ሲኾን ፡ በአልፍ ፡ አ ፡ እንጂ ÷ በዐይን ፡ አይጣፍም ፤ በዐይኑ ፡ ዐ ፡ ሲጣፍ ፡ ትርጓሜው ፡ ሌላ ፡ ነው ፤ ግእዘንና ፡ ግዕዘን ፡ ተመልከት ። ከኼታችን ፡ ልደት ፡ በፊት ፡ በዘመነ ፡ ብሉይ ፡ ኋላም ፡ በዘመነ ፡ ሐዲስ ፡ እስከ ፡ አብርሀ ፡ ወአጽብሐ ፡ ዘመን ፡ ድረስ ፡ ካዕብ ÷ ሣልስ ÷ ራብዕ ÷ ኃምስ ÷ ሳድስ ÷ ሳብዕ ፡ ሳይኖር ፡ በግእዙ ፡ ብቻ ፡ ይጥፉበትና ፡ ያነቡበት ፡ ይናገሩበት ፡ ነበረና ፤ ግእዝ ፡ የተባለ ፡ ስለዚህ ፡ ነው ።

፮ ፤ ይኸውም ፡ ሊታወቅ ፡ በጥንታዊ ፡ ፊደል ፡ ተጥፎ ፡ ከአኵስም ፡ ሐውልት ፡ የተገኘ ፡ ጥንታዊው ፡ የግእዝ ፡ ንባብ ፡ እንዲህ ፡ ይላል ።

«ዘ ፡ ሐወለተ ፡ ዘአገበረ ፡ አገዘ ፡ ለአበወሀ ፡ ወሰሐበ ፡ መሐዘተ ፡ አወየ ፡ ለነ ፡ ፀበለነ ፡ ወሐለፈነ ፡ ወመጸ ፡ ነገሠ ፡ ወፈተወ ፡ የነገሠነ ፡ አነዘ ፡ ሀለከ ፡ በአከሰመ ፡ ዘከመ ፡ ገአዘ ፡ አበወሀ ፡ በነደየ ፡ ፀወወነ ፡ ፀወ ፡ መፀ ፡ አከሰመ ፡ ወፀአየ ፡ ዘአደወየ ፡ ወወከሐ ፡ ዘመጸአ ፡ አመ ፡ ቀደመ ፡ የተከፀወ ፡ ደመ ፡ ቀነየከ ፡ ነገሠ ፡ አከሰመ ፡ ወፈነወከወ ፡ የነጸረ ፡ አከሰመ ፡ በሐረ ፡ መነገሠተየ» ይህን ፡ የመሰለ ፡ ብዙ ፡ ንባብ ፡ አለ ፤ መልክአ ፡ ፊደሉም ፡ እንደ ፡ ሰው ፡ መልክ ፡ ብዙ ፡ ጊዜ ፡ በየዘመኑ ፡ ተለዋውጧል ። ከፊተኞች ፡ ይልቅ ፡ የኋለኞች ፡ አሻሽለውታል ፤ አሠራረሩንም ፡ ከሰማርያና ፡ ከፊንቂ ፡ አመሳስለውታል ፤ ካህኑ ፡ ዕዝራ ፡ ዕብራይስጥን ፡ ከአሶር ፡ ፊደል ፡ እንዳመሳሰለ ።

ስለ ፡ ፊደላት ፡ ፯ ፡ ፯ነት ።

፯ ፤ ቋንቋነቱና ፡ ፊደሉም ፡ ያረጀ ፡ ያፈጀ ፡ ግእዝ ፡ ብቻ ፡ ኹኖ ፡ ለሐዲሱ ፡ ዘመን ፡ አነጋገር ፡ ንባብ ፡ የሚያከፋ ፡ ምስጢር ፡ የሚያጠፋ ÷ አፍ ፡ የሚያስከፍት ፡ ነገር ፡ የሚያስጐትት ፡ ስለ ፡ ኾነ ÷ ከሣቴ ፡ ብርሃን ፡ ሰላማ ፡ በዘመነ ፡ ሐዲስ ፡ መጻሕፍትን ፡ ከጽርእ ፡ ወደ ፡ ግእዝ ፡ ሲመልስና ፡ ሲያስመልስ ፡ በግእዝ ፡ ቃል ፡ ብቻ ፡ ለመተርጐም ፡ አልመችኽ ፡ ቢለው ÷ ያይሁዶችንና ፡ ያረቦችን ፡ የጽርኣችን ፡ ፊደል ፡ እንደ ፡ ቋንቋው ፡ ሥርዐት ፡ ድምጥ ፡ እየለወጠ ፡ በሚያስኬድ ፡ በነቍጣና ፡ በዋየል ፡ ፈንታ ፡ ከካዕብ ፡ እስከ ፡ ሳብዕ ፡ ድረስ ፡ ያሉትን ፡ ስድስቱን ፡ አዕጹቅ ፡ አግብቶ ÷ በጽርእ ፡ ቋንቋ ፡ ሽ ፡ የሚሉ ፡ ፊደል ፡ ስለ ፡ ሌለ ፡ ሽን ፡ ሠ ፡ ብሎ ፡ ከሽነቱ ፡ አውጥቶ ÷ በንባቡና ፡ በገባቡ ፡ ከጽርእ ፡ ፊደል ፡ አሰማምቶ ፡ እንደ ፡ ዕብራይስጥ ፡ ዐድሶታል ፤ ለብሉይና ፡ ለሐዲስ ፡ የበቃና ፡ የተቀደሰ ፡ ብርሃን ፡ የለበሰ ፡ ከዚያ ፡ ወዲህ ፡ ነው ።

፰ ፤ ይኸውም ፡ ሊታወቅ ፡ ከጥንት ፡ ከአበው ፡ የተገኘ ፡ ከውሉድም ፡ የተሰናኘ ፡ ትርጓሜ ፡ ፊደል ÷ ያባ ፡ ሰላማን ፡ ትጋትና ፡ ሥራ ፡ ሲተርክ ፤ ወአምጽአ ፡ ለነ ፡ ሰላማ ፡ ጳጳስ ፡ ፊደለ ፡ እምሕርክትያኑስ ፤ ወሚጠሙ ፡ በአዱ ፡ ልሳን ÷ ወእሙንቱ ፡ ሰብዐቱ ፡ ፊደላት ፡ ብሎ ፡ ይመሰክራል ። ሰባት ፡ ማለቱ ፡ ከግእዝ ፡ ጋራ ፡ ነው ፤ ከሰባቱ ፡ ደግሞ ፡ ስድስቱ ÷ ከነዚያውም ፡ ፩ ፡ ፩ቱ ፡ ግእዝና ፡ ሳድስ ÷ ካዕብና ፡ ሳብዕ ÷ ሣልስና ፡ ኃምስ ፡ ሱቱፋን ፡ ናቸው ፤ ይወራረሳሉ ። ይኸውም ፡ በገቢር ፡ አንቀጽ ÷ ሞአ ፡ ፀረ ፡ ወጸላኤ ÷ ሐነጸ ፡ ቤቶ ፡ ወጽርሐ ፡ ያለውን ፡ በተገብሮ ÷ ተሞአ ፡ ፀር ፡ ወጸላኢ ÷ ተሐንጸ ፡ ቤቱ ፡

ወጽርሐ ፡ እያለ ፡ መኼዱን ፡ መናገር ፡ ነው ። ራብዕ ፡ ግን ፡ ኃምስና ፡ ሳብዕ ፡ ሳይቀሩ ፡ ከኹሉም ፡ ተፈቃቃሪ ፡ ነው ፥ መልኩንና ፡ ድምፁን ፡ ሳይለውጥ ፡ ኹሉን ፡ ይከታል ፤ ይህም ፡ በልዐ ፡ ሥጋ ፡ ወመና ፥ ተበልዐ ፡ ሥጋ ፡ ወመና ፡ ማለቱን ፡ ያሳያል ። ኃምስ ፡ ሳብዕ ፡ ደግሞ ፡ እንደ ፡ ራብዕ ፡ ናቸው ፤ ቀሠመ ፡ ጾጌ ፡ ወፍሬ ፥ ተቀሥመ ፡ ጾጌ ፡ ወፍሬ ፡ አኀዘ ፡ ዖርሆ ፡ ወአንቆቅሖ ፥ ተእኀዘ ፡ ዖርሆ ፡ ወአንቆቅሖ ፡ እያሰኙ ፡ ገቢር ፡ ተገብሮ ፡ ይከታሉ ። ፯ ፡ ያልናቸው ፡ ፫ቱ ፡ መዋርስቶች ፡ በይንና ፡ በዠሮ ፡ በፍንጫ ፡ ይመሰላሉ ፤ ራብዕ ፡ በአፍ ፡ ይመሰላል ። ባለቅዳሴዎች ፡ ግን ፡ ሰባቱን ፡ ኹሉ ፡ በሰባቱ ፡ ዕለታትና ፡ በሰባቱ ፡ ሀብታት ፥ በሰባቱ ፡ ምስጢራት ፡ ይመስሏቸዋል ።

፱ ፤ ሕርከትያኑስ ፡ የዐረብ ፡ ቃል ፡ ነው ፥ ጫፉ ፡ የጽርእ ፡ ይመስላል ፤ ዐረብ ፡ ግን ፡ ሐረከ ፡ ብሎ ፡ አማሰለ ፡ ይላልና ፥ ሕርከት ፡ ከዚህ ፡ ይወጣል ፤ የፊደልን ፡ ድምጥ ፡ የሚለዋውጡ ፡ ነቍጣትንም ፡ መወልጣን ፡ ሲል ፡ እልሐረካት ፡ ይላል ። ትርጓሜውም ፥ የተማሰለ ፡ ፩ ፡ ወገን ፡ እንዲኾን ፡ እንዲቀላቀል ፤ ነቍጣው ፡ ወይም ፡ ዋየሉ ፡ ከፊደሉ ፡ ጋራ ፡ ፩ ፡ የኾነ ፡ የተቀላቀለ ፡ ማለት ፡ ነው ። ዋየል ፡ ነቍጣ ፡ የሚባል ፡ ቅጥሉ ፡ ነው ፤ ቅጥልም ፡ ባይኖረው ፡ ሰባሩና ፡ ዐንካሳ ፡ መኾኑ ፡ ራሱን ፡ ማጽነኑ ፡ እንደ ፡ ቅጥል ፡ ኹኖ ፡ ዋየል ፡ ይባላል ፤ ወይም ፡ እንደ ፡ ነቍጣ ፡ ይታሰባል ። ዋየል ፡ የላቲን ፡ ቃል ፡ ነው ፤ መላው ፡ የአ ፡ ቤት ፡ ፊደል ፡ ፯ቱ ፡ ዐይነት ፡ ኹሉ ፡ በሮማይስጥ ፡ ዋየል ፡ ይባላል ፤ ድምፅ ፡ ወይም ፡ ጕህና ፡ ማለት ፡ ነው ፥ መወልጠ ፡ ድምፅም ፡ ይሉታል ፤ ድምፅ ፡ ለራሱ ፡ መወልጥ ፡ ለሌላው ። እኛ ፡ በሰዋስው ፡ ግእዝ ፡ ዐመል ፡ ደጊመ ፡ ቃል ፡ የምንላቸውን ፡ እነዚህን ፡ ሦስቱን ፡ ኤውሮፖች ፡ ኮንሶን ፡ ዋየል ፡ ዱብል ፡ ይሏቸዋል ። አሊሁም ፡ ከነሰ ፡ ወየለ ፡ ደበለ ፡ ከማለት ፡ ጋራ ፡ ፩ ፡ ናቸው ፥ በንባብ ፡ በምስጢር ፡ ይገጥማሉ ፤ እንዲያውም ፡ በጯራሽ ፡ ከነዚህ ፡ የወጡ ፡ ይመስላሉ ። በግእዝና ፡ በማርኛም ፡ በሌላ ውም ፡ በሴም ፡ ቋንቋ ፡ ኹሉ ፡ በዐረብ ፡ በሱርስት ፡ በዕብራይስጥ ፥ አና ፡ ሀ ፡ ወና ፡ የ ፡ አሊህ ፡ ፬ቱ ፡ እንደ ፡ ዋየል ፡ ናቸው ፤ ለራሳቸው ፡ ድምፅ ፡ እየኾኑ ፡ የሌሎቹን ፡ ድምፅ ፡ ይለዋውጣሉ ። አለዋወጣቸው ፡ እንዴት ፡ እንደ ፡ ኾነ ፡ ድምጣቸውንና ፡ ድምጥነታቸውን ፡ በግስ ፡ ዐመል ፡ ፍች ፡ ተመልከት ።

አዕጹቅ ፡ ያልናቸው ፡ የ፮ቱ ፡ ፊደላት ፡ ጠባይ ።

፲ ፤ በካዕብ ፡ በሳብዕ ፡ ወ ፥ በሣልስ ፡ በኃምስ ፡ የ ፥ በራብዕ ፡ በሳድስ ፡ አና ፡ ሀ ፡ አሉ ። የወ ፡ ጠባይ ፡ ራሱን ፡ ጐርዶ ፡ ሌላውን ፡ ፊደል ፡ ካዕብና ፡ ሳብዕ ፡ ማድረግ ፡ ነውና ፤ የካዕብ ፡ የሳብዕ ፡ ቅጥይ ፡ ዐንካስነት ፡ ህየንተ ፡ ወ ፡ ኹኖ ፡ በወ ፡ ፈንታ ፡ ገብቷል ። የየ ፡ ጠባይ ፡ ደግሞ ፡ እንደ ፡ ወ ፡ ራሱን ፡ ጐርዶ ፡ ሌላውን ፡ ፊደል ፡ ሣልስና ፡ ኃምስ ፡ ማድረግ ፡ ነውና ፤ የሣልስ ፡ የኃምስ ፡ ቅጥይ ፡ ኹሉ ፡ ህየንተ ፡ የ ፡ ኹኖ ፡ በየ ፡ ፈንታ ፡ ገብቷል ። የአና ፡ የሀም ፡ ጠባይ ፡ እንደ ፡ ወና ፡ እንደ ፡ የ ፡ ራስን ፡ ጐርዶ ፡ ወይም ፡ ሳይጐርዱ ፡ ሌላውን ፡ ፊደል ፡ ራብዕ ፡ ሳድስ ፡ ማድረግ ፡ ነውና ፤ የራብዕና ፡ የሳድስ ፡ ቅጥይ ፡ ሰባርነትና ፡ ዐንካስነት ፡ ስለ ፡ አ ፡ ስለ ፡ ሀ ፡ የገባ ፡ ነው ፤ እንደ ፡ አና ፡ እንደ ፡ ሀ ፡ ይታሰባል ፤ አና ፡ ሀ ፡ ጠባያቸው ፡ ፩ ፡ ስለ ፡ ኾነ ፡ ፪ቱ ፡ ስላንድ ፡ ይቈጠራሉ ።

ለዜማ ፡ ምልክት ፡ ሥረይ ፡ እንዳለው ፥ ለፊደልም ፡ ድምፅ ፡ ለጠበዩና ፡ ለቅጥዩ ፡ ሥረ
ዩቹ ፡ ዉ.ዎ ፡ ዩ.ዮ ፥ ኣ—ሀ ፡ ናቸው ፤ ቅጥይ ፡ ኹሉ ፡ ባለቤት ፡ አከል ፡ ነውና ፤ ጉንደ ፡
ፊደሉን ፡ ነዉ ፡ ነዎ ፡ ነዩ ፡ ነዮ ፡ ነኣ ፡ ነሀ ፡ በማለት ፡ ፈንቃ ፥ ኑ ፡ ኖ ፡ ኒ ፡ ኔ ፡ ና ፡ ን ፡ እያ
ሰኘ ፡ በ፯ ፡ ስልት ፡ ማስኬዱ ፡ የነዚህ ፡ ምልክት ፡ ስለ ፡ ኾነ ፡ ነው ። የርሳቸውም ፡ ቅጥይ ፡
ምልክትነቱ ፡ ሥረይ ፡ እንደ ፡ ማለት ፡ ነው ፤ የድምጣቸውን ፡ ስልት ፡ ልዩ ፡ ልዩነቱን ፡
እያገላ ፡ እያጋነነ ፡ ያሳያል ። እንደ ፡ ኤውሮፖችም ፡ ብዙውን ፡ ፊደል ፡ ጠቅልሎ ፡ አሳ
ንሶ ፡ በእጅ ፡ መኪና ፡ ለመጣፍ ፤ ግእዞችን ፡ ብቻ ፡ በኡ—ቡ ፥ በኢ—ቢ ፥ በኣ—ባ ፥
በኤ—ቤ ፥ በእ—ብ ፥ በኦ—ቦ ፡ እያሉ ፡ በአ ፡ ብቻ ፡ ማስኬድ ፡ ይቻላል ፤ ይህነንም ፡ ኋላ ፡
በ፯ኛው ፡ ማዕርገ ፡ ፊደል ፡ እናመጣዋለን ።

፲፩ ፤ ዳግመኛም ፡ ያራቱ ፡ ዲቃሎች ፡ የነገ•ነ•ኬ•ቄ ፡ ቅጥይ ፡ ከግእዛቸው ፡ በቀር ፡
ኹሉም ፡ መንቃ ፡ መንቃ ፡ ዐይነት ፡ መኾኑ ፥ ዋየሎቻቸው ፡ ፪ ፡ ፪ ፡ ስለ ፡ ኾነ ፡ ነው ፤
የግእዛቸው ፡ ቅጥል ፡ ግን ፡ እንደነሆሎፎ ፡ እንደነሮቆቶ ፡ መኾኑ ፥ ፩ ፡ ዋየል ፡ ብቻ ፡
ወን ፡ ያሳያል ፤ ቀለበቱ ፡ ሀየንተ ፡ ወ ፡ ነው ። ይህም ፡ ገወ—ጎ ፥ ገወዩ—ጉ ፥ ገውዋ—ጓ ፥
ገወዮ—ጔ ፥ ገወሀ—ጕ ፥ እያለ ፡ ኹሉን ፡ ያሳያል ። ከዕብና ፡ ሱበዕ ፡ መተዋቸው ፡ የከዕ
ቡን ፡ ድምጥ ፡ ሣልሳቸውና ፡ ሳድሳቸው ፡ ጐ ፡ ጕ ፥ የሳብዑን ፡ ድምጥ ፡ ግእዛቸው ፡
ጎ ፡ ደርበ ፡ ስለ ፡ ወረሰው ፡ ነው ። ሳድሳቸው ፡ የካዕብ ፡ ድምጥ ፡ ስለ ፡ ደረበ ፡ ከኹን ፡
ቀደም ፡ ጎ ፡ ጕ ፥ ኈ ፡ ኍ ፥ ኰ ፡ ኵ ፥ ቈ ፡ ቍ ፡ እያለ ፡ በቃውን ፡ ትቶ ፡ አለበቃው ፡ ገብቶ ፡
በካዕብ ፡ በቃ ፡ ይጣፍ ፡ ነበር ፤ ዛሬ ፡ ግን ፡ ከበቃው ፡ ገብቶ ፡ መጨረሻ ፡ ኹኗል ። ሳድስ
ነቱም ፡ ጕሕቈ ፡ ኵሕሰ ፡ በለው ፡ ይታወቃል ፤ ግስ ፡ በካዕብ ፡ በሣልስ ፡ አይነሣምና ።
ግእዛቸው ፡ በቅኔና ፡ በመልክ ፡ ከግእዝ ፡ ጋራ ፡ እንዲገባ ፡ ሳድሳቸውም ፥ ሰርጕ ፡ እኍ ፡
ጽኵ ፡ ጽጕ ፡ ኍልቍ ፡ እያለ ፡ ከሳድስ ፡ ጋራ ፡ ይገባል ፤ ከካዕብ ፡ ግን ፡ አይተባበርም ፤
ቤት ፡ ያፈርሳል ።

፲፪ ፤ ከናባ ፡ ሰላማም ፡ በኋላ ፡ እስከናጫ ፡ ካሌብ ፥ ከዚያም ፡ በኋላ ፡ እስከ ፡ ብዙ ፡
ዘመን ፡ ሕዝቡ ፡ ሰራዊቱ ፡ ይህን ፡ ሐዲስ ፡ ግእዝ ፡ አንለምድኽ ፡ ብለው ፡ እንደ ፡ ካህ
ናቱ ፡ ታዜና ፡ ወልደ ፡ አልዐሜዳ ፡ ካሌብ ፡ በማለት ፡ ፈንቃ ፥ ተዘካ ፡ ወለደ ፡ አለፀመደ ፡
ከለበ ፡ እያሉ ፡ በዚያው ፡ ባሮጌው ፡ ግእዝ ፡ ሲጥፉ ፡ እንደ ፡ ኖሩ ፥ ባኵስምና ፡ በሽማ
ዛና ፡ በደንጊያ ፡ ተጥፎ ፡ የሚገኝ ፡ ጥንተ ፡ ጥፈታቸው ፡ ይመሰክራል ።

ፍናወ ፡ ፊደል ፡ ወሑረታቲሁ ።

፲፫ ፤ የጥንቱ ፡ ግእዝ ፡ ፍጹም ፡ የሴም ፡ ቋንቋ ፡ ስለ ፡ ኾነ ፡ አካኼዱና ፡ መንገዱ ፡
እንደ ፡ ወንድሞቹ ፡ እንዳረብና ፡ እንደ ፡ ሱርስት ፡ እንደ ፡ ዕብራይስጥ ፡ ከቀኝ ፡ ወደ ፡
ግራ ፡ ነበረ ፤ ይህነንም ፡ በየመን ፡ ያሉ ፡ ሕምያር ፡ ነገደ ፡ ዮቅጣን ፥ ዕብራውያንም ፡
ሳይቀሩ ፡ በቃል ፡ በታሪክ ፡ ይመሰክራሉ ። ፪ኛም ፡ ፊደሉና ፡ ቋንቋው ፡ ቅን ፡ ስለ ፡ ኾነ ፡
እንደርሻ ፡ አካኼድ ፡ ከቀኝ ፡ ወደ ፡ ግራ ፡ ከግራ ፡ ወደ ፡ ቀኝ ፡ በ፪ ፡ ወገን ፡ ይጣፍና ፡
ይነበብ ፡ ነበረ ፡ ይባላል ። ይህነንም ፡ እኔ ፡ ከቃላቸው ፡ እንደ ፡ ሰማኹ ፥ በትግሬ ፡
መሬት ፡ ከዚያውም ፡ ባጋሜ ፡ ወረዳ ፡ ከዋሻ ፡ ውስጥ ፡ በደንጊያ ፡ ተጥፎ ፡ ያዩትና ፡

ያገኙት ፡ አሉ ። ኋላ ፡ ግን ፡ በሰላማ ፡ ጊዜ ፡ በአብርሀና ፡ በአጽብሐ ፡ ዘመን ፥ የያፌት ፡ ልጆች ፡ ጽርአውያን ፥ የካም ፡ ልጆች ፡ ግብጻውያን ፡ ከያፌት ፡ ቋንቋ ፡ ሊያሰማሙ ፡ በጭራሽ ፡ ከግራ ፡ ወደ ፡ ቀኝ ፡ አዙረውት ፡ ከሴም ፡ ቋንቋ ፡ መንገድ ፡ ወጥቷል ። ከዚያ ፡ ወዲህ ፡ በጕረሮ ፡ የሚነገረው ፡ ቃል ፡ የሐውት ፡ ሐና ፡ የዐይኑ ፡ ዐ ፡ ድምጥ ፡ እየደከመና ፡ እያነሰ ፡ እየጠፋ ፡ ኼደ ። ትግሮች ፡ ግን ፡ እስከ ፡ ዛሬ ፡ ድረስ ፡ ከቋንቋቸው ፡ አላጠፉትም ፤ እንዳይሁድና ፡ እንዓረቦች ፡ ለይተው ፡ ጠንቅቀው ፡ ይናገሩታል ።

፲፬ ፤ ፊደሉ ፡ ግእዝ ፡ ብቻ ፡ ኹኖ ፡ ከቀኝ ፡ ወደ ፡ ግራ ፡ መኼዱም ፡ በዚህ ፡ ይታወቃል ፤ በጥንታዊ ፡ ፊደል ፡ ተጥፎ ፡ ከአኩስም ፡ የተገኘው ፡ አንቀጽ ፡ እንሆ ፡ እንዲህ ፡ ይላል ።

| የማናይ ። | ፀጋማይ ። |
|---|---|
| መሐጸበወ | ወበጺሐሙ ፡ |
| መረሐበ | ብሒሮሙ ፡ |
| መሰለፈአ | አፍለሰሙ ፡ |
| መሀሰሰነአ | እንስሳሆሙ ፡ |
| ረበከየ | ይክበር ፥ ማለት ፡ ነው ፡ ብለው ፡ ቃል ፡ |

በቃል ፡ ተርጕመውታል ። አኩስሞች ፡ ግን ፡ ከቀኝ ፡ ወደ ፡ ግራ ፡ ስለ ፡ ተጣፈ ፡ ዕብራይስጥ ፡ ይሉታል ። (ተረት) አባቱን ፡ አያውቅ ፡ አያቱን ፡ ናፈቅ ፡ እንዲሉ ። ወዲያ ፡ ማዶም ፡ በየመንና ፡ በናግራን ፡ እንደዚህ ፡ ያለ ፡ ይህን ፡ የመሰለ ፡ አንቀጽ ፡ ጥፈት ፡ በየዋሻውና ፡ በየደንጊያው ፡ በየመቃብሩ ፡ ይገኛል ፤ የብራናም ፡ መጽሐፍ ፡ አይታጣ ፤ ሕምያሮች ፡ ግን ፡ ግእዝ ፡ ቋንቋቸውን ፡ አጥፍተው ፡ እንደ ፡ ግብጦች ፡ ዐረቦች ፡ ኹነዋል ።

## ፍልሰተ ፡ ፊደላት ፡ ወአኃዛቲሆን ።

፲፭ ፤ የፊደል ፡ ተራ ፡ የተፋለሰና ፡ አልፍ ፡ አ ፡ ከርስቱ ፡ ከቀዳማዊነት ፡ ተነቅሎ ፡ በርሱ ፡ ፈንታ ፡ ሆይ ፡ ሀ ፡ መዠመሪያ ፡ ፊደል ፡ የኾነ ፡ ከፍሬ ፡ ምናጦስ ፡ ወዲህ ፡ ነው ፤ አበገደህ ፡ የነበረውን ፡ ሀለሐመሠ ፡ ብለው ፡ ከላይ ፡ እስከ ፡ ታች ፡ ያፋለሱትም ፡ ከርሱ ፡ ጋራ ፡ ዐብረው ፡ የነበሩ ፡ ጽርአውያንና ፡ ቅብጣውያን ፡ ናቸው ፡ ይባላል ። ያፋለሱበትም ፡ ምክንያት ፡ የግእዝን ፡ ፊደል ፡ ከአኃዝነት ፡ አውጥቶ ፡ የርሳቸውን ፡ ፊደል ፡ አልፋ ፡ ቤታ ፡ ጋማ ፡ የነበረውን ፡ ፩ ፡ ፪ ፡ ፫ ፡ እያሉ ፡ በግእዝ ፡ ፊደል ፡ ላይ ፡ አኃዝ ፡ አድርጎ ፡ ለማግባት ፡ እንዲመቻቸው ፡ ነው ፤ አኃዛችን ፡ ኹሉ ፡ የጽርእና ፡ የቅብጥ ፡ ፊደል ፡ መኾኑን ፡ ኋላ ፡ በበታው ፡ እናመጣዋለን ። ይህም ፡ ሥራ ፡ የግእዝን ፡ ፊደል ፡ ከሴም ፡ ቋንቋ ፡ ዐዋጅ ፡ አውጥቶ ፡ ጥርጊያ ፡ መንገዱን ፡ አጥፍቶ ፡ ቍጥሩን ፡ አሳስቶ ፡ በዚህ ፡ ብቻ ፡ የቀረ ፡ አይዶለም ፤ በሄኖስ ፡ ራእይ ፡ ተመሥርቶ ፡ የታነጸውን ፡ ያልፋ ፡ ወያን ፡ ምስጢር ፡ አፍርሷል ።

፲፮ ፤ ከዚያ ፡ ወዲህ ፡ በኢትዮጵያ ፡ አበገደ ፡ እየተረሳና ፡ እየጠፋ ፥ ሀለሐመ ፡ እየሰፋ ፡ ኼደ ፤ ኋላ ፡ ግን ፡ በኹሉ ፡ አገር ፡ ጠፍቶ ፡ በሺዋ ፡ በስሜን ፡ ስለ ፡ ተገኘ ፡ እኩሉ ፡ የሺዎች ፡ ፊደል ፥ እኩሉ ፡ የስሜኖች ፡ ፊደል ፡ ይሉታል ፤ ርሱ ፡ ግን ፡ ከጥ

ንት ፡ ከሰላማ ፡ በፊት ፡ የነበረ ፡ አንቲካ ፡ ፊደል ፡ ነው ። አንቲካነቱንም ፡ ዐረቦች ፡ ሳይ ቀሩ ፡ ሴማውያንም ፡ ያፌታውያንም ፡ በፊደል ፡ ታሪክ ፡ ይመሰክራሉ ፤ በሀገራችንም ፡ ባሎስም ፡ ሐውልት ፡ በስሜን ፡ መጻሕፍት ÷ በሺዋም ፡ በያድባራቱ ፡ በየገዳማቱ ÷ ይል ቁንም ፡ በደብረ ፡ ሊባኖስ ፡ እስከ ፡ ዛሬ ፡ አለ ፤ ያስተምሩበታል ። ስሙንም ፡ ከሀለሐመ ፡ ለይተው ፡ በዚያው ፡ በጥንቱ ፡ አጠራር ፡ አበገደ ፡ ወይም ፡ አቡጊዳ ፡ ይሉታል ፤ አቡጊ ዳም ፡ ማለት ፡ የግእዙ ፡ ተራ ፡ ሳይፋለስ ፡ ከካዕብ ፡ እስከ ፡ ሳብዕ ፡ ያሉት ፡ ፮ቱ ፡ አዕጹቅ ፡ በመፋለስና ፡ በመዋረስ ፡ እየተዛነቁ ፡ ይጣፋሉና ÷ ስለዚህ ፡ ነው ፤ መዛነቃቸውም ፡ ውጥ ንቅጥ ፡ ኹኖ ፡ የሕዝቅኤልን ፡ ምግብ ፡ ይመስላል ፡ (ሕዝ፬ ፡ ፱) ።

## ማዕርገ ፡ ፊደላት ።

፳፪ ፤ የፊደላት ፡ ማዕርግ ፡ ባጣጣፍና ፡ በትምርት ፡ ከ፫ ፡ ይከፈላል ፤ ፫ቱ ፡ ክፍል ፡ የግእዝ ፡ ብቻ ፤ ፩ኛው ፡ ያማርኛ ፡ ብቻ ፤ ፫ኛው ፡ የግእዝና ፡ ያማርኛ ፡ መድበል ÷ ጉ ባኤ ፡ ፊደል ፡ ነው ። የግእዙ ፡ ማዕርግ ፡ ከ፫ ፡ መክፈሉ ÷ የወጣኒና ፡ የማእከላዊ ፡ የፍ ጹም ፡ ትምርት ፡ መኾኑን ፡ ያሳያል ፤ ያማርኛውና ፡ መድበሉም ፡ ከ፫ቱ ፡ የሚበልጥ ፡ የፍጹም ፡ ፍጹም ፡ ነው ።

## ፩ኛ ፡ ማዕርግ ።

| ፳፪ ፤ ፊደል ። | ስመ ፡ ፊደል ። | ኍልቈ ፡ ፊደል ። |
|---|---|---|
| አ | አልፍ ፡ | አሐድ ፡ |
| በ (ጰ) | ቤት ፡ | ክልኤት ፡ |
| ገ (ጐ) | ገምል ፡ | ሠለስት ፡ |
| ደ | ድልት ፡ | አርባዕት ፡ |
| ሀ | ሆይ ፡ | ኀምስት ፡ |
| ወ | ዋዌ ፡ | ሰድስት ፡ |
| ዘ | ዛይ ፡ | ሰብዐት ፡ |
| ሐ (ኀ—ኈ) | ሐውት ፡ | ሰምንት ፡ |
| ጠ | ጠይት ፡ | ተስዐት ፡ |
| የ | የማን ፡ | ዐሥርት ፡ |
| ከ (ኰ) | ካፍ ፡ | ዕሥራ ፡ |
| ለ | ላዊ ፡ | ሠላሳ ፡ |
| መ | ማይ ፡ | አርብዓ ፡ |
| ነ | ነሐስ ፡ | ኀምሳ ፡ |
| ሠ | ሠውት ፡ | ስሳ ፡ |
| ዐ | ዐይን ፡ | ሰብዓ ፡ |
| ፈ (ፐ) | ፈፍ ፡ | ሰማንያ ፡ |
| ጸ (ፀ) | ጸደይ ፡ | ተስዓ ፡ |

| | | |
|---|---|---|
| ቀ (ቈ) | ቆፍ ፡ | ምእት ፡ |
| ረ | ርእስ ፡ | በ ፡ ምእት ፡ |
| ሰ | ሳት ፡ (ሰዓት) ፡ | ገ ፡ ምእት ፡ |
| ተ | ታው ፡ | ደ ፡ ምእት ። |

## ሐተታ ።

፲፱ ፤ እሊህም ፡ ፳፪ቱ ፡ ፊደላት ፡ የመልክ ፡ ልዩነት ፡ ያላቸው ፡ ፬ቱ ፡ ድርቦች ፡ (ኀፀጸፐ) ፡ ሳይቀሩ ፡ በ፭ ፡ ጸታ ፡ ተከፍለው ፡ በ፭ቱ ፡ ሕዋሳተ ፡ አፍ ፡ በጕረሮና ፡ በትናጋ ፡ በምላስና ፡ በከንፈር ፡ በጥርስ ፡ ይነገራሉ ፤ ጸታቸውና ፡ ክፍላቸውም ፡ ይህ ፡ ነው ።

፩ኛ ፤ — በጕረሮ ፡ የሚነገሩ ፡ ፭ ፤ — አ ፡ ሀ ፡ ሐ ፡ ኀ ፡ ዐ ።
(እነዚህ ፡ ፭ቱ ፡ ከመላላት ፡ በቀር ፡ መጥበቅ ፡ የላቸውም) ።
፪ኛ ፤ — በትናጋ ፡ የሚነገሩ ፡ ፬ ፤ — ገ ፡ የ ፡ ከ ፡ ቀ ።
፫ኛ ፤ — በምላስ ፡ የሚነገሩ ፡ ፭ ፤ — ደ ፡ ጠ ፡ ለ ፡ ነ ፡ ተ ።
፬ኛ ፤ — በከንፈር ፡ የሚነገሩ ፡ ፮ ፤ — በ ፡ ወ ፡ መ ፡ ፈ ፡ ጰ ፡ ፐ ።
፭ኛ ፤ — በጥርስ ፡ የሚነገሩ ፡ ፮ ፤ — ዘ ፡ ሠ ፡ ጸ ፡ ፀ ፡ ረ ፡ ሰ ።

## ፪ኛ ፡ ማዕርግ ።

፳ ፤ መላው ፡ የግእዝ ፡ ፊደል ፡ ከናበጋዙና ፡ ከነጓዙ ፡ ከነአኃዙ ።

| | | | | | | | |
|---|---|---|---|---|---|---|---|
| አ | ኡ | ኢ | ኣ | ኤ | እ | ኦ | ፩ |
| በ | ቡ | ቢ | ባ | ቤ | ብ | ቦ | ፪ |
| ገ ጐ | ጉ | ጊ ጒ | ጋ ጓ | ጌ ጔ | ግ ጕ | ጎ | ፫ |
| ደ | ዱ | ዲ | ዳ | ዴ | ድ | ዶ | ፬ |
| ሀ | ሁ | ሂ | ሃ | ሄ | ህ | ሆ | ፭ |
| ወ | ዉ | ዊ | ዋ | ዌ | ው | ዎ | ፮ |
| ዘ | ዙ | ዚ | ዛ | ዜ | ዝ | ዞ | ፯ |
| ሐ | ሑ | ሒ | ሓ | ሔ | ሕ | ሖ | ፰ |
| ኀ ኈ | ኁ | ኂ ኊ | ኃ ኋ | ኄ ኌ | ኅ ኍ | ኆ | ፱ |
| ጠ | ጡ | ጢ | ጣ | ጤ | ጥ | ጦ | ፲ |
| የ | ዩ | ዪ | ያ | ዬ | ይ | ዮ | ፳ |
| ከ ኰ | ኩ | ኪ ኲ | ካ ኳ | ኬ ኴ | ክ ኵ | ኮ | ፴ |
| ለ | ሉ | ሊ | ላ | ሌ | ል | ሎ | ፵ |
| መ | ሙ | ሚ | ማ | ሜ | ም | ሞ | ፶ |
| ነ | ኑ | ኒ | ና | ኔ | ን | ኖ | ፷ |
| ሠ | ሡ | ሢ | ሣ | ሤ | ሥ | ሦ | ፸ |
| ዐ | ዑ | ዒ | ዓ | ዔ | ዕ | ዖ | ፹ |

| | | | | | | | |
|---|---|---|---|---|---|---|---|
| ፈ | ፉ | ፊ | ፋ | ፌ | ፍ | ፎ | ፺ |
| ጸ | ጹ | ጺ | ጻ | ጼ | ጽ | ጾ | ፻ |
| ፀ | ፁ | ፂ | ፃ | ፄ | ፅ | ፆ | ፪፻ |
| ቀ ቈ | ቁ | ቂ ቍ | ቃ | ቄ ቋ | ቅ ቍ | ቆ | ፫፻ |
| ረ | ሩ | ሪ | ራ | ሬ | ር | ሮ | ፬፻ |
| ሰ | ሱ | ሲ | ሳ | ሴ | ስ | ሶ | ፭፻ |
| ተ | ቱ | ቲ | ታ | ቴ | ት | ቶ | ፮፻ |
| ጰ | ጱ | ጲ | ጳ | ጴ | ጵ | ጶ | ፯፻ |
| ፐ | ፑ | ፒ | ፓ | ፔ | ፕ | ፖ | ፰፻ |

## ፫ኛ ፡ ማዕርግ ፤ አቡጊዳ ።

፳፩ ፤ አቡጊዳሰ ፡ ውእቱ ፡ ኅዉሥ ፡ ዘርዕ ፡ ወሥርጽ ፤ ወቱሱሐ ፡ መልክእ ፡ ሐንፈጽ ። ሑረቱ ፡ አምሳለ ፡ ፍርዝ ፡ እንዘ ፡ በየማኑ ፡ ወበፀጋሙ ፡ አኃዝ ፤ ወፍናዊሁኒ ፡ መብእስ ፡ ወደጋን ፥ አዕቃጼ ፡ ረዋጺ ፡ ሕፃን ።   የፊደሉና ፡ የአኃዙ ፡ ተራ ፡ ከታው ፡ በታች ፡ ፬ቱን ፡ ድርቦች ፡ ኀፀጸፐንና ፡ ፪ቱን ፡ ዲቃሎች ፡ ኈቈን ፡ ጨምሮ ፡ እስከ፲፻ ፡ ይወርድና ፡ ፻ ፡ ለማለት ፡ የአልፍ ፡ አን ፡ ሳድስ ፡ እን ፡ ይጥፋል ፤ አጣጣፉም ፡ ይህ ፡ ነው ።

| | | | | | | | | |
|---|---|---|---|---|---|---|---|---|
| ፩ | አ | ቡ | ጊ | ዳ | ሄ | ው | ዘ | ፯ |
| ፪ | በ | ጉ | ዲ | ሃ | ዌ | ዝ | ሐ | ፰ |
| ፫ | ገ | ዱ | ሂ | ዋ | ዜ | ሕ | ጠ | ፱ |
| ፬ | ደ | ሁ | ዊ | ዛ | ሔ | ጥ | ዮ | ፲ |
| ፭ | ሀ | ዉ | ዚ | ሓ | ጤ | ይ | ከ | ፳ |
| ፮ | ወ | ዙ | ሒ | ጣ | ዬ | ክ | ሎ | ፴ |
| ፯ | ዘ | ሑ | ጢ | ያ | ኬ | ል | ሞ | ፵ |
| ፰ | ሐ | ጡ | ዪ | ካ | ሌ | ም | ኖ | ፶ |
| ፱ | ጠ | ዩ | ኪ | ላ | ሜ | ን | ሦ | ፷ |
| ፲ | የ | ኩ | ሊ | ማ | ኔ | ሥ | ዖ | ፸ |
| ፳ | ከ | ሉ | ሚ | ና | ሤ | ዕ | ፎ | ፹ |
| ፴ | ለ | ሙ | ኒ | ሣ | ዔ | ፍ | ጸ | ፺ |
| ፵ | መ | ኑ | ሢ | ዓ | ፌ | ጽ | ቆ | ፻ |
| ፶ | ነ | ሡ | ዒ | ፋ | ጼ | ቅ | ሮ | ፪፻ |
| ፷ | ሠ | ዑ | ፊ | ጻ | ቄ | ር | ሶ | ፫፻ |
| ፸ | ዐ | ፉ | ጺ | ቃ | ሬ | ስ | ቶ | ፬፻ |
| ፹ | ፈ | ጹ | ቂ | ራ | ሴ | ት | ኆ | ፭፻ |
| ፺ | ጸ | ቁ | ሪ | ሳ | ቴ | ኅ | ፆ | ፮፻ |
| ፻ | ቀ | ሩ | ሲ | ታ | ኄ | ፅ | ጶ | ፯፻ |

| | | | | | | | | |
|---|---|---|---|---|---|---|---|---|
| ፪፻ | ረ | ሉ | ቲ | ኃ | ዔ | ጵ | ፖ | ፰፻ |
| ፫፻ | ሰ | ቱ | ኂ | ፃ | ጼ | ፕ | አ | ፩ |
| ፬፻ | ተ | ኁ | ፂ | ጻ | ፔ | እ | በ | ፪ |
| ፭፻ | ኀ | ፀ | ጺ | ፓ | ኤ | ብ | ጎ | ፫ |
| ፮፻ | ፀ | ጹ | ፒ | አ | ቤ | ግ | ዶ | ፬ |
| ፯፻ | ጸ | ፑ | ኢ | ባ | ጌ | ድ | ሆ | ፭ |
| ፰፻ | ፐ | ኡ | ቢ | ጋ | ዴ | ሀ | ዎ | ፮ |
| ፱፻ | ጐ | | | | | | | |
| ፲፻ | ቈ | | | | | | | |
| ፼ | ኧ | | | | | | | |

ያቡጊዳ ፡ ተረፍ ።

፳፪ ፤ መልካቸውንና ፡ ድምጣቸውን ፡ አካኼዳቸውን ፡ ለውጠው ፡ ከዕብና ፡ ሳብዕ ፡ ትተው ፡ ፭ ፡ ፭ ፡ ብቻ ፡ እየኾኑ ፡ በሕጹጽነት ፡ የሚጣፉ ፡ ፬ቱ ፡ ሕጹጻን ፡ ዲቃሎች ፡ ከናባቶቻቸው ።

| | | | | | |
|---|---|---|---|---|---|
| ገ | — | ጐ | ጕ | ጓ | ጔ | ጕ |
| ኀ | — | ኈ | ኍ | ኋ | ኌ | ኍ |
| ከ | — | ኰ | ኵ | ኳ | ኴ | ኵ (ዅ) |
| ቀ | — | ቈ | ቍ | ቋ | ቌ | ቍ |

የኀና ፡ የከ ፡ ዲቃሎች ፡ ኋና ፡ ኯ ፡ ቅጥላቸውና ፡ ድምጣቸው ፡ ፩ ፡ ዐይነት ፡ ፩ ፡ ስልት ፡ ስለ ፡ ኾነ ፡ በማርኛ ፡ ይዋረሳሉ ፤ እናንተ ፡ በሚል ፡ ባ፬ኛው ፡ መደብ ፡ አይታችኋል=አይታችኻል ፥ ሰምታችኋል=ሰምታችኻል ፥ ኋላ=በኋላ ፡ እያሰኙ ፡ ይዋረሳሉና ፤ ከ፪ቱ ፡ ባንዱ ፡ በወደዱት ፡ መጣፍ ፡ ይቻላል ።

ሐተታ ፤ ስለ ፡ ፊደል ፡ ቍጥር ።

፳፫ ፤ ፊደላችንና ፡ የፊደል ፡ ቍጥራችን ፡ በሀለሐ ፡ አካኼድ ፡ ተፋልሶ ፡ ከላይ ፡ እስከ ፡ ታች ፡ ስለ ፡ ተሳሳተ ፥ ቍጥሩም ፡ በዚያው ፡ በስሕተቱ ፥ ዛሬም ፡ በውነቱ ፡ ፰፻ ፡ ብቻ ፡ ስለ ፡ ኾነ ፥ የዘጠኝ ፡ መቶና ፡ ያሥር ፡ መቶ ፡ የእልፍ ፡ ምልክት ፡ ፊደል ፡ አልነበረውም ። ዛሬ ፡ ግን ፡ ባቡጊዳ ፡ ቍጥር ፡ ምእት ፡ ብሎ ፡ አምኣት ፡ ሳይሉ ፡ እልፍ ፡ ማለት ፡ ስሕተትና ፡ ግድፈት ፡ እንዳይኾን ፥ ከፐ ፡ በታች ፡ ፫ ፡ ፊደላት ፡ ጐ ፡ ቈ ፡ ኧ ፡ ተጨምረውለት ፡ እስከ ፡ እልፍ ፡ መልቷል ። እስከ ፡ እልፍም ፡ በፊደል ፡ መቍጠር ፡ የጥንት ፡ ልማድ ፡ ነው ፡ እንጂ ፤ ያኹን ፡ ልብ ፡ ወለድ ፡ አይዶለም ። የሴም ፡ ቋንቋ ፡ ኹሉ ፡ እንደዚህ ፡ ነው ፤ በየፊደሉ ፡ እስከ ፡ እልፍ ፡ ይቈጥራል ።

፳፬ ፤ ጐ ፡ ስለ ፡ ቀለበቱ ፡ የ፱፻ ፡ አኃዝ ፡ መኾኑ ፥ አባቱ ፡ ኀርም ፡ ኀ ፡ የሐ ፡ ተወራጅ ፡ ነውና ፥ በተራ ፡ ቍጥር ፡ እንደ ፡ ጠ ፡ ዘጠነኛነት ፡ ስላለው ፡ ነው ። ቈም ፡ ስለ ፡ ቀለበቱ ፡ ያ፲፻ ፡ ወይም ፡ የሺሕ ፡ አኃዝ ፡ መኾኑ ፥ ቆፍ ፡ ፻ ፡ ነውና ፤ የርሱን ፡ አሥር ፡

ተከትሎ፡ነው ። እ፡ ደግሞ፡እልፍ፡መባሉና፡ያ፲፡ሺሕ፡አኀዝ፡መኾኑ፥በራሱ፡ላይ፡ስለ፡ተቀዳጃት፡ስላንዲቱ፡ቅንጣት፡ነቍጣ፡ነው ። የአልፍ፡አ፡ ጠባይ፡በዕብራይስጥም፡እንደዚህ፡ነው ፤ ብቻውን፡አሐዱ፡ይባል፡የነበረው፡በራሱ፡ላይ፡ነቍጣ፡ሲኾንበት፡፩፡እልፍ፡ይባላል ። ዕብራውያን፡ግን፡እልፍ፡የሚሉት፡እንዳረቦች፡ዐሥሩን፡መቶ፡ነው ። የግእዝም፡እልፍ፡ጥንታዊው፡እንደዚህ፡ነበረ ፤ ይኸውም፡በአኀዙ፡አካኼድ፡ይታወቃል፡ምእት፡ብሎ፡እልፍ፡በማለቱ ። ዐሥሩን፡መቶ፡ወይም፡አንዱን፡ሺሕ፡አምእት፡ብሎ፡፲ሩን፡ሺሕ፡፩፡እልፍ፡ማለት፡ከጽርእና፡ከቅብጥ፡የመጣ፡የሐዲስ፡ግእዝ፡ልማድ፡ነው ።

፹፫ ፤ ካኹን፡ቀደም፡በፊደል፡ተራ፡የቃጣነው፡የአኀዙም፡ነገር፡እንዲህ፡ነው ፤ ጥንታዊው፡የግእዝ፡አኀዝ፡እንደ፡ሱርስት፡እንደ፡ዕብራይስጥ፡እንደ፡ጽርእ፡እንደ፡ቅብጥ፡ያው፡ራሱ፡ፊደሉ፡ነው፡እንጂ፥እንዳረብና፡እንደ፡ላቲን፡ሌላ፡ቍጥር፡ልዩ፡ዐይነት፡አኀዝ፡አልነበረውም ፤ ይህነንም፡ባንደኛው፡ማዕርግ፡አሳይተናል ። በኋላ፡ዘመን፡ግን፡ከሰላማ፡ጋራ፡የነበሩ፡ቅብጣውያንና፡ጽርአውያን፡አስቀድመን፡እንደ፡ተናገርነ ፤ የግእዝን፡ፊደል፡ተራውን፡አፋልሰው፡ከአኀዝነት፡አውጥተው፡የጽርእን፡ፊደል፡ለግእዝ፡ፊደል፡አኀዝ፡አድርገው፡አላኳያውና፡አላምሳያው፡አለፈርጁ፡አላጣማጁ፡እያቈራኙ፡ስለ፡ጣፉት ፤ እንሆ፡ይህ፡ከአሐዱ፡እስከ፡እልፍ፡(፩—፼)፡ያለ፡አኀዝ፡ከሰብዓ፡(፸)፡በቀር፡ኹሉም፡የጽርእና፡የቅብጥ፡ፊደል፡ነው ።

፹፬ ፤ የፊደል፡ትውልድ፡አወራረዱና፡አቀዳዱ፡እንዴት፡ነው፡ብትል ፤ የፊንቅያ፡ፊደል፡ከዕብራይስጥ፥የጽርእ፡ፊደል፡ከፊንቅያ፥የላቲን፡ፊደል፡ከጽርእ፡ተቀድቷል ። የጽርእ፡ፊደላት፡መላው፡፳፬፡ናቸው ፤ የቅብጥ፡ደግሞ፡በነዚህ፡ላይ፡፯፡ጨምሮ፡፴፩፡ነው ። ለኛ፡ግን፡አኀዝ፡የኾኑልን፡፲፯፡ናቸው ፤ ከነዚሁም፡፯ቱና፡፫፡አኀዝ፡እንጂ፡ፊደል፡አይባሉም ፤ ፊደልነት፡ስለሌላቸው፡በፊደላት፡ተራ፡አይጣፉም ። ፬ቱ፡ደ፡ነው ፤ መልኩ፡ተለውጦ፡ዐይኑ፡ዐን፡ይመስላል ፤ በወዲያ፡ግን፡ዴልታ፡፫፡ማእዝን፡ነው ። ፭ቱም፡ሄ፡ነው ፤ ኤ፡ይሉታል ። ፮ቱም፡ዛይ፡ነው ፤ በጽርእ፡ፊደል፡ዋው፡ስለሌለ፡ዛይን፡፯፡ጊዜ፡ጥፈው፡እግሮቹን፡ዘርግተው፡ቈልፈው፡የገን፡ሣልስና፡ኃምስ፡አስመስለው፡፯ና፡፮፡አድርገውታል ፤ ቈላፉው፡ዛይ፡ነው ፤ ዝርጉ፡ስም፡የለውም ። አንዱን፡አልፋ፡ጎዳና፡ቀንዳም፡አድርገው፡ጎዳውን፡አሐዱ፡፩፥ቀንዳሙን፡ዕሥራ፡፳፡እንዳሉት፡ይህም፡እንደዚያ፡ነው ። ፰ቱም፡ሔት፡ነው ፤ እንደ፡ሬሳ፡ተጋድሞ፡ተጥፏል ፤ በጽርእ፡ኤታ፡በሮማይስጥ፡ሐሽ፡ይባላል ። ፱ቱና፡፲ቱም፡ጤትና፡ዮድ፡ናቸው ፤ ቴታ፡ዮታ፡ይኟቸዋል ። ባለቀንዱም፡፳፡፩፡ነው ፤ ፩ዱም፡አልፋ፡ነው ። ፴ና፡፵ም፡ተዛውረው፡ተዘቅዝቀው፡አለመልካቸው፡ተጥፈዋል ፤ ፴፡እንደ፡ሥዕለ፡ጴጥሮስ፡ቍልቍሊት፡ተጥፎ፡ራብዑን፡ሃ፡ይመስላል ፤ አቅንቶ፡ሲያዩት፡ላምዳ፡ነውና፥በጽርእ፡ሠላሳ፡ይባላል ። ፶ም፡ኑን፡ነውና፥በጽርእ፡ኀምሳ፡ይባላል ። ፵ም፡ሚም፡ነው ፤ እንደ፡ላምዳ፡ቍልቍሊት፡ተጥፎ፡ራብዑን፡ሣ፡ይመስላል ።

፷፯፤ ፴ ፡ ግን ፡ የግእዝ ፡ ሮ ፡ ነው ፤ ፆሚክሮን ፡ የሚሉት ፡ ቃናሹ ፡ ፆ ፥ በዴልታ ፡ ምትክ ፡ አድርገው ፡ ፬ቱ ፡ ካሉት ፡ ከዐይኑ ፡ ዐ ፡ ጋራ ፡ በስምና ፡ በመልክ ፡ ተባብሮ ፡ ፩ ፡ ዐይነት ፡ ስለ ፡ ኾነባቸው ፥ በፆ ፡ ፈንታ ፡ ሮን ፡ አግብተው ፡ አለስሙና ፡ አለቍጥሩ ፡ ሰብዓ ፡ ብለውታል ። ፹ም ፡ ፈ ፡ ነው ፤ በጽርእ ፡ ፐ ፡ ይባላል ፤ መልኩ ፡ አልተለወጠም ። ፺ ፡ ግን ፡ አኃዝ ፡ ብቻ ፡ እንጂ ፡ ፊደል ፡ ስላልኾነ ፡ ከቍጥር ፡ ስም ፡ በቀር ፡ የፊደልነት ፡ ስም ፡ የለውም ፤ መልኩ ፡ ተለውጦ ፡ እንደ ፡ ን ፡ ኹኗል ፤ ጥንተ ፡ መልኩ ፡ ግን ፡ ራሱ ፡ ገጥሞ ፡ እግሩ ፡ ቀጥ ፡ ያለ ፡ ነው ። በጽርእ ፡ ፊደል ፡ ዋውና ፡ ጻዴ ፡ ቆፍ ፡ እነዚህ ፫ቱ ፡ ስለሌሉ ፡ በታቸውን ፡ በአኃዝነት ፡ ሌሎች ፡ ወርሰውታል ። ፻ ፡ የተባለም ፡ ሬስ ፡ ነው ፤ መልኩ ፡ የግእዝን ፡ የ ፡ ይመስላል ፤ በጽርእና ፡ በቅብጥ ፡ ሮ ፥ በሮማይስጥ ፡ ፐ ፡ ይባላል ፤ ሬስ ፡ መቶ ፡ መባሉ ፡ በታውን ፡ ትቶ ፡ በቆፍ ፡ በታ ፡ ገብቶ ፡ ነው ፡ እንጂ ፥ በግእዝና ፡ በዕብራይስጥ ፡ ኹለት ፡ መቶ ፡ ነው ። ፻፻ም ፡ ኹለት ፡ ሮ ፡ ነው ፤ በጽርእ ፡ ሚርያ ፡ ይባላል ፤ ፪ቱን ፡ ሮ ፡ አቈራኝቶና ፡ አስተሳስሮ ፡ እልፍ ፡ ማለት ፥ እንደ ፡ ጽርአውያን ፡ መቶ ፡ ጊዜ ፡ መቶ ፡ ማለት ፡ ነው ፡ እንጂ ፥ እንደ ፡ ሴማውያን ፡ ፲ ፡ ጊዜ ፡ መቶ ፡ ወይም ፥ ሺሕ ፡ ማለት ፡ አይዶለም ።

፬ኛ ፡ ማዕርግ ።

ከግእዝ ፡ ፊደላት ፡ የተዴቀለ ፡ ያማርኛ ፡ ፊደል ።

፷፰፤ ምሉ ፡ ዐማርኛ ፡ ያላቸው ፡ ፊደላት ፡ ፯ ፡ ብቻ ፡ ናቸው ፤ ለቀሩት ፡ ግን ፡ ከራብዖቻቸው ፡ በቀር ፡ ያማርኛ ፡ ቅጥል ፡ የላቸውም ፤ ከነራብዑም ፡ በጜራሽ ፡ የሌላቸው ፡ አሉ ፤ (አ—ዐ ፡ ሀ—ሐ ፡ ወ—የ ፡ ጰ—ፐ) ። ፯ ፡ ያልናቸውም ፡ ምሉአንና ፡ ፍጹማን ፡ ፊደላት ፡ እነዚህ ፡ ናቸው ።

| | | | | | | | | |
|---|---|---|---|---|---|---|---|---|
| ደ | — | ጀ | ጁ | ጂ | ጃ | ጄ | ጅ | ጆ |
| ዘ | — | ዠ | ዡ | ዢ | ዣ | ዤ | ዥ | ዦ |
| ጠ | ጸፀ | ጨ | ጩ | ጪ | ጫ | ጬ | ጭ | ጮ |
| ከ | — | ኸ | ኹ | ኺ | ኻ | ኼ | ኽ | ኾ |
| ነ | — | ኘ | ኙ | ኚ | ኛ | ኜ | ኝ | ኞ |
| ሰ | — | ሸ | ሹ | ሺ | ሻ | ሼ | ሽ | ሾ |
| ተ | — | ቸ | ቹ | ቺ | ቻ | ቼ | ች | ቾ |

ሐተታ ።

፷፱፤ ጨ ፡ የወጣ ፡ ከጠና ፡ ከጸፀ ፡ ነው ፡ እንጂ ፥ ከጠ ፡ ብቻ ፡ አይዶለም ፤ በግእዝ ፡ ጸ—ፀ ፡ የሚባለው ፡ ባማርኛ ፡ ጠና ፡ ጨ ፡ ይኾናል ። ማስረጃ ፡ ጸመ ፡ ጠመ ፡ ጸልአ ፡ ጠላ ፤ ጸጕር ፡ ጠጕር ፡ ጬገር ፤ ጸልመ ፡ ጨለመ ፤ ጼው ፡ ጨው ፤ ጻጹት ፡ ጫጩት ፤ ጸርቅ ፡ ጨርቅ ። ፀመደ ፡ ጠመደ ፤ ፀመረ ፡ ጨመረ ፤ ፀበጠ ፡ ጨበጠ ።

ዐማርኛና ፡ ትግሬ ፡ ትግሪኛ ፡ ካባታቸው ፡ ከግእዝ ፡ ጕያ ፡ ሳይወጡ ፡ ጀሸኸ ፡ በማለት ፡ ከዐረብ ፡ ከሱርስት ፡ ከዕብራይስጥ ፥ ዠኘቸ ፡ በማለት ፡ ከሮማይስጥና ፡ ከልጆቹ ፡ ይስማማሉ ፤ ጨ ፡ በማለት ፡ ግን ፡ ከማንም ፡ ከማን ፡ የማይገጥሙ ፡ ብቸኞች ፡ ናቸው ። ሸን ፡ ከጥንታዊ ፡ ግእዝ ፡ ወርሰውታል ፤ ጀ ፡ የዐረቦች ፡ ገ ፡ ነው ፥ ዐረብ ፡ ገ ፡ ሲል ፡ ጂም ፡ ጀመል ፡ ይላል ። ከን ፡ ኸ ፡ ማለት ፡ የዕብራይስጥና ፡ ያማርኛ ፡ የትግሬኛም ፡ ነው ፤ ባረብና ፡ ባሮጌው ፡ ግእዝ ፡ ግን ፡ ኸ ፡ የሚባለው ፡ ኀርም ፡ ኀ ፡ ነው ፡ እንጂ ፥ ከፍ ፡ አልነበረም ። ሸ ፡ የሚባለውም ፡ ንጉሡ ፡ ሠ ፡ እንጂ ፥ ሳቱ ፡ ሰ ፡ አልነበረም ፤ ሠውት ፡ ሠና ፡ ሳት ፡ ሰ ፡ ተዛውረውና ፡ ተፋልሰው ፡ አለቦታቸው ፡ ተጥፈዋል ፤ መፋለሳቸውም ፡ በዚህ ፡ ይታወቃል ፤ ነጋሢ ፡ ነጋሽ ፥ ሢመት ፡ ሹመት ፥ ሦክ ፡ ሾኽ ፤ የመሰለው ፡ ኹሉ ።

በጓኋኳቋ ፡ አንጻር ፡ ከግእዙም ፡ ካማርኛውም ፡
የሚገኙ ፡ የራብዕ ፡ ዲቃሎች ፡ ራብዖች ፡ ብቻ ።

(ከግእዙ) ።

፴፤ በ ዳ ዛ ጣ ላ ማ ና ሣ ፋ ጳ ፃ ራ ሳ ታ ።
ቧ ዷ ዟ ጧ ሏ ሟ ኗ ሧ ፏ ጿ ሯ ሷ ቷ ።

(ካማርኛው) ።

ጃ ዣ ጫ ኻ ኛ ሻ ቻ ።
ጇ ዧ ጯ ዃ ኟ ሿ ቿ ።

ለነዚህ ፡ ፊደሎች ፡ ለኹሉም ፡ ዋየላቸው ፡ ዋ ፡ ነው ፤ ቅጥላቸው ፡ ኹሉ ፡ ሀየንተ ፡ ዋ ፡ ኹኖ ፡ በዋ ፡ ፈንታ ፡ ገብቷል ። ቅጥላቸው ፡ ቀርቶ ፡ በዝርዝር ፡ ፊደል ፡ ሲጣፉ ፡ ግን ፡ ቡአ ፡ ዱአ ፡ ጁአ ፡ ጬአ ፡ ያሰኛሉ ፤ በዚህም ፡ ዉአ ፡ ይገኛል ፤ ይኸውም ፡ ዋ ፡ ማለት ፡ ነው ። ኹሉንም ፡ ዘርዝሮ ፡ ሲጥፉት ፥ በዉአ ፡ ደዉአ ፡ ጀዉአ ፡ እያሰኘ ፡ የቅጥላቸው ፡ መንታነት ፡ ስለ ፡ ፪ቱ ፡ መኾኑን ፡ ያሳያል ። ሟኗሧጿሯቷ ፡ እነዚህ ፡ ፯ቱ ፡ እንደ ፡ ጓኋኳቋ ፡ ናቸውና ፥ ለግእዝም ፡ ይስማሙታል ። ተሟቅሐ ፡ ይትመዋቃሕ ፡ ይትሟቃሕ ። ተኗለወ ፡ ይትነዋሉ ፡ ይትኗሉ ፤ ምሧዕ ፡ መሧዕት ። መጸተ ፡ መጿቴ ፡ ምጿት ። ምሯጽ ፡ ስሯጽ ። ተቷስሐ ፡ ይተዋሳሕ ፡ ይቷሳሕ ፤ ተቷሳሒ ። አስተቷስሐ ፡ ያስተተዋስሕ ፡ ያስተቷስሕ ፤ አስተቷሳሒ ፡ መስተቷስሕ ። ዋ ፡ ከዕብና ፡ ራብዕ ፡ ማዛመዱ ፡ ቅጥሉ ፡ የአ ፡ ምስለኔ ፡ ስለ ፡ ኾነለት ፡ ነው ፡ (ቍ፲) ።

፲፰ኛ ፡ ማዕርግ ።

፴፩፤ ጉባኤ ፡ ዝርዋን ፡ ፊደላት ፥ ፊደላተ ፡ ግእዝ ፡ ወዐምሐራ ፡ እለ ፡ ምስለ ፡ ሱርስት ፡ ወዐረብ ፡ ወምስለ ፡ ዕብራይስጥ ፡ የኀብራ ።

| | | | | | | | |
|---|---|---|---|---|---|---|---|
| አ | ኡ | ኢ | ኣ | — | ኤ | እ | ኦ |
| በ | ቡ | ቢ | ባ | ቧ | ቤ | ብ | ቦ |
| ገ | ጉ | ጊ | ጋ | — | ጌ | ግ | ጎ |
| ጐ | » | ጒ | ጓ | — | ጔ | ጕ | » |
| ደ | ዱ | ዲ | ዳ | ዷ | ዴ | ድ | ዶ |
| ጀ | ጁ | ጂ | ጃ | ጇ | ጄ | ጅ | ጆ |
| ሀ | ሁ | ሂ | ሃ | — | ሄ | ህ | ሆ |
| ወ | ዉ | ዊ | ዋ | — | ዌ | ው | ዎ |
| ዘ | ዙ | ዚ | ዛ | ዟ | ዜ | ዝ | ዞ |
| ዠ | ዡ | ዢ | ዣ | ዧ | ዤ | ዥ | ዦ |
| ሐ | ሑ | ሒ | ሓ | — | ሔ | ሕ | ሖ |
| ኀ | ኁ | ኂ | ኃ | — | ኄ | ኅ | ኆ |
| ኈ | » | ኊ | ኋ | — | ኌ | ኍ | » |
| ጠ | ጡ | ጢ | ጣ | ጧ | ጤ | ጥ | ጦ |
| ጨ | ጩ | ጪ | ጫ | ጯ | ጬ | ጭ | ጮ |
| የ | ዩ | ዪ | ያ | — | ዬ | ይ | ዮ |
| ከ | ኩ | ኪ | ካ | — | ኬ | ክ | ኮ |
| ኰ | » | ኲ | ኳ | — | ኴ | ኵ | » |
| ኸ | ኹ | ኺ | ኻ | ዃ | ኼ | ኽ | ኾ |
| ለ | ሉ | ሊ | ላ | ሏ | ሌ | ል | ሎ |
| መ | ሙ | ሚ | ማ | ሟ | ሜ | ም | ሞ |
| ነ | ኑ | ኒ | ና | ኗ | ኔ | ን | ኖ |
| ኘ | ኙ | ኚ | ኛ | ኟ | ኜ | ኝ | ኞ |
| ሠ | ሡ | ሢ | ሣ | ሧ | ሤ | ሥ | ሦ |
| ዐ | ዑ | ዒ | ዓ | — | ዔ | ዕ | ዖ |
| ፈ | ፉ | ፊ | ፋ | ፏ | ፌ | ፍ | ፎ |
| ጸ | ጹ | ጺ | ጻ | ጿ | ጼ | ጽ | ጾ |
| ፀ | ፁ | ፂ | ፃ | — | ፄ | ፅ | ፆ |
| ቀ | ቁ | ቂ | ቃ | — | ቄ | ቅ | ቆ |
| ቈ | » | ቊ | ቋ | — | ቌ | ቍ | » |
| ረ | ሩ | ሪ | ራ | ሯ | ሬ | ር | ሮ |
| ሰ | ሱ | ሲ | ሳ | ሷ | ሴ | ስ | ሶ |
| ሸ | ሹ | ሺ | ሻ | ሿ | ሼ | ሽ | ሾ |
| ተ | ቱ | ቲ | ታ | ቷ | ቴ | ት | ቶ |
| ቸ | ቹ | ቺ | ቻ | ቿ | ቼ | ች | ቾ |
| ጰ | ጱ | ጲ | ጳ | — | ጴ | ጵ | ጶ |
| ፐ | ፑ | ፒ | ፓ | — | ፔ | ፕ | ፖ |

## ቍጥር ፡ በፊደልና ፡ በአኃዝ ።

አ በ ገ ደ ሀ ወ ዘ ሐ ጠ የ ከ ለ መ ነ ሠ ዐ ፈ ጸ ቀ ቄ እ
፩ ፪ ፫ ፬ ፭ ፮ ፯ ፰ ፱ ፲ ፳ ፴ ፵ ፶ ፷ ፸ ፹ ፺ ፻ ፲፻ ፼

## ፮ኛ ፡ ማዕርግ ።

## ስለ ፡ እጅ ፡ መኪና ፡ ፊደል ።

፴፪ ፤ ኤውሮፖች ፡ ፊደላቸውን ፡ ሳያሳንሱና ፡ ሳይከፍሉ ፡ እናሳንስም ፡ ሳይሉ ፡ መላውን ፡ ፊደል ፡ ፳፮ቱን ፡ ዘር ፡ ከነአኃዙና ፡ ከነጓዙ ፡ አሳክተውና ፡ አስማምተው ፡ በ እጅ ፡ መኪና ፡ እንዲጥፉ ፥ የኛም ፡ ፊደል ፡ በኤውሮፖች ፡ ልክ ፡ ፳፮ ፡ ዘር ፡ ነውና ፤ እንደ ፡ መዠመሪያው ፡ ማዕርግ ፡ ጭፍራውን ፡ ትቶ ፡ አበጋዙን ፡ ብቻ ፡ ግእዝ ፡ ግእዙን ፡ ባንድ ፡ አይቅር ፡ ሰብስቦ ፡ በ፯ ፡ ዋየል ፡ ቢያስኬዱት ፡ ከእጅ ፡ መኪና ፡ ተስማምቶ ፡ እንደ ነሱ ፡ ፊደል ፡ ይኼዳል ። አኃዙንም ፡ ፲ኛውን ፡ ዘሮ ፡ አድርጎ ፡ የላይ ፡ የታች ፡ ሠረዝ ፡ ቀርቶበት ፡ ከ፩ ፡ እስከ ፡ ፱ ፡ ያለውን ፡ በ፲ቱ ፡ ዘሮነት ፡ ቢያስኬዱት ፡ ከአኃዛቸው ፡ ይሰ ማማል ። ዘሮ ፡ ማለት ፡ የአኃዝ ፡ ዋየል ፡ ወይም ፡ ምእላድ ፥ ወላጤ ፡ ፍቅድ ፡ ወመፈ ድፍድ ፡ ማለት ፡ ነው ፤ ብቻውን ፡ ሲኾን ፡ ባዶ ፡ ጠፍ ፥ አኃዝ ፡ ሲከተለው ፡ አብዢ ፡ ይባላል ፤ ጥሬነቱም ፡ ዘረወንና ፡ ዘርዘረን ፡ ይመስላል ።

## ፊደልና ፡ ዋየል ፡ ከነአኃዙና ፡ ከነጓዙ ።

አ በ ገ ደ ሀ ወ ዘ ሐ ኀ ጠ የ ከ ለ
መ ነ ሠ ዐ ፈ ጸ ፀ ቀ ረ ሰ ተ ጰ ፐ ።

## ዲቃሎች ።

ጐ ጀ ዠ ኈ ጨ ኰ ኸ ኘ ቈ ሸ ቸ ።

## ዋየሎች ።

ኡ ኢ ኣ—ዋ ኤ እ ኦ ።

## አኃዞች ።

፩ ፪ ፫ ፬ ፭ ፮ ፯ ፰ ፱ ፲ ።

## ምልክቶች ።

. ፡ ፥ ፤ ፦ ። . . . ? ! ( ) - « » — × +

## ዐዋጅና ፡ አገባብ ።

፴፫ ፤ ግእዝ ፡ ፊደል ፡ በግእዝነት ፡ ዋየልም ፡ በፊደልነት ፡ ሲነገር ፡ ኹሉም ፡ ራሱን ፡ ችሎ ፡ በየጠባዩ ፡ ይነገራል ። ግእዝ ፡ ኹሉ ፡ ዋየል ፡ መፈለጉ ፡ ከካዕብ ፡ እስከ ፡

ሳብዕ ፡ ነው ፤ ዋየልም ፡ ድምፁን ፡ የሚያወርስ ፡ ለግእዝ ፡ ብቻ ፡ ነው ። ይህም ፡ ራሱን ፡ ችሎ ፡ ገደለ ፡ ተገደለ ፡ ቀበረ ፡ ተቀበረ ፡ እያለ ፥ በዋየልም ፡ ታዝሎ ፥ በኡ—ቡ ፡ በኢ—ቢ ፡ በኣ—ባ ፡ በዋ—ቧ ፡ በኤ—ቤ ፡ በእ—ብ ፡ በኦ—ቦ ፡ እያሰኘ ፡ ከገ ፡ እስከ ፡ ፐ ፡ ያሉትን ፡ የኹሉን ፡ አካኼድ ፡ ያሳያል ። ዋየልም ፡ በፊደልነቱ ፡ መነሻ ፡ መድረሻ ፡ መካከልም ፡ ቢኾን ፡ እንደ ፡ ግእዝ ፡ ራሱን ፡ ይችላል ፤ ይህም ፡ ኡረኡኤለእ—ኡሩኤል ፤ ኢየአ በእ—ኢዮብ ፤ አፈእአ ፡ አፍአ ፤ ኤለእየአሰእ—ኤልያስ ፤ እነኤ—እኔ ፤ እኘአ—እኛ ፤ ኦረኢተእ—ኦሬት ፡ እያሰኘና ፡ በቁም ፡ ቀሪነቱን ፡ መደብ ፡ አድርጎ ፡ ዋየልነቱንም ፡ ያሳያል ። ዋ ፡ ደግሞ ፡ በመነሻና ፡ በመድረሻ ፡ ፊደል ፡ በአንቀጽ ፡ ሲገባ ፥ በጥሬ ፡ መነሻም ፡ ሲገባ ፡ ልዩነት ፡ የለውም ። ምሳሌ ፤ ጐዋጐረ—ጓጐረ ፡ ጐዋጐዋረአ—ጓጓራ ፤ ተነእፈዋፈዋ—ተንፏፏ ፤ ፈዋፈዋተኤ—ፏፏቴ ። በጥሬ ፡ መድረሻ ፡ ሲገባ ፡ ግን ፡ የሩቅ ፡ ሴት ፡ ዝርዝር ፡ ይኾናል ። ምሳሌ ፤ በአለዋ—ባሏ ፤ ለእጅዋ—ልጇ ፤ ዐመአ ቸዋ—ዐማቿ ። የጥሬው ፡ መድረሻ ፡ ሣልስና ፡ ራብዕ ፡ ኃምስና ፡ ሳብዕ ፡ ሲኾንበት ፡ ርሱ ፡ ራሱ ፡ ብቻ ፡ ይበቃል ፤ ይህም ፡ ሰነእጠኢ—ሰንጢ ፡ ሰንጢዋ ፤ ከአረአዋ—ካራዋ ፤ ጐፈረኤዋ—ጐፈሬዋ ፤ መኢደኦዋ—ሚዶዋ ፡ ማለቱን ፡ ያሳያል ። ማእከል ፡ ኹኖ ፡ ግእዝ ፡ ሲቀድመውና ፡ ሲከታተል ፡ ግን ፥ ድምፁን ፡ ለግእዝ ፡ እንዳያወርስና ፡ በቁም ፡ ቀሪ ፡ ኹኖ ፡ እንዲነገር ፡ በራሱ ፡ ላይ ፡ ፪ ፡ ነቍጥ ፡ ይደረግበታል ፤ ይህም ፡ አስተዋ̈ለ ፤ ተዋ̈ዋለ ፤ ከኡ̈ረ ፥ ለኢ̈የ ፡ እያለ ፡ ሌላውን ፡ ኹሉ ፡ ያሳያል ። የኤውሮፓን ፡ ቋንቋ ፡ ተምረው ፡ ለሚጥፉና ፡ ለሚያነቡ ፡ ስላገር ፡ ቋንቋና ፡ ስለ ፡ እጅ ፡ መኪናም ፡ ለሚያ ስቡ ፡ ማመልከቻ ፡ ይኸው ፡ ይበቃል ። የአኃዙም ፡ ነገር ፡ ዐሥርቱ ፡ ዘሮ ፡ ስለ ፡ ኾነ ፡ ዐረቦች ፡ ከህንዶች ፡ ኤውሮፖች ፡ ከረቦች ፡ እንደ ፡ ወሰዱት ፡ እንደዚያው ፡ እንደ ፡ ህንዶች ፡ አኃዝ ፡ ይኼዳል ፤ ከመልክ ፡ በቀር ፡ ያካኼድ ፡ ልዩነት ፡ የለውም ። አኃዝነ ቱና ፡ ፊደልነቱም ፡ የጽርእና ፡ የቅብጥ ፡ እንደ ፡ ኾነ ፡ በ፫ኛው ፡ ማዕርግ ፡ ተነግሯል ፡ (ቍ፳፫ና ፡ ፳፯) ። የምልክቶችም ፡ አገባብ ፡ ከነስማቸው ፡ ገና ፡ ወደ ፡ ፊት ፡ ይነገራል ።

ያልተነገረውም ፡ ያራቱ ፡ ዐይነት ፡ ቍጥር ፡ ምልክት ፡ ይህ ፡ ነው ።

\+ የመደመር ፡  
— የመቀነስ ፡  
× የማብዛት ፡  
÷ የማካፈል ።

የንባብ ፡ ማሳያ ።

መኦአ ፡ አነእበሰአ ፡ ዘእ̈መእነገደ ፡ የእሀኡደአ ፤ ቀደአመአወኢ ፡ ኀየእለ ፡ ሠእ ለአሰኤ ፡ ሠእየኡመ ፡ እገእዘኢአበእሐኤረእ ፡ ነእገኡሠ ፡ ነገሠእተእ ፡ ዘኢ̈ተእየኦጰእ የአ ። ሞአ ፡ አንበሳ ፡ ዘእምነገደ ፡ ይሁዳ ፤ ቀዳማዊ ፡ ኀይለ ፡ ሥላሴ ፡ ሥዩመ ፡ እግ ዚአብሔር ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ ዘኢትዮጵያ ። ፲፱፻፵ ፡ ወይም ፡ 1942 ፡ ፲፱፻፵፪ ፡ ዓ ፡ ም ፡

## የጥፈትና ፡ የመጻሕፍት ፡ መልክ ።

፴፬ ፤ ከንገት ፡ በላይ ፡ በለው ፡ በፍጥረት ፡ ኹሉ ፡ መልክ ፡ በየራሱና ፡ በየገጹ ፡ ልዩ ፡ ልዩነት ፡ ያላቸው ፡ ብዙ ፡ ሕዋሳት ፡ እንዳሉ ፥ በመጻሕፍትም ፡ መልክ ፡ በያንዳንዱ ፡ ገጽ ፡ ብዙ ፡ ስም ፡ ያለው ፡ ክፍል ፡ አለበት ። ያልተቀጻው ፡ ብራና ፡ ወረቀት ፡ አንዳንዱ ፡ ጥቅል ፡ ሰሌዳ ፥ ወይም ፡ ሉሕ ፡ ይባላል ፤ ዝርግ ፡ ማለት ፡ ነው ። ከዚያ ፡ የሚቀጻው ፡ አንዳንዱ ፡ ክፍል ፡ ሳይታጠፍ ፡ ቅጽ ፥ ሲታጠፍ ፡ ቅጠል ፡ ይባላል ። ፪ኛ ፡ ቅጠል ፡ የሌለው ፡ እኩሌታ ፡ ቅጽ ፡ ሲኾን ፡ ኅላፍ ፡ ይባላል ። ፬ቱ ፡ ወይም ፡ ፰ቱ ፡ ቅጽ ፡ እየታጠፈ ፡ በንድነት ፡ ሲታሰር ፡ ጥራዝ ፡ ይባላል ። አንዱ ፡ ቅጽ ፡ ተሠምሮ ፡ ሲታጠፍ ፡ ባላ፬ ፡ ገጽ ፡ ከኾነ ፡ ዘንድ ፡ ባንድ ፡ ወገን ፡ ያለው ፡ የ፪ቱ ፡ ገጽ ፡ ስምና ፡ መልክ ፡ በየክፍሉ ፡ ይህ ፡ ነው ፤ ውግ ፡ ያለበት ፡ ክፍል ፡ ግራና ፡ ቀኙ ፡ ጠርዝ ፥ መግለጫውና ፡ መግለጫው ፡ ግልየት ፥ ላይኛው ፡ አርእስት ፥ ታችኛው ፡ ኅዳግ ፥ መካከለኛው ፡ ዐምድ ፤ ዕጥፋቱን ፡ እንደ ፡ ወንዝ ፡ አማክሎ ፡ ወደ ፡ ጥራዝ ፡ ያለው ፡ ማዶና ፡ ማዶው ፡ ምስማክ ፡ ይባላል ፤ መከዳ ፡ ማለት ፡ ነው ። በመካከልም ፡ በያንዳንዱ ፡ ውግ ፡ ፊት ፡ ወስፌውና ፡ ርሳሱ ፡ ያለፈበት ፡ ሰንበር ፡ ሰንበሩ ፡ ሢራክ ፥ ቀለም ፡ የሚወድቅበት ፡ ቃዳው ፡ ተለላው ፡ መሥመር ፥ በፊደልና ፡ በፊደል ፡ መካከል ፡ ያለው ፡ ክፍት ፡ ክፍቱ ፡ ኖኅት ፥ በየፊደሉ ፡ ውስጥ ፡ ያለው ፥ ከርሥ ፡ ይባላል ፤ የነጩ ፡ ስም ፡ ይህ ፡ ነው ። የመሥመርም ፡ ሥራ ፡ አብነቱ ፡ የተገኘና ፡ የተቀዳ ፡ ከሙዝ ፡ ቅጠልና ፡ ከጕናጕና ፡ ነው ፡ ይባላል ። የጥቍሩ ፡ ደግሞ ፡ አንዳንዱ ፡ ፊደል ፥ ቀለም ፡ ወይም ፡ ኅር(ወ)መት ፡ ይባላል ፤ ቅርጽ ፡ ማለት ፡ ነው ። ከነቍጥ ፡ እስከ ፡ ነቍጥ ፡ የሚሰደረው ፡ አንዳንዱ ፡ ስክ ፡ ንባብ ፡ ይባላል ፤ ቃል ፡ ማለት ፡ ነው ። ቃልንም ፡ ከቃል ፡ በየንባቡና ፡ በየስልቱ ፡ በየብልቱ ፡ ለይተው ፡ ነጥለው ፡ ዘርዝረው ፡ ደምረው ፡ ፩ ፡ ፈርጅ ፡ አድርገው ፡ የሚያሳዩ ፡ የቃል ፡ ምልክቶች ፡ ፬ ፡ ናቸው ፤ መልካቸውና ፡ ስማቸውም ፡ ይህ ፡ ነው ።

| መልካቸው ። | ስማቸው ። |
|---|---|
| . | ነጥብ ፥ አው ፡ (ወይም) ፡ ነቍጥ ፥ ማጥበቂያ ። |
| ፡ | ንኡስ ፡ ነጥብ ፥ አው ፡ ንጻል ፡ (ነጠላ) ። |
| ፤ ፥ | ንኡስ ፡ ሠረዝ ፥ አው ፡ ንጻል ። |
| ፤ | ዐቢይ ፡ ሠረዝ ፥ አው ፡ ክዑብ ፡ (ድርብ) ። |
| ። | ዐቢይ ፡ ነጥብ ፥ አው ፡ ክዑብ ። |

## ሐተታ ።

፴፭ ፤ ነጥብና ፡ ነቍጥ ፡ ፩ ፡ ስም ፡ ናቸው ፤ ነጥብ ፡ የግእዝ ፡ ብቻ ፡ ነቍጥ ፡ የዐረብና ፡ የዕብራይስጥ ፡ ነው ፤ ያውም ፡ አንዳንዱ ፡ ጠብታ ፡ ነው ፡ እንጂ ፥ ፪ቱና ፡ ፬ቱ ፡ አይዶለም ፤ ሲበዛ ፡ ነቍጣት ፡ ነጥባት ፡ ወይም ፡ ነጠብጣብ ፡ ያሰኛል ። የጥንቱ ፡ ነጥብ ፡ እንደ ፡ ዜማ ፡ ይዘት ፡ ፩ ፡ ቅንጣት ፡ ብቻ ፡ ነበረ ፡ ይባላል ፤ ፪ኛም ፡ በንዱ ፡ ነጥብ ፡ ፈንታ ፡ እንዳ፲ቱ ፡ ያለ ፡ ዘንግ ፡ ነበረ ፤ ፫ኛ ፡ ግን ፡ አንዱ ፡ ነጥብ ፡ የመጥበቅ ፡ ምልክት ፡ ስለ ፡

ኾነ ፡ እንዳይሞከሽ ፡ በዘንጉ ፡ ፈንታ ፡ ፪ ፡ ነጥብ ፡ ኹኗል ። ፪ቱን ፡ ፬ቱን ፡ ነቍጥ ፡ ነጥብ ፡ ብሎ ፡ ባንድነት ፡ ስም ፡ መጥራት ፡ በዚያው ፡ በጥንቱ ፡ ባንዱ ፡ ቅንጣት ፡ ልማድ ፡ ነው ፡ እንጂ ፤ በሰዋስው ፡ መንገድ ፡ አይዶለም ። ባማርኛ ፡ ፪ ፡ ነጥብ ፡ ፬ ፡ ነጥብ ፡ ተብሎ ፡ ከቅጽል ፡ ጋራ ፡ ይነገራል ፤ ጣፎችና ፡ ባለመጣፎች ፡ ግን ፡ ነቍጥን ፡ ለ፪ቱ ፡ ብቻ ፡ ነጥብን ፡ ላ፬ቱ ፡ ብቻ ፡ ሰጥተው ፡ አለቅጽል ፡ ፪ቱን ፡ ነቍጥ ፡ ፬ቱን ፡ ነጥብ ፡ ብለው ፡ በተለየ ፡ ስም ፡ ውስጠ ፡ ብዙ ፡ አድርገው ፡ ይጠሩታል ። ባለቅኔዎችም ፥ ቃልከ ፡ ነቍጥ ፡ እንዘ ፡ ክልኤቲ ፤ ልሳንከ ፡ አሐቲ ፡ ይእቲ ። ፍቅደ ፡ ነጥብ ፡ በዓላተ ፡ ወልድ ፡ ተስዐቱ ፡ ውእቱ ፡ እያሉ ፡ በውስጠ ፡ ብዙነት ፡ ያገቡታል ። ነጥብን ፡ ተስዐቱ ፡ ማለት ፡ ፱ ፡ ቀይ ፡ ሲጨመርበት ፡ ነው ።

## አገባባቸውም ፡ ይህ ፡ ነው ።

፴፮ ፤ ነቍጥ ፡ የንኡሳን ፡ ቃላት ፡ መለያ ፡ ነው ፤ በንባብ ፡ ኹሉ ፡ ራስ ፡ በያንዳንዱ ፡ ስክ ፡ ይገባል ። ነጠላ ፡ ወይም ፡ ንኡስ ፡ ሠረዝ ፡ ጠባዩ ፡ ፩ ፡ ሲኾን ፡ መልኩ ፡ ፪ ፡ ነው ፤ ልዩነት ፡ ስላላቸው ፡ እየራሳቸው ፡ በሚታሰሩና ፡ በማይጫፈሩ ፡ በጫጭር ፡ ቃሎች ፡ ይገባል ። ምሳሌ ፤ አነ ፡ ቀዳማዊ ፤ ወአነ ፡ ደኃራዊ ፥ ርእስ ፡ ወማኅለቅት ፤ ጥንት ፡ ወተፍጻሜት ፣ አንተ ፡ ዘአሜሃ ፤ ወአንተ ፡ ዘይእዜ ፥ አንተ ፡ ዘእሙንቱ ፤ ወአንተ ፡ ዘለነ ። ተፈለጥ ፡ የማነ ፤ አው ፡ ፀጋመ ፥ ወእመ ፡ አኮ ፡ ግበእ ፡ ድኅረ ፤ ወኢትሑር ፡ ቅድመ ። ድርብ ፡ ወይም ፡ ዐቢይ ፡ ሠረዝ ፥ በፍጹም ፡ ቃል ፡ ማኽል ፡ በንዳንዱ ፡ ፈርጅ ፡ (ፍራዝ) ፡ ውስጥ ፡ እየራሱ ፡ በሚታሰርና ፡ በሚነገር ፡ ባስረጅና ፡ ባፍራሽ ፡ ይገባል ። ምሳሌ ፤ ወምድርሰ ፡ ኢታስተርኢ ፤ ወኢኮነት ፡ ድሉተ ፤ ወጽልመት ፡ መልዕልተ ፡ ቀላይ ፤ ወመንፈሰ ፡ እግዚ ፡ ይጼልል ፡ መልዕልተ ፡ ማይ ። ወይቤ ፡ እግዚ ፤ ለይኩን ፡ ብርሃን ፤ ወኮነ ፡ ብርሃን ። ነዐ ፡ ንበር ፡ ማእከሌነ ፡ ወንግረነ ፤ እስመ ፡ ኪያከ ፡ አልሀቀ ፡ እግዚ ። ፈርሀ ፡ ወደንገፀ ፤ ባሕቱ ፡ ኢጐየ ፡ ወኢገገጸ ። ነጥብ ፡ (።) ንኡስ ፡ ምዕራፍ ፡ ነው ፤ አንባቢን ፡ እንደ ፡ ልጓም ፡ ኹኖ ፡ ይገታል ። አንዱ ፡ ፍጹም ፡ ቃል ፡ ወይም ፡ አንዱ ፡ ፈርጅ ፡ ዐጭርም ፡ ረዥምም ፡ ቢኾን ፡ ተሳቢው ፡ ተከቶ ፡ ነገሩ ፡ ሲጨረስ ፡ እንደ ፡ ጒልላት ፡ በጫፉ ፡ በቍንጮው ፡ ይገባል ። ረዥም ፡ ቃል ፥ ወምድርሰ ፡ እንዳል ነው ፡ ያለ ፡ ነው ። ዐጭር ፡ ቃል ፥ በቀዳሚ ፡ ገብረ ፡ እግዚ ፡ ሰማያተ ፡ ወምድረ ። ያማርኛውም ፡ እንደ ፡ ግእዙ ፡ ነው ፤ ለብቻው ፡ የተለየ ፡ ዐዋጅ ፡ የለውም ።

፴፯ ፤ በነዚህ ፡ ባራቱ ፡ ላይ ፡ ደግሞ ፤ . . . . ነጠብጣብና ፡ ( ) ቀርን ፡ « » አቅርንት ፡ ሲጨመሩ ፡ ቍጥራቸው ፡ ፯ ፡ ይኾናል ፤ የነዚህም ፡ የ፫ቱ ፡ አገባብ ፡ እንዲህ ፡ ነው ። ነጠብጣብ ፡ ከያንዳንዱ ፡ ምዕራፍና ፡ አንቀጽ ፡ ፍሬ ፡ ፍሬው ፡ ጥቅስ ፡ በጥፈት ፡ ሲለቀም ፡ በቀሪው ፡ ቃል ፡ ፈንታ ፡ ይገባል ። ምሳሌ ፤ መጽሐፈ ፡ ልደቱ ፡ ለኢ ፡ ክር ፡ ወልደ ፡ ዳዊት ፡ ወልደ ፡ አብርሃም ። አብርሃም ፡ ወለዶ ፡ ለይሥሐቅ ፤ . . . . ወእሴይኒ ፡ ወለደ ፡ ዳዊትሀ ፡ ንጉሠ ፤ . . . . ወኵሎንኬ ፡ ትውልድ ፡ እምአብርሃም ፡ እስከ ፡ ዳዊት ፡ ዐሥርቱ ፡ ወአርባዕቱ ። ቀዳሚሁ ፡ ቃል ፤ . . . . ወውእቱ ፡ ቃል ፡ ሥጋ ፡ ኮነ ። ዳግመኛም ፡ በቋንቋ ፡ መጣፍ ፡ ውስጥ ፡ የተጣፈውን ፡ ቃል ፡ አንዱን ፡ ስም ፡ መላ

ልሶ ፡ በመጣፍ ፡ ፈንታ ፡ በቀሪው ፡ ፊደል ፡ ልክ ፡ ይገባል ። ምሳሌ ፤ ጎግ ፥ ማ . . ። ዳዊት ፥ መዝሙረ ፡ . . . ። አምላክ ፥ ወልደ ፡ . . . . ። ቀርን ፡ እንደ ፡ ዋዌና ፡ እንደ ፡ አው ፡ ነው ፤ ሞክሼና ፡ ባዕድ ፡ አስረጅ ፡ ወይም ፡ ተወላጅ ፡ ስለ ፡ ኾነ ፡ ተጥፎ ፡ በማይነበብ ፥ በ ፡ ዘይቤ ፡ በሚያሰኝ ፡ ነገር ፡ በትርፍ ፡ ንባብ ፡ ይገባል ። ምሳሌ ፤ ወንጌል ፡ ብሂል ፡ በልሳነ ፡ ጽርእ ፤ ወትርጓሜሃ ፡ ስብከት ፡ (ብሥራት) ። እስመ ፡ ክርስቶስ ፡ ብሂል ፡ ቅቡዕ ፡ (መሲሕ) ። ፲፱፻፷፩ ፡ (፵፪) ፡ ዓ ፡ ም ፡ በግስም ፡ ሲገባ ፡ ጽሒፍ ፤ (ጸሐፈ ፡ ይጽሕፍ ፡ ይጽሐፍ) ፡ መጣፍ ፡ አጣጣፍ ። ጸሓፊ ፤ (ፊት ፡ ፍያን ፡ ያት ፤ ጸሐፍት) ፡ ያሰኛል ። አቅርንት ፡ ያንዱን ፡ ደራሲ ፡ ቃል ፡ ከሌላው ፡ ድርሰት ፡ ለመለየት ፡ ባለድርሳኑ ፡ ሌሎች ፡ ከደረሱት ፡ ከድርሳን ፡ ከተግሣጽ ፡ አብዝቶ ፡ አሳንሶ ፡ በሚጠቅሰው ፡ ቃል ፡ በጥቅስና ፡ በስሑጽ ፡ ይገባል ፤ ጥቅስና ፡ ስሑጽ ፡ የንባብ ፡ የምስጢር ፡ የድርሰት ፡ ማቅኛ ፡ ስለ ፡ ኾኑ ፥ እነዚህ ፡ ፪ቱ ፡ ፩ ፡ ወገን ፡ ናቸው ። ምሳሌ ፤ ከመ ፡ ዝ ፡ ነአምን ፡ ወከመ ፡ ዝ ፡ ንትአመን ፤ ወንበል ፡ ጸሎተ ፡ ሃይማኖት ። «ነአምን ፡ በአሐዱ ፡ አምላክ ፡ . . . . ። ወንሴፎ ፡ ትንሣኤ ፡ ሙታን ፤ ወሕይወተ ፡ ዘይመጽእ ፡ ለዓለመ ፡ ዓለም» ። ንግበእኬ ፡ ኀበ ፡ ጥንተ ፡ ነገር ።

፴፰ ፤ ጣፎችና ፡ ዐታሞች ፡ የፊደላትን ፡ ዘር ፡ በብራና ፡ ማሕፀናቸው ፡ በወረቀት ፡ ሰፋድላቸው ፡ ከመምህራን ፡ እየተቀበሉ ፡ ፀንሰውና ፡ አምጠው ፡ በቀለም ፡ በብርዕ ፡ የሚወልዱት ፡ የጥፈትና ፡ የመጻሕፍት ፡ መልክ ፡ ድርሰቱ ፡ መድበሉ ፡ ከምሉ ፡ በክፍሉ ፡ ይህ ፡ ነው ። ይህ ፡ የጣፍነው ፡ ኹሉ ፡ ስምና ፡ መልክ ፡ ታትሞ ፡ ተጥፎ ፡ ተጠርዞና ፡ ታፍፎ ፥ ድጕሱና ፡ ማኅደሩ ፡ ተከናውኖ ፥ ግዙፍና ፡ ምእዙን ፡ ኹኖ ፡ ሥራው ፡ ካለቀለት ፡ በኋላ ፤ መጽሐፉ ፡ በጽላት ፥ ማኅደሩ ፡ በታቦት ፥ ዙሪያው ፡ በ፬ቱ ፡ ማእዝን ፡ ይመሰላል ። ከዚያውም ፡ ዘንድ ፥ ቀኙ ፡ የምሥራቅ ፡ ግራው ፡ የምዕራብ ፥ ራሱ ፡ የሰሜን ፡ እግሩ ፡ የደቡብ ፤ ፬ቱ ፡ ቀርን ፡ በነዚህ ፡ ውስጥ ፡ ያለው ፡ የንኡስ ፡ ማእዝን ፡ ምሳሌ ፡ ነው ።

፴፱ ፤ ለንባቡም ፡ ትምርት ፥ ለስልቱና ፡ ለማዕርጉ ፡ እንዳሪቱ ፡ ጸዋትወ ፡ ዜማ ፡ ፭ ፡ ክፍል ፡ አለው ፤ ፩ኛው ፡ ቍጥር ፥ ፪ኛው ፡ ግእዝ ፥ ፫ኛው ፡ ወርድ ፥ ፬ኛው ፡ ዐቢይ ፥ ፭ኛው ፡ ድጋም ፡ ወይም ፡ ማነብነብ ፡ ይባላል ። እነዚህም ፡ ፭ቱ ፡ ክፍሎች ፡ ጸዋትወ ፡ ንባብ ፡ ተብለው ፡ ኹሉም ፡ በሕፃን ፡ አካኼድ ፡ ይመሰላሉ ፤ ቍጥር ፡ እንደ ፡ መንኰቀቅ ፥ ግእዝ ፡ እንደ ፡ መዳኽ ፡ ነው ፤ እነዚህ ፡ ፪ቱ ፡ በሣር ፡ በሥንጥር ፡ ይነገራሉ ። ቍጥር ፡ በኖኅትና ፡ በኖኅት ፡ መካከል ፡ ያለውን ፡ የያንዳንዱን ፡ ፊደል ፡ ራስ ፡ ራሱን ፡ በሣር ፡ እየነኩ ፥ ፩ ፡ ፪ ፡ ፫ ፡ እንደ ፡ ማለት ፡ ኹሉ ፡ ስም ፡ ስሙን ፡ ለይቶ ፡ መጥራት ፡ ነው ። ግእዝ ፥ ከነቍጥ ፡ እስከ ፡ ነቍጥ ፡ በያንዳንዱ ፡ ስክ ፡ ያሉትን ፡ ፊደሎች ፡ እንደ ፡ መሠረዝ ፡ ሣሩን ፡ በላያቸው ፡ እያሳለፉ ፡ በቅርብ ፡ በቅርቡ ፡ ማጋጠም ፡ ነው ። ወርድ ፥ ዘርፍና ፡ ባለቤት ፡ ሳቢና ፡ ተሳቢ ፡ በማዛረፍና ፡ በማናበብ ፡ የሚወድቅና ፡ የሚነሣ ፡ የሚጠብቅና ፡ የሚላላ ፡ ቀለም ፡ ለይቶ ፡ በሐዘንዚን ፡ ቃል ፡ እየጮኹና ፡ እያለፉ ፡ እየተደገፉ ፡ ማንበብ ፡ ነው ። ይኸውም ፡ እጅን ፡ ተይዞ ፡ አቱ ፡ ሥግሩ ፡ ታቱ ፡ ሥግሩ ፥ ወይም ፡ ዳዴ ፡ ዳዴ ፥ አንድ ፡ ኹለት ፡ እየተባሉ ፡ በመኼድና ፡ በመራመድ ፥ በማንገር

ገር ፡ በመወናከር ፡ ይመሰላል ፡፡ አቡጊዳና ፡ ወርድ ፡ ንባብ ፡ ለተማሪ ፡ በጣም ፡ ይጠቅማሉ ፤ አለነዚህ ፡ አለኹለቱ ፡ በፊደል ፡ በንባብ ፡ ቶሎ ፡ መሠልጠን ፡ አይቻልም ፡፡ ዐቢይ ፡ ንባብ ፥ ራስን ፡ ችሎ ፡ እየተቀናጡ ፡ ቶሎ ፡ ቶሎ ፡ እንደ ፡ መኼድ ፡ ኹሉ ፤ በነቍጥ ፡ በሠረዝ ፡ የተለየውን ፡ ቃል ፡ ከነጥብ ፡ እስከ ፡ ነጥብ ፡ እንደሚገባው ፡ እያሰሙ ፡ እያሰ ማሙ ፡ ማንበብ ፡ ነው ፡፡ ድጋም ፡ ከደጋሚው ፡ በቀር ፡ ሌላ ፡ የማይሰማው ፡ ስለ ፡ ኾነ ፡ በሩጫ ፡ አካኼድ ፡ ይመሰላል ፡፡ የሚጠብቅና ፡ የሚላላ ፡ ቀለም ፡ ያልነውም ፡ ልዩ ፡ ልዩነቱ ፡ በንባብ ፡ ብቻ ፡ አይዶለም ፥ በምስጢርም ፡ እንጂ ፤ መላላት ፡ የሥራ ውን ፡ ቀሊልነትና ፡ ገርነት ፥ መጥበቅ ፡ ግን ፡ ከባድነቱን ፥ በኀይልና ፡ በግድ ፡ መኾ ኑን ፡ ያሳያል ፡፡ ከግእዝም ፡ ይልቅ ፡ ዐማርኛ ፥ ገደለ ፡ ሰበረ ፥ ዐረሰ ፡ ቈፈረ ፥ ዐጨደ ፡ ነቀለ ፡ እያሰኘ ፡ አጥብቆ ፡ ያሳያል ፤ ዕብራይስጥም ፡ እንዳማርኛ ፡ ነው ፡፡ ጸዋትወ ፡ ፊደል ፡ የተባለው ፡ የሰዋስውና ፡ የግስ ፡ መቅድም ፡ እስከዚህ ፡ ነው ፡፡

## የታሪክ ፡ መርገፍ ፡ የመቅድም ፡ አጫዋች ፡፡

ውዳሴ ፡ ዕበያ ፡ ወክብራ ፡ ለብእሲተ ፡ ሰማይ ፡ ፊደል ፡ አርአያ ፡ ድንግል ፡፡

፴ ፤ ንግባእኬ ፡ ኀበ ፡ ጥንተ ፡ ነገር ፡ ወባህል ፤ ወንሕትታ ፡ ከዕበ ፡ ለቅድስት ፡ ፊደል ፥ በዘዘ ፡ ዚአሁ ፡ አርአያ ፡ ወዘዘ ፡ ዚአሁ ፡ አምሳል ፡ እንዘ ፡ ኪያሃ ፡ ንሜስል ፡ ወናስተማስል ፡፡ በመኑ ፡ በአምሳለ ፡ መኑ ፡ ትትሜሰል ፡ ፊደል ፤ በምድረ ፡ ሎዛኑ ፡ ወዳቤር ፡ ሀገረ ፡ ሰዋስው ፡ ወመጽሐፍ ፥ ወሚመ ፡ በሲና ፡ ጉባኤ ፡ መላእክት ፡ አእ ላፍ ፤ አው ፡ በጽዮን ፡ ሀገረ ፡ ዳዊት ፥ ወእመ ፡ አኮ ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ቅድስት ፤ ጽዮ ንሰ ፡ ወሳሌም ፥ መካነ ፡ ርእሱ ፡ ለአዳም ፥ ወመክፈልተ ፡ ርስቱ ፡ ለሴም ፤ እስመ ፡ እም ጽዮን ፡ ይወፅእ ፡ ሕግ ፡ ወቃለ ፡ እግዚአብሔር ፡ እምኢየሩሳሌም ፡ በከመ ፡ ጽሑፍ ፡፡ ፊደልሰ ፡ አሚን ፡ መሠረተ ፡ ነገር ፡ ወጥንት ፤ ወከልአኒሃ ፡ መጻሕፍት ፡ ሕንጻ ፡ ወንድቅ ፡ ከመ ፡ እንተ ፡ ምግባር ፡ ወትሩፋት ፡፡ ሥረዊሃ ፡ ሥርወ ፡ ቀለማት ፥ ዐቃቢረ ፡ ፈውስ ፡ ወመድኀኒት ፡ ዘመህሮ ፡ ለኖኅ ፡ አሐዱ ፡ እመላእክት ፡ ዐቃቤ ፡ ሥራይ ፡ ታቦት ፤ ወሥ ርወ ፡ ነገራ ፡ ይቀውም ፡ በስምዐ ፡ ሠለስቱ ፡ ገጻት ፡ ከመ ፡ ሥርወ ፡ እሴይ ፡ ወዳዊት ፡፡ ሠናይትኬ ፡ ሠናይት ፡ እምኵሎን ፡ ሠናያት ፥ ላሕየ ፡ ፈጣሪ ፡ ሕያው ፡ ወሥነ ፡ ኵሉ ፡ ፍጥ ረት ፤ እስመ ፡ ጕላቲሃ ፡ ዕሥራ ፡ ወክልኤት ፤ ወሱባዔሃኒ ፡ ፍጹም ፡ ሱባዔ ፡ ዕለት ፡ እም ዕለተ ፡ እሑድ ፡ ግእዝ ፡ እስከነ ፡ ሳብዕት ፡፡ አርአያሃኒ ፡ አዳም ፡ አርአያ ፡ ሥላሴ ፡ ቅድስት ፤ ወአምሳሊሃኒ ፡ ንዮሙ ፡ ዐሠርቱ ፡ ቃላት ፥ ወሰሌዳቲሃ ፡ ጽላት ፡፡ ጽሕፈታሂ ፡ መንክር ፡ ዘእ ግዚአብሔር ፡ ጽሕፈት ፡ በጸፍጸፈ ፡ ሰማይ ፡ ሳብዕ ፡ ሰሌዳ ፡ እሳት ፤ ወግብረታሂ ፡ ዕጹብ ፡ ግብረ ፡ መለኮት ፡ እምኀበ ፡ አልበ ፡ ማየ ፡ ሕመት ፡፡ ታበታ ፡ ደቂቀ ፡ ሴት ፤ ወደብተራሃ ፡ ሰብአ ፡ ትካት ፡፡ አዕማዲሃሰ ፡ ኖኅ ፡ ወሴም ፡ ካም ፡ ወያፌት ፤ ወምዕማዲሃ ፡ ነቢያት ፡ ወካ ህናት ፡፡ አርእስቲሃ ፡ አብርሃም ፡ ይሥሐቅ ፡ ወያዕቆብ ፡ አርእስተ ፡ አበው ፡ ቀደምት ፤ ወደመና ፡ ርእሳ ፡ ብሩህ ፡ መንፈስ ፡ ትንቢት ፡፡ አረፋቲሃ ፡ ዘዕንቍ ፡ እእባነ ፡ ልብሰ ፡ አሮን ፡ ሕስት ፤ ወመሠረታ ፡ ዘጽድቅ ፡ ኰኵሐ ፡ ሃይማኖት ፤ ወኰኵሕሰ ፡ ክርስቶስ ፡ ሊቀ ፡ ካህናት ፡ እብነ ፡ ርእሰ ፡ ኵሉ ፡ ማእዘንት ፡ ዘመነንዎ ፡ ነደቅት ፡፡ ቅድስተ ፡

ቅዱሳን፡አበው፡ነቅዐ፡ምስጢራት፤ወመንበረ፡ስብሐት፡ድልው፡እምአፈ፡ደቂቀ፡ወሕፃናት ። ኵለንታሃ፡ወርቅ፡ተቋመ፡ማኅቶት፥ወመድሎተ፡ወርቃ፡ጽሩይ፡መጠነ፡መክሊት፤ አዕጹቂሃኒ፡አዕጹቀ፡ዘይት፡አምሳለ፡ሰብዐቱ፡ሀብታት፥ወመሳውሪሃ፡አእላፍ፡ብሩሃነ፡አልባብ፡ጸሐፍት ። ጸዳለ፡ብርሃና፡ወሥና፡ብዝኀ፡ትምህርት፤ወብርሃናስ፡ውእቱ፡ገባሬ፡ብርሃናት፡ዐበይት፡ዘበጸዳሉ፡ብርሃኑ፡ሰሰለ፡ጽልመት ።

፶፩ ፤ ጥብልልት፡ራእዩ፡ወፋእሙ፡ለበላዔ፡መጽሐፍ፡ሕዝቅኤል፤ወስቴ፡ጽዋዑ፡ለዕዝራ፡ደመ፡ሕብረ፡እሳት፡አስካል፡ዘያውዒ፡ልበ፡ወያንበለብል ። ይእቲኬ፡ድንግል፡ወላዲተ፡ቃል፡በብሥራተ፡መልአክ፡ገብርኤል፤መጥበቢተ፡አብዳን፡ኖሎት፡ወሰብአ፡ሰገል፡እለ፡ውስተ፡ዓለም፡ኀል፤እስመ፡ሀላዌሁ፡ለቃል፡ሀላዌ፡ፊደል፡በከመ፡ተነበየ፡ዳንኤል፡ወፈከረ፡ላቲ፡በብዙኅ፡አምሳል ። ወኮከበኒ፡ታው፡ጽዱል፡ኮከበ፡ወንጌል፡ዘቦቱ፡ትእምርተ፡መስቀል ።　አበዊነሂ፡ይብልዋ፡በዘአበዊሆሙ፡በህል፡ወለቱ፡ለሄኖስ፡ንእስተ፡አካል፡ወእኅተ፡አቡሁ፡ለመላልኤል ። ፍኅርቱ፡ለያሬድ፡ልሂቅ፡ብሉየ፡መዋዕል፤ወመፅመርተ፡ብርዑ፡ለሔኖክ፡ጸሓፌ፡ጥበቡ፡ለልዑል ። ሱታፌ፡ንባቡ፡ወቃሉ፡ለማቱሳላ፡ባዕል፤ወፍቅርተ፡ላሜኅ፡ወኖኅ፡ወራዙተ፡ኀይል ።

፶፪ ፤ ልህቅት፡ይእቲ፡እምሰብዓ፡ሊቃናት፤ወብሊት፡ዘእምቅድመ፡ብሉይ፡ኦሪት ። ሐፃኒተ፡ሙሴ፡ሕፃን፡ዘአኮ፡ይብስተ፡አጥባት፤ወጥልልተ፡ርሥአን፡ዕቤርት፡እሞን፡ለዕቤራተ፡ሕግ፡መጻሕፍት፡ወለአዋልድ፡ንኡሳት፤በከመ፡ተብህለ፡ስሳ፡እማንቱ፡ንግሥታት፡ወሰማንያ፡ዕቁባት፥አዋልድሰ፡እለ፡አልቦን፡ኈልቍ፡ወመስፈርት ። ወላዲቱ፡ለጥበብ፡ሕያው፡ወላዬ፡ሕይወት፤ወእምሔውቱ፡ለነገረ፡ኵሎን፡በሓውርት ። ጽዕዳዌ፡ሥዕርታ፡ክርስቶስ፡ቅቡዐ፡መንፈስ፡ከመ፡ፀምረ፡በግዕ፡ጌዴዎን፡ወከመ፡ሜላት፡ፍሑስ፤ወቂሐተ፡ገጻ፡ልሁብ፡መንፈሰ፡ጸጋሁ፡ለአብ፡መስተፍሥሔ፡ልብ ። ድምድማሃ፡ድሉል፡በመሥዕርተ፡ብርዕ፥ወሕብረ፡ቀለማ፡ጸሊም፡ከመ፡ሕብረ፡ቋዕ፤ወቀይሕ፡ከመ፡ደመ፡በግዕ ።　በእንተዝ፡ትልሒ፡እምፀሓይ፡ወእምኵሉ፡ንብረተ፡ከዋክብት ። እንዘ፡ምስለ፡ብርሃን፡ትትቃወም፡ትትረከብ፡ከመ፡ቀዳማዊት፤ወእንዘ፡በርሥእ፡ሀለወት፡ኵሎ፡ትሔድስ፤ወለትውልደ፡ትውልድ፡ውስተ፡ነፍስ፡ጻድቃን፡ትትፋለስ ።

፶፫ ፤ ይእቲ፡ትኄይስ፡እምዕንቍ፡ክቡር፤ወኵሉ፡ክብር፡ኢመጠና ። ላቲ፡ምክር፡ወዕዘዝ፤ወላቲ፡ጽንዕ፡ወአእምሮ ። ባቲ፡ነገሥት፡ይነግሡ፤ወባቲ፡ኀያላን፡ይጽሕፉ፡ጽድቀ ። ባቲ፡ዐቢያን፡ይከብሩ፤ወባቲ፡መኳንንት፡ይእኅዙ፡ምድረ ። እለ፡ያፈቅርዋ፡ታፈቅር፥ወእለ፡የዐቅብዋ፡ተዐቅብ፤ወእለ፡የኅሥዋ፡ላቲ፡ይረክቡ፡ሞገሰ ። ውስተ፡ፍናወ፡ጽድቅ፡ታንሶሱ፤ወውስተ፡አሠረ፡ጽድቅ፡ትትመየጥ፡ከመ፡ተሀበሙ፡ለእለ፡የአምርዋ፡ጥሪተ፡ወመዛግብቲሆሙ፡ከመ፡ትምላእ፡ተድላ ። ዘኵሎ፡የአምር፡ውእቱ፡የአምራ፤ወዘኵሎ፡ይመልክ፡ውእቱ፡አሠነየ፡

ፍኖታ ። ውእቱ ፡ ወሀበ ፡ ለሄኖስ ፡ ቀኖልዔሁ ፡ ወለቃይናን ፡ ቅዱሱ ። ወእምዝ ፡ አስተ ርአየት ፡ ዲበ ፡ ምድር ፤ ወአንሶሰወት ፡ ውስተ ፡ ዕጓለ ፡ መሕያው ። ናሁ ፡ ሐነጸት ፡ ላቲ ፡ ቤተ ፤ ወአቀመት ፡ ሰብዐተ ፡ አዕማደ ። ዘብሐት ፡ ዘዚአሃ ፡ ጥብሐ ፥ ወቶስሐት ፡ ውስተ ፡ ስያሓ ፡ ዘዚአሃ ፡ ወይና ፤ ወአስተዳለወት ፡ ዘዚአሃ ፡ ማእደ ። ወፈነወት ፡ ዘዚአሃ ፡ አግ ብርተ ፡ በነዋኅ ፡ ስብከት ፡ እንዘ ፡ ትብል ፡ ዘአብድ ፡ ውእቱ ፡ ይትገሐሥ ፡ ኀቤየ ፤ ወለ እለሂ ፡ የሐጽሙ ፡ አእምሮ ፡ ትጼውዕ ፡ እንዘ ፡ ትብል ፥ ንዑ ፡ ብልዑ ፡ ኅብዝትየ ፡ ወስ ተዩ ፡ ወይንየ ፤ ወኅድግዋ ፡ ለእበድ ፡ ወሕየዉ ። ፊደልሰ ፡ ውእቱ ፡ እግዚአብሔር ፡ ዘለክአ ፡ ወእደ ፡ መንፈሱ ፡ ቅዱስ ፡ ዘአስተናበሮ ፡ ወሠርዖ ፥ ዲበ ፡ ዕፀ ፡ መስቀል ፡ ይኩን ፡ ስፉሐ ፡ ሰሌዳ ፡ ተሰብአ ፥ ወምስለ ፡ ኃጥአን ፡ ይትኈለቍ ፡ በሱባዔ ፡ ኅለት ፡ ተኰርዖ ፥ ኢየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ አልፋ ፡ ወዖ ፤ በበ ፡ ስብዕ ፡ ስብዐ ፡ እንበለ ፡ አጽርዖ ፡ እስመ ፡ ኵሉ ፡ ትውልድ ፡ ያስተበፅዖ ፥ በአሐዱ ፡ ቃለ ፡ አውሥአ ፡ እንዘ ፡ ይብል ፡ እግ ዚኦ ፡ እግዚኦ ። ሎቱ ፡ ስብሐት ፡ ወአኰቴት ፡ ዕበይ ፡ ወበርከት ፥ ውዳሴ ፡ ወማሕሌት ፤ ክብር ፡ ወብዕል ፡ ዕዘዝ ፡ ወኀይል ፡ ለልዑል ፡ ወሃቤ ፡ ፊደል ፤ ይእዜኒ ፡ ወዘልፈኒ ፡ ወ ለዓለመ ፡ ዓለም ፤ አሜን ። ወለእለሂ ፡ ነሥእዋ ፡ እምኔሁ ፡ በአሚን ፡ ከመ ፡ ጽላተ ፡ ሕግ ፡ ወኪዳን ፡ ወከመ ፡ ቅዱስ ፡ ቍርባን ፥ ለርእሰ ፡ ነቢያት ፡ ሄኖስ ፡ ወለበኵረ ፡ ነገ ሥት ፡ ቃይናን ፤ እስመ ፡ ከመ ፡ ሙሴ ፡ ወአሮን ፡ ክቡዳነ ፡ ክልኤ ፡ አቅርንት ፡ ወአም ርሕተ ፡ ሠናይ ፡ ፍኖት ፡ ለዕዉራነ ፡ ልብ ፡ ሰብአ ፡ ትካት ። ፍኖትሰ ፡ ፊደል ፡ ዕንስተ ፡ ወንጌል ፥ ወስፍሕተ ፡ ማሕፀን ፡ ትንቢት ፡ ለወሊደ ፡ ተስፋ ፡ ሥግው ፡ እምኍልቄ ፡ ዕ ሥራ ፡ ወክልኤቱ ፡ ዘመደ ፡ ፍጥረት ፡ አበው ፥ ወእምዝርዐ ፡ ያዕቆብ ፡ ሰዋስው ።

## ዐጭርና ፡ ቍርጭኝ ፡ ሰዋስው ፡

የመምህራን ፡ ዐይን ፡ ያዕቆብ ፡ እንደ ፡ ረኸሙ ፡ አጥርቶና ፡ ቀምሎ ፡
ያላየው ፥ ቀርበም ፡ እንደ ፡ ሐኪም ፡ ያልዳሰሰውና ፡ ያልፈወሰው ።

ሰዋስው ፡ ማለት ፡ ዘይቤው ፡ መሰላል ፡ ማለት ፡ ነው ፤ እሙን ፡ ትርጓሜው ፡ ግን ፡ የግእዝ ፡ ቋንቋ ፡ ዐዋጅ ፥ ያሰካኩና ፡ ያጣጣፉ ፡ ያነጋገሩ ፡ ፈርጅ ፥ የንባቡ ፡ ኹሉ ፡ እ ጅና ፡ ፍንጅ ፥ አስተሳሰሩና ፡ አፈታቱ ፡ ተለይቶ ፡ የሚታወቅበት ፡ የትምርት ፡ ደንብ ፡ ፍርድና ፡ አገባብ ፡ ማለት ፡ ነው ፤ ፍትሐ ፡ ነገሥት ፡ እንደ ፡ ማለት ፡ ኹሉ ።

አዝመራ ፡ ታጭዶ ፡ ሲሰበሰብ ፡ ብዙው ፡ አገዳ ፡ ፩ ፡ እስር ፡ ነዶ ፥ ብዙው ፡ ነዶ ፡ ፩ ፡ ሙሉ ፡ ዕቅፍ ፥ ብዙው ፡ ዕቅፍ ፡ ፩ ፡ ጕቶ ፥ ብዙው ፡ ጕቶ ፡ ፩ ፡ ታላቅ ፡ ክምር ፡ እንዲ ኾን ፤ የሰዋስውም ፡ ክፍል ፡ እንዲሀ ፡ ነው ፤ ምዕራፍ ፡ በታላቅ ፡ ክምር ፡ ይመሰላል ። ብዙው ፡ ብትን ፡ ቃል ፡ እንደ ፡ ሥነ ፡ ፍጥረት ፡ በየወገኑና ፡ በያይነቱ ፡ ሲሰበሰብና ፡ ሲ ለቀም ፡ ነዶውና ፡ ዕቅፉ ፡ ጕቶው ፡ በ፫ ፡ ዐይነት ፡ ቍጥር ፡ ተቈጥሯል ፤ ብትኑ ፡ ቃል ፡ በነዶው ፡ ቍጥር ፥ ነዶው ፡ ቃል ፡ በዕርከን ፥ ዕርከንም ፡ በዐቢይ ፡ ክፍል ፡ ተጠቅልሎ ፡ ፫ ፡ ብቻ ፡ ኾኗል ። በያንዳንዱ ፡ ክፍል ፡ ውስጥ ፡ የሚገኝ ፡ አርእስተ ፡ ቃል ፡ ንኡስ ፡

ክፍል ፡ እንደ ፡ መኾኑ ፡ ዕርከን ፡ ተብሏል ፤ ፩ ፡ ክፍል ፡ ትምርት ፡ ማለት ፡ ነው ፤ ፩ ፡ ሙሉ ፡ ዕቅፍ ፡ እንደ ፡ ማለት ። ከ፯ቱ ፡ ደግሞ ፡ ፬ቱና ፡ ፫ቱ ፡ አንዳንድ ፡ ወገን ፡ ኹነው ፡ በ፪ ፡ ምዕራፍ ፡ ይከፈላሉ ፤ ክፍላቸውና ፡ ስማቸውም ፡ ይህ ፡ ነው ።

የሰዋስው ፡ ክፍሎች ፡ ስምና ፡ ተራ ።

መዠመሪያ ፡ ምዕራፍ ፡ ባላ፬ ፡ ክፍል ።

፩ኛ ፡ ክፍል ፡ ጸዋትወ ፡ ቅምር ፡ ባለብዙ ፡ ሕብር ።
፪ኛ ፡ ክፍል ፡ ጸዋትወ ፡ ርባ ፡ የሰዋስው ፡ ሆድና ፡ ዠርባ ።
፫ኛ ፡ ክፍል ፡ ጸዋትወ ፡ ጥሬ ፡ የርባታ ፡ ቅንጣትና ፡ ፍሬ ።
፬ኛ ፡ ክፍል ፡ ጸዋትወ ፡ ቅጽል ፡ ባለቤት ፡ አከል ።

፪ኛ ፡ ምዕራፍ ፡ ባለ፫ ፡ ክፍል ።

፭ኛ ፡ ክፍል ፡ ጸዋትወ ፡ ንባብ ፡ ሳቢና ፡ ተሳቢ ፡ ተናባቢ ።
፮ኛ ፡ ክፍል ፡ ጸዋትወ ፡ አገባብ ፡ የዘርና ፡ የነባር ፡ ሕንባብ ።
፯ኛ ፡ ክፍል ፡ ጸዋትወ ፡ ቅኔ ፡ የሠምና ፡ የወርቅ ፡ ዡርጓኔ ።

፫ኛ ፡ ምዕራፍ ፡ ጸዋትወ ፡ ግስ ፡

ባለ፳፯ ፡ ክፍልና ፡ ራስ ፡ ከአ ፡ እስከ ፡ ፐ ፡ ድረስ ።

ጸዋትውም ፡ ማለት ፡ ጓዝና ፡ ወገን ፡ ቤት ፡ ሰብ ፡ ማለት ፡ ነው ፤ ጸዋትወ ፡ ቀዳሴ ፡ እንዲሉ ። ያጭሩ ፡ ሰዋስው ፡ ልክና ፡ መልክ ፥ ወርዱና ፡ ቁመቱ ፡ አርእስቱ ፡ ይህ ፡ ነው ። የቀረውን ፡ በየነዶውና ፡ በየቅፉ ፡ በየጕችው ፡ ቃል ፡ ተመልከት ፤ አንዱ ፡ ክፍል ፡ ላንዱ ፡ መቅድምና ፡ አርእስት ፡ እየኾነ ፡ ሰዋስውነቱን ፡ ስንስለት ፡ አድርጎ ፡ ያሳይ ኻል ። ከዚህም ፡ ሰዋስው ፡ የቀረውን ፡ ረዥም ፡ ትምርት ፡ ኅሊናችን ፡ ዐጥሮ ፡ ስላልደረሰበት ፡ ለኋላ ፡ ልጆች ፡ ትተነዋል ፡ (ማቴ፯ ፡ ፯ና ፡ ፰) ።

መዠመሪያ ፡ ምዕራፍ ፡ ባለ፬ ፡ ክፍል ፡ ጎረ ፡ ቤተ ፡ ወንጌል ።

፩ኛ ፡ ክፍል ።

የሰዋስው ፡ ዐዋጅ ፡ ርባ ፡ ቅምር ።

የፍጥረት ፡ ኹሉ ፡ ዐይነት ፡ ፪ ፡ ፪ ፡ ብቻ ፡ እንደ ፡ ኾነ ፡ ያውም ፡ ወንድና ፡ ሴት ፡ ተባትና ፡ እንስት ፡ እንዲባል ፤ ሰዋስው ፡ ተብሎ ፡ የሚጠራ ፡ የቋንቋም ፡ ዐይነት ፡ ፪ ፡ ነው ፤ ዘርና ፡ ነባር ፥ ወይም ፡ ስምና ፡ ግብር ። ወንድና ፡ ተባት ፡ ሴትና ፡ እንስት ፡ አንዳንድ ፡ ወገን ፡ ኹነው ፡ በ፪ነት ፡ እንዲታዩ ፥ እነዚህም ፡ ፬ቱ ፡ ስሞች ፡ ዘርና ፡ ግብር ፡ ነባርና ፡ ስም ፡ አንዳንድ ፡ ወገን ፡ ናቸው ። ፪ኛም ፡ የመሰላል ፡ ዕርከን ፡ ብዙ ፡ ሲኾን ፡ በ፪ ፡ አዕማድ ፡ እንዲወሰን ፤ የቋንቋም ፡ ትምርት ፡ ስሙና ፡ ክፍሉ ፥ ስልቱና ፡ ባህሉ ፡ ብዙ ፡ ሲኾን ፡ ዐይነቱና ፡ ሕብሩ ፡ አርእስተ ፡ ነገሩ ፡ በነዚህ ፡ በ፪ቱ ፡ ብቻ ፡ ተወስኗል ፤ ከስ ምና ፡ ከግብር ፡ አይወጣም ። ሲዘረዘሩ ፡ ግን ፡ አንቀጽና ፡ ርባታ ፥ ዝርዝር ፥ ቅጽልና ፡

ጥሬ ፥ አገባብ ፥ ሠምና ፡ ወርቅ ፥ ሙሻዘር ፥ ሠረዝ ፥ አንጻር ፡ ተብለው ፡ ፲ ፡ ይኾናሉ ፤ ዝርዝር ፡ ከርባታ ፥ አገባብ ፡ ከጥሬ ፡ ሲደረቡ ፡ ግን ፡ ፳ ፡ ብቻ ፡ ኹነው ፡ ይቀራሉ ። የሰዋስውን ፡ ክፍል ፡ ዝቅ ፡ ብለው ፡ ፫ና ፡ ፬ ፡ ፮ ፥ ከፍ ፡ ብለው ፡ ፲፪ና ፡ ፲፰ ፡ የሚሉ ፡ አሉ ።

መዠመሪያ ፡ ዕርከን ፡ ወይም ፡ ቀዳማይ ።

የዘርና ፡ የነበር ፡ ጠባይ ።

ዘር ።

፩ ፤ ነጠላ ፡ ግስን ፡ ከነርባው ፡ የሚያስገኝ ፥ ጥሬ ፡ ዘርን ፡ ኹሉ ፡ የሚወልድ ፡ በሊዕ ፡ ሰትይ ፡ ጸጊብ ፡ ሰኪር ፡ መዊት ፡ ሐዪው ፡ እያለ ፡ በሦስት ፡ ፊደል ፡ በቅሎ ፡ የሚኼድ ፥ ይህን ፡ የመሰለ ፡ ኀጠተ ፡ ቃል ፥ አባት ፡ ዘር ፡ ይባላል ፤ አባትነቱም ፡ አዳምን ፡ ይመስላል ። አባት ፡ ዘር ፥ ርሱ ፡ ራሱ ፡ እንደ ፡ ሥር ፡ ኹኖ ፡ ሌላውን ፡ ፍሬ ፡ ቃል ፡ ቢያስገኝ ፡ እንጂ ፡ ለርሱ ፡ አስገኝና ፡ አባት ፡ የለውም ። ፪ኛም ፡ ሥረ ፡ ነገር ፡ መሠረተ ፡ ቃል ፡ ስለ ፡ ኾነ ፥ አርእስት ፡ ይባላል ። ፫ኛም ፡ ዐጕል ፡ አንቀጽ ፡ ስለ ፡ ኾነ ፥ ንኡስ ፡ ይባላል ። ስሞቹ ፡ እንደ ፡ ፊደሎቹ ፡ ፫ ፡ ናቸው ፤ አባት ፡ ዘር ፥ አርእስት ፥ ንኡስ ፡ አንቀጽ ።

፪ ፤ ዘር ፡ በቋንቋ ፡ ኹሉ ፡ የግስ ፡ ጥንት ፡ የርባ ፡ መሠረት ፡ ስለ ፡ ኾነ ፥ ከአናቅጽ ፡ በፊት ፡ ይጣፋል ፤ ከርባታ ፡ በፊት ፡ ይነገራል ። ጣፊም ፡ አንባቢም ፡ ወንጌል ፡ ዘዮሐንስ ፡ ሳይል ፡ ቀዳሚሁ ፡ ቃል ፡ እንዳይል ፤ አርእስትን ፡ በጥፈትም ፡ በመነገርም ፡ ንባብ ፡ እንዳይቀድመው ፥ ዘርንም ፡ አንቀጽና ፡ ጥሬ ፡ አይቀድሙትም ። የዚህ ፡ መጽሐፈ ፡ ግስ ፡ ቀዋሚ ፡ ግብሩ ፡ ደገኛ ፡ ነገሩ ፡ ይህ ፡ ነው ፤ እናት ፡ ዘር ፡ ሳትቀበል ፡ እንዳትፀንስ ፡ ርሱም ፡ ዘር ፡ ሳያስቀድም ፡ አንቀጽ ፡ አይጥፍም ። ምንጩን ፡ አሳይቶ ፡ ውሃውን ፥ ዛፉን ፡ አሳይቶ ፡ ፍሬውን ፡ እንደ ፡ መስጠት ፡ ኹሉ ፥ ዘሩን ፡ በፊት ፡ አንቀጹን ፡ በኋላ ፡ ያመጣዋል ፤ ባፈ ፡ ታሪክም ፡ የቀድሞ ፡ መምህራን ፡ ዘር ፡ ሳያስቀድሙ ፡ አይገሱም ፡ ነበር ፡ ይባላል ።

፫ ፤ ዘር ፡ መባሉም ፡ በምሳሌ ፡ ነው ፤ ዘር ፡ በዘሩት ፡ ጊዜ ፡ አንዱ ፡ ቅንጣት ፡ ብዙ ፡ ቅንጣቶች ፡ እንዲያፈራ ፥ ንኡስ ፡ አንቀጽም ፡ በረቡትና ፡ በገሰሱት ፡ ጊዜ ፡ አንዱ ፡ ቃል ፡ ብዙ ፡ ቃላት ፡ ያፈራልና ፤ ስለዚህ ፡ ዘር ፡ ተባለ ፡ (ዮሐ ፲፪ ፡ ፳፬) ። በዕብራይስጥም ፡ ሾሬሽ ፡ ምቁር ፡ ይባላል ፤ ሥርው ፡ ነቅዕ ፡ ማለት ፡ ነው ፤ ዘር ፡ ከማለት ፡ ጋራ ፡ ይሰማማል ። አማናዊው ፡ የባሕርይ ፡ ስሙ ፡ ግን ፡ ግብር ፡ ይባላል ፤ ግብርነቱም ፡ ሠራተኛው ፡ ያልታወቀለት ፥ ለሠራተኛ ፡ ያልተሰጠ ፥ ገና ፡ ወደ ፡ ፊት ፡ የሚሰጥ ፥ በኀላፊና ፡ በትንቢት ፡ መካከል ፡ የቆመ ፡ ዐጓጕል ፡ ማእከላዊ ፡ ነው ። ዳግመኛም ፡ ካባት ፡ ዘር ፡ የሚገኝ ፡ ጥሬ ፡ ዘር ፥ ስምና ፡ መስም ፥ ርሱም ፡ እንዳባቱ ፡ ሲገሰስ ፥ ዘርነቱ ፡ ወዳንቀጽነት ፡ ተለውጦ ፡ ጥሬ ፡ ግስ ፡ ይኾናል ። ካባቱ ፥ አባት ፡ የመሰለ ፡ የ፫ ፡ ፊደል ፡ ግስ ፡ እንዲገኝ ፥ ከጥሬውም ፡ ጥሬ ፡ የመሰለ ፡ ይገኛል ፤ አገኛኘቱንም ፡ በግስ ፡ አርእስት ፡ ውስጥ ፡ ባ፵፬ ፡ ቍጥር ፡ ተመልከት ።

፬፤ በ፫፡ፊደል፡እግር፡የቆሙ፡ዘርና፡ግስ፡የሚነሡባቸው፡ፊደላት፡ወይም፡ቀለማት፡፫፡ናቸው፤ በላገባቦች፡መራኁት፡ይሏቸዋል፤መክፈቻች፡ማለት፡ነው። እሊሁም፡ግእዝ፡ራብዕ፡ኃምስ፡ሳድስ፡ሳብዕ፡ናቸው፤ ዘርና፡ግስ፡በነዚህ፡ብቻ፡ቢነሡ፡እንጂ፡በካዕብ፡በሣልስ፡አይነሡም። የዘርና፡የግስ፡አነሣሥ፥አከኼድና፡አገሣገሥ፡እንዴት፡እንደ፡ኾነ፡በግስ፡አርእስት፡ተመልከት። የዘር፡መድረሻ፡ወይም፡መጨረሻ፡፪፡ናቸው፤ሳድስና፡ሳብዕ፥ይህም፡ነዊም፡ነቂህ፥ሰብሖ፡ዘምሮ፡እያለ፡በነዚህ፡ብቻ፡መድረሱን፡ያሳያል። ግስ፡ግን፡ምንም፡እንደ፡ዘር፡በላ፫፡መነሻ፡ቢኾን፥በላንድ፡መድረሻ፡ነውና፤ቀደሰ፡ባረከ፡ሤመ፡ጥሕረ፡ሖረ፡እያለ፡በግእዝ፡ብቻ፡ይጨርሳል፤ ይኸውም፡የሩቅ፡ወንድ፡አንቀጽ፡ስለ፡ኾነ፡ነው፤ ግእዝ፡የሩቅ፡ዝርዝር፡ነውና። ሲረባና፡ሲዘረዘር፡ግን፡ከኃምስ፡በቀር፡በሌሎቹ፡ኹሉ፡ይጨርሳል።

፭፤ አባት፡ዘር፡ከ፫ቱ፡ልጆቹ፡(ቀዳማይ፡ካልአይ፡ሣልሳይ)፡ከዐበይት፡አና ቅጽ፡በኋላ፡፬ኛ፡ንኡስ፡አንቀጽ፡ኹኖ፥ቀቲል፡ቀቲሎት፥ቀድሶ፡ቀድሶት፥ባርኮ፡ባርኮት፥ብሂል፡ብሂሎት፡እያለ፡በደጊመ፡ቃል፡መነገሩና፡ምእላድ፡ፊደል፡ትን፡እየጨመረ፡መኼዱ፥ለመዘርዘርና፡ለማዘረፍ፡ለማብዛትና፡ለማብለጥ፡ንባብ፡ለማስጌጥ፡ነው። በዝርዝር፡ጊዜ፥ቀቲልሁ፡ቀቲሎቱ፥ቀድሶሁ፡ቱ፥ባርኮሁ፡ቱ፥ብሂልሁ፡ብሂሎቱ፡ቢል፡እንጂ፥ቀቲሉ፡ቀድሱ፡ባርኩ፡ብሂሉ፡ብሎ፡በዘመድ፡አይዘረዝርም፤ ይህ፡በለ፡ሲያዛርፍ፡ነው። በዘና፡በግእዝ፡ሲያዛርፍ፡ግን፡እንዳለ፡ይገባል፤ይህም፡ቀቲል፡ዘዳዊት፥ዘዳዊት፡ቀቲሎት፥ቀቲለ፡ዳዊት፡ቀቲሎተ፡ዳዊት፡ኀልያድህ፡እያለ፡ሌላውን፡ኹሉ፡ያሳያል። በላገባቦችም፡ለብሂል፡ለ፡የለው፥ለብሂሎት፡ዘ፡የለው፡ብለው፡ያውጃሉ፤ ይህም፡ብሂሉ፡ለዳዊት፥ብሂሎት፡ዘዳዊት፡አለማለቱን፡ያሳያል፤ በብሂል፡ኹሉን፡መናገር፡ነው። ሲያበዛና፡ሲዘረዝርም፥ሀልዎታት፡ሀልዎታቱ፡ቲሁ፡ያሰኛል።

፮፤ ዘር፡ጥንቱን፡ሲፈጠር፡ሲታነጽ፡ሲቀረጽ፡ከ፫፡ፊደል፡በሕርይ፡መገኘቱና፡በ፫፡ፊደል፡ብቻ፡መመሥረቱ፥ወደ፪ና፡ወዳ፬፡አለመውረድ፡አለመውጣቱ፡ስለ፡ምን፡ነው፡ብትል፤እግዜር፡በ፮ኛ፡ቀን፡ንግበር፡ሰብአ፡በአርአያነ፡ወበአምሳሊነ፡ብሎ፡አዳምን፡ሲፈጥር፡ቋንቋውንም፡አርአያና፡አምሳል፡አድርጎታልና፥ስለዚህ፡ነው። ይኸውም፡አነ፡ውእቱ፡አልፋ፡ወዖ፡ወይም፡አሌፍ፡ወታው፡ባለው፡ይታወቃል፡(ራእ፳፪፡፲፫)። ኋላም፡በባቢሎን፡ንዑ፡ንረድ፡ወንክዐው፡ሀየ፡ነገሮሙ፡ከመ፡ኢይስማዕ፡ብእሲ፡ከንፈረ፡ቢጹ፡ብሎ፡የልጆቹን፡ቋንቋ፡ሲለያይ፡ይህ፡የአዳም፡ቋንቋ፡በሴም፡ብቻ፡ቀርቷል፡(ዘፍ፩፡፳፮። ፲፩፡፯)። በሴም፡ዘር፡የቀረ፡ቋንቋው፡ብቻ፡አይዶለም፤ ተስፋውና፡ሃይማኖቱም፡እንጂ። ስለዚህ፡ነገር፡የሴም፡ቋንቋ፡ኹሉ፡ዘሩ፡ሥረ፡ነገሩ፥ዋሕድ፡ቃል፡ሥሉስ፡ፊደል፡እየ ኾነ፡በ፫፡ፊደላት፡ተወስኗል፤ከ፫፡ቅንጣት፡ፊደል፡አይወጣም፤ወደ፡፪፡ፊደል፡አይወርድም። ከዚህ፡የተነሣ፡ፊደሉ፡አርአያ፡አካላት፥ቃሉ፡አምሳለ፡መለኮት፡ተብሏል።

፲ ፤ ግእዝም ፡ ከላይ ፡ ከአዳም ፡ የነቃ ፡ ከታችም ፡ ከኖኅ ፡ የፈለቀ ፡ ሴማዊና ፡ አዳማዊ ፡ ቋንቋ ፡ ስለ ፡ ኾነ ፥ ዘሩን ፡ በኖኅ ፡ ልጆች ፡ አምሳል ፡ ሲሰፍርና ፡ ሲቈጥር ፡ ከ፫ ፡ ፊደላት ፡ አያበልጥም ፤ አያሳንስም ፡፡ ቀቲል ፡ ገቢር ፥ ቀዊም ፡ ሐዊር ፥ ሣርሮ ፡ ሐድሶ ፥ ሐውጾ ፡ ገሥጾ ፡ እያለ ፡ እንደ ፡ ወንድሞቹ ፡ እንዳረብና ፡ እንደ ፡ ሱርስት ፡ እንደ ፡ ዕብራይስጥ ፡ በ፫ ፡ ፊደላት ፡ ይኼዳል ፡፡

«ዋዜማ ፡ ዘሰሜቴ ፡ ሠርጸ ፡ ድንግል ፡፡

አካልከ ፡ ነጋዴ ፡ ሕግ ፡
ለአጥርዮ ፡ ሕማም ፡ ሲሳዩ ፡ ውስተ ፡ ቀራንዮ ፡ ወረደ ፤
ጊዮርጊስ ፡ መብረቀ ፡ ስባሔ ፡ ዘትጸውር ፡ ነደ ፡፡
ወበውስተ ፡ ዓለም ፡ ይዝራዕ ፡ ገቢረ ፡ ተአምር ፡ ዘመደ ፡
ከማድከ ፡ ኖኅ ፡ ሠለስተ ፡ ወለደ ፤
ወበእሉ ፡ ኢወሰከ ፡ ባዕደ» ፡፡

፲፩ ፤ መጻሕፍት ፡ ከጽርእ ፡ ወደ ፡ ግእዝ ፡ ሲመለሱ ፡ ያን ፡ ጊዜ ፡ የገባ ፡ የሰባ ፡ የኖባ ፥ የጽርእ ፡ የቀብጥ ፡ ቃል ፡ የኋላ ፡ ቅጥል ፡ ካልኾነ ፡ በቀር ፥ ከለዳዊና ፡ ዮቅጣናዊ ፡ ሕምያራዊ ፡ ለሚባለው ፡ ለጥንታዊው ፡ ግእዝ ፡ ከዕብራይስጥ ፡ ልዩነት ፡ የለውም ፡፡ ኋላ ፡ ግን ፡ በታደሰ ፡ ጊዜ ፡ ብዙ ፡ ባዕድ ፡ ቋንቋ ፡ ገብቶበታል ፤ ባዕድ ፡ የተባለም ፡ የካ ምና ፡ የያፌት ፡ ቋንቋ ፡ ነው ፡፡ የሴም ፡ ቋንቋ ፡ ግን ፡ ምንም ፡ ከ፫ ፡ ከ፬ ፡ ቢከፈል ፡ ነቁ ፡ ሥር ፡ መሠረቱ ፡ እንደ ፡ ምንጭ ፡ እንደ ፡ ዛፍ ፡ እንደ ፡ ሕንጻ ፡ አንድ ፡ ስለ ፡ ኾነ ፥ ርስ ፡ በርሱ ፡ ይስማማልና ፤ አንዱ ፡ ላንዱ ፡ ዘመድ ፡ እንጂ ፥ ባዕድ ፡ አይባልም ፡፡ የጐደለው ንም ፡ አንዱ ፡ ካንዱ ፡ ቢወስድ ፡ ብድር ፡ አይኾንም ፥ ገንዘቡ ፡ ነውና ፤ የቅርብ ፡ ዘመድ ፡ ወንድም ፡ እኅት ፡ ወዳጅ ፡ ጎረ ፡ ቤት ፡ እያለ ፡ ከባዕድ ፡ መበደር ፡ አይገባም ፥ ታላቅ ፡ ስንፍና ፡ ነው ፤ ሳይቸገሩም ፡ መበደር ፡ ዝሙት ፡ ይባላል ፡፡

ነባር ፡፡

፲፪ ፤ ዘርነት ፡ የሌለው ፥ ከዘር ፡ ከአንቀጽ ፡ የማይገኝ ፡ የቋንቋ ፡ ቤት ፡ ሰብ ፡ እየ ኾነ ፡ በውጥንቀጥነት ፡ የሚገኝ ፡ ጥሬ ፡ ቃል ፡ ኹሉ ፡ ነባር ፡ ይባላል ፤ ትርጓሜውም ፡ የማይፈልስ ፡ የማይናወጥ ፡ የማይጠፋ ፡ የማይለወጥ ፡ ስም ፡ ማለት ፡ ነው ፡፡ ከነባር ፡ የሚገኝ ፡ ስም ፡ ብቻ ፡ አይዶለም ፥ አንቀጽና ፡ አገባብም ፡ እንጂ ፤ ከዘሩ ፡ ዘር ፡ የመሰለ ፡ አንቀጽ ፡ እንዲገኝ ፥ ከነባሩም ፡ ነባር ፡ የመሰለ ፡ ይገኛል ፡፡ ከባት ፡ ዘር ፡ የሚገኝ ፡ ጥሬ ፡ ዘር ፥ አንቀጽ ፡ እየኾነ ፡ እንዲገሰስ ፡ ግስነቱም ፡ ዲቃላ ፡ እንዲባል ፥ ከነባርም ፡ ጥሬ ፥ አንቀጽ ፡ እየኾነ ፡ የሚገሰስ ፡ ብዙ ፡ ስም ፡ አለ ፤ ነባር ፡ ስም ፡ ኹሉ ፡ እንደ ፡ ዘር ፡ ኹኖ ፡ ሊረባ ፡ ሊገሰስ ፡ አንቀጽ ፡ ሊወጣለት ፡ ይቻላል ፡፡ ይህም ፡ ሰብእ ፡ ብሎ ፡ ተሰብአ ፥ ወይን ፡ ወየነ ፡ አውየነ ፥ እብን ፡ አበነ ፡ አእበነ ፥ ክርስቲያን ፡ ክረስተነ ፥ ደብተራ ፡ ደብ ተረ ፡ ተደብተረ ፡ እያለ ፡ ሌላውን ፡ ኹሉ ፡ ያሰያል ፡፡ ከተጸውዖ ፡ ስም ፡ በቀር ፡ የማይበ ዛና ፡ የማይረባ ፡ የማይገሰስ ፡ ስም ፡ የለም ፤ ከነባር ፡ ስም ፡ የሚወጣ ፡ አንቀጽ ፡ ነባር ፡ ግስ ፡ ይባላል ፡፡

፲ ፤ ነባር ፡ መባሉም ፡ ሥሩና ፡ ምንጩ ፡ ስላልታወቀ ፡ እንጂ ፥ ዘር ፡ የሌለው ፡ ኹኖ ፡ አይዶለም ፤ ልጅ ፡ አላባት ፡ አለናት ፡ እንዳይገኝ ፥ ነባርም ፡ አለዘር ፡ በቅሎ ፡ አይገኝም ። ጥሬ ፡ ዘር ፡ እንደ ፡ ሚስት ፡ ልጅ ፡ ነው ፤ ነባር ፡ ግን ፡ ከባት ፡ ከናቱ ፡ እንደ ሚጣልና ፡ ሌሎች ፡ አንሥተው ፡ እንደሚያሳድጉት ፥ ወይም ፡ እናቱ ፡ ታውቃ ፡ አባቱ ፡ እንደማይታወቅ ፡ ዲቃላ ፡ ነው ። ከዘር ፡ አንቀጽም ፡ እየተዴቀለ ፡ ስሙና ፡ ጠባዩ ፡ ተለውጦ ፡ ነባር ፡ አንቀጽ ፡ የሚባል ፡ አለ ፤ ሐሰወ ፡ ሐሰ ፥ ነዐወ ፡ ነዐ ፥ አበየ ፡ እንቢ ፤ የመሰለው ፡ ኹሉ ፤ የቀረውን ፡ በደቂቅ ፡ ርባታ ፡ ተመልከት ።

፲፩ ፤ ለጥሬ ፡ ለነባር ፡ እንደ ፡ ዘር ፡ እንደ ፡ ግስ ፡ የፊደል ፡ ውሳኔ ፡ የለውም ፤ ከግእዝ ፡ እስከ ፡ ሳብዕ ፡ ባሉት ፡ በ፯ቱ ፡ ኹሉ ፡ ተነሥቶ ፡ ከግእዝ ፡ በቀር ፡ በ፮ቱ ፡ ኹሉ ፡ ይጨርሳል ። ያገባብም ፡ ቃል ፡ አመ ፡ ሶበ ፡ ከመ ፡ ሌላውም ፡ ኹሉ ፡ መድረሻው ፡ ግእዝ ፡ መኾኑ ፡ ሲናበብ ፡ ነው ፡ እንጂ ፥ ሲያርፍና ፡ ሲወድቅ ፡ ሳድስ ፡ ነው ። ከዚህም ፡ አካኼድ ፡ የተነሣ ፡ ነባር ፡ ከዘርና ፡ ከግስ ፡ ተዛንቆ ፥ የፊደሉን ፡ ተራ ፡ ጠብቆ ፥ ተባብሮ ፡ ተጫፍሮ ፡ በንድነት ፡ ይጣፋል ፡ እንጂ ፤ ለብቻው ፡ የተለየ ፡ ቦታ ፡ የለውም ። ያለም ፡ ቋንቋ ፡ ኹሉ ፡ ሲጣፍ ፡ ሲነገር ፡ እንደዚህ ፡ ነው ፤ ነባርን ፡ ከዘር ፡ አይለየውም ። የፊደሉም ፡ ተራ ፡ ሥሩን ፡ መነሻውን ፡ እንጂ ፥ እንደ ፡ መልክና ፡ እንደ ፡ ቅኔ ፡ እንደ ፡ ሙሾና ፡ እንደ ፡ ዘፈን ፡ ግጥም ፡ ጫፉን ፡ መድረሻውን ፡ አይሻም ።　ባለቅኔዎች ፡ ግን ፡ ከቅኔያቸው ፡ እንዲስማማላቸው ፡ መነሻውን ፡ ትተው ፡ መድረሻውን ፡ ብቻ ፡ ይሻሉ ፤ ግሱንም ፡ ሎሐ ፡ ለብሐ ፡ ለስሐ ፡ እያሉ ፡ በቅኔያቸው ፡ መንገድ ፡ ስላስኬዱት ፤ የርባታው ፡ መንገድ ፡ የዘሩና ፡ የነባሩ ፡ አካኼድ ፡ የጥፈቱ ፡ ረገድ ፡ ተበላሽቶ ፡ ካለም ፡ ቋንቋ ፡ መንገድ ፡ ወጥቷል ። የሐ ፡ ግስ ፡ የሚባል ፡ በሐ ፡ የሚነሣ ፡ ነው ፡ እንጂ ፥ በሌላ ፡ ተነሥቶ ፡ በሐ ፡ የሚጨርስ ፡ አይዶለም ፤ የሌላውም ፡ ፊደል ፡ እንዲሁ ፡ ነው ። ዳግመኛም ፡ ፊደልና ፡ ግስ ፡ ፩ ፡ ወገን ፡ ነውና ፤ ፪ቱንም ፡ ያፋለሷቸው ፡ ሰባክያን ፡ ናቸው ፡ ይባላል ፥ አስቀድመን ፡ እንደ ፡ ተናገርን ፡ (መቅ ፡ ፲፭) ።

፲፪ ፤ የርባታውም ፡ መበላሸትና ፡ መሳሳት ፡ በዚህ ፡ ይታወቃል ፤ አመረ ፡ በመላላቱ ፡ የቀተለ ፡ ቤት ፡ ሲኾን ፤ አመረ ፡ (የአምር ፡ ይእምር ፤ አሚር ፡ አሚሮት) ፡ ዐወቀ ፡ በማለት ፡ ፈንታ ፤ አስደራጊውን ፡ አእመረን ፡ መደበኛ ፡ ያ፬ ፡ ፊደል ፡ ግስ ፡ አድርጎ ፤ አእመረ ፡ (የአምር ፡ ያእምር ፤ አእምሮ ፡ ሮት) ፡ አሳወቀ ፡ እንደ ፡ ማለት ፡ ኹሉ ፡ ዐወቀ ፡ እያሉ ፡ በደንገፀ ፡ ቤት ፡ መግሰስና ፡ ማርባት ፡ የስሕተት ፡ ስሕተት ፡ ነው ። አስደራጊውን ፡ መደበኛ ፡ ትንቢቱን ፡ ኀላፊ ፡ ስላሉት ፡ የአእመረና ፡ የይቤ ፡ ርባታ ፡ ከሥር ፡ እስከ ፡ ጫፍ ፡ ተበላሽቷልና ፤ ሌላውንም ፡ እንደነዚህ ፡ እየው ። አእኰተ ፡ አግመረ ፡ አድምዐ ፡ አጥብዐ ፡ አጥመቀ ፡ አልጸቀ ፡ አይድዐ ፡ አርመመ ፡ አዕረፈ ፡ አፍቀረ ፤ ተገበረ ፡ ተወከለ ፡ ተለዐለ ፡ ተሰፈወ ፡ ይህን ፡ የመሰለ ፡ ዐመል ፡ ያለበት ፡ ግሥ ፡ ኹሉ ፡ እንደ ፡ ይቤና ፡ እንደ ፡ አእመረ ፡ ያልታረመ ፡ ያልተጠነቀቀ ፡ ሕገ ፡ ወጥ ፡ ነው ።

፲፫ ፤ አንቀጽ ፡ የሌላቸው ፡ አገባቦችና ፡ የመጠሪያ ፡ ስሞች ፡ ፊደልና ፡ አኃዝም ፡ አንዳንድ ፡ ቅንጣት ፡ ዘሮች ፡ ስለ ፡ ኾኑ ፡ ቍጥራቸውና ፡ ክፍላቸው ፡ ከነባሮች ፡ ነው ። ዘርና ፡ ነባርን ፡ በጥፈት ፡ በትምርት ፡ ለመለየት ፡ በግእዝ ፡ ንባብ ፡ ውስጥ ፡ ያለ ፡ ቍጥ

ርን ፡ አሐድ ፡ ዱ ፤ ክልኤት ፡ ቱ ፤ ዐሥርት ፡ ቱ ፡ እያሉ ፡ ኹሉን ፡ በፊደል ፡ ብቻ ፡ እንጂ ፡ በአኃዝ ፡ ብቻ ፡ ፩ ፡ ፪ ፡ ፫ ፡ ብሎ ፡ ወይም ፡ አኃዝና ፡ ፊደል ፡ አቈራኝቶ ፡ ፩ዱ ፡ ፪ቱ ፡ ፫ቱ ፡ ይልቁንም ፡ ፳ኤል ፡ እያሉ ፡ መጣፍ ፡ አይገባም ፤ የንባቡና ፡ የትርጓሜው ፡ የምስጢሩ ፡ ጣዕም ፡ ይበላሻል ፡፡ በአኃዝ ፡ ሊጣፍ ፡ የሚገባው ፡ ምዕራፍና ፡ ክፍል ፡ በውስጡ ፡ ያ ለው ፡ ነዶ ፡ ቃል ፡ ያማርኛ ፡ ንባብ ፡ ነው ፡ እንጂ ፤ ለግእዝ ፡ ቋንቋ ፡ አይስማማውም ፡፡

## ፪ኛ ፡ ዕርከን ፡፡

## የግስ ፡ ዐመሎች ፡፡

፲፬ ፤ ግስ ፡ ማለት ፡ የቋንቋ ፡ ጓዝ ፡ የዘርና ፡ የነባር ፡ እክት ፡ ወይም ፡ ዕቃ ፡ ግሴት ፡ ማለት ፡ ነው ፤ ሰማይ ፡ ከነግሱ ፡ ምድር ፡ ከነልብሱ ፡ እንዲሉ ÷ ከነጓዙ ፡ ሲሉ ፡፡ የሚያ ጠግበውና ፡ የሚያረካው ፡ እሙን ፡ ትርጓሜው ፡ ግን ፡ ተወራራሽና ፡ ተመላላሽ ፡ ቃል ፡ ማለት ፡ ነው ፡፡ ፩ዱ ፡ አንቀጽ ፡ እስከ ፡ ፹ ፡ ጥሬው ፡ እስከ ፡ ፫ ፡ መደብ ፡ መረባቱና ፡ መ ዘርዘሩ ፡ ያንዱ ፡ ለብዙ ፡ የወንዱ ፡ ለሴት ፡ የሩቁ ፡ ለቅርብ ፡ እየተሰጠ ፡ በመፋለስና ፡ በ መዋረስ ፡ በመመላለስ ፡ ነውና ፡፡ በገሲስ ፡ ዘይቤም ፡ ሲፈቱት ፡ መደቦችና ፡ መደበኞች ፡ ኹነው ፡ የሚዳሰሱና ፡ የሚያዙ ፡ ዐሥሩን ፡ ሰራዊት ፡ ያሳያል ፡ (ቍ፶፯) ፡፡ ለግስ ፡ አከፋፈል ፡ ብዙ ፡ ስም ፡ አለው ፡፡ መዠመሪያ ፡ ትርጓሜና ፡ አፈታት ፡ እንደ ፡ ገጠመው ፡ ሲነገር ፡ ከተማ ፡ ግስ ፤ ፪ኛ ፡ እንደ ፡ ተገኘ ፡ ሲነገር ፡ መንደር ፡ ግስ ፤ ፫ኛ ፡ እንደ ፡ ፊደሉ ፡ ተራ ፡ በየወገኑና ፡ በየቤቱ ፡ በየሰራዊቱ ፡ ሲነገር ፡ ተራ ፡ ግስ ፡ ይባላል ፡፡ የቀረውም ፡ ኋላ ፡ በ፯ኛ ፡ ዕርከን ፡ ይመጣል ፡፡

፲፭ ፤ ነጠላ ፡ ግስ ፡ ከ፪ ፡ ፊደል ፡ አይወርድም ፤ ከ፬ ፡ ፊደል ፡ አይወጣም ፤ ልማ ድና ፡ ባዕድ ፡ ሲጨመር ፡ ግን ፡ ፭ም ፡ ፮ም ፡ ፯ም ፡ ይኾናል ፤ ከ፯ ፡ በላይ ፡ ግን ፡ አይወ ጣም ፤ ይህን ፡ ኋላ ፡ በቦታው ፡ እናመጣዋለን ፡፡ በግስ ፡ ያሉ ፡ ዐመሎች ፡ ፫ ፡ ናቸው ፤ አና ፡ ሀ ÷ ወና ፡ የ ÷ ደጊመ ፡ ቃል ፡፡ አና ፡ ሀ ፡ ስላንድ ÷ ወና ፡ የ ፡ ስላንድ ፡ ይቈጠራሉ ፤ ደጊመ ፡ ቃል ፡ ግን ፡ ለብቻው ፡ ፩ ፡ ነው ፤ እሊህ ፡ ፫ቱ ፡ ዐመሎች ፡ ያሉበት ፡ ግስ ፡ ቤቱን ፡ ሳይለቅ ፡ ድምጥና ፡ መንገድ ፡ ይለውጣል ፡፡ ዐመሎችን ፡ ሕርመት ፡ ወይም ፡ ጸዋትው ፡ የሚሉ ፡ አሉ ፡፡

### ከመላላት ፡ በቀር ፡ መጥበቅ ፡ የሌላቸው ፡ አ—ዐ ፡ ሀ—ሐ—ኀ ፡፡

አና ፡ ሀ ፡ በመካከሉ ፡ ያሉበት ፡ ግስ ፡ የቀተለ ፡ ሰርዌ ፡ አርእስቱ ፡ በግእዝ ፡ ይነሣ ፡ የነበረውን ፡ ለውጦ ፡ ሳድስ ፡ ያደርጋል ፤ ይህም ፡ ልኢክ ፡ ለአከ ÷ ልሒክ ፡ ለሐኰ ፡ ጽዒል ፡ ጸዐለ ÷ ምሂር ፡ መሀረ ÷ ግሒሥ ፡ ገሐሠ ÷ ዝኒር ፡ ዘኀረ ፡ እያለ ፡ ሌላውን ፡ ኹሉ ፡ ያሳያል ፡፡ አንዳንድ ፡ ጊዜም ፡ አንቀጹ ፡ ሳይቀር ፡ ፪ቱንም ፡ በሳድስ ፡ ያስነሣል ፤ ይህም ፡ ንኢድ ፡ ንእደ ÷ ጥዒም ፡ ጥዕመ ÷ ብሂል ፡ ብህለ ÷ ጥሒር ፡ ጥሕረ ÷ ጕሒቍ ፡ ጕሕቈ ÷ ድኂን ፡ ድኅነ ፡ እያለ ፡ መኼዱን ፡ ያሳያል ፡፡ አና ፡ ሀ ፡ ማእከል ፡ ኹነው ፡ እን ዲህ ፡ ከለወጡት ፡ በቀር ፡ ዘርና ፡ አንቀጽ ፡ በሳድስ ፡ ፊደል ፡ አይነሣም ፡፡ ዳግመ ኛም ፡ በመካከሉ ፡ ዐመል ፡ ያለበት ፡ ግስ ፡ እንደ ፡ ኀሥሥት ፡ የሚለዋወጥ ፡ ስለ ፡ ኾነ ፡

ተዝኅረ፡ ተዘኀረ ፥ ተልዕለ፡ ተለዐለ ፥ ተውዕረ፡ ተወዐረ ፥ ተምህረ፡ ተመሀረ ፥ ተክዕወ፡ ተከዐወ፡ እያለ፡ ይገኛል ። በክህለም፡ ያለ፡ ህ፡ እስከ፡ ፳፡ ሰራዊት፡ በካልአይ፡ ኹሉ፡ ይታጣል ፤ ይህም፡ ክህለ፡ ይክል ፥ ክህልከ፡ ትክል ፥ ክህልኩ፡ እክል፡ እያለ፡ ጭራሽ፡ መታጣቱን፡ ያሳያል ። የብህለም፡ አካኼድ፡ እንደ፡ ክህለ፡ ነው ፤ ህን፡ በካልአይ፡ ኹሉ፡ ይውጣል ። ይህም፡ ብህለ፡ ይብል ፥ ብህልኩ፡ እብል ፥ ብህልነ፡ ንብል፡ ማለቱን፡ መደብ፡ አድርጎ፡ ይብህል፡ እብህል፡ ንብህል፡ አለማለቱን፡ ያሳያል ። በቤለ፡ አካኼድ፡ ግን፡ መሪና፡ ተከታይ፡ የሌለው፡ ባሕታዊ፡ ፍኖት፡ ነው ፤ ቤለን፡ ተመልከት ።

፲፮ ፤ ፫ኛም፡ ከቀተለ፡ እስከ፡ ማህረከ፡ ባሉት፡ በ፯ቱ፡ አርእስት፡ አና፡ ሀ፡ መድረሻ፡ ሲኾኑ፡ ፪ኛው፡ ፊደል፡ ወይም፡ ፫ኛው፡ ግእዝ፡ ይኾን፡ የነበረውን፡ ለውጠው፡ ሳድስ፡ ያደርጉታል ። ይህም፡ ገብአ፡ ፈርሀ ፥ ጸውዐ፡ ሰብሐ ፥ ሰርሐ፡ ሣርን፡ ባልሐ ፥ ቈቅሐ፡ ቶስሐ፡ ሞቅሐ ፥ ገፍትዐ፡ ቀሕቅሐ ፥ ላዕልዐ፡ ላሕልሐ፡ እያለ፡ ሌላውን፡ ኹሉ፡ ያሳያል ። ፯ቱ፡ አርእስቶች፡ ማን፡ ማን፡ እንደ፡ ኾኑ፡ ባመል፡ መጨረሻ፡ ተመልከት ።   ፬ኛም፡ በ፫፡ ፊደል፡ ግስ ፥ ከዚያውም፡ በቀተለ፡ ቤት፡ በሣልሳይ፡ አንቀጽ፡ ሳድስ፡ ይኾን፡ የነበረውን ፥ ይግበእ፡ ይፍራህ ፥ ይብላዕ፡ ይክላሕ፡ ይበእ፡ ይፃእ፡ ይብዛኅ፡ እያሰኙ፡ ወደ፡ ራብዕ፡ ይለውጡታል ። ፪ነታቸው፡ ስላንድ፡ የሚቈጠር፡ የአና፡ የሀ፡ ግብር፡ ይህ፡ ነው ።

ወና፡ የ ።

፲፯ ፤ የወና፡ የየ፡ ዐመል፡ መጕረድና፡ ድምጥ፡ መለወጥ፡ ነው ፤ ራሳቸውን፡ እየጐረዱና፡ እየዋጡ ፥ ወይም፡ በጥፈት፡ እየታጡ፡ እየተዋጡ፡ ለሌሎቹ፡ መወልጣነ፡ ድምፅ፡ ይኾናሉ ። የድምጣቸውም፡ ስልት፡ በፊደላት፡ ጠባይ፡ በ፲ኛው፡ ቍጥር፡ በመቅድም፡ ውስጥ፡ እንደ፡ ተነገረ፡ ፪፡ ፪፡ ነው ፤ የወ፡ ካዕብና፡ ሳብዕ፡ ማድረግ ፥ የየ፡ ሣልስና፡ ኃምስ፡ ማድረግ ።

ወ ።

፲፰ ፤ ወ፡ መድረሻ፡ ወይም፡ መጨረሻ፡ ሲኾን ፥ ካልአዩ፡ ሳድስ፡ ይኾን፡ የነበረውን፡ ጕርዶ፡ ካዕብና፡ ሳብዕ፡ ያደርጋል ፤ ይህም ፥ በገቢር፡ ዘረወ፡ ይዘሩ ፥ ሠረወ፡ ይሤሩ ፥ ፈነወ፡ ይፌኑ፡ ማለቱን ፤ በተገብሮም፡ ተዘርወ፡ ይዘሮ ፥ ተሠረወ፡ ይሤሮ ፥ ተፈነወ፡ ይትፌኖ፡ ማለቱን፡ ያሳያል ። ደጊም፡ ሲኾን፡ በጭራሽ፡ አይጐርድም ፤ ይህም ፥ ከወወ፡ ይከውው ፥ ለወወ፡ ይለውው ፥ ዔወወ፡ ይዔውው፡ እያለ፡ መኼዱን፡ ያሳያል ። ሳድስ፡ ቅጽሉንም፡ መከከሉ፡ ካዕብ፡ ይኾን፡ የነበረውን፡ ሳድስ፡ ያደርጋል ፤ ይህም፡ ዝርው፡ ሥርው፡ ፍንው፡ ህልው፡ ቅንው፡ ጊውው፡ ምጥው፡ ማለቱን፡ ያሳያል ።

፲፱ ፤ ኹለተኛም፡ ወ፡ በቀተለ፡ ሰርዌ፡ ማእከል፡ ሲኾን፡ ያንቀጹ፡ መነሻ፡ ግእዝ፡ ይኾን፡ የነበረውን፡ ጕርዶ፡ ሳብዕ፡ ያደርጋል ፤ ይህም፡ ሀዊብ፡ ሆበ፡ የሀውብ፡ ይሁብ ፥ ሐዊር፡ ሖረ ፥ ጸዊር፡ ጾረ ፥ ነዊም፡ ኖመ ፥ ቀዊም፡ ቆመ፡ እያለ፡ መኼዱን ፤

ሕንዳርእስቱ፡ ሀወበ፡ ሐወረ፡ ጸወረ፡ ነወመ፡ ቀወመ፡ አለማለቱን፡ ያሳያል ። በ፬፡ ፊደል፡ ግስ፡ ማእከል፡ ሲኾን፡ ግን፡ ያርእስቱንም፡ ጣፍ፡ እንደ፡ ሥሩ፡ ሳብዕ፡ ያደርጋል ። ይህም፡ ኖልዎ፡ ኖለወ፥ሰስዎ፡ ሰሰወ፥ ቶስሐ፡ ቶስሐ፥ቆጽሮ፡ ቆጸረ፡ እያለ፡ በ፫፡ ፊደል፡ ብቻ፡ መኼዱን፤ ነውልዎ፡ ነውለወ፥ ሰውስዎ፡ ሰውሰወ፥ ተውስሐ፡ ተውስሐ፥ ቀውጽሮ፡ ቀውጸረ፡ አለማለቱን፡ ያሳያል ።

፳ ፤ ሦስተኛም፡ ወ፡ ለሦስት፡ ፊደል፡ ግስ፡ መነሻ፡ ሲኾን፥ ጥሬ፡ ዘሩ፡ ፬፡ ፊደል፡ ይኾን፡ የነበረውን፡ ጐርዶ፡ ፫፡ ፊደል፡ ብቻ፡ ያደርጋል ። ይህም፡ ወጊስ፡ ወገሰ፡ ብሎ፡ ሞገስ፤ ወጥሐ፡ ወጥሐ፡ ብሎ፡ ሞጥሕ፤ ወቂሕ፡ ወቅሐ፡ ብሎ፡ ሞቅሕ፤ ወጊድ፡ ወገደ፡ ብሎ፡ ሞገድ፤ ወገረ፡ ሙጋር፥ ወደየ፡ ሙዳይ፥ ወድቀ፡ ሙዳቅ፥ ውሕዘ፡ ሙሓዝ፥ ወለደ፡ ሙላድ፡ ማለቱን፡ ያሳያል ። ሳቢ፡ ዘሩ፡ ግን፥ ልደት፡ ፀአት፡ ድቀት፡ ርደት፡ እያለ፤ ወይም፡ ሳይጐርድ፡ ውግረት፡ ውኀደት፡ ውኀጠት፡ ውጥነት፡ ውፅፈት፡ እያለ፡ ይኼዳል ። ሣልሳዩንም፡ ከቀደሰና፡ ከባረከ፡ ቤት፡ በቀር፡ ኹሉን፡ ይጐርዳል፤ ይህም፡ ወሀበ፡ ይውህብ፡ ብሎ፡ የሀብ፤ ይገስ፡ ይቃሕ፡ ይገድ፡ ይገር፤ ይደቅ፡ የሐዝ፡ ይለድ፡ ይፈጥ፥ ይፀፍ፡ ይረድ፡ ማለቱን፡ ያሳያል ።

፳፩ ፤ አራተኛም፡ ከ፪ቱ፡ ዐመሎች፡ ሲገናኝ፡ አርእስቱ፡ ሳድስ፡ ይኾን፡ የነበረውን፡ ወደ፡ ራብዕ፡ ይለውጠዋል፤ ይህም፡ ዋሕይ፡ ዋሕዮት፥ ዋሐየ፡ ይዋሒ፡ ይዋሒ፡ እያለ፡ መኼዱን፡ ያሳያል ። ዳግመኛም፡ ውዕይ፡ ውዕዮት፡ ውዕየ፡ ወይም፡ ወዐየ፡ ይውዒ፡ የዐይ፡ ይላልና፥ ዋሐየም፡ እንደ፡ ውዕየ፡ ሊኼድ፡ ይችላል፤ ይህም፡ አካኼድ፡ በቀተለ፡ ቤት፡ ነው ። በቀደሰና፡ በባረከ፡ ቤት፡ ግን፤ ወደሰ፡ ይዌድስ፡ ይወድስ፥ ወጥሐ፡ ይዌጥሕ፡ ይወጥሕ፥ ወሠረ፡ ይዌሥር፡ ይወሥር፥ ዋሐደ፡ ይዋሕድ፡ ይዋሕድ፥ ዋከየ፡ ይዋኪ፡ ይዋኪ፥ ዋነየ፡ ይዋኒ፡ ይዋኒ፡ ይላል፡ እንጂ፤ እንደ፡ ቀተለ፡ ቤት፡ አይጐርድም ። ወ፡ መነሻም፡ መድረሻም፡ ማእከልም፡ ኹኖ፡ ከልጐረደው፡ በቀር፥ የግእዝ፡ ቋንቋ፡ ግስ፡ በሳብዕ፡ ቀለም፡ አይነሣም፤ በካዕብ፡ በሳብዕ፡ አይጨርስም፤ ጥሬ፡ ዘሩም፡ በካዕብ፡ በሳብዕ፡ አይነሣም ። ከዚህ፡ የቀረውን፡ የወን፡ ጠባይና፡ ዐመል፡ እኹል፡ ገብ፡ ፊደል፡ መኾኑን፡ በቦታው፡ ተመልከት ።

የ ።

፳፪ ፤ የ፡ መድረሻ፡ ወይም፡ መጨረሻ፡ ሲኾን፥ ከልአዩ፡ ሳድስ፡ ይኾን፡ የነበረውን፡ ጐርዶ፡ ሣልስ፡ ያደርጋል፤ ያርእስቱንም፡ ማእከል፡ ሣልስ፡ ይኾን፡ የነበረውን፡ ለውጦ፡ ሳድስ፡ ያደርጋል ። ይህም፥ ሐቅይ፡ ሐቀየ፡ የሐቂ፤ ሰቅይ፡ ሰቀየ፡ ይሰቂ፤ ፈድይ፡ ፈደየ፡ ይፈዲ፤ ገንይ፡ ገነየ፡ ይገኒ፤ ኀርይ፡ ኀረየ፡ የኅሪ፡ እያለ፡ ሌላውን፡ ኹሉ፡ ያሳያል ። በቦዝ፡ አንቀጽም፡ እንዲሁ፡ ነው፤ ሣልስ፡ ይሆን፡ የነበረውን፡ ሳድስ፡ ያደርጋል ። ወርእያ፡ ደንገፀት፤ በሊዖ፡ ወሰትዮ፤ አዕሚቆ፡ ወኀልዮ፡ እንዲል ።

፳፫ ፤ ፪ኛም፡ የ፡ በቀተለ፡ ሰርዌ፡ በ፫፡ ፊደል፡ ግስ፡ ማእከል፡ ሲኾን፡ መነሻው፡ ግእዝ፡ ይኾን፡ የነበረውን፡ ለውጦና፡ ጐርዶ፡ ኃምስ፡ ያደርጋል ። ይህም፡ ገዩሥ፡

ጌሠ፥ጠዴስ፡ጤሰ፥መዴጥ፡ሜጠ፥ሠዴም፡ሤመ፥ዐዴል፡ዔለ፥በዴል፡ቤለ፡እ
ያለ፡መኼዱን፡መደብ፡አድርጎ፤እንዳርእስቱ፥ገየሠ፡ጠየሰ፥መየጠ፡ሠየመ፤ዐ
የለ፡በየለ፡አለማለቱን፡ያሳያል።በ፬፡ፊደል፡ግስ፡ማእከል፡ሲኾን፡ግን፡አርእስ
ቱንም፡እንዳንቀጹ፡በኃምስ፡ያስነሣል፤ይህም፡ዴግኖ፡ዴገነ፥ጌግዮ፡ጌገየ፥ሌልዮ፡
ሌለየ፥ቄቅዮ፡ቄቀየ፥ሴስዮ፡ሴሰየ፡ማለቱን፡መደብ፡አድርጎ፤ደይግኖ፡ደይገነ፥
ገይግዮ፡ገይገየ፥ለይልዮ፡ለይለየ፥ቀይቅዮ፡ቀይቀየ፥ሰይስዮ፡ሰይሰየ፥አለማለ
ቱን፡ያሳያል። የ፡ማእከልና፡መድረሻ፡እየኾነ፡ከልጐረደው፡በቀር፥ግስ፡በኃምስ፡
ፊደል፡አይነሣም፤በሣልስ፡ፊደል፡አይጨርስም፤ጥሬና፡ነባርም፡እንደዚህ፡ነው።

## ሐተታ፡ስለ፡ብህለና፡ስለ፡ቤለ።

፳፬፤ ሀሎ፡የሀለወ፡ክፋይ፡ወይም፡ካዕቡ፥መንቲያው፡ድርቡ፡እንደ፡ኾነ፤
ቤለም፡የብህለ፡ካዕብ፡መንቲያና፡ድርብ፡ይባላል፤ያንዱ፡ቅንጣት፡ዘር፡ግስ፡
ባለ፪፡ዐመል፡ስለ፡ኾነ፡በሀና፡በየ፡ስልት፡በ፪ቱ፡አካኼድ፡ይኼዳል። የሀውን፡
አካኼድ፡በሀ፦ተናግረናል፤የየውም፡አካኼድ፡እንዲህ፡ነው። በሀ፡ማእከልነት፡
ብሂል፡ብሂሎት፡ብህለ፦የተባለው፤፪ኛ፡ደግሞ፡በየ፡ማእከልነት፥በዩል፡በዩ
ሎት፡ቤለ፡ተብሎ፥አስደራጊውንም፥አበለ፡ያብል፡እያሰኘ፡ልውጥና፡ግልብጥ፡
ሕግ፡ወጥ፡አካኼድ፡ይኼዳል፤ብህለም፡ቤለ፡መባሉ፡በወዲያኛው፡ትግሬ፡በሐ
ባቦች፡ቋንቋ፡ይታወቃል፤በወዲህኛውም፡ትግሪኛ፥ሐማሴኖች፡የለ፥አኵስም
ችና፡ዐዶች፡በለ፡ይሉታል።ያካኼዱም፡ሕግ፡ወጥነት፡ይህ፡ነው፤ቤለ፡ይበይል፡
ይቢል፡ብሎ፥እንደ፡ዔለና፡እንደ፡ሤመ፡ፊት፡ለፊት፡በመኼድ፡ፈንታ፥ቤለ፡
ይቤ፡ይበል፡ይበል፤ቤልከ፡ትቤ፡ትበል፡በል፤ቤለት፡ትቤ፡ትበል፡ትበል፤
ቤልኩ፡እቤ፡እበል፡እበል፤ቤልነ፡ንቤ፡ንበል፡ንበል፡እያለ፡በነዚህ፡በ፰ቱ፡
ሰራዊት፡ለን፡እያሰገደ፥የን፡እየጐረደ፡በዔለና፡በሤመ፡አካኼድ፡ግእዝ፡ይኾን፡
የነበረውን፡በ፥በካልአይ፡ኹሉ፡ኃምስ፡ያደርጋል። በቀሩት፡ደግሞ፡በ፰ቱ፡
ኹሉ፥ቤሉ፡ይቤሉ፡ይበሉ፡ይበሉ፤ቤልክሙ፡ትቤሉ፡ትበሉ፡በሉ፤ቤላ፡ይቤላ፡
ይበላ፡ይበላ፤ቤልክን፡ትቤላ፡ትበላ፡በላ፤ቤልኪ፡ትቤሊ፡ትበሊ፡በሊ፡እያሰኘ፡
የን፡በመጕረዱ፡ላይ፡ለን፡እየጨመረ፡ይኼዳል። ትንቢትነቱንም፥ይቤ፡ትቤ፡
እቤ፡ንቤ፡ብሎ፡በሥርወ፡ቀለሙ፡ያስረዳል፤ይህነንም፡በአሥራውና፡በብሂል፡
አፈታት፡ተመልከት። ባላገባቦች፡ግን፡ባለመጽሐፎችም፡ሳይቀሩ፥የይቤ፡ቀዳ
ማይ፡ቤለ፡መኾኑን፡ስላላስተዋሉ፤፪ኛም፡ቀዳማይ፡አንቀጽ፤ሥርወ፡ፊደል፡አለ
መለወጡን፥በሣልስ፡በኃምስ፡አለመጕረዱን፥አጥብቀው፡አጥልቀው፡ስላልመረ
መሩ፥ይቤን፡በቤለ፡ፈንታ፦ቀዳማይ፡አንቀጽ፡አድርገው፥እኩሉ፡ዘርና፡አርእ
ስት፡የሌለው፡ለብቻው፡የቆመ፡ነበር፡ቀዳማይ፡ነው፤እኩሉም፡የቀዳማይ፡አን
ቀጽ፡የብህለ፡ድርብ፡ነው፡እያሉ፡በቀዳማይነት፡ስላቆሙት፥ርባታውና፡አፈታቱ፡
ከሥር፡እስከ፡ጫፍ፡ተበላሽቷል፡(ቍ፲፪)።

፳፭፤ የአንና፡የሀን፥የወንና፡የየን፡የነዚህን፡የኹለቱን፡ስልት፥የመንገዳ
ቸውን፡ልዩነት፥ያካኼዳቸውን፡መጥፎነት፥ነውጠኞችና፡ዐመለኞች፡ኹነው፡የግ

ብቻ ፤ ፪ቱም ፡ ፩ ፡ ወገን ፡ ናቸው ። ባሕቱም ፡ ግን ፡ ብቻ ፡ ይኸናል ፤ ግን ፡ ሲኾን ፡ ቀድሞ ፡ ተከትሎ ፡ በኹሉ ፡ ይገባል ። ባሕቱ ፡ ዘንተ ፡ ረከብኩ ። መበለተ ፡ ባሕቱ ፡ ኢታውስብ ። ወን ፡ እየደረበም ፡ ሲገባ ፤ ወባሕቱ ፡ እብለክሙ ። ወእቤለክሙ ፡ ባሕቱ ። ብቻ ፡ ሲኾን ፡ እንደ ፡ ዳእሙ ፡ እጅግ ፡ አይገኝም ፤ አላ ፡ ነቅዐ ፡ ማይ ፡ የዐርግ ፡ ባሕቱ ፡ እምነ ፡ ምድር ። በዝንቱ ፡ ባሕቱ ፤ አንተ ፡ ባሕቱ ። በብቻም ፡ ፈንታ ፡ ይልቅ ፡ ሲሉት ፡ ያምራል ። አኮ ፡ ይእዜ ፤ አላ ፡ ባሕቱ ፡ እምድኅረ ፡ ኅዳጥ ፡ መዋዕል ። እንበለም ፡ ዘ ፡ እያጋነነው ፡ በዘንድ ፡ አንቀጽ ፡ ገብቶ ፡ ሳ ፡ ይኸናል ። ዘእንበለ ፡ ያእምር ፡ ሕፃን ፡ ሰምየ ፡ አቡሁ ፡ ወእሙ ። ዘእንበለ ፡ ይቊሙ ፡ አድባር ። ፫ኛም ፡ እንበለ ፡ ደቂቅ ፡ አገባብ ፡ ሲኾን ፤ በቀር ፡ አለ ፡ ያለ ፡ እንጂ ፡ ይኸናል ። ዘ ፡ እያጋነነው ፡ ሳያጋንነውም ፡ በጥሬ ፡ ኹሉ ፡ ይገባል ፤ በቀር ፡ ሲኾን ፡ በሉታና ፡ በክፍል ፡ ይገባል ። በሉታ ፤ ወኢታገምር ፡ ፍኖታ ፡ ዘእንበለ ፡ አሐቲ ፡ ኪደተ ፡ እግረ ፡ ብእሲ ። አልብነ ፡ ዝየ ፡ ዘእንበለ ፡ ኀምስ ፡ ኅብስት ። በክፈል ፤ ወተዘርዉ ፡ ኵሎሙ ፡ ዘእንበለ ፡ ሐዋርያት ። አለ ፡ ያለ ፡ ሲኾን ፤ እንበለ ፡ ኀጢአት ፡ ተሰቅለ ፤ ወእንበለ ፡ ድልወት ፡ ተገፍዐ ፡ ያሰኛል ። እንጂ ፡ ሲኾን ፤ አዘዘሙ ፡ ኢይንግሩ ፡ ዘርእዩ ፡ በደብር ፤ ዘእንበለ ፡ አመ ፡ ተንሥአ ፤ በተነሣ ፡ ጊዜ ፡ እንጂ ። አልቦኬ ፡ ዘይበቍዕ ፡ ዘእንበለ ፡ ለገዲፍ ፡ አፍአ ። ሲዘረዝርም ፤ እንበሌሁ ፡ ሃ ፡ ሆሙ ፡ ሆን ፤ እንበሌከ ፡ ኪ ፡ ክሙ ፡ ክን ፡ የ ፡ ነ ፡ እያሰኘ ፡ አለ ፡ ያለ ፡ በቀር ፡ ይኸናል ።

፹፪ ፤ ዓዲ ፤ ዐቢይ ፡ አገባብ ። እንጂ ፡ ም ፡ ይኸናል ፤ ቀድሞ ፡ ተከትሎ ፡ ይነገራል ፤ አላ ፡ ዳእሙ ፡ ባሕቱ ፡ በገቡበት ፡ ኹሉ ፡ ይገባል ። እንጂ ፡ ሲኾን ፡ ዋዌነቱ ፡ አይቀርም ፤ አሉታውን ፡ በጽድቅ ፡ ሲያናግር ፤ አኮ ፡ በመቄዶንያ ፡ ወአካይያ ፡ ባሕቲቱ ፤ ዓዲ ፡ በኵሉ ፡ በሓውርት ፤ በገሩም ፡ ኹሉ ፡ እንጂ ። ያሉታውን ፡ ውጥን ፡ በጽድቅ ፡ ሲጨርስ ፤ ምሕሮ ፡ ወአኮ ፡ ሎቱ ፡ ለባሕቲቱ ፤ ዓዲ ፡ ሊተኒ ፤ እኔንም ፡ ደግሞ ፡ ይቅር ፡ አለኝ ፡ እንጂ ። ዳእሙ ፡ ዓዲ ፡ እያለ ፡ ሲገባ ፡ እንጂነቱን ፡ ዳእሙ ፡ ወርሶት ፡ ዋዌ ፡ ብቻ ፡ ኹኖ ፡ ይቀራል ። አኮ ፡ ክመ ፡ ሰንበተ ፡ ባሕቲቶ ፡ ዘይስዕር ፡ ዳእሙ ፡ ዓዲ ፡ አባሁ ፡ ይሬስዮ ፡ ለእግዚ ፤ እግዜርንም ፡ አባቱ ፡ ያደርጋል ፡ እንጂ ። ንኡስ ፡ አገባብም ፡ ሲኾን ፡ ገና ፤ ደግሞ ፡ ዳግመኛ ፤ አኹን ፡ ም ፡ ይኸናል ። ገና ፡ ሲኾን ፡ በኅላፊና ፡ በትንቢት ፡ በትእዛዝና ፡ በነባር ፡ ይገባል ። ይህም ፡ ዓዲ ፡ ሀሎኩ ፡ ምስሌከ ። ይዌስክ ፡ ዓዲሁ ። ተዐገሡ ፡ ዓዲ ፡ ኅዳጠ ። ዓዲ ፡ ብየ ፡ ነገር ። ዘትብሉ ፡ ከመ ፡ ዓዲ ፡ ሕያው ፡ ማለቱን ፡ ያሳያል ። እስመ ፡ ዓዲ ፡ እንዘ ፡ ዓዲ ፡ ዘዓዲ ፡ ከመ ፡ ዓዲ ፡ እያሰኘም ፡ በነባር ፡ አንቀጽ ፡ ከሚገቡ ፡ አገባቦች ፡ ጋራ ፡ ይነገራል ። በኅላፊ ፡ ግን ፡ ብዙ ፡ ጊዜ ፡ በሉታ ፡ ይገባል ። ዓዲ ፡ ኢበጽሐ ፡ ጊዜሁ ። ዓዲሁ ፡ ሃ ፡ እያለም ፡ ሲዘረዝር ፡ ገና ፡ ይኸናል ፤ እንዘ ፡ ዓዲሁ ፡ ጽልመት ። እስመ ፡ ዓዲሃ ፡ ኢተዐውቀት ። ዓዲየ ፡ ኢነሣእኩ ። ደግሞ ፡ ዳግመኛ ፡ ሲኾን ፡ በኹሉ ፡ ይገባል ፤ ወገብረ ፡ እግዚአብሔር ፡ ዓዲ ፡ አራዊተ ። ወትቤ ፡ ይእዜ ፡ ዓዲ ፡ አአምኖ ። አኹን ፡ ሲኾን ፤ ዓዲ ፡ መጽአ ፡ ዓዲ ፡ ይመጽእ ፡ እያሰኘ ፡ ይህን ፡ በመሰለ ፡ ይገባል ። ዓዲ ፡ ኅዳጠ ፤ አኹን ፡ ጥቂት ፤ ወዓዲ ፡ ኅዳጥ ፤ ጥቂት ፡ ቈይቶ ፤ ከጥቂት ፡ በኋላ ፡ ይኸናል ። ም ፡ ሲኾን ፡ ዋዌ ፡ ነውና ፤ ከወንድሞቹ ፡ ከወሂ ፡ ጋራ ፡ ኋላ ፡ በቦታው ፡ ይነገራል ።

፫፻፫ ፤ ብሂል ፤ ዐቢይ ፡ አገባብ ፡፡ ዘይቤው ፡ ማለት ፡ ይኾናል ፤ የብህለና ፡ የይቤ ፡ ራስ ፡ ነው ፡፡ ብሂል ፡ ፫ ፡ ነገር ፡ ይኾናል ፤ እነዚህም ፡ ፫ቱ ፡ አንቀጽነትና ፡ አገባብነት ፡ ሰዋስውነት ፡ ናቸው ፡፡ ባንቀጽነቱ ፡ አንቀጽን ፡ ኹሉ ፡ ይስባል ፤ ሲነገርም ፡ ቀድሞ ፡ ተከትሎ ፥ ዐርፎ ፡ ተናቦ ፡ ይገባል ፡፡ ይህም ፥ ብሂል ፡ ሠረቀ ፡ ብሂል ፡ ተወልደ ፤ ወይም ፡ ሠረቀ ፡ ብሂል ፡ ተወልደ ፡ ብሂል ፡፡ ብሂለ ፡ ሠረቀ ፡ ብሂለ ፡ ተወልደ ፡ ውእቱ ፡፡ በካልአይና ፡ በሣልሳይም ፥ ብሂለ ፡ ይሠርቅ ፡ ኮከብ ፡ እምያዕቆብ ፡፡ ብሂለ ፡ ንበር ፡ በየማንየ ፡፡ በነባርም ፡ አይምሰልክሙ ፡ በብሂለ ፡ አብ ፡ ብነ ፡ ማለቱን ፡ ያሳያል ፡፡ ፪ኛም ፡ በገባብነቱ ፡ ዘማች ፡ አንቀጽና ፡ ነባር ፡ አንቀጽ ፡ ኹሉ ፡ እንዳያስሩ ፡ ይከለክላል ፡፡ ይህም ፥ ብሂል ፡ ከፈለ ፡ ሙሴ ፡ ባሕረ ፥ ብሂል ፡ ዐደወ ፡ ብንያም ፡ ብሂል ፡ ለሊቀ ፡፡ በዚምህ ፡ አንቀጽነቱ ፡ መሳቡን ፡ ሳይለቅ ፡ በገባብነቱ ፡ ከፈለና ፡ ዐደወ ፡ እንዳያስሩ ፡ ማሰሪያነትን ፡ አስለቀቀ ፤ ይህ ፡ ሲደረደር ፡ ነው ፡፡ ሲነባበር ፡ ደግሞ ፥ ብሂለ ፡ ብሂል ፡ ተወልደ ፡ አምላክ ፡ እማርያም ፡ ለሊቀ ፡ ይላል ፡፡ ግብር ፡ እንዲተረጐም ፡ ስም ፡ ይተረጐማል ፤ ግብር ፡ ያለፈው ፡ ነው ፤ ስም ፡ ሲተረጐም ፥ ሚካኤል ፡ ብሂል ፡ በልሰነ ፡ ዕብራይስጥ ፥ መኑ ፡ ከመ ፡ አምላክ ፤ ጴጥሮስ ፡ ብሂል ፡ በልሳነ ፡ ጽርእ ፥ ኰኵሓዊ ፥ አው ፡ ብእሴ ፡ ኰኵሕ ፡፡ ፫ኛም ፡ በሰዋስውነቱ ፡ ዘርፍና ፡ ምሳሌ ፡ ይኾናል ፡፡ ዘርፍና ፡ ምሳሌም ፡ ሲኾን ፡ ለዘርፍነቱ ፡ ብዙ ፡ ስምና ፡ ግብር ፡ አለውና ፤ ኋላ ፡ በቅኔ ፡ ክፍል ፡ በሠምና ፡ በወርቅ ፡ ይነገራል ፡፡

ሐተታ ፤ ያለፈውን ፡ ዕርከን ፡ መልሶ ፡ የሚፈታና ፡ የሚያፍታታ ፤
ያበይት ፡ አገባቦች ፡ ዳግም ፡ ሕግ ፥ ማሰሪያና ፡ አገባብ ፡ የሚያዛውግ ፡፡

፫፻፬ ፤ ከብሂል ፡ በፊት ፡ ከእስመ ፡ እስከ ፡ ብሂል ፡ ከተነገሩቱ ፡ ተመርጠውና ፡ ተለይተው ፡ ዳግመኛ ፡ መነገር ፡ የሚያሻቸው ፡ ዐበይት ፡ አገባቦች ፡ እሊህ ፡ ናቸው ፤ መደገማቸውም ፡ ስለ ፡ ማሰሪያ ፡ ነው ፡፡ ንኡስና ፡ ደቂቅ ፡ መኾናቸው ፡ ሳይቀር ፡ ጠባያቸው ፡ ኹሉ ፡ ተለቅሞ ፡ ተቃርሞ ፡ ተከቶ ፡ ተነግሯል ፡፡ የማሰሪያም ፡ ነገር ፡ እንዲህ ፡ ነው ፤ እስመ ፡ በእንተ ፡ በይነ ፡ እንበይነ ፡ ስለ ፡ ስላ ፡ ሲኾኑ ፡ በራሳቸውና ፡ በባዕድ ፡ ያሳስራሉ ፡፡ በራሳቸው ፡ ማለት ፡ በነባር ፡ አንቀጽ ፥ በባዕድ ፡ ማለት ፡ በዘማች ፡ አንቀጽ ፡ ማለት ፡ ነው ፤ በባዕድ ፡ ሲያሳስሩ ፡ ለነገሩ ፡ ፯ ፡ አገባቦች ፡ ይሰማሙታል ፡፡ አገባቦቹም ፡ እሊህ ፡ ናቸው ፤ እስመ ፡ አምጣነ ፡ አኮኑ ፡ ና ፡ ሲኾኑ ፤ እመ ፡ ሶበ ፡ ብቢ ፡ ሲኾኑ ፤ እመ ፡ እምከመ ፡ ከ ፡ ካ ፡ ሲኾኑ ፤ ኀበ ፡ ዘንድ ፡ ሲኾን ፤ ከመ ፡ እንደ ፡ ሲኾን ፤ እንዘ ፡ እየ ፡ ሲኾን ፤ እንተ ፡ እለ ፡ ዘ ፡ የ ፡ ሲኾኑ ፡ ነው ፡፡ በራሳቸው ፡ ሲያሳስሩ ፥ ሞቱ ፡ ለእግዚእ ፡ እስመ ፡ ሞተ ፡ አዳም ፡ በእንተ ፡ በይነ ፡ እንበይነ ፡ ዘሞተ ፡ አዳም ፤ የጌታ ፡ ሞቱ ፡ አዳም ፡ ስለ ፡ ሞተ ፡ ነው ፡፡ በባዕድ ፡ ሲያሳስሩ ፥ እስመ ፡ ተዋረደ ፡ በእንተ ፡ በይነ ፡ እንበይነ ፡ ዘተዋረደ ፡ አዳም ፡ ሞተ ፡ እግዚእ ፡ ያሰኛል ፡፡

፫፻፭ ፤ ለነገሩም ፡ ፯ቱ ፡ አገባቦች ፡ ሲሰማሙት ፥ ሞቱ ፡ ለእግዚእ ፡ እስመ ፡ እስመ ፡ ሞተ ፡ አዳም ፥ አምጣነ ፡ በእንተ ፡ ዘሞተ ፡ አዳም ፥ አኮኑ ፡ በይነ ፡ እንበይነ ፡ ዘሞተ ፡ አዳም ፥ ሎቱ ፡ ስብሐት ፤ የጌታ ፡ ሞት ፡ አዳም ፡ ስለ ፡ ሞተ ፡ ነውና ፥ ምስጋና ፡ ይገባ

ዋል ። ኵሉ ፡ ፍጥረት ፡ ይሴብሖ ፡ ለእግዚ ፡ እመ ፡ ሰበ ፡ ተሰቅሎቱ ፡ እስመ ፡ ተዋረደ ፥ በእንተ ፡ በይነ ፡ እንበይነ ፡ ዘተዋረደ ፡ አዳም ፤ መሰቀሉ ፡ አዳም ፡ ስለ ፡ ተዋረደ ፡ ቢ ኸን ። በይነ ፡ ምንት ፡ መነንዎ ፡ አይሁድ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ እምከመ ፡ ተወልዶቱ ፡ እስመ ፡ አፍቀረ ፡ ሰብአ ፥ እመ ፡ ተወልዶቱ ፡ በእንተ ፡ በይነ ፡ እንበይነ ፡ ዘአፍቀረ ፡ ሰ ብአ ፤ መወለዱ ፡ ሰውን ፡ ስለ ፡ ወደደ ፡ ከኸነ ፡ አይሁድ ፡ ጌታን ፡ ስለ ፡ ምን ፡ ናቁት ። እግ ዚእ ፡ ተሰምየ ፡ ጻድቀ ፡ ኀበ ፡ እስመ ፡ መሐለ ፥ ኀበ ፡ በእንተ ፡ በይነ ፡ እንበይነ ፡ ዘመ ሐለ ፡ ለአዳም ፡ ሞቱ ፤ ሞቱ ፡ ለአዳም ፡ ስለ ፡ ማለ ፡ ከኸነ ፡ ዘንድ ። ተዐውቀ ፡ ወተጠ የቀ ፡ ከመ ፡ ተሰምዮቱ ፡ ለተክለ ፡ ሃይማኖት ፡ ተክለ ፥ እስመ ፡ ተኀርየ ፡ በእንተ ፡ በይነ ፡ እንበይነ ፡ ዘተኀርየ ፡ እምከርሠ ፡ እሙ ፤ ስለ ፡ ተመረጠ ፡ እንደ ፡ ኸነ ። እፎ ፡ ይምሕል ፡ ሰብእ ፡ እንዘ ፡ እስመ ፡ መሐለ ፥ እንዘ ፡ በእንተ ፡ በይነ ፡ እንበይነ ፡ ዘመሐለ ፡ ተሰቅሎቱ ፡ ለእግዚእ ፤ የጌታ ፡ መሰቀል ፡ ስለ ፡ ማለ ፡ ሲ ኸን ። ተሰብሐ ፡ እግዚእ ፡ ዘበእንተ ፡ በይነ ፡ እንበይነ ፡ መሐለ ፡ ለአዳም ፡ ሞቱ ። ሞቱ ፡ ለአዳም ፡ ስለ ፡ ማለ ፡ የኸነ ፡ ጌታ ። የቀሩ ትም ፡ ስለ ፡ የሚኸኑ ፡ ዐበይት ፡ አገባቦች ፡ እንደዚሁ ፡ ናቸው ። ኀበ ፡ መንገለ ፡ ውእደ ፡ ዘንድ ፡ ሲኸኑ ፡ በራሳቸውና ፡ በባዕድ ፡ ያሳስራሉ ፤ ይህም ፡ በቦታው ፡ ተነግሯል ። አገ ባቦችም ፡ ሲሰማሙት ፥ ሚ ፡ የአከ ፡ ኀጢአት ፡ እስመ ፡ ኀበ ፡ ገብረ ፥ አምጣነ ፡ መንገለ ፡ ገብረ ፥ አኮኑ ፡ ውእደ ፡ ገብረ ፡ አዳም ፡ ኀጢአተ ፡ ሞተ ፡ እግዚእ ። የቀሩትንም ፡ እን ዲሁ ፡ አግባ ።

፹፯ ፤ እንዘ ፥ ስ ፡ ሲ ፡ ኹኖ ፡ ሲነገር ፤ አገባቦችም ፡ ሲሰማሙት ፥ ጸጊቦቱ ፡ ለር ኁብ ፡ እስመ ፡ እንዘ ፡ ይበልዕ ፡ ኅብስተ ፥ እምከመ ፡ እንዘ ፡ ይበልዕ ፡ ኅብስተ ፥ ንብላዕ ፡ ኪያሁ ። መጠነ ፡ አምጣነ ፡ ዐቅመ ፥ ያኽል ፡ ሲኸኑ ፡ በራሳቸውና ፡ በባዕድ ፡ ያሳስራሉ ። በራሳቸው ፥ ተዋርዶቱ ፡ ለፈርዖን ፡ መጠነ ፡ አምጣነ ፡ ዐቅመ ፡ አስተዋረዶሙ ፡ ለእስራ ኤል ። በባዕድ ፥ ተዋረደ ፡ ፈርዖን ፡ መጠነ ፡ አስተረዋዶሙ ፡ ለእስራኤል ። አገባቦችም ፡ ሲሰማሙት ፥ አብደሩ ፡ ጻድቃን ፡ መከራ ፡ ሥጋ ፡ እምተድላ ፡ ሥጋ ፤ እስመ ፡ መጠነ ፡ አፈድፈዱ ፡ መከራ ፡ ይፈደፍድ ፡ ፍሥሓሆሙ ። ለምንት ፡ ሰብእ ፡ ይጸልእ ፡ መከራ ፡ እመ ፡ ክብሩ ፡ አምጣነ ፡ ያበዝኅ ፡ መከራ ። ከመ ፥ እንደ ፡ ሲኸን ፡ በራሱ ፡ በባዕድ ፡ ያሳ ስራል ፤ በራሱ ፡ ተቀሥፎቱ ፡ ለእግዚእ ፡ ከመ ፡ ተቀሥፎተ ፡ ሰራቂ ። በባዕድ ፡ ሲያሳ ስር ፥ ይደልዎሙ ፡ ክበር ፡ ለሰማዕታት ፤ እስመ ፡ ተሣቅዮቶሙ ፡ ከመ ፡ ተሣቀየ ፡ ክር ስቶስ ። የቀሩትንም ፡ እያሰማማኽ ፡ እንዲሁ ፡ አግባ ።

፹፰ ፤ እመ ፤ ሰበ ፤ ብ ፡ ቢ ፡ ሲኸኑ ፡ በራሳቸው ፡ በባዕድ ፡ ያሳስራሉ ፤ በራሳቸው ፡ አድኅኖተ ፡ ሰብአ ፡ ነፍሰ ፡ እመ ፡ ሰበ ፡ በሃይማኖቱ ፡ ይዌስክ ፡ ምግባረ ። በባዕድ ፥ ያድ ኅን ፡ ሰብእ ፡ ነፍሶ ፡ እመ ፡ ሰበ ፡ ይዌስክ ፡ ምግባረ ፡ በሃይማኖቱ ። አገባብም ፡ ሲሰማማ ቸው ፥ ይጽሕቅ ፡ ሰብእ ፡ ለከዊነ ፡ ባዕል ፤ እስመ ፡ እመ ፡ ሰበ ፡ ይብዕል ፡ ክብሩ ፡ ያሰኛሉ ፤ የቀሩትንም ፡ እንዲህ ፡ አግባ ። እስከ ፥ በራሱ ፡ በባዕድ ፡ ያሳስራል ፤ በራሱ ፥ ንብረ ቶሙ ፡ ለሙታን ፡ ውሳጤ ፡ መቃብር ፡ እስከ ፡ አመ ፡ ይከውን ፡ ንፍኀተ ፡ ቀርን ። በባ ዕድ ፥ ኢትቅናዕ ፡ ላዕለ ፡ ባዕል ፤ እስመ ፡ እስከ ፡ ይመውት ፡ ብዕሉ ። የቀሩትንም ፡ እን ዲህ ፡ አግባ ። ቅድመና ፡ ድኅረም ፡ በራሳቸውና ፡ በባዕድ ፡ ያሳስራሉ ። በራሳቸው ፥

ሞቱ ፡ ለሰብእ ፡ ቅድመ ፡ ትንሣኤ ፤ ወድኅረ ፡ ትንሣኤ ፡ ሞተ ፡ ዓለም ። ተፈንዎቱ ፡ ለጰራቅሊጦስ ፡ ኀበ ፡ ሐዋርያት ፡ እምድኅረ ፡ ዐርገ ፡ እግዚእነ ። በባዕድም ፥ መንክር ፡ ኀይሉ ፡ ለጰራቅሊጦስ ፤ እስመ ፡ እምድኅረ ፡ ወረደ ፡ ሎሙ ፡ ጥበዐተ ፡ ሐዋርያት ፡ እለ ፡ እም ቅድሜሁ ፡ ኢኮኑ ፡ ጥቡዓነ ። የቀሩትንም ፡ እንዲሁ ፡ አሰማምተኽ ፡ አግባ ።

## ፳ኛ ፡ ዕርከን ።

## ንኡሳን ፡ አገባቦች ።

፺፰ ፤ ሰ ፤ ና ፡ ስ ፡ ሳ ፡ ማ ፡ ግን ፡ ትች ፡ ይኾናል ፤ ምስጢሩ ፡ ግን ፡ የኹሉም ፡ አፍራሽ ፡ ነው ። ሲገባም ፡ ትራስ ፡ እየኾነ ፡ በቃል ፡ መጨረሻ ፡ ይገባል ። ሰ ፡ ስ ፡ መኾኑን ፡ ሳይለቅ ፡ ጸንሐ ፡ ተርፈ ፡ ተኀድገ ፡ በሚሉ ፡ በነዚህ ፡ በ፫ቱ ፡ በሣልሳይ ፡ ብቻ ፡ እየገባ ፡ ና ፡ ይኾናል ። አገባቡም ፡ ይህ ፡ ነው ፤ ኢፈጸሙ ፡ አይሁድ ፡ ሕገ ፡ ወንጌል ፤ ይጸናሕሰ ፡ ይትርፍሰ ፡ ይትኀደግሰ ፡ ዝንቱ ፤ ሕገ ፡ ኦሪትሂ ፡ ኒ ፡ ጥቀ ፡ ኢፈጸሙ ፤ ሲፈታም ፡ ይህስ ፡ ይቅርና ፡ የኦሪትን ፡ ሕግ ፡ ስንኳ ፡ አልፈጸሙም ። ስ ፡ ብቻ ፡ ሲኾን ፡ በብትን ፡ በቅጽል ፡ ይገባል ፤ ወልድየሰ ፡ መዊቶ ፡ ህለወ ፥ ወበእንተ ፡ ዝ ፡ ጐንደየ ፤ ልጄስ ፡ ሙቷል ። ውእቱሰ ፡ ሕያው ፤ ርሱስ ፡ ደኅና ፡ ነው ። ሳ ፡ ሲኾን ፡ ደግሞ ፡ እንደዚሁ ፡ በቅጽል ፡ በብትን ፡ እየገባ ፡ ጥያቄ ፡ ይከተለዋል ። ይቤሎ ፡ ለዘይቤሎ ፡ መጽኡ ፡ ሳእካኒሁ ፡ ለንጉሥ ፥ ውእቱሰ ፡ ተርፈኑ ፤ ርሱሳ ፡ ቀረን ። አንተሰ ፡ መጻእከ ፥ እኑከሰ ፤ አንተስ ፡ መጣኽ ፥ ወንድምኽሳ ። ማ ፡ ሲኾን ፡ ደግሞ ፡ በቅጽል ፡ በብትን ፡ ባገባብ ፡ ገብቶ ፡ በጥያቄ ፡ ምላሽ ፡ ይነገራል ። ይቤሎ ፡ ለዘይቤሎ ፡ ሕያውኑ ፡ እኁከ ፥ ውእቱሰ ፡ ሞተ ፤ ርሱማ ፡ ሞተ ። ግን ፡ ሲኾን ፡ ብቻውን ፡ በብትን ፡ ይገባል ፤ ሰብእሰ ፡ እንዘ ፡ ክቡር ፡ ውእቱ ፡ ኢያእመረ ። መብልዕሰ ፡ ጽኑዕ ፡ ለልሂቅ ። ትች ፡ ሲኾን ፡ ወ ፡ ሂ ፡ ኒ ፡ ሰ ፥ ግን ፡ እየኾኑ ፡ ይከተሉታል ። ይህም ፥ ሰብእሰ ፡ ገጸ ፡ ይሬኢ ፡ ወእግዚአብሔርሰ ፡ ልበ ፡ ይሬኢ ። እሙንቱሰ ፡ ተዐቅጹ ፡ ወወድቁ ፡ ወንሕነሰ ፡ ተንሣእነ ፡ ወረታዕነ ። ለአድግሰ ፡ አቅሕሞ ፤ ወለገብርኒ ፡ ገሥጾ ፡ ባለው ፡ ይታወቃል ። ባገባብና ፡ ባንቀጽም ፡ ኹሉ ፡ ይገባል ፤ ሶበሰ ፡ ተአምሬ ፥ እመሰ ፡ አማን ፥ እንከሰ ፥ ይረትዕሰ ፥ እፈቱሰ ፡ እፍልስ ።

፺፱ ፤ እም ፤ ንኡስ ፡ አገባብ ። በ ፡ ባ ፡ ከ ፡ ካ ፡ ኪ ፡ ክ ፡ ይኾናል ፤ ኪ ፡ ክ ፡ ሲኾን ፡ በትርፍ ፡ ዐማርኛ ፡ ይልቅ ፡ ያሰኛል ። እመና ፡ ሶበ ፡ ቀድመውት ፡ ወይም ፡ ተከትለውት ፥ ብቻውንም ፡ ኹኖ ፡ በኀላፊ ፡ አንቀጽ ፡ እየገባ ፡ በጽንዕ ፡ ሲፈታ ፡ በ ፡ ባ ፡ ይኾናል ፤ ምስጢሩም ፡ ባለፈ ፡ ነገር ፡ ጸጸት ፥ በሚመጣ ፡ ነገር ፡ ምኞት ፡ ያሳያል ። እመ ፡ ይኔስሕ ፡ ይሁዳ ፡ እምጸድቀ ፤ በጸደቀ ፡ ነበር ። እምኀየሶ ፡ ሶበ ፡ ኢተወልደ ። እመ ፡ ኢይበልዕ ፡ አዳም ፡ በለሰ ፡ እምኢኀጥአ ፡ ጸጋሁ ፡ ዘተውህበ ፤ ሶበሰ ፡ ትሄሉ ፡ ዝየ ፡ እምኢሞተ ፡ እኁየ ፤ ባልሞተም ፡ ነበር ። የእመና ፡ የሶበ ፡ ጠባይ ፡ እንዴት ፡ እንደ ፡ ኾነ ፡ (ዕር ፲፱ኛ ፡ ቍ፷፯) ፡ ተመልከት ። ብቻውንም ፥ እምደለወከ ፡ ታግብእ ፡ ወርቅየ ፥ ወመጺእየ ፡ እምአስተገበርክዎ ፡ ለልየ ። መኑ ፡ እምወሀበኒ ፡ ማየ ፡ እያለ ፡ ይገባል ። ከ ፡ ካ ፡ ሲኾን ፡ ከመንና ፡ ዘን ፡ በር ፡ ከፋች ፡ አድርጎ ፡ እንደዚሁ ፡ በኀላፊ ፡ አንቀጽ ፡ ይገባል ፤ እምዘ ፡ እምከመ ፡ የሚባል ፡ አገባብ ፡ የለምና ፤ እምዘ ፡ ከበዘ ፡ ጋራ ፡ በቦታው ፡

ተነግሯል ፤ ከመም ፤ እምከመ ፡ ለምለመ ፡ ዐጽቁ ፤ ወእምከመ ፡ ወፅአ ፡ መንፈስ ፡ ርኩስ ፡
እያለ ፡ ይገባል ። ዘእም ፡ እያለም ፡ ሲገባ ፡ እምዘ ፡ ተብሎ ፡ ይፈታል ፤ ይህም ፡ ጸልኡ ፡
ዘእምአፍቀሩ ፤ ከወደዱት ፡ ይልቅ ። አኅሰረከ ፡ ዘእምአክበረከ ፤ ካከበረኽ ፡ ይልቅ ።
ሊወዱት ፡ የነበር ፥ ሊያከብርኽ ፡ የነበር ፡ ብለው ፡ ኀላፊውን ፡ በዘንድ ፡ የሚፈቱ ፡
አሉ ። ሕቀ ፡ ክመ ፡ ዘእምድኅፀ ፡ ሰኰናየ ፤ ዘእምተንተና ፡ እገርየ ፡ ያለውም ፤ እን
ዲሁ ፡ ይፈታል ። ኪ ፡ ክ ፡ ሲኾን ፡ በዘንድ ፡ እየገባ ፡ ይልቅ ፡ ያሰኛል ፤ ማሰሪያውም ፡
ቀለ ፡ ኀየሰ ፡ አፍቀረ ፡ ኀረየ ፥ ይህን ፡ የመሰለ ፡ ነው ። ይቀልል ፡ ኀልፈተ ፡ ሰማይ ፡
እምትደቅ ፡ አሐቲ ፡ ቃል ። ይኄይሰነ ፡ ንቅትል ፡ አሐደ ፡ ብእሴ ፡ እምይትሀጐል ፡
ኵሉ ፡ ሕዝብ ። ደቂቅ ፡ አገባብም ፡ ሲኾን ፥ ከ ፡ ይልቅ ፡ የተነሣ ፡ ዠምሮ ፥ ኋላ ፡ ወ
ዲያ ፡ ወዲህ ፡ ይኾናል ። እም ፡ ከ ፡ ካ ፡ እየኾነ ፡ በሰዋስው ፡ ላይ ፡ ሲወድቅ ፥ ተወላጅ ፡
ተከፋይ ፡ መገኛ ፡ ሰጭ ፡ ይኾናል ። ተወላጅ ፡ ሲኾን ፡ ተወልደ ፡ ቃል ፡ እምአብ ፤ ተከ
ፋይ ፡ ሲኾን ፡ ተወልደ ፡ ቃል ፡ እምድንግል ፤ ተወላጅና ፡ ተከፋይ ፡ ሲኾን ፡ ተወልደ ፡
ወልድ ፡ አው ፡ ሕፃን ፡ እምአቡሁ ፡ ወእሙ ። መገኛ ፡ ሲኾን ፡ ወፅአ ፡ ቃል ፡ እምአብ ፤
ተሰብከ ፡ ወንጌል ፡ ለአሕዛብ ፡ እምቃለ ፡ ሐዋርያት ። ሰጭ ፡ ሲኾን ፡ ተውህበ ፡ ወርቅ ፡
እምንጉሥ ፡ ለወዓሊሁ ፡ ያሰኛል ። አለግሱ ፡ የተነበበ ፡ እም ፡ ቦዝ ፡ አንቀጽ ፡ ይመረመ
ርበታል ፤ ይህም ፡ ዜነዋ ፡ ገብርኤል ፡ ለማርያም ፡ እምእግዚአብሔር ፤ ታዞ ፡ ተልኮ ።
ለዘሐወጸነ ፡ እምአርያም ፥ ወርዶ ፡ መጥቶ ። ተንሥአ ፡ እሙታን ፥ ተለይቶ ፡ ቀድሞ ፡
አስቀድሞ ። ሰብሕዎ ፡ ለእግዚ ፡ እምሰማያት ፤ ከመላእክት ፡ አብነት ፡ ነሥታችኹ ።
እምከርሥ ፡ ስሕቱ ፡ ወነበቡ ፡ ሐሰተ ፤ ከማሕፀን ፡ ዠምረው ፡ ማለቱን ፡ ያሳያል ። እም ፡
ይልቅ ፡ እጅግ ፡ ሲኾን ፡ በተመሳሳይ ፡ ቃል ፡ ይነገራል ፤ ይትበደር ፡ ሰብእ ፡ እምዕንቌ ፡
ሰንፔር ፡ ክቡር ፤ እምወርቅ ፡ ወእምብሩር ፡ ይትበደሩ ፡ ጻድቃን ። አንቲ ፡ ተዐብዪ ፡
እምብዙኃት ፡ አንስት ። ውጥንም ፡ ሲጨርስ ፡ የዐቢ ፡ ክብራ ፡ ለማርያም ፡ እምኵሎሙ ፡
ቅዱሳን ፡ ይላል ። የተነሣ ፡ ሲኾን ፡ ነ ፡ መንገለ ፡ በር ፡ ከፋቾች ፡ ኹነው ፡ ሳይኾኑም ፡
ብቻውን ፡ ምክንያት ፡ ባለው ፡ ቃል ፡ ይገባል ። ሰቀልዎ ፡ አይሁድ ፡ ለክርስቶስ ፡ እምነ ፡
እመንገለ ፡ ቅንአቶሙ ። የብሰ ፡ እምድንጋጼ ፡ ወጕየ ፡ እምፍርሀት ። ዠምሮ ፡ ሲኾን ፡
በቦታ ፡ በጊዜ ፡ ይገባል ፤ በቦታ ፥ እምጽንፍ ፡ እስከ ፡ ጽንፍ ፤ እምኢየሩሳሌም ፡ እ
ስከ ፡ ግብጽ ። በጊዜ ፥ እምአዳም ፡ እስከ ፡ ሙሴ ፤ እምትንሣኤ ፡ እስከ ፡ ዕርገት ። ኋላ ፡
ሲኾን ፡ በጸፉ ፡ ይገባል ፤ ወእምዝ ፡ ወሰዶ ፡ መንፈስ ፡ ገዳመ ፤ ወእምዝ ፡ መጽኡ ፡ አር
ዳኢሁ ፤ ከዚህ ፡ በኋላ ። ወዲያ ፡ ወዲህ ፡ ሲኾን ፥ ኢያበርህ ፡ ፀሓይ ፡ እምአድማስ ፡
አላ ፡ እምአድማስ ፡ ይላል ። ሲዘረዘርም ፤ እምኔሁ ፡ ሃ ፡ ሆሙ ፡ ሆን ፤ እምኔከ ፡ ኪ ፡
ክሙ ፡ ክን ፡ የ ፡ ነ ፡ እያሰኘ ፡ እንደሚስማማው ፡ ይፈታል ። እም ፡ ነን ፡ በር ፡ ከፋች ፡
ሳይዝ ፡ በ ፡ ፈ ፡ ሰ ፡ ጰ ፡ ፐ ፡ ብሎ ፡ በሚነሣ ፡ ቃል ፥ እምበረከት ፡ እምፈቃድ ፡ እምሰ
ማይ ፡ እምጳፉ ፡ እምፓና ፡ እያለ ፡ በቅኔ ፡ ሲገባ ፡ አፈ ፡ ጸያፍ ፡ ነው ። ፪ኛም ፡ ከግእዝ ፡
እስከ ፡ ሳብዕ ፡ ባለው ፡ በመ ፡ ፊደል ፡ በሚነሡ ፡ ቃላት ፡ ሲገባ ፡ ደጊመ ፡ ቃልነት ፡ ስላ
ለው ፡ እየጠበቀና ፡ እየዋጠ ፡ ቀለም ፡ ያስቀራል ። ይህም ፡ እመብረቅ ፡ እሙላድ ፡ እሚ
ናስ ፡ እማርያም ፡ እሜሎስ ፡ እምሥራቅ ፡ እሞት ፡ ማለቱን ፡ ያሳያል ።

፫ ፤ አይ ፡ ምንት ፡ መኑ ። ማእዜ ፤ አይቴ ፤ ስፍን ። በለቤት ፡ ሲኖር ፡ ቅጽል ፥ በለቤት ፡ ሲቀር ፡ በቂ ፡ ይኾናሉ ፤ ማእዜ ፡ ግን ፡ ብቻውን ፡ ይበቃል ። ቅጽልነታቸው ፡ በ፩ኛና ፡ በ፫ኛ ፡ ክፍል ፡ ተነግሯል ። አኹንም ፡ በዚህ ፡ የጥያቄ ፡ አገባብ ፡ ስለ ፡ ኹኑ ፡ ዐብሮ ፡ ይነገራል ። በንባብ ፡ ጥያቄ ፡ ብቻ ፡ ሲመስሉ ፡ በምስጢር ፡ አሉታ ፡ ናቸው ፤ ሁ ፡ ኑ ፡ ያጋንኗቸዋል ፤ አላ ፡ ዳእሙ ፡ በሕቱ ፡ ያጸድቋቸዋል ። አይ ፡ ምንት ፡ በበቂነትም ፡ በቅጽልነትም ፡ የግብር ፡ የነገድ ፡ የተቀብዖ ፡ ስም ፡ ይፈልጋሉ ። ይህም ፡ አይ ፤ ምንት ፡ ተሰቅለ ፤ ወይም ፡ አይ ፡ ብእሲ ፥ ምንት ፡ ሰብእ ፡ ተሰቅለ ፡ በቀራንዮ ፤ ነቢይሁ ፡ ኑ ፥ ወሚመ ፡ ሐዋርያ ፥ አው ፡ ረድእ ፡ ወእመ ፡ አኮ ፡ አሐዱ ፡ ጻድቅ ፤ አኮ ፡ ነቢይ ፡ ወአኮ ፡ ሐዋርያ ፥ ኢረድእ ፡ ወኢጻድቅ ፥ ዳእሙ ፡ አምላክ ፡ ሥግው ። ናሁ ፡ ተሰቅለ ፡ አሐዱ ፡ ብእሲ ፥ ምንት ፡ ብእሲሁ ፡ በለ ፡ ጊዜ ፥ አይሁዳዊ ፡ ወይም ፡ ክርስቲያናዊ ፡ መኾኑን ። ወናሁ ፡ ብእሲ ፡ ዲበ ፡ መንበር ፤ አይ ፡ ብእሲ ፡ ብሎ ፡ ጳጳስ ፡ ንጉሥ ፡ መኾኑን ፡ ይፈልጋል ። ምንት ፡ ሲቀር ፡ አይ ፡ መኑ ፡ በካል ፡ የተለየ ፡ የተጸውዖ ፡ ስም ፡ ይሻሉ ። ይህም ፥ አይ ፡ መኑ ፡ ተሰቅለ ፡ እምሐዋርያት ፡ ቍልቍሊተ ፡ በትዕይንተ ፡ ሮም ፥ ጳውሎስኑ ፡ ወሚመ ፡ ዮሐንስ ፤ አልቦ ፡ ዘተሰቅለ ፡ ዘእንበለ ፡ ጴጥሮስ ፡ ማለቱን ፡ ያሰያል ። ሂ ፡ ኒ ፡ ትራስ ፡ ሲኾኗቸው ፥ ማንም ፡ ይኾናሉ ፤ አይኒ ፡ ዘተምዐ ። በአይኒ ፡ ግብር ፡ እምግብራት ። ዘይዘብጥ ፡ መነሂ ፤ ማንንም ፡ ማን ። ኢአይኒ ፡ ወኢመኑሂ ፤ አንድስ ፡ እንኳ ፡ ያሰኛሉ ። ኢተገብረ ፡ ዘከማሁ ፡ ወኢበአይኒ ፡ መንግሥት ። አልቦ ፡ ዘርእየ ፡ ወኢመኑሂ ። በከፊል ፡ ሲገቡም ፡ እንዲሁ ፡ ናቸው ። ምንት ፡ ደግሞ ፡ ሂ ፡ ኒ ፡ ትራስ ፡ ሲኾኑት ፡ ምንምን ፡ አንዳች ፡ ይኾናል ። አሌዕል ፡ እደውየ ፡ ኀበ ፡ ሰማይ ፡ ከመ ፡ ኢይንሥእ ፡ ምንተኒ ፡ እምንዋይከ ። ዘወሀቦ ፡ አሐዱ ፡ ለካልኡ ፡ ምንተኒ ። ኢ ፡ ወኢ ፡ ሲገባበት ፡ ያልተፈጠረ ፡ ከንቱ ፥ ስምና ፡ ህላዌ ፡ የሌለው ፡ ተብሎ ፡ ይፈታል ። ሰፍሐ ፡ ለመስዕ ፡ ዲበ ፡ ኢምንት ፡ አው ፡ ዲበ ፡ ወኢምንት ።

አይ ፡ ማእዜ ፤ መቼ ፡ ይኾናሉ ፤ አየ ፡ ዘመነ ፡ በአይ ፡ ዘመን ፥ ማእዜ ፡ ተወልደ ፡ ክርስቶስ ። አይ ፡ ለኹሉ ፡ ይኾናል ፤ ማእዜ ፡ ግን ፡ ለጊዜ ፡ ብቻ ፡ ነው ፤ ሂ ፡ ኒ ፡ ትራስ ፡ ሲኾኑት ፡ ኢ ፡ ሲጨመርበት ፡ ማሰሪያው ፡ አሉታ ፡ ነው ። ኢለከሮን ፡ ፀሓይ ፡ ማእዜሂ ። ወኢማእዜኒ ፡ ኢኮኑ ፡ ሕያዋነ ፤ መቼም ፡ መች ። አይቴ ፤ ሔት ፡ ወዴት ፡ ይኾናል ፤ ዐዋጁ ፡ እንደ ፡ ማእዜ ፡ ነው ። በአይቴ ፡ ኀበ ፡ አይቴ ፡ እንተ ፡ አይቴ ፡ እምአይቴ ፡ እስከ ፡ አይቴ ፡ እያሰኙ ፡ የቦታ ፡ አገባቦች ፡ ይሰማሙታል ። ለ ፡ ሲሰማማው ፡ ኀበን ፡ በር ፡ ከፋች ፡ አድርጎ ፡ ለኀበ ፡ አይቴ ፡ ያሰኛል ። ሂ ፡ ኒ ፡ ትራስ ፡ ኹነውት ፡ ሳይኾኑትም ፡ ኢ ፡ ወኢ ፡ ሲጨመርበት ፡ ማሰሪያው ፡ አሉታ ፡ ነው ። ኢትፃእ ፡ እምህየ ፡ ወኢትሑር ፡ አይቴሂ ፤ ኢአይቴኒ ፥ የትም ፡ የት ፥ ወዴትም ፡ ወዴት ። ግሙራ ፡ ኢያስተርእየ ፡ ዘከመ ፡ ዝ ፡ ወኢበአይቴኒ ፤ በየትም ፡ በየት ፥ ባንድ ፡ስንኳ ፡ ቦታ ፡ ያሰኛል ። ስፍን ፡ እስፍንት ፡ ቱ ፤ ስንት ፡ ምን ፡ ያኽል ፡ ይኾናሉ ፤ ስፍን ፡ ያንድ ፥ እስፍንት ፡ የብዙ ፡ ነው ፤ ምስጢራቸው ፡ አኃዝ ፡ ስለ ፡ ኾነ ፡ በከፊል ፡ ይነገራሉ ። ሲገቡም ፡ በበቂነት ፥ እስፍንተ ፡ ኀረየ ፤ ወይም ፡ በቅጽልነት ፥ እስፍንተ ፡ ሐዋርያተ ፡ ኀረየ ፡ ክርስቶስ ፡ እምእስራኤል ፥ ክልኤተኑ ፡ አው ፡ ሠለስተ ፤ ዳእሙ ፡ ዐሠርተ ፡ ወክልኤተ ፡ ያሰኛሉ ። ሂ ፡ ኒ ፡ ትራስ ፡ ይኾኗቸዋል ፡ ማለት ፡ የለም ፡ እንጂ ፡ ዐዋጃቸው ፡ ኹሉ ፡ እንደ ፡ ሌሎቹ ፡ ነው ።

፺፩ ፤ መ ። ሚ ። መ ፡ ነገር ፡ ያበረታል ፥ ቃል ፡ ያገነታል ፤ አዳማቂ ፡ ኹኖ ፡ ይቀ ራል ፡ እንጂ ፥ ንኡስ ፡ አገባብ ፡ እንደ ፡ መኾኑ ፡ የተለየ ፡ ፍች ፡ የለውም ። እውነተኛ ፡ ፍችው ፡ ማ ፡ ነበረ ፤ በመምህራን ፡ ልማድ ፡ ከሰ ፡ ተደርበ ፡ ተነግሯል ። ከአይ ፡ እስከ ፡ እፎ ፡ ባሉት ፡ በንኡሳንና ፡ በደቂቅ ፡ ቅጽሎች ፡ በአንቀጽም ፡ ሳይቀር ፡ ትራስ ፡ እየ ኾነ ፡ በኹሉ ፡ ይገባል ። የጥያቄ ፡ አገባብ ፡ ኑ ፡ ሲንተራሰው ፡ ጥርጥር ፡ ያሳያል ። መ ኑመ ፡ አንተ ፤ ምንተኑመ ፡ ትርአዩ ፡ ወፃእክሙ ። ዝኑመ ፡ ብቻውንም ፡ አይቴመ ፥ እፎመ ፥ እስኩመ ፡ ውእቱመ ፥ ከልእመ ። በአንቀጽም ፡ መጽአመ ፡ ዘይመጽእ ፡ እያለ ፡ ይገባል ። ከንኡሳን ፡ በቀር ፡ በሌሎቹ ፡ ማ ፡ ተብሎ ፡ ሲፈታ ፡ ያምርለታል ። ሚ ፤ ምን ፡ ምንድር ፥ ምንኛ ፡ ስንት ፡ ይኾናል ። ምን ፡ ምንድር ፡ ሲኾን ፡ በአናቅጽ ፡ ኹሉ ፡ ይገባል ፤ ምስጢሩም ፡ ጥያቄ ፡ ምርመራ ፡ አንክሮ ፡ ነው ። ሚ ፡ የዐቢ ፡ እምረኃብ ፡ ወሚ ፡ ያሐምም ፡ እምቍር ። ሚ ፡ እግበሮ ፡ ለዝ ፡ ሕዝብ ። ሚ ፡ ላዕሌነ ፤ ምን ፡ አለ ብን ። ምንኛ ፡ ስንት ፡ ምን ፡ ሲኾን ፡ በኀላፊና ፡ በትንቢት ፡ በቅጽል ፡ ይገባል ፤ ሚ ፡ በዝኁ ፡ እለ ፡ ይሣቅዩኒ ። ሚ ፡ ይበዝኅ ፡ ሐዘነ ፡ እምየ ። ሚ ፡ መጠን ፡ ግርምት ፡ ዛቲ ፡ ዕለት ። እምን ፡ ተከትሎ ፡ በጸጸት ፡ በምኞት ፡ ሲገባ ፡ ምነው ፡ ይኾናል ። ሚ ፡ እሞትነ ፡ በግብጽ ፤ ምነው ፡ በሞትነ ። መጽሐፍ ፡ ግን ፡ እመ ፡ ሞትነ ፡ ሰበ ፡ ሞትነ ፡ ይላል ፡ (ዘፀ ፲፮ ፡ ፫) ። ሚመ ፡ ተብሎ ፡ በንድነት ፡ ሲነገር ፡ አማራጭ ፡ ነውና ፤ ኋላ ፡ ከአው ፡ ጋራ ፡ ይነገራል ።

፺፪ ፤ እፎ ። እንዴት ፡ ረግ ፥ ምን ፡ ምንኛ ፤ በ ፡ ሲወድቅበት ፡ ስለ ፡ ምን ፡ ይኾ ናል ። ኢ ፡ ኬ ፡ ኑ ፡ መ ፡ እንጋ ፡ እያጋነኑት ፡ ሳያጋንኑትም ፡ በኀላፊና ፡ በትንቢት ፡ በነ ባር ፡ በቅጽል ፡ ይገባል ፤ ምስጢሩም ፡ ጥያቄና ፡ አንክሮ ፡ ድንጋፄ ፡ ነው ፤ መዓትም ፡ ያሳያል ። እንዴትና ፡ ረግ ፡ ፩ ፡ ወገን ፡ ናቸው ፤ እፎ ፡ ወድቀ ፡ ኮከበ ፡ ጽባሕ ፡ እምሰ ማይ ። እፎ ፡ አግመርኪዮ ፡ ለዘኢይትገመር ። ኢ ፡ ኬ ፡ ሲያጋንኑት ፡ ራብዕ ፡ ያናግ ራል ፤ ኢ ፡ ደግሞ ፡ ኤ ፡ ይኾናል ። እፎኢ ፡ እንዘ ፡ አይሁዳዊ ፡ አንተ ፡ ትስእል ፡ በኀቤየ ፡ ትስተይ ፡ ማየ ፡ እንዘ ፡ ሳምራዊት ፡ አነ ፤ ኤ ፡ እንዴት ፡ ነዋ ፡ ረግና ። እፎኬ ፡ ሰቀልዎ ፤ እንዴት ፡ ነዋ ፡ ሰቀሉት ። በቀሩትም ፡ እፎኑ ፡ ንዜኑ ። እፎመ ፡ ዘኢያምጻእክምዎ ። እፎኑመ ፡ ይኳንን ፡ ዓለመ ። እፎ ፡ እንጋ ፡ ማሕፀነ ፡ ድንግል ፡ ጾሮ ፡ እያለ ፡ ይገባል ። ምን ፡ ምንኛ ፡ ሲኾን ፥ እፎ ፡ ትቤ ። እፎ ፡ ተሰባሕከ ፡ ኤልያስ ፡ ያሰኛል ። በቅጽልም ፡ ኦ ፡ ሞት ፡ እፎ ፡ ዝክርከ ፡ መሪር ፡ እያለ ፡ ምንኛ ፡ ይኾናል ። ስለ ፡ ምን ፡ ሲኾን ፥ በእፎ ፡ ትነውኅ ፡ ዕለት ፡ እምዕለት ፡ ይላል ። በደጊመ ፡ ቃልም ፡ ሲነገር ፡ በደጊመ ፡ ቃል ፡ ይፈ ታል ፤ ይህም ፡ እፎ ፡ እፎ ፥ ወይም ፡ እፈፎ ፤ ምንምን ፥ ምን ፡ ምን ፡ ምንኛ ፥ እንዴት ፡ እንዴት ፥ ረግ ፡ ረግ ። እፈፎ ፡ ትቤ ፡ (ቄር) ። እፎያዊ ፤ እንዴት ፡ ያለ ፥ እንደ ፡ ምን ፡ ያለ ፡ ያሰኛል ።

፺፫ ። ሁ ፤ ኑ ። ጥያቄና ፡ አጋናኝ ፡ ናቸው ፤ በነገር ፡ ኹሉ ፡ ትራስ ፡ እየኾኑ ፡ ይገ ባሉ ። ጥያቄ ፡ ባለው ፡ ቃል ፡ ሲገቡ ፡ን ፡ ይኾናሉ ፤ ምስጢራቸውም ፡ ጥያቄን ፡ መደብ ፡ አድርጎ ፡ ማድነቅና ፡ መናቅ ፡ መሰልቸት ፡ ያሳያል ። ጥያቄና ፡ ድንቅ ፡ ሲኾኑ ፡ በንድ ፡ ቃል ፡ አንዳንድ ፡ ጊዜ ፡ ብቻ ፡ ይነገራሉ ፤ ትሳአሉኒሁ ፡ መጻእክሙ ። ይትከሀልኑ ፡

ይፃእ ፡ ኄር ፡ እምናዝሬት ፡፡ ድኩምኑ ፡ ከመ ፡ ዝ ፡ ይገብር ፡፡ መናቅና ፡ መሰልቸት ፡ ሲኾኑ ፡ ተመላልሰው ፡ ይነገራሉ ፤ መኑ ፡ ያኀድገነ ፡ ፍቅሮ ፡ ለክርስቶስ ፡ ሕማምኑ ፡ ምንዳቤኑ ፡ መጥባሕትኑ ፡፡ ይቤ ፡ ነዳይ ፡ ዘጸንዐ ፡ ቦቱ ፡ ምንዳቤ ፡ ምንት ፡ ይኄይሰኒ ፡ ሞትኑ ፡ ስደትኑ ፡ ሰሪቅኑ ፤ ስርቆትን ፡ ያሰኛል ፡፡ አጋናኝ ፡ ሲኾኑ ፡ ከአይ ፡ እስከ ፡ እፎ ፡ ባሉት ፡ ይገባሉ ፡፡ ዳግመኛም ፡ ቦሁ ፡ ቦኑ ፡ እያሉ ፡ ሲገቡ ፡ በውኑ ፡ ተብለው ፡ ይፈታሉ ፡፡ ቦኑ ፡ መሢዕተ ፡ ወቍርባነ ፡ አባእክሙ ፡ ሊተ ፡፡ ቦኑ ፡ ይብሎ ፡ ጽቡር ፡ ለለብሓዊ ፡ ኢትግበረኒ ፡ ከመ ፡ ዝ ፡፡ ቦኑ ፡ ለባሕቲቶሙ ፡ ለአይሁድ ፡ እግዚ ፡፡ በቅጽልና ፡ በጥሬ ፡ ግን ፡ አለን ፡ ያሰኛሉ ፡፡ ቦሁ ፡ ዘይሴወር ፡ እምኔየ ፡፡ ቦኑ ፡ ዘተርፈ ፡ ኀቤከ ፡፡ ይቤላሁ ፡ ለዘይቤሎን ፡ ቦኑ ፡ ረአይ ፡ በዛቲ ፡ ሀገር ፡ እወ ፡ ቦ ፡፡

፺፩ ፤ አ ፡፡ የጥሬ ፡ አገባብ ፡ ነው ፤ ሆይ ፡ ምን ፡ ወዮ ፡ ይብላኝ ፡ ይኾናል ፡፡ በተለየም ፡ ላራቱ ፡ ቅርቦች ፡ የሰሚ ፡ አገባብ ፡ ነው ፡፡ ሆይ ፡ ሲኾን ፡ ቃለ ፡ ጽዋዔ ፡ ነው ፤ ምስጢሩም ፡ አክብሮና ፡ አፍቅሮ ፡ አራኅርኖና ፡ ምክር ፡ አፍርሆና ፡ አኅስሮ ፡ ወቀሣም ፡ ያሳያል ፡፡ ጽዋዔ ፡ ለሩቅም ፡ ለቅርብም ፡ ሲነገር ፡ የሩቁ ፡ ተጠሪ ፡ የቅርቡ ፡ ሰሚ ፡ ይባላል ፤ ምስጢሩ ፡ አክብሮ ፡ ሲኾን ፡ አ ፡ ኢየሱስ ፡ ወልደ ፡ ዳዊት ፡ ተሣሀለነ ፡፡ አፍቅሮ ፡ አ ፡ ማርያም ፡ በእንተ ፡ ዝ ፡ ናፈቅረኪ ፡፡ አራኅርኖ ፡ አ ፡ መስተምሕርት ፡ አስተምሕሪ ፡ ኀበ ፡ ወልድኪ ፡፡ አ ፡ ዮሴፍ ፡ ወልደ ፡ ዳዊት ፡ ኢትፍራህ ፡ ነሢአታ ፡ ለማርያም ፡ ፍኅርትከ ፡፡ ምክር ፡ ሲኾን ፡ አ ፡ ወልድየ ፡ ስምዐኒ ፡ ዘእብለከ ፡፡ አፍርሆ ፡ አ ፡ ሀገረ ፡ ሰዶም ፡፡ አኅስሮ ፡ አ ፡ ይሁዳ ፡ አ ፡ ሐናንያ ፡ እፎ ፡ መልአ ፡ ሰይጣን ፡ ውስተ ፡ ልብከ ፡፡ ወቀሣም ፡ ሲኾን ፡ አ ፡ አዳም ፡ ምንተኑ ፡ ረሰይናከ ፡ ማለቱን ፡ ያሳያል ፡፡ ምን ፡ ሲኾን ፡ ቃለ ፡ አንክሮ ፡ ነው ፤ ለክፉም ፡ ለበጎም ፡ ይነገራል ፤ ለ ፡ እየተከተለው ፡ ሳይከተለውም ፡ በቅጽል ፡ በጥሬ ፡ ይገባል ፡፡ አ ፡ ዝንቱ ፡ ምስጢር ፡፡ አ ፡ ዕሙቀ ፡ ብዕለ ፡ ጥበቡ ፡፡ አ ፡ ለዝ ፡ ዝንጋዔ ፡፡ አ ፡ ለዝ ፡ ኀሊና ፡፡ ወዮ ፡ ይብላኝ ፡ ሲኾን ፡ ቃለ ፡ ሰቈቃው ፡ ነው ፤ እምና ፡ ለ ፡ ይስማሙታል ፡፡ አ ፡ ሞት ፤ አ ፡ እምዝንቱ ፡ ሞት ፡ ዘሥሉጥ ፡ ላዕለ ፡ ዕጓለ ፡ መሕያው ፡፡ አ ፡ ለዘሞተ ፡፡ አ ፡ ለይሁዳ ፤ እስመ ፡ ሤጠ ፡ ለእግዚኡ ፡፡ ፪ኛም ፡ የሰሚ ፡ አገባብ ፡ ሲኾን ፡ ምስጢሩ ፡ ከጽዋዔነት ፡ አይወጣም ፤ ሰሚዎቹም ፡ ፬ ፡ ናቸው ፤ አንተ ፡ አንቲ ፡ አንትሙ ፡ አንትን ፤ አቀራቢቻቸውም ፡ ዝርዝሮች ፡ ፬ ፡ ናቸው ፤ ከ ፡ ኪ ፡ ክሙ ፡ ክን ፡፡ አ ፡ እየገባባቸው ፡ ሳይገባባቸውም ፡ ብቻቸውን ፡ እየተጠሩ ፡ ይሰማሉ ፡፡ አ ፡ ሰገባ ፡ አ ፡ አግዚአ ፡ አ ፡ ብእሲቶ ፡ አ ፡ አንትሙ ፡ ሕዝበ ፡ ክርስቲያን ፡ አ ፡ አዋልድየ ፡፡ አ ፡ ሲቀር ፡ ስምዐኒ ፡ እግዚኦ ፤ ስምዒ ፡ ወለትየ ፤ አጽምዑ ፡ ሕዝብየ ፤ አዋልደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ ኢትብክያ ፡ ላዕሌየ ፡ እያለ ፡ ሌላውን ፡ ኹሉ ፡ ያሳያል ፡፡ እነዚህም ፡ ፬ቱ ፡ ቅርቦች ፡ በ፮ ፡ ነገር ፡ ይሰማሉ ፤ በማሰሪያ ፡ አቅራቢ ፡ ባንቀጽ ፡ አቅራቢ ፡ በቅጽል ፡ አቅራቢ ፡ በባለቤት ፡ አቅራቢ ፡ በዘርፍ ፡ አቅራቢ ፡ ባገባብ ፡ አቅራቢ ፡ ይሰማሉ ፡፡ በማሰሪያ ፡ አቅራቢ ፡ ሲሰሙ ፡ አ ፡ አብ ፡ ፈኖከ ፡ ወልደ ፡፡ ባንቀጽ ፡ አቅራቢ ፡ አመ ፡ ፈኖከ ፡ ወልደ ፡፡ በቅጽል ፡ አቅራቢ ፡ ፍቁርከ ፡፡ በባለቤት ፡ አቅራቢ ፡ ተሰቅለ ፡ ወልድከ ፡፡ በዘርፍ ፡ አቅራቢ ፡ ወልደ ፡ ባሕርይከ ፡፡ ባገባብ ፡ አቅራቢ ፡ አንቃዕደወ ፡ ኀቤከ ፡፡ ሰሚ ፡ ከክፍል ፡ ወዲህ ፡ ኹኖ ፡ ከክፍል ፡ ወዲያ ፡ ያለውን ፡ አይሰማም ፤ ይህም ፡ አ ፡ አብ ፡ ይነብሩ ፡ አሕዛብ ፡ በአም

ሏከ ፡ ጣፆት ፤ ባሕቱ ፡ እሉ ፡ አከ ፡ ሕዝብከ ፡ አለማለቱን ፡ ያሳያል ። እንደዚሁ ፡ ደግሞ ፡ ከዋዌ ፡ በታች ፡ ኹኖ ፡ ከዋዌ ፡ በላይ ፡ ያለውን ፡ አይሰማም ፤ ይህም ፥ አ ፡ አብ ፡ አይሁድ ፡ ዐለዉ ፡ ሕገ ፡ ወሰቀሉ ፡ ወልደከ ፡ አለማለቱን ፡ ያሳያል ።   ፫ኛም ፡ ኡኡ ፡ ተብሎ ፡ በደጊመ ፡ ቃል ፡ ሲነገር ፡ ኡኡ ፡ ይኸናል ፤ የሪታና ፡ የቡታ ፡ ቃል ፡ ነው ፤ የሰው ፡ ያለኸ ፡ ድረሱልኝ ፡ ማለት ፡ ይሰማበታል ። ሆይ ፡ ሆይ ፡ ተብሎም ፡ ሲፈታ ፡ የክፉ ፡ አንክሮና ፡ ቃለ ፡ አፍርሆ ፡ ነው ፤ የጭንቅና ፡ የመከራ ፡ ብዛት ፡ ያሳያል ። ኡኡ ፡ ጕዩ ፡ እምሰሜን ።

፺፫ ፤ አሌ ፤ ወይ ፤ ወይሌ ፤ ሰይ ።   ኹሉም ፡ ቃለ ፡ ብካይ ፡ ናቸው ፤ ወዮ ፡ ወየው ፡ ወዮታ ፡ እዬዬ ፡ ይኸናሉ ። አሌ ፡ ሎ ፡ አሌ ፡ ላ ፤ ወይ ፡ ሊተ ፡ ሰይ ፡ ልየ ፤ ወይሌ ፡ ለቅጥቃጤየ ፡ እያሰኙ ፡ በለ ፡ ሲገቡ ፥ ወዮልኝ ፡ ወዮታ ፡ አለብኝ ፡ ወዮታ ፡ ይገባታል ፤ ወይሌ ፡ ላዕለ ፡ ናበው ፤ ወዮታ ፡ አለባት ፡ ያሰኛሉ ። ብቻቸውንም ፡ ወይ ፡ እኍየ ፡ ወይ ፡ እግዚእየ ፡ እያሉ ፡ በቅርብ ፡ በቅርብ ፡ ይገባሉ ።

አህ ፥ አሀህ ፤ ዬ ፤ ሐዊሳ ።   አህ ፡ አሀህ ፥ የአንክሮና ፡ የደስታ ፡ የሐዘንና ፡ የነቀፌታ ፡ ነው ፤ የአንክሮና ፡ የደስታ ፡ ሲኾን ፡ አዬ ፡ አዬ ፥ ዋይ ፡ ዋይ ፡ ይኸናል ። አህ ፡ አህ ፡ አንደደኒ ፡ ፍቅርከ ። አህ ፡ አህ ፡ ለድምፀ ፡ ቅኔሆሙ ። ሐዘንና ፡ ነቀፌታ ፡ ሲኾን ፡ ወዲያ ፡ ወዲያ ፡ ጓድግ ፡ ይኸናል ፤ አህ ፡ አህ ፡ እምዛቲ ፡ ኀፍረት ። አህ ፡ አህ ፡ እምዛቲ ፡ ሕሠም ።   ዬ ፤ የልቅሶና ፡ የደስታ ፡ ቃል ። የልቅሶ ፡ ሲኾን ፡ በቁሙ ፡ ወዮ ፡ ወየው ፡ እዬዬ ፡ ይኸናል ። ዬ ፡ ዬ ፡ ዬ ፡ አውረድዎ ፡ እምዕፅ ። የደስታ ፡ ሲኾን ፡ እንሆ ፡ ዕሠይ ፡ ይኸናል ። ዬ ፡ መስቀል ፡ ጸገየ ። አንፈርዐጹ ፡ ሰብአ ፡ ሰገል ፡ ረኪቦሙ ፡ ሕፃነ ፡ ዘተወልደ ፡ ለነ ፥ ዬ ፡ ዬ ፡ ዬ ።   ሐዊሳ ፤ የደስታና ፡ ያንክሮ ፡ ቃል ፤ ዕሦ ፡ ዕሦ ፡ ይኸናል ። ሐዊሳ ፡ ለምጽአትከ ። ሐዊሳ ፡ ሐዊሳ ፡ ለዝንቱ ፡ ሐዋርያ ። ምስጢሩ ፡ ደስ ፡ የሚያሰኝ ፡ ነገር ፡ ከማየት ፡ ከመስማት ፡ የተነሣ ፡ ራስን ፡ ዐንገትን ፡ በመነቅነቅና ፡ በማድነቅ ፥ ወሰው ፡ ወሰው ፥ መልካም ፡ መልካም ፥ ይበል ፡ ይበል ፡ ማለትን ፡ ያሳያል ።   በሓ ፤ በአድንኖተ ፡ ርእስ ፡ የሚነገር ፡ የሰላምታ ፡ ቃል ፥ ሰላም ፡ ለከ ፡ ይኸናል ፤ በሓከ ፡ ኪ ፡ ክሙ ፡ ክን ፡ እያለ ፥ ሳይዘረዘርም ፡ በሓ ፡ ንጉሦሙ ፡ ለአይሁድ ፡ እያሰኘ ፡ ባሩቱ ፡ ቅርቦች ፡ ይነገራል ።

፺፬ ፤ እስኩ ፤ ዮጊ ። እንጋ ፤ እንዳዒ ።   እስኩ ፥ እስኪ ፡ ይኸናል ፤ ጥያቄ ፡ ባለው ፡ ቃል ፡ በሣልሳይ ፡ አንቀጽ ፡ ቀድሞ ፡ ተከትሎ ፡ ይገባል ። እስኩ ፡ ንግረኒ ፡ ምንትኑ ፡ ዝ ፡ ነገር ፡ ዘትሜህር ። ንግረኒ ፡ እስኩ ፥ ሰብአ ፡ ሮሜኑ ፡ አንተ ። እስኩ ፡ ፍትሑ ፡ ለሊክሙ ። እስኩ ፡ በሎሙ ።   ዮጊ ፤ እንሆ ፡ አኹን ፥ ወይ ፡ ምናልባት ፡ ይኸናል ፤ በኀላፊና ፡ በትንቢት ፡ ይገባል ። እምትሡዒ ፡ ለአማልክት ፡ ወእምዕጣነ ፡ ታዕርጊ ፥ ተመትሮተ ፡ ክሣድ ፡ አብደርኪ ፡ ወኀረይኪ ፡ ዮጊ ። ገሥጾ ፡ ለዐርክከ ፡ ዮጊ ፡ ኢገብረ ። ኢትፍቅድ ፡ ከዊነ ፡ መኰንን ፤ ዮጊ ፡ ኢትክል ፡ ተበቅሎቶ ፡ ለዘአበሰ ፥ ወዮጊ ፡ ታደሉ ፡ ለገጸ ፡ ዐቢይ ። እንጋ ፡ እንዳዒ ፤ ንኡስ ፡ ቅጽልና ፡ የጥያቄ ፡ አገባብ ፡ እየተከተሉ ፡ ሲገቡ ፡ እንጃ ፡ ይኸናሉ ፤ ምስጢራቸው ፡ ምኞትና ፡ አንክሮ ፡ ጥርጥር ፡ ያሳያል ። አሐዩኑ ፡ እንጋ ፡ እስከ ፡ እማንቱ ፡ መዋዕል ። መኑ ፡ እንጋ ፡ ይክል ፡ ድኅነ ። እንዳዒ ፡ እመ ፡ ቦ ፡ ዘኀለየ ፡ ልብከ ። እንጋ ፡ ተለይቶ ፡ አለጥያቄ ፡ በኀላፊ ፡ አንቀጽ ፡ ሲገባ ፡ እንሆ ፡ ይኸናል ። እንጋ ፡ በጽ

ሐት ፡ ኅቤክሙ ፡ መንግሥተ ፡ እግዚአብሔር ። በነባር ፡ አንቀጽም ፡ አነሁ ፡ እን.ጋ ፡ እማ ዚ.አ ፡ እያለ ፡ ይገባል ።   እንዳዒ ፥ እንጂ. ፡ ሲ.ኾን ፡ ርእየ ፡ ሰምዐ ፡ አእመረ ፡ እኒህን ፡ የመሰሉ ፡ ግሶች ፡ ይወርሳል ። እንጃ ፡ ማለት ፡ አላየኹም ፡ አልሰማኹም ፡ አላውቅም ፡ ማለት ፡ ነው ። እንዳዒ ፡ ኢ.ያእመርነ ፡ ከመ ፡ ይመልእ ፡ ኵሉ ፡ ዝቅ ፡ ወይነ ፡ እንዳዒ ፡ እመ ፡ በ ፡ ዘኀለይከ ። አሉታውንም ፡ በጽድቅ ፡ ውጥን ፡ ይጨርሳል ። አልቦ ፡ ዘየዐብየኒ ፡ በዝንቱ ፥ እንዳዒ ፡ ገብርኤል ።

፺፯ ፤ ክመ ። ጽመ ፡ ጽሚ.ተ ። ኳ ። እንቋዕ ። ጥቀ ።   ክመ ፡ ብቻ ፡ መቼም ፡ መች ፥ ድንት ፡ ይኾናል ፤ ኹሉም ፡ የጊዜ ፡ ነው ። ብቻ ፡ ሲ.ኾን ፥ ሐቀ ፡ ክመ ፤ ንስቲተ ፡ ክመ ፥ ተርፎሙ ፡ ይላል ፤ ጥቂት ፡ ብቻ ፡ ማለት ፡ ነው ። መቼም ፡ መች ፡ ሲ.ኾን ፡ ሂ ፡ ኒ ፡ ትራስ ፡ እየኾኑት ፡ ሳይኾኑትም ፡ ብቻውን ፡ ይገባል ። ክመኒ ፡ ኢ.ወረደ ፡ እይኅ ፡ ከመ ፡ አመ ፡ ኖኅ ። ክመ ፡ ኢ.ኮነ ፡ ዕረፍት ፡ ለእስራኤል ፡ ከመ ፡ አመ ፡ ነገሠ ፡ ሰሎሞን ። አንተሰ ፡ አንተ ፡ ክመ ። ድንት ፡ ሲ.ኾን ፡ በጸጸት ፡ በምኞት ፡ ይገባል ፤ ሶበ ፡ ኢ.ዐለወ ፥ አው ፡ ሶበ ፡ ኢ.የዐሉ ፡ አዳም ፡ ትእዛዘ ፡ እግዚ.አ ፡ ክመ ፡ እምነበረ ፡ ውስተ ፡ ገነት ፡ በከመ ፡ ይነብሩ ፡ ሔኖክ ፡ ወኤልያስ ። ንበር ፡ ክመ ፥ ያንብርከ ፡ ክመ ፡ እያለም ፡ በሣልሳይ ፡ አንቀጽ ፡ ይገባል ።   ጽመ ፤ ዝም ፡ ብሎ ፥ ቀስ ፡ ብሎ ፥ ዝግ ፡ ብሎ ፡ ይኾናል ። መጽአ ፡ ጽመ ፥ ይመጽእ ፡ ጽመ ፥ ነዐ ፡ ጽመ ፥ ሐ.ር ፡ ጽመ ፥ ብላዕ ፡ ጽመ ፡ እያለ ፡ በዘማች ፡ አንቀጽ ፡ ይገባል ።   ጽሚ.ተ ፡ ጽምሚ.ተ ፤ በዝምታ ፡ በቀስታ ፡ በስውር ፡ ይኾናል ፤ ኢ.ፈቀደ ፡ ይክሥታ ፡ አላ ፡ መከረ ፡ ጽሚ.ተ ፡ ይኅድጋ ። አልቦ ፡ ዘተናገርኩ ፡ ጽሚ.ተ ፤ ሰውሬ ፡ በስ ውር ።   ኳ ፤ እኮ ፡ በ.ያ ፡ እንኳ ፡ ይኾናል ፤ ትራስ ፡ እየኾነ ፡ በቃል ፡ መጨረሻ ፡ ይገ ባል ። እኮ ፡ በ.ያ ፡ ሲ.ኾን ፥ አገባቡ ፡ እንደ ፡ እስመ ፡ ነው ፤ የእስመን ፡ ፫ኛውን ፡ ፍች ፡ ተመልከት ። እንኳ ፡ ሲ.ኾን ፥ በብትን ፡ ይገባል ፤ ሕሡመ ፡ ይሜንኖ ፡ ኃጥእ ፡ ለጻድቅ ፥ ዝሰ ፡ ይትርፍ ፡ ቀቲሎቶ ፡ ኳ ፥ ይቅትሎ ፡ ኳ ፡ ይትሜነይ ። መግደሉን ፡ እንኳ ፥ ሊ.ገድ ለው ፡ እንኳ ፡ ይመኛል ።   እንቋዕ ፤ የደስታ ፡ ቃል ፥ እንኳዕ ፡ ይኾናል ፤ ዕሡይ ፡ ዕሦ ፡ ወሰው ፡ ውሽን ፡ ማለት ፡ ነው ፤ በኀላፊና ፡ በትንቢ.ት ፡ ይገባል ። እንቋዕ ፡ ተሰብረት ፡ ማዕጾ ፡ አሕዛብ ። እለ ፡ ይብሉኒ ፡ እንቋዕ ፡ እንቋዕ ።   ጥቀ ፤ ስንኳን ፡ ይኾናል ። ወ ፡ ሂ ፡ ኒ ፡ ስንኳን ፡ ሲ.ኾኑ ፡ ይሰማሙታል ። ይቤሎ ፡ ለዘይቤሎ ፡ ትፈቅድኑ ፡ ይሙት ፡ እጐየ ፥ ጥቀ ፡ ይሙት ፥ ጥቀ ፡ ሞት ፥ ሕማምኒ ፡ ወሕማምሂ ፥ ሕማም ፡ ኳ ፡ ኢ.ይርከበ ። አብርሃም ፡ ጥቀ ፡ ሞተ ፥ ወነቢ.ያትኒ ፡ ሞቱ ። አልቦ ፡ ዘመድ ፡ ጊዜ ፡ ተዋርዶ ፤ ወይከ ውን ፡ ባዕደ ፡ ጊዜ ፡ ተዋርዶ ፡ ዘመድ ፤ እመሰ ፡ ይትሌዐል ፡ በንብረተ ፡ ሥጋ ፡ ማእድ ፥ ጥቀ ፡ ዘመዱ ፡ ወጥቀ ፡ ነገድ ፥ ባዕድ ፡ ይዘመድ ። እንኳንና ፡ እንኳ ፡ እንኳዕና ፡ ስንኳን ፡ ልዩ ፡ ልዩዎች ፡ እንደ ፡ ኾኑ ፡ አስተውል ። እንኳን ፡ የእኮ ፡ ፍች ፡ ነው ፤ ምስጢሩም ፡ አሉታ ። እንኳ ፡ የኳ ፡ ፍች ፡ ነው ፤ ምስጢሩም ፡ አንክሮና ፡ ምኞት ፡ ማበላለጥ ፡ ነው ፤ በማበላለጡ ፡ ከጥቀ ፡ ይጎራበታል ። እንኳዕ ፡ የእንቋዕ ፡ ብቻ ፡ ነው ፤ ምስጢሩም ፡ ደስታ ። ስንኳን ፡ ግን ፡ የማማረጥና ፡ የማሻሻል ፡ ቃል ፡ ነው ፤ ከኳ ፡ ብቻ ፡ እንጂ. ፡ ከ፫ቱ ፡ አይመሳሰልም ።

፺፰ ፤ እንከ ። እምዮም ፥ እምይእዜ ። እንከ ፥ እንከ.ያ ፥ እንግዴ.ህ ፡ ከንግዴ.ህ ፡ ወዲ.ህ ፥ ከዚ.ያ ፡ ወዲ.ያ ፡ እንሆ ፡ ይኾናል ፤ የነገር ፡ ዚ.ቅ ፡ ወይም ፡ ዘዬ ፡ ይባላል ። ከኹን ፡

ዠምሮ ፡ ወደ ፡ ፊት ፡ በሚመጣ ፡ ነገር ፡ ቃልን ፡ ተከትሎ ፡ ይገባል ፤ ሰና ፡ ኬ ፡ ትራስ ፡ ሲኾኑት ፡ ግን ፡ በፊትም ፡ በኋላም ፡ ይገባል ። እንኪያ ፡ ሲኾን ፡ ይቤሎ ፡ ለዘይቤሎ ፡ አልብየ ፥ መፍቅድ ፡ ኀቤከ ፡ ለምንት ፡ እንከ ፡ መጻእከ ፡ ኀቤየ ፤ እንኪያ ፡ ወደኔ ፡ ለምን ፡ መጣኽ ። ዘትገብር ፡ እንከ ፡ ፍጡነ ፡ ግበር ። ትሬኢ ፡ እንከ ፡ ዘየዐቢ ፡ ኀጢአተ ፤ እን ግዴህ ፡ ከንግዴህ ፡ ወዲህ ። እንከሰ ፡ አወቅሥ ። ግበሩ ፡ እንከሰ ። እንከሰኬ ፡ ይብልዑ ፡ ፍሬ ፡ ምግባሮሙ ፤ እንግዴህስ ። ኀደገት ፡ እንከ ፡ ብሂሎታ ። ወኢይሰማዕ ፡ እንከ ፡ ፀመፃ ። አልቦ ፡ እንከ ፡ መዓልት ፡ ወኢሌሊት ፤ ከዚያ ፡ ወዲያ ። ሀለወ ፡ እንከ ፡ ኀቤነ ፡ ክልኤቱ ፡ አኀው ፤ እንሆ ። እንከ ፥ እንሆ ፡ መኾኑ ፡ በናሁ ፡ ፈንታ ፡ ሲገባ ፡ ነው ። እም ዮም ፡ እምይእዜም ፡ እንከ ፡ በገባበት ፡ እየገቡ ፡ የርሱን ፡ አፈታት ፡ ይወርሳሉ ።

፺፱ ፤ አ ፤ ሰ ፤ ኬ ።   አ ፥ ቃለ ፡ መልእክት ፡ ነው ፤ ትራስ ፡ እየኾነ ፡ በኹሉ ፡ ይገ ባል ፤ ምስጢሩም ፡ ቍልምጫና ፡ ከበሬታ ፡ ነው ። በቅርብ ፡ ሲገባ ፡ ቃለ ፡ አጋኖ ፡ ቃለ ፡ አስተብቍዖ ፡ ቃለ ፡ ተጋንዮ ፡ ይኾናል ። አስተብቍዖ ፡ ሲኾን ፡ ፍችው ፡ እባክኽ ፡ ነው ፤ ያንኑ ፡ በደጊመ ፡ ቃል ፡ ያናግራል ። ተጋንዮ ፡ ሲኾን ፡ መድረሻውን ፡ ፊደል ፡ እንደ ፡ ኬ ፡ ራብዕ ፡ ያደርጋል ፤ በትርፍ ፡ ዐማርኛም ፡ እኮ ፡ ይኾናል ። መልእክት ፡ ሲኾን ፡ ፈነውኩአ ፡ ይዜንውዎአ ፡ ለእግዚእየአ ፡ ዒሳውአ ፡ ከመአ ፡ እርከብአ ፡ ሞገ ሰአ ፡ ይላል ። አጋኖ ፡ አንተኑአ ፡ ውእቱ ፡ ግብጻዊ ። አንተኑአ ፡ ዘይመጽእ ፥ ወሚመ ፡ ካልእ ። አስተብቍዖ ፥ አ ፡ እግዚአ ፡ አድኅንአ ፡ አድኅነነአ ፤ እባክኽ ፡ አድነን ፤ ወይም ፡ በደጊም ፡ እባክኽ ፡ እባክኽ ፥ አድነን ፡ አድነን ፡ ያሰኛል ። ተጋንዮ ፥ እግዚእየአ ፡ እኁ የአ ፡ እያለ ፡ ይህን ፡ በመሰለ ፡ ሲገባ ፥ ጌታዬዋ ፡ ወንድሚዋ ፥ ወይም ፡ እንደ ፡ ፊቱ ፡ ጌ ታዬ ፡ ጌታዬ ፡ ወንድሜ ፡ ወንድሜ ። ሀበኒአ ፡ ኅድገኒአ ፡ እያለም ፡ ሲገባ ፡ በደጊም ፡ ይፈታል ፤ ወይም ፡ ስጠኛ ፡ ተወኛ ፤ ስጠኝ ፡ እኮ ፡ ተወኝ ፡ እኮ ፡ እያሰኘ ፡ ለክፉም ፡ ለበጎም ፡ ይኾናል ።   ሰ ፤ ከአ ፡ የበረታ ፡ የልመና ፡ ቃል ፡ ነው ፤ ቍርጥ ፡ ባለው ፡ ነገር ፡ በሣልሳይ ፡ አንቀጽ ፡ እየገባ ፡ እባክኽ ፡ ይኾናል ። ወይም ፡ አንቀጽ ፡ ይዘረዝ ራል ። አምላከ ፡ ኀያላን ፡ ተመየጥሰ ፤ ተመየጠነ ፥ ተመየጥ ፡ ለነ ። አድኅንሰ ፥ ሠርሕሰ ፤ አድኅነነ ፥ ሠርሐነ ፡ ሠርሕ ፡ ለነ ።   ኬ ፤ እንደ ፡ አ ፡ ትራስ ፡ እየኾነ ፡ በኹሉ ፡ ሲገባ ፡ መድረሻውን ፡ ፊደል ፡ ራብዕ ፡ ያደርጋል ፤ ምስጢሩም ፡ ማጋነንና ፡ ማስደነቅ ፡ ነው ። አንዳንድ ፡ ጊዜም ፡ ራብዕ ፡ ሳያደርግ ፡ አጋኖ ፡ ይቀራል ፤ ወይም ፡ ማ ፡ ይኾናል ፤ ማ ፡ መኾኑም ፡ በመ ፡ ፈንታ ፡ ገብቶ ፡ ሲገኝ ፡ ነው ፤ ይምጽኡኬ ፡ ይርአዩ ። ውእቱኬ ፡ ዘወ ረደ ። ዝኬ ፡ እፎ ፡ ይሀሳ ። ምንትኬ ፡ ሰብእ ። ምንትኬ ፡ ዘአሚሃ ፡ ዐውያት ። ማ ፡ ሲኾን ፡ ጽናሕኬ ፡ ጽንሕኒኬ ። አንተኬ ፡ ትሰመይ ፡ ኬፋ ፡ እያሰኘ ፡ ይህን ፡ በመሰለ ፡ ይገባል ።

አሉታ ፡ የጽድቅ ፡ መከታ ።

፻ ፤ አል ፤ ኢ ።   አል ፡ የኢ ፡ ፍች ፡ ነው ፤ አሉታነቱም ፡ ያማርኛና ፡ የዕብራይ ስጥ ፡ እንጂ ፡ የግእዝ ፡ አይዶለም ። ይኸውም ፡ ሊታወቅ ፡ ከበ ፡ በቀር ፡ በሌላ ፡ አንቀጽ ፡ ገብቶ ፡ አይገኝም ፤ በ ፡ አልበ ። ኢ ፡ በአናቅጽ ፡ ኹሉ ፡ እየገባ ፡ ጽድቁን ፡ አሉታ ፡ ያደ ርጋል ፤ ሲፈታም ፡ ም ፡ ጽንዕ ፡ እየኾነው ፡ ሳይኾነውም ፡ በኀላፊ ፡ አል ፥ በትንቢትና ፡

ብትእዛዝ ፡ አ፥በዘንድ ፡ እንዳ ፡ ላ ፡ ሳ ፡ ይኾናል ። ይህም ፡ ኢ.በልዐ ፡ አልበላ፥አልበላም ፤
ወይም ፡ እንደ ፡ ጕዛግም ፡ አልበልቶም ፤ ኢ.ይበልዕ ፡ አይበላ፥አይበላም ። ኢ.ይብላዕ ፡
እንዳይበላ፥ላይበላ ፡ ሳይበላ፥ኢ.ይብላዕ ፤ አይብላ ፡ ማለቱን ፡ ያሳያል ። በበዝም ፡ ሲገባ ፡
ኢ.ነጊሦ ፡ ዳዊት ፤ ኢ.ተዘኪ.ሮ ፡ አበሳነ ፡ ብሎ ፥ ሳይነግሥ ፡ ሳያስብ ፡ ያሰኛል ፡ (፪ኛ ፡ ክ
ፍል ፡ ፰ና ፡ ፺) ። በሣልስ ፡ ቅጽልም፥ቃል ፡ ኢ.ሐማሚ ፡ በባሕርየ ፡ ሥጋ ፡ ዘሐመ ፤ ት
ውልድ ፡ ኢ.አማኒት ፡ እያለ ፡ ሲገባ፥ያላመነች ፡ የማታምን ፡ ተብሎ ፡ በዘ ፡ ዐማርኛ ፡ ይ
ፈታል ። በሳድስ ፡ ቅጽልም ፡ ኢ.ርቱዕ፥ኢ.መፍትው ፡ ሲል ፡ ያልቀና ፡ ያልተገባ ፡ ያሰ
ኛል ። በዘ ፡ ዐማርኛ ፡ መፈታቱ ፡ ቅጽሉ ፡ በቂ ፡ ሲኾን ፡ ነው ፤ አለዚያ ፡ ግን ፡ ኢ. ፡ እን
ዳንቀጽነቱ ፡ አይዶለም ፡ ተብሎ ፡ ይፈታል ። ማሰሪያውም ፡ አሉታ ፡ ኹኖ ፡ ወን ፡ እያ
ስከተለ ፡ ሲደረደር ፡ አንቀጽ ፡ እንጂ ፡ አገባብ ፡ አይኾንም ። ፍችው ፡ ግን ፡ ኹኖ ፡ ሲ
ብል ፡ ንኡስ ፡ አገባብ ፡ ነው ፤ የኹኖም ፡ ምስጢር ፡ እንደ ፡ ወ ፡ ማጫፈር ፡ ነውና ፤ አልቦ ፡
ብዝ ፡ መዋዕል ፡ መልአክ፥ኢ.ነቢ.ይ ፡ ወኢ.ንጉሥ ፡ ኢ.ቍርባን ፡ ወኢ.መሢዕት ፤ ነቢ.ይ ፡
የለም ፡ ንጉሥም ፡ የለ ፤ ቍርባን ፡ የለም ፡ መሢዕትም ፡ የለ ፡ እያሰኘ ፡ በየደጁ ፡ ያስራል ፤
አገባብ ፡ ሲኾን ፡ ግን፥ነቢ.ይ ፡ ኹኖ ፡ ንጉሥም ፡ ኹኖ ፥ ቍርባን ፡ ኹኖ ፡ መሢዕትም ፡
ኹኖ ፡ እያለ ፡ በአልቦ ፡ ያስራል ። ደቂቅ ፡ አገባብም ፡ ሲኾን ፡ እንደ ፡ እንበለ ፡ ነው ፤
አለ ፡ ያለ ፡ ይኾናል ፤ በብትን ፡ ባርእስት ፡ በጥሬ ፡ ይገባል ። እንበለንም ፡ እየተከተለ ፡
ዘእንበለ ፡ ተምያጥ ፡ ወኢ.ተውላጥ፥ኢ.ቡዓዴ ፡ ወኢ.ቱስሕት ፡ ብሎ ፡ ሲገባ፥አንቀጽና ፡
አገባብ ፡ እየኾነ ፡ ባንቀጽነቱ ፡ ሳይኖር ፤ ባገባብነቱ ፡ አለ ፡ ያለ ፡ ያሰኛል ። በ ፡ ለ ፡
በጥሬ ፡ ባርእስት ፤ ዘ ፡ በቅጽል ፡ ይሰማሙታል ። ግብር ፡ ዘይትገበር ፡ በኢ.ምክር ፡
ወበኢ.ለብዎ ፡ እበድ ፡ ውእቱ ። ማርያምሰ ፡ ፍጎርተ ፡ ብእሲ. ፡ ከመ ፡ ዘኢ.ፍጎርት ፡ ምኵ
ራብ፥ማኅደሩ ፡ ለኢ.ሩካቤ ፡ ወምዕራፉ ፡ ለኢ.ሰብሳብ ። አብዳን ፡ ወጕንዱያን ፡ ልብ ፡
ለኢ.አሚን ። ዘ ፡ ሲሰማማው ፡ በቅጽል ፡ ይገባል ፤ ምንት ፡ ብከ ፡ ዘኢ.ነሣእከ ፡ እምካል
እከ ። ኢ.ትንሣእ ፡ ዘኢ.ያንበርከ ። ባርእስትም ፡ ብቻውን ፡ ሲገባ፥ኢ.በሊ.ዐ ፡ ሥጋ ፡
ወኢ.ሰትየ ፡ ወይን ፡ ብሎ ፤ አለመብላት ፡ አለመጠጣት ፡ ያሰኛል ። በማርኛም ፡ ኢ. ፡ በ
ቊሙ ፡ ኢ. ፡ ወይም ፡ አዩ. ፡ አዬ ፡ ተብሎ ፡ ሲነገር ፡ ቃለ ፡ አኅስሮ ፡ ነው ፤ ሐዘንና ፡ አን
ክሮም ፡ ይኾናል ። ያሉታም ፡ ዐዋጅ ፡ በብሂል ፡ ሲነገር ፡ ባህሉ ፡ ፪፥ክፍሉ ፡ ፬ ፡
ነው ፤ ፩ኛውና ፡ ፫ኛው ፡ ፪ኛውና ፡ ፬ኛው ፡ አንዳንድ ፡ ወገን ፡ ናቸው ። ፩ ፡ አሉታ ፡
ፍጹም ፡ አሉታ ፤ ፪ ፡ አሉታ ፡ ፍጹም ፡ ጽድቅ ፤ ፫ ፡ አሉታ ፡ ፍጹም ፡ አሉታ ። ፬ ፡ አ
ሉታ ፡ ፍጹም ፡ ጽድቅ ፡ ይኾናል ። አንድ ፡ አሉታ ፥ ምንት ፡ ውእቱ ፡ ደዌ ፡ ንስጥሮስ ፡
ባዕል፥እንበለ ፡ ኢ.ብሂል ፡ ብሂለ ፡ ወላዲ.ተ ፡ አምላክ ፡ ድንግል ። ፪ ፡ አሉታ፥ኢ.ደለዎ ፡
ለክርስቶስ ፡ በሰብእናሁ ፡ ኢ.ብሂል ፡ ከማነ ፡ አምላኪ.የ ፡ ወላዲ.ሁ ። ሦስት ፡ አሉታ፥ደ
ለዎ ፡ ለክርስቶስ ፡ በመለኮቱ ፡ ኢ.ብሂል ፡ አከ ፡ አነ ፡ ወአብ ፡ አሐዱ ፡ ንሕነ፥በከመ ፡
ደለዎ ፡ ኢ.ብሂል ፡ ዘርእየ ፡ ኪ.ያየ ፡ ርእዮ ፡ ለአቡየ ። አራት ፡ አሉታ ፥ ተውህበ ፡ ለጴጥ
ሮስ ፡ ጸጋ ፡ ኢ.ብሂል ፡ ኢ.ሞተ ፡ ክርስቶስ ፡ በሥጋ ፥ በከመ ፡ ተውህበ ፡ ለጳውሎስ ፡
ሀብተ ፡ ኢ.ብሂል ፡ ኢ.ተሣሀለነ ፡ አብ ፡ በሞተ ፡ ወልዱ ።

፻፩ ፤ አው ፤ ሚመ ። ወይ ፡ ወይም ፡ ወይስ ፡ ይኾናሉ ፤ ጥያቄ ፡ በለው ፡ ቃል ፡ ተ
ከትለው ፡ ሳይከተሉም ፡ በነገር ፡ ኹሉ ፡ ይገባሉ ። ምስጢራቸውም ፡ ማሻሻልና ፡ ማማ

ረጥ ፥ ማነጻጸርና ፡ ማበላለጥ ፡ ነው ፤ ዋዌነትም ፡ አለው ። ሲገቡም ፡ አው ፡ ቀድሞ ፡
ሚመ ፡ ይከተላል ። ኢትቁም ፥ አው ፡ ንበር ፥ ወሚመ ፡ ሑር ። እየብቻቸውም ፥ በሕ
ርኑ ፡ አነ ፥ አው ፡ ቀላይ ። እምሰማይኑ ፡ ወሚመ ፡ እምሰብእ ፡ ያሰኛሉ ። ተደጋግመ
ውም ፡ ሲነገሩ ፡ አው ፡ ብቻውን ፥ ሚመ ፡ በወ ፡ ይደገማል ። አው ፡ ሠምዐ ፥ አው ፡ ዘ
ይት ። ሚመ ፡ ተፈጥሮ ፡ ወሚመ ፡ ኢተፈጥሮ ። አው ፡ ተለይቶ ፡ ዋዌ ፡ ይኾናል ፤ አው ፡
ሑር ፡ ኅበ ፡ ንህብ ። አው ፡ ካልእት ፡ ሀገር ።

፻፬፤ ወ ። ስሙ ፡ በፊደልነት ፡ ሲጠራ ፡ ዋዌ ፡ ይባላል ፤ ሜንጦ ፡ ቍልፍ ፡ ዘለ
በት ፡ ማለት ፡ ነው ። በዕብራይስጥም ፡ ዋው ፡ የመስኰት ፡ ስናግ ፡ ቈላፋ ፡ ብረት ፡ ነው ፤
በተገናኝ ፡ እንደ ፡ ዳኛ ፡ የወል ፡ እንደ ፡ ምሰሶ ፡ የመካከል ፡ ኹኖ ፡ ግራና ፡ ቀኙን ፡ የሚ
ያያይዝና ፡ የሚያቈራኝ ፡ አያያዥ ፡ ማለት ፡ ነው ። ዘለበትም ፡ ሲባል ፡ በግብሩ ፡ ላይ ፡
መልኩን ፡ ጨምሮ ፡ ያሳያል ። ወ ፤ በገባብነቱ ፡ ም ፥ ና ፡ ዘተረስዐ ፥ ቸልታ ፥ ው
ጥን ፡ ጨራሽ ፥ ጠቅላይ ፥ ከ ፥ ጊዜ ፥ ስንኳ ፥ እንጂ ፥ ግን ፥ ል ፥ ስ ፥ አዳማቂ ፡ ይኾናል ፤
ምንም ፡ ያማርኛው ፡ ስልት ፡ ቢበዛ ፡ ምስጢሩ ፡ ማያያዝና ፡ ማጫፈር ፡ ብቻ ፡ ነው ።
ም ፡ ሲኾን ፡ ተሳቢውን ፡ ከቶ ፡ በሚጫፈር ፡ አንቀጽ ፡ ይገባል ፤ ናሁ ፡ ትፀንሲ ፡ ወ
ትወልዲ ፡ ወልደ ፥ ወትሰምዩዮ ፡ ስሞ ፡ ኢየሱስ ። ተሳቢ ፡ በሌለው ፡ በድርድር ፡ አ
ንቀጽ ፡ ግን ፡ ጠቅላይ ፡ እንጂ ፡ ም ፡ አይኾንም ፤ ሐመ ፡ ወሞተ ፡ ወተቀብረ ። ወተን
ሥአ ፡ እሙታን ፡ አመ ፡ ሣልስት ፡ ዕለት ፡ ሲል ፡ ብቻ ፡ ስለ ፡ ተሳቢው ፡ ም ፡ ይኾናል ።
ና ፡ ሲኾን ፡ ዘተረስዐ ፡ ነው ፤ በስምና ፡ ባንቀጽ ፡ እየገባ ፡ በሎደቀበት ፡ ላይ ፡ የኋሊት ፡
ይፈታል ። በስም ፡ ሚካኤል ፡ ወገብርኤል ፤ ጴጥሮስ ፡ ወጳውሎስ ። ባንቀጽ ፥ ሖረ ፡ ወመ
ጽአ ፥ ቦአ ፡ ወወፅአ ፥ ሐመ ፡ ወሞተ ፤ ኼደና ፡ መጣ ፥ ወይም ፡ ኼዶ ፡ መጣ ፡ እያሰኘ ፡
ዘተረስዐነቱን ፡ ያሳያል ። ቸልታ ፡ ሲኾን ፡ ወደ ፡ ፊት ፡ በወደቀበት ፡ ላይ ፡ ይፈታል ፤
ተንሥአ ፡ ወኀደገ ፡ ልብሰ ፥ ተጠምቀ ፡ ወአድኀነ ፡ ርእሰ ፥ ልብሱን ፡ ጥሎ ፡ ራሱን ፡
አዘንብሎ ። ውጥንም ፡ ሲጨርስ ፡ በኋላ ፡ ኹኖ ፡ የፊቱን ፥ በፊት ፡ ኹኖ ፡ የኋላውን ፥
የወንዱን ፡ በሴት ፡ ያንዱን ፡ በብዙ ፥ የብዙውን ፡ ባንድ ፡ ያናግራል ። በኋላ ፡ ኹኖ ፡
የፊቱን ፥ ሰማይ ፡ ወምድር ፡ የኀልፍ ፤ ሰማይ ፡ ያልፋል ፥ ምድርም ፡ ታልፋለች ፤ ም
ድር ፡ የፍጥረት ፡ ኹሉ ፡ እናት ፡ ስለ ፡ ኾነች ፡ በሴት ፡ አንቀጽ ፡ እንጂ ፡ በወንድ ፡ አት
ጠራም ። በፊትም ፡ ኹኖ ፡ የኋላውን ፥ መጽአ ፡ ዝኩ ፡ ብእሲ ፡ ወብእሲቱኒ ። በሉቃም ፡
ኢኮነ ፡ ደብር ፡ ገብረ ፡ ወኢይከውን ፤ ወኢወግር ፡ አመተ ፡ ለብእሲት ። ያንዱን ፡ በብዙ ፥
ተውህበ ፡ ጳውሎስ ፡ ሙቁሕ ፡ ወካልአንሂ ፡ ሙቁሓን ። አገብኦ ፡ ለኤልዛቤል ፡ ወለ
እለ ፡ ዘመዉ ፡ ምስሌሃ ። የብዙውን ፡ ባንድ ፥ ተሰቅሉ ፡ ፈያት ፡ ወክርስቶስኒ ፡ ኅቡረ ፡
ምስሌሆሙ ። ሩቅና ፡ ቅርብም ፡ ሲወጥን ፡ እንደዚሁ ፡ ያናግራልና ፤ አሰማምተኽ ፡ አ
ግባ ። ጠቅላይ ፡ ሲኾን ፡ ባንቀጽና ፡ በስም ፡ በአኃዝ ፡ ይገባል ፤ ያንቀጹ ፡ ተነግሯል ።
በ፫ ፡ ስሞች ፡ ሲገባ ፡ ፩ኛውና ፡ ፪ኛው ፡ ጠቅላይ ፡ ይኾናል ። ጳውሎስ ፡ ወስልዋኖስ ፡
ወጢሞቴዎስ ። በሌላውም ፡ ጥሬ ፥ ክብር ፡ ወስብሐት ፡ ወዕዘዝ ፡ ሲል ፡ እንዲሁ ፡ ነው ።
በአኃዝ ፡ ሲገባ ፡ ካሥር ፡ እስከ ፡ ሺሕ ፡ ይጠቀልላል ፤ ዐሥርቱ ፡ ወአሐዱ ፤ ተስዐቱ ፡
ምእት ፡ ተስዓ ፡ ወተስዐቱ ፤ ከሺሕ ፡ በላይ ፡ ግን ፡ ከ ፡ ይኾናል ፤ ምስጢሩም ፡ ብዙውን ፡

ከጥቂት ፡ ማመፈር ፡ ነው ። ኀምሳ ፡ ወኀምስቱ ፡ ምእት ፤ እልፍ ፡ ወዕሥራ ፡ ምእት ።
ጊዜ ፡ ሲኾን ፡ በቦዝ ፡ ይገባል ፤ አገባቡም ፡ በ፱ኛ ፡ ዕርከን ፡ በ፰ ፡ ቍጥር ፡ ተነግሯል ።
ስንኳ ፡ እንጂ ፡ ግን ፡ ሲኾን ፡ ነቃፊ ፡ ነውና ፣ በሉታና ፡ ባፍራሽ ፡ ይገባል ፤ ኢ.ወሀበ ፡
ርስቶ ፡ ወኢመጠነ ፡ ምሥጋረ ፡ እግር ፣ አንዲት ፡ ርምጃ ፡ ስንኳ ። በልዐ ፡ ወኢሰትየ ፣
አልጠጣም ፡ እንጂ ። እግር ፡ በሙ ፡ ወኢየሐውሩ ፡ ያለውም ፣ እንጂ ፡ ተብሎ ፣ ወይም ፡
ጠቅላይ ፡ ኹኖ ፡ በትች ፡ ቃል ፣ አለዚያም ፡ ዘተረስዐ ፡ ኹኖ ፡ በእንዘ ፡ ዐማርኛ ፡ ይፈ
ታል ። አንተ ፡ ጴጥሮስ ፡ ዕድሜሁ ፡ ስብከተ ፣ ወይሁዳ ፡ አኀጸረ ፡ ዕለተ ፤ ይሁዳ ፡ ግን ።
ል ፡ ሲኾን ፡ ስምዐኒ ፡ ወእንግርከ ፤ ቅረበኒ ፡ ወእግስስከ ፡ እያሰኘ ፡ በሣልሳይ ፡ አንቀጽ ፡
ይገባል ። ሲ ፡ ሲኾን ፡ በንኡስ ፡ ይገባል ፤ አይቴኑ ፡ አሐውር ፣ ወአይቴ ፡ እጐይይ ፤ ወዴ
ትስ ። ምንተ ፡ በልዐ ፣ ወምንተ ፡ ሰትየ ፤ ምንስ ፡ ጠጣ ። አዳማቂ ፡ ሲኾን ፡ በጥንተ ፡
ነገር ፡ ይገባል ፤ ወሀሎ ፡ አሐዱ ፡ ብእሲ ። ወኮነ ፡ በሠላሳ ፡ ክረምት ። ምስጢሩ ፡ ግን ፡
ከማቈራኘት ፡ አይወጣም ፤ የሚቀድመው ፡ መጽሐፍ ፡ አለና ። ወንድና ፡ ሴትም ፡ ሲያ
መፍር ፣ ተፈጥሩ ፡ አዳም ፡ ወሔዋን ፡ ይላል ፡ እንጂ ፣ ሔዋን ፡ ወአዳም ፡ አይልም ።
ተመፋሮች ፡ ፫ ፡ ሲኾኑ ፡ አንዳንድ ፡ ጊዜ ፡ ሴት ፡ ያስቀድማል ፤ ወረከብዎሙ ፡ ለማር
ያም ፡ ወለዮሴፍ ፡ ወለሕፃንኒ ። ባመፋሪነቱም ፡ ዘርፍና ፡ ቅጽል ፡ አያተርፍም ፤ ዘርፍ ፡
አለማትረፉ ፡ ባለቤት ፡ መንታ ፡ ሲኾን ፡ ነው ፤ ይህም ፡ ኅሩያነ ፡ ወሠናያነ ፡ ሊባኖስ ፡
ያለውን ፣ ኅሩያነ ፡ ሊባኖስ ፡ ብሎ ፡ ወሠናያን ፡ አለማለት ፡ ነው ። ቅጽል ፡ አለማትረ
ፉም ፡ ብፁዕ ፡ ጴጥሮስ ፡ ወጳውሎስ ፡ ሲል ፡ ነው ። በወ ፡ የማይወርዱ ፡ ፰ ፡ ናቸው ፤ የግ
እዝ ፡ ወራሽ ፡ ሀ ፡ የሙሻዘር ፡ ውስጠ ፡ ዘ ፡ ዊ ፣ ዝርዝር ፣ አሉታ ፤ እም ፡ ጸጸትና ፡ ተም
ኔት ፡ ሲኾን ። ኀረዩ ፡ እስጢፋኖስሀ ፡ ወፊልጶስሀ ። ክርስቶስ ፡ ሰማያዊ ፡ ወምድራዊ ።
ነአምን ፡ ሕማሞ ፡ ወሞቶ ። ኢገብረ ፡ ኀጢአተ ፡ ወኢተረክበ ፡ ሐሰት ፡ ውስተ ፡ አፉሁ ።
እመ ፡ ነስሐ ፡ ይሁዳ ፡ እምጸድቀ ፡ ብሎ ፣ ወእምኢተኰነነ ፡ ይላል ፡ እንጂ ፤ ወ ፡ እምን ፡
ያወርድልኛል ፡ ብሎ ፡ ወኢተኰነነ ፡ አይልም ።

፻፫ ፤ ሂ ፡ ኒ ፡ ዓዲ ። ስማቸው ፡ ማሰሪያ ፡ ከፋዮች ፣ ማንጸሪያ ፤ ትርጓሜያቸው ፡
ም ፣ ደግሞ ፡ ይኾናል ። ሂ ፡ ኒ ፡ በኋላ ፣ ዓዲ ፡ በፊትም ፡ በኋላም ፡ እየገቡ ፡ ይነገራሉ ። ንት
ሜሰሎ ፡ በሕይወቱሂ ። የኀድግ ፡ ለክሙኒ ። ዓዲ ፡ ናቄርብ ፡ ለከ ፤ ፈነውነ ፡ ምስሌሁ ፡
ዓዲ ። ሂ ፡ ወሂ ፣ ኒ ፡ ወኒ ፡ ም ፡ ወይም ፡ ደግሞ ፡ ተብለው ፡ ሲፈቱ ፡ ምስጢራቸው ፡ ማመ
ፈርን ፡ መደብ ፡ አድርጎ ፡ አንጻርነትና ፡ ከፋይነት ፡ አማራጭነት ፡ ነው ። ዘንተሂ ፡ ወዝ
ክተሂ ። ዝኒ ፡ የኀልፍ ፡ ወይሰዐር ፡ ዝኒ ። ተደርድረውም ፡ ሲያመፍሩ ፣ ከሃሊ ፡ አንሰ ፡
ተጽናሰሂ ፡ ወተደልዎሂ ፣ ርኂበሂ ፡ ወጸጊበሂ ፣ ሐሚመሂ ፡ ወተፈሥሖሂ ፡ ያሰኛሉ ።
፪ኛም ፣ ሂ ፡ ኒ ፡ ሰ ፡ ባሕቱ ፡ ግን ፡ ሲኾኑ ፡ ክፍል ፡ ናቸውና ፣ ወ ፡ ግን ፡ ሲኾን ፡ እንደ ፡
ገባው ፡ አግባ ። ፫ኛም ፡ ሂ ፡ ኒ ፡ ጥቀ ፡ ኑ ፡ በብትን ፡ ሲገቡ ፡ ስንኳ ፡ ይኾናሉና ፤ ወ ፡ ስንኳ ፡
ሲኾን ፡ እንደ ፡ ገባው ፡ አግባ ። ጥቀ ፡ ኑ ፡ በየቦታቸው ፡ ተነግረዋል ፤ የቀረውም ፡ የሂና ፡
የኒ ፡ አገባብ ፡ በእመ ፡ ተነግሯል ።

፻፬ ፤ ቅድመ ። ንኡስ ፡ አገባብ ። እም ፡ እያዳመቀው ፣ ሳያዳምቀውም ፡ ብቻ
ውን ፡ በዘንድ ፡ አንቀጽ ፡ ገብቶ ፡ ሳ ፡ ይኾናል ። እምቅድመ ፡ ይትረበባ ፡ ሰማያት ። በሰ

ማይኒ ፡ ቅድመ ፡ ይትፈጠር ፡ ኪሩብ ፤ ሰማዮች ፡ ሳይዘረጉ ፤ ኪሩብ ፡ ሳይፈጠር ። ደቂቅ ፡ አገባብም ፡ ሲኾን ፡ በፊት ፡ ይኾናል ፤ እምና ፡ በ ፡ እየተሰማሙ ፡ በቦታ ፡ በጊዜ ፡ ይገባል ፤ በቦታ ፡ ዘሀሎ ፡ እምቅድመ ፡ ሀገር ። በቅድመ ፡ ቤተ ፡ እግዚአብሔር ። በጊዜም ፡ ሲገባ ፡ እምቅድመ ፡ ዳዊት ፡ በቅድመ ፡ ዳዊት ፥ ቅድመ ፡ ዳዊት ፡ ነግሡ ፡ ሳኦል ፡ ያሰኛል ። ሲዘረዝርም ፡ ቅድሚሁ ፡ ሃ ፡ ብሎ ፡ እስከሦር ፡ ይዘምታል ። የሚገባም ፡ ፊት ፡ በተደረገ ፡ ኋላም ፡ በማይቀር ፡ በቍርጥ ፡ ነገር ፡ ነው ፤ የቦታና ፡ የጊዜ ፡ ጥሬ ፡ ስለ ፡ ኾነ ።

## የጊዜያት ፡ ጥሬ ።

፩፫ ፤ ትካት ፤ ዓለም ። ዱሮ ፡ ጥንት ፡ ቀድሞ ፡ ይኾናሉ ። ትካት ፡ ብቻውን ፥ ሰብአ ፡ ትካት ። ሕዝብ ፡ ዘኢተአምሪ ፡ ትካት ፡ እያለ ፥ ከገባብም ፡ ጋራ ፥ እምትካት ፥ ኀበ ፡ ዘትካት ፡ እያለ ፡ ይገባል ። ዓለም ፡ ግን ፡ አገባብ ፡ ሳይዝ ፡ ብቻውን ፡ አይገባም ፤ ነቢያት ፡ እለ ፡ እምዓለም ። ተዘከርኩ ፡ ፍትሐከ ፡ ዘእምዓለም ፤ ከዱሮ ፡ ከጥንት ፡ ከቀድሞ ፡ ዠምሮ ፡ የነበረ ። ለ ፡ ሲወድቅበት ፡ ወትሮ ፡ ዘወትር ፡ ድንት ፡ ይኾናል ። አንተሰ ፡ ትነብር ፡ ለዓለም ። ዘ ፡ ሲጨመርበት ፥ አምላክ ፡ ዘለዓለም ፡ ብሎ ፥ ለድንት ፡ የሚኖር ፡ የማይጠፋ ፡ የማይለወጥ ፥ ጥንትና ፡ ፍጻሜ ፡ የሌለው ፡ ያሰኛል ። ለዓለመ ፡ ዓለም ፤ ለዘላለም ፥ በጊዜው ፡ በዘመኑ ፡ ኹሉ ፡ ያለማቋረጥ ፤ እምዓለም ፡ ወእስከ ፡ ለዓለም ፤ ከመዠመሪያ ፡ እስከ ፡ መጨረሻ ፤ ከፍጥረት ፡ እስከ ፡ ምጽአት ።

፩፬ ፤ ቅድም ፤ ትማልም ። ቅድም ፡ ብቻውን ፡ ሲነገር ፡ ፊት ፡ መዠመሪያ ፡ ይኾናል ፤ ከትማልም ፡ ጋራ ፡ ሲናበብ ፡ ግን ፡ በስቲያ ፡ ወዲያ ፥ ሐች ፡ ይኾናል ። ትማልም ፡ ደግሞ ፡ ትላንት ፡ ዓምና ፡ ይኾናል ፤ ዕለት ፡ እንተ ፡ ትማልም ፡ ኀለፈት ። በተገናኝ ፡ ቅድመ ፡ ትማልም ፡ ብሎ ፡ ከትላንት ፡ በስቲያ ፥ ወይም ፡ ወዲያ ፥ ሐች ፡ ዓምና ፥ የወዲያኛው ፡ ዓመት ፡ ያሰኛል ።

ዮም ፡ ይእዜ ። ዛሬ ፡ አኹን ፡ ዘንድሮ ፡ ይኾናሉ ፤ ዘትማልም ፡ ወዮም ። እም ይእዜ ፡ ወእስከ ፡ ለዓለም ። ቅድምና ፡ ትማልም ፡ ዘመነ ፡ ብሉይ ፡ ሲባሉ ፡ ዮምና ፡ ይእዜም ፡ ዘመነ ፡ ሐዲስ ፡ ይባላሉ ። ዳግመኛም ፡ በመምህራን ፡ ልማድ ፥ አሜር ፡ አስፌር ፡ ዓምና ፤ ኀሪፍ ፡ ገሪፍ ፡ ዘንድሮ ፡ ይባላሉ ፤ በመጻሕፍት ፡ ግን ፡ ከኀሪፍ ፡ በቀር ፡ የሦስቱ ፡ ምስክር ፡ አይገኝም ። ጎድጋ ፡ ኀሪፈኒ ፡ እመ ፡ ትፈሪ ፡ ለዓመ ። ምናልባት ፡ ለሚመጣው ፡ ዓመት ፡ ብታፈራ ፥ ዓምና ፡ እንደ ፡ ተውኻት ፡ ዘንድሮም ፡ ተዋት ። ይኸውም ፡ አትክልት ፡ የሚታገሉበት ፡ የርጥበት ፡ ወራት ፡ ጊዜ ፡ ገሚድ ፡ ነው ።

፩፭ ፤ ጌሠም ፤ ሳኒታ ። ነገ ፡ ነገታ ፥ ማግስት ፡ የዮም ፡ ተከታይ ፥ ፪ኛ ፡ ቀን ። ዮምኬ ፡ ሰብእ ፡ ወጌሠመ ፡ መሬት ። ወበሳኒታ ፡ እምድኀረ ፡ ዐርብ ። በዘመን ፡ ሲገባም ፡ ከርሞ ፡ የዛሬ ፡ ዓመት ፡ ይኾናል ። ኢትበሉኬ ፡ ለጌሠም ፤ እስመ ፡ ጌሠምሰ ፡ ትኄሊ ፡ ለርእሳ ። ዘልፍ ፡ ወትር ፤ ዘልፈ ፡ ወትረ ፤ ወትሮ ፡ ዘወትር ፥ ያለማቋረጥ ፡ ይኾናሉ ። ልማድ ፡ ዘዘልፍ ፥ ዘወትረ ፡ ይሴብሑ ። ለዝሉፉ ፡ ለዝላፉ ፥ ለወትሮ ፡ ለዘወትር ፡ ለዘላለም ፡ ይኾናል ። ግሙራ ፡ ለግሙራ ፥ ለፍጻሜ ፤ ከቶ ፡ አካቶ ፡ ፈጽሞ ፡ ጭራሽ ፡ ይኾናሉ ። በተገብሮም ፡ አንቀጽ ፡ ሲገቡ ፡ ተከቶ ፡ ተካቶ ፡ ተጨርሶ ፡ ያሰኛሉ ። እምድ

ሩም ፡ እንደ ፡ ግሙራ ፡ ነው ፤ አካቶ ፡ ፈጽሞ ፡ ጭራሽ ፡ ይኾናል ፡፡ እመ ፡ እምድሩ ፡ ትኰሲ ፡ ልደቶ ፡፡ ነቅዐ ፡ ኀጢአትየ ፡ ለገብረከ ፡ እምድሩ ፡ ይሠሮ ፡፡ ብዛትና ፡ ብልጫ ፡ የሚያሳዩ ፥ ጥቀ ፡ ፈድፋደ ፡ በሕቁ ፤ እጅግ ፡ በጣም ፡ ይኾናሉ ፡፡ ጥቀ ፡ ተሰብሐ ፡፡ ፈድፋደ ፡ ተለዐለ ፡፡ ለእመ ፡ ኢተኀፅቡ ፡ በሕቁ ፡፡ ቅጽልና ፡ በቂ ፡ እየኾኑ ፡ ሕጸጽ ፡ የሚያሳዩ ፤ ኅዳጥ ፡ ንስቲት ፡ ሕቅ ፤ ጥቂት ፡ ይኾናሉ ፤ ዓዲ ፡ ኅዳጠ ፡ ኢትሬእዩኒ ፤ ወካዕበ ፡ ኅዳጠ ፡ ትሬእዩኒ ፡፡ ንስቲት ፡ ሕቅ ፡ ከክመ ፡ ጋራ ፡ ተነግረዋል ፡፡

፻፰ ፤ መድረሻቸው ፡ ግእዝ ፡ እየኾነ ፡ ወይም ፡ በ ፡ ወድቆባቸው ፡ ንኡስ ፡ አገባብ ፡ የሚኾኑ ፡ ሳድስ ፡ ቅጽሎች ፡ በዐበይትና ፡ በንኡሳት ፡ በአናቅጽ ፡ ኹሉ ፡ እየገቡ ፡ እንደሚስማማቸው ፡ ይፈታሉ ፡፡ ይህም ፡ እነግረክሙ ፡ ከሡተ ፥ አው ፡ በከሡት ፡ ብሎ ፡ ገልጬ ፡ ወይም ፡ በግልጥ ፡ ማለቱን ፡ ያሳያል ፡፡ የቀሩትም ፡ ድሎትና ፡ መፍትው ፡ ብዉሕ ፥ በለ ፡ ተዘርዝረው ፡ ሳይዘረዘሩም ፡ በዘንድ ፡ አንቀጽና ፡ ባርእስት ፡ በሳቢ ፡ ዘር ፡ ገብተው ፡ ሲነገሩ ፡ ማሰሪያቸው ፡ ነባር ፡ አንቀጽ ፡ ነው ፡፡ አኮ ፡ ድሎት ፡ ሊተ ፡ አንቃዕዶ ፡ ወእርአይ ፡፡ መፍትው ፡ ትግበሩ ፡ ዘንተ ፡ ወዝክተኒ ፡፡ አኮ ፡ ድሎት ፡ ወአኮ ፡ መፍትው ፡ አስተርእዮ ፡ በመንታ ፡ ፍናው ፡፡ ብዉሕ ፡ ሊተ ፡ አንብራኒ ፡ ወእሚማኒ ፡፡ ጽድቅና ፡ አሉታ ፡ አንቀጽ ፡ የሚያሰሙ ፡ ዮጊ ፡ ዬ ፡ ናሁ ፡ ነዋ ፡ በኹሉ ፡ እየገቡ ፡ እንሆ ፡ ተብለው ፡ ይፈታሉ ፤ ዮጊና ፡ ዬ ፡ በየበታቸው ፡ ተነግረዋል ፡፡ ናሁና ፡ ነዋ ፡ ከነባር ፡ አንቀጽ ፡ ከነ ፡ የወጡ ፡ ናቸው ፤ ርባታቸውም ፡ ነዮ ፡ ያ ፡ በ፲፩ኛ ፡ ዕርከን ፡ ተነግሯል ፡ ፤(ቍ፹፰)፤፡፡ እነዚህ ፡ ኹለቱ ፡ በቅርብ ፡ አነጋገር ፡ እንሆ ፡ እያሉ ፡ ሩቁን ፡ እንደ ፡ ቅርብ ፡ ሲያደርጉ ፡ ቅርብ ፡ ቅርቡንም ፡ ሲዳርጉ ፥ ደቂቅ ፡ ቅጽል ፡ እንጂ ፡ አገባብ ፡ አይመስሉም ፡፡ ናሁ ፡ ለወንድም ፡ ለሴትም ፥ ነዋ ፡ ላንድ ፡ ወንድ ፡ ብቻ ፡ ይነገራል ፡፡ ናሁ ፡ ኢመጽአ ፡ ለበዓል ፤ ወናሁ ፡ ኤልሳቤጥኒ ፡፡ ነዋ ፡ ወልድከ ፡፡ ናሁ ፡ ተሊይቶ ፡ ቃለ ፡ አንክሮ ፡ ይኾናል ፤ ይኸውም ፡ መጽሐፍ ፡ መላሾች ፥ ዕብራይስጡ ፡ ሚ ፡ ሠናይ ፡ ወሚ ፡ አዳም ፡ ያለውን ፥ ናሁ ፡ ሠናይ ፡ ወናሁ ፡ አዳም ፡ ብለው ፡ ስላገቡት ፡ ነው ፡፡ ፪ኛም ፡ በእስመ ፡ ፈንታ ፡ እየገባ ፡ ዐቢይ ፡ አገባብ ፡ ይኾናል ፤ ወሥጋሁኒ ፡ እምድኅረ ፡ ትንሣኤሁ ፡ ከነ ፡ ዘኢይማስን ፡ ወዘኢይመውት ፤ ናሁ ፡ ከነ ፡ አሐደ ፡ ምስለ ፡ እግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ ዘእንበለ ፡ ፍልጠት ፡፡ እስመ ፡ ደግሞ ፡ በናሁ ፡ ፈንታ ፡ እየገባ ፡ ንኡስ ፡ ይኾናል ፤ እስመ ፡ ቆሙ ፡ ላዕሌየ ፡ ሰማዕተ ፡ ዐመፃ ፡፡ እወ ፡ አማን ፡ አሆ ፡ እንቢ ፡ አህ ፡ ብሥራት ፤ ሀብ ፡ ነዐ ፥ ና ፡ ቶሎ ፡ በል ፤ ሕንክ ፥ ዕንካ ፡፡ እነዚህ ፡ ኹሉ ፡ በ፫ኛው ፡ ክፍል ፡ ውስጥ ፡ በ፲፫ኛ ፡ ዕርከን ፡ ከነርባታቸው ፡ ተነግረዋል ፡ (ቍ፻፲፩) ፡፡ አኢ ፡ አኢ ፤ ዐዋጅ ፡ ዐዋጅ ፥ ስማ ፡ ስማ ፡ ይኾናል ፡፡ በጽሐ ፡ ጊዜ ፡ ዘይትበሀል ፡ አኢ ፡ እንዲል ፡ (ገድ ፡ ተክ) ፡፡ በላገባቦች ፡ ግን ፡ በአኢ ፡ ፈንታ ፡ ኤር ፡ ኤር ፥ ወይም ፡ ኤል ፡ ኤል ፡ አብሬል ፡ ይላሉ ፤ የአብሬልንም ፡ ፍች ፡ ገብር ፡ ከነ ፡ እግዚአ ፡ ይሉታል ፤ ኹሉም ፡ የተሳሳተ ፡ ነው ፡፡ ኤር ፡ ኤል ፡ በአሪት ፡ የለም ፤ አብሬል ፡ ብቻ ፡ አብሬኽ ፡ ተብሎ ፡ ይገኛል ፥ ፍችውም ፡ ብርክ ፡ አስተብርክ ፥ ስግድ ፡ ወአምኃ ፥ ግነይ ፡ ወባርክ ፡ ማለት ፡ ነው ፡፡ ይኸውም ፡ ስለ ፡ ዮሴፍ ፡ ሹመት ፡ የተነገረ ፡ የፈርዖን ፡ ዐዋጅ ፡ ነው ፤ ቃሉም ፡ ዕብራይስጥ ፡ ነው ፡፡

## ኛ፩ኛ ፡ ዕርከን ።

## ደቂቅ ፡ አገባቦች ።

፻፱ ፤ ቤዛ ፡ ተክለ ። በብትን ፡ ገብተው ፡ ስለ ፡ ይኾናሉ ፤ ቤዛ ፡ ለውጥነት ፡ ባለው ፡ ተክለ ፡ ምትክነት ፡ ባለው ፡ ይገባል ። እሜጡ ፡ ነፍስየ ፡ ቤዛ ፡ አባግዕየ ። ተወልደ ፡ ሴት ፡ ተክለ ፡ አቤል ፤ ስለ ፡ በጎቼ ፡ ቤዛ፥ ስለ ፡ አቤል ፡ ምትክ ። ፪ኛም ፡ በጥሬነታቸው ፡ የበጎቼን ፡ ቤዛ ፡ ነፍሴን፥የአቤል ፡ ምትክ ፡ ሴት ፡ ተብለው ፡ ሲፈቱ ፡ ቅጽል ፡ ይኾናሉ ። ዐስበና ፡ ዕሴተም ፡ እንደዚሁ ፡ ነው ፤ ዋጋነትን ፡ ሳይለቅ ፡ ይፈታል ። ሲዘረዝርም ፡ ቤዛሁ ፡ ሃ፥ ተክሉ ፡ ላ ፡ እያለ ፡ ስለ ፡ ርሱ፥ ቤዛው ፡ ምትኩ ፡ ያሰኛል ።

የቦታ ፡ አገባቦች ፤ ዲበ ፡ ላዕለ ፡ መልዕልተ ። ላይ ፡ በላይ ፡ ወደ ፡ ላይ ፡ በ ፡ ስለ ፡ ይኾናሉ ። ዘሐነጸ ፡ ቤቶ ፡ ዲበ ፡ ኰኵሕ ። ዐርገ ፡ ዲበ ፡ ሰግላ ። ክልብ ፡ ይገብእ ፡ ዲበ ፡ ቂያኡ ። ዲበ ፡ ሀጕለ ፡ ውሉዶሙ ፡ ይግዕሩ ፤ በልጆቻቸው ፡ ጥፋት ፤ ስለ ፡ ልጆቻቸው ፡ ጥፋት ። ላዕለ ፡ መልዕልተም ፡ እንደዚሁ ፡ ናቸው ። አዕረፈት ፡ በረከት ፡ ላዕለ ፡ ያዕቆብ ። ወመጽአ ፡ ቃል ፡ ላዕለ ፡ ዮሐንስ ። ዐርጉ ፡ መልዕልተ ፡ ወግር ። ወጽልመት ፡ መልዕልተ ፡ ቀላይ ። ስለ ፡ ሲኾን ፡ ጸልዩ ፡ ላዕሌየ ፡ ወላዕለ ፡ ዝንቱ ፡ መሢዕት ፡ እያሰኘ ፡ ይህን ፡ በመሰለ ፡ ይገባል ። አንዳንድ ፡ ጊዜም ፡ ጥቅም ፡ ባለው ፡ ነገር ፡ ሲገባ ፡ ለ ፡ ይኾናል ፤ ግበሩ ፡ ምሕረተ ፡ ወምጽ.ተ ፡ ላዕለ ፡ አኀዊክሙ ፤ ለወንድሞቻችኹ ። ሲዘረዝሩም ፡ ዲቤሁ ፡ ላዕሉ ፡ ሌሁ፥መልዕልቱ ፡ ቴሁ ፡ እያሰኙ ፡ እንዳንቀጹ ፡ ስልት ፡ ይፈታሉ ። ፫ ፡ አገባቦች ፡ በ ፡ እም ፡ እንተ ፡ ይሰማሟቸዋል ። ጸጋ ፡ በዲበ ፡ ጸጋ ። ቀነጸ ፡ እምዲበ ፡ ሐመር ፤ አዝዘኒ ፡ እምጻእ ፡ ኀቤከ ፡ እንተ ፡ ዲበ ፡ ባሕር ። ፪ኛም ፡ በጥሬነታቸው ፡ ዘርፍ ፡ ይዘው ፡ ወይም ፡ ተዘርዝረው ፡ ቅጽል ፡ ይኾናሉ ። ጠፈር ፡ ዲበ ፡ ላዕለ ፡ መልዕልተ ፡ ምድር ፡ ዓለመ ፡ ብርሃናት ፤ ወሰማይኒ ፡ ላዕለ ፡ ጠፈር ፡ ዓለመ ፡ መላእክት ፡ ውእቱ ። ሲፈታም ፡ የምድር ፡ ላይ ፡ ጠፈር፥ የጠፈር ፡ ላይ ፡ ሰማይ፥ ወይም ፡ አቅንቶ ፡ ከምድር ፡ በላይ ፡ ያለ፥ ከጠፈር ፡ በላይ ፡ ያለ ፡ እያሰኘ ፡ ሌላውን ፡ ኹሉ ፡ ያሳያል ።

፻፲ ፤ ታሕተ ፡ መትሕተ ። ታች ፡ በታች ፡ ወደ ፡ ታች ፡ ይኾናሉ ፤ ያቦታ ፡ አገባቦች ፡ በ ፡ እም ፡ ኀበ ፡ መንገለ ፡ ውስተ ፡ ወደ ፡ ሲኾኑ ፡ ይሰማሟቸዋል ። በታሕተ ፡ እምታሕተ ፡ ሰማይ፥ኀበ ፡ መትሕት ። ሲዘረዝርም ፡ ታሕቴ ፡ መትሕቴ ፡ ቴሁ፥በታቹ ፡ ከርሱ ፡ በታች ፡ ያሰኛል ። በጥሬነቱም ፡ ሲነገር ፡ ተዘርዝሮና ፡ ዘርፍ ፡ ይዞ ፡ ቅጽል ፡ ይኾናል ። በሰማይ ፡ በላዕሉ፥ወበምድር ፡ በታሕቱ ። ምድር ፡ ታሕተ ፡ ጠፈር ፡ ወመትሕተ ፡ ደመናት ፡ ዓለመ ፡ ሰብእ ፡ ወእንስሳት ። ስትፈታም ፡ በሰማይ ፡ ላዕሉ ፡ ለምድር ፡ ወበምድር ፡ ታሕቱ ፡ ለሰማይ ፡ ብለኽ ፡ ግጠም ።

፻፲፩ ፤ ውስተ፥ ውሳጤ፥ ማእከለ ። ውስተ ፡ ውስጥ ፤ በውስጥ ፡ በማኽል፥በ ፡ ወደ ፡ ይኾናል ። ዓሣ ፡ ዘውስተ ፡ ባሕር ። ሡርዌ ፡ ዘውስተ ፡ ዐይንከ ። ከመ ፡ አንበሳ ፡ ውስተ ፡ እንስሳ ። ኢሀሎ ፡ ውስተ ፡ መካኑ፥ በቦታው ። ሖርከ ፡ ውስተ ፡ ሲኦል፥ ወደ ። ምስጢሩ ፡ ውስጥን ፡ አይለቅም ፤ የቦታ ፡ አገባብ ፡ ስለ ፡ ኾነ ፡ በ ፡ እም ፡ እንተ ፡ ይሰማሙታል ። የበ ፡ መሰማማት ፡ ተነግሯል ። ዘይወፅእ ፡ እምውስተ ፡ አፍ ። ወፅአት ፡ ሐጽ ፡

እንተ ፡ ውስተ ፡ ልቡ ፤ በደረቱ ። ሲዘረዝርም ፡ በ ፡ እም ፡ እንተ + ውስቴቱ ፡ ታ ፡ እያሰኙ ፡ ይሰማሙታል ። ውስጥና ፡ ውሳጤም ፡ ከውስተ ፡ ጋራ ፡ ፩ ፡ ዘር ፡ ናቸው ፤ ውስተ ፡ የተ በለው ፡ ውስጥ ፡ ነውና ። ውሳጤም ፡ ውስተ ፡ በገባበት ፡ እየገባ + ውስጥ ፡ በውስጥ ፡ ይኾናል ። ይትኀብኡ ፡ አራዊት ፡ ውሳጤ ፡ ግብ ። በ ፡ እም ፡ ይሰማሙታል ፤ ሲዘረዝ ርም ፡ ውሳጤሁ ፡ ሃ ፡ እያለ ፡ ውስጡ ፡ ውስጧ ፡ ያሰኛል ። ማእከለም ፡ ማኽል ፡ በማኽል ፡ ወደ ፡ ማኽል ፡ ይኾናል ፤ ምስጢሩ ፡ ውስጥ ፡ ነው ፤ ግራና ፡ ቀኝ ፡ ላይና ፡ ታች ፡ ከበብ ፡ ባለው ፡ ነገር ፡ ይገባል ። ጽንፍ ፡ ወማእከል ። ቁም ፡ ማእከለ ። በእ ፡ ማእከለ ፡ ሀገር ። በ ፡ እም ፡ እንተ ፡ ውስተ ፡ ይሰማሙታል ። በማእከለ ፡ ማኅበር ፡ እሴብሐከ ። አወፅ አሙ ፡ እማእከላ ። እንተ ፡ ማእከላ ። ውስተ ፡ ማእከሎሙ ። ሲዘረዝርም ፡ ማእከሉ ፡ ላ + ማእከሌሁ ፡ ሃ ፡ እያሰኘ ፡ በዘመድ ፡ በባዕድ ፡ ይነገራል ።

፻፲፱ ፤ በ ። በቁም ፡ ቀሪ ፤ ም ፡ ን ፡ ለ ፡ ጊዜ ፡ ጋራ ፡ እንደ ፡ ቸልታ ፡ ይኾናል ። በቁም ፡ ቀሪ ፡ ሲኾን ፡ በማሰሪያ ፡ ኹሉ ፡ እየገባ ፡ ማድረጊያ ፡ ይኾናል ። አድኅነነ ፡ በመ ለኮቱ ፡ ወቤዘወነ ፡ በትስብእቱ ። ም ፡ ሲኾን + ለእግዚአብሔር ፡ ምድር ፡ በምልኣ ። እስመ ፡ ዚአየ ፡ ውእቱ ፡ ኵሉ ፡ ዓለም ፡ በምልኡ ፡ ይላል ። ወምልኣ ፡ ወምልኡ ፡ ማለት ፡ ነው ፤ በውስጧም ፡ ያለው ፡ ማለትን ፡ ያሰማል ። ይኸውም ፡ መላሾች ፡ በወ ፈንታ ፡ ስላገቡት ፡ ነው ፤ ከዚህ ፡ በቀር ፡ በሌላ ፡ አይገኝም ። ን ፡ ሲኾን + የግእዝ ፡ ወራሽ ፡ ነው ፤ ለምሁራነ ፡ ልብ ፡ በጥበብ ። ኢቀባዕክኒ ፡ በዘይት ፤ ጥበበ ፡ ዘይት ፡ ማለት ፡ ነው ። ይኄይስ ፡ ተአምኖ ፡ በእግዚ ፡ እምተአምኖ ፡ በዕጓለ ፡ መሕያው ፡ ሲል + በቁም ፡ ቀሪ ፡ ኹኖ + ወይም ፡ ን ፡ ተብሎ ፡ ይፈታል ። ለ ፡ ሲኾን ፡ መንታነትና ፡ ተነጻጻሪነት ፡ ባላቸው ፡ በሕዋሳት ፡ ኹሉ ፡ ይገባል ፡ አንቀጹም ፡ ተደራራጊና ፡ አደራራጊ ፡ ነው ። ተናጸሩ ፡ ገጸ ፡ በገጽ ፤ ፊት ፡ ለፊት ። ይትጓድዑ ፡ ክንፈ ፡ በክንፍ ። አስተአኀዘሙ ፡ እደ ፡ በእድ + ወእግረ ፡ በእግር ። ወተናገሮ ፡ ቃለ ፡ በቃል ። ጊዜ ፡ ሲኾን ፡ የእመ ፡ ወራሽ ፡ ነው ፤ ኢመፍትው ፡ አድልዎ ፡ በፍትሕ ፤ በፍርድ ፡ ጊዜ ። ጋራ ፡ ሲኾን ፤ የም ስለ ፡ ወራሽ ፡ ነው ፤ ተዋሐደ ፡ ቃል ፡ በሥጋ ። እንደ ፡ ሲኾን ፡ የከመ ፡ ወራሽ ፡ ነው ፤ ጽድቅ ፡ በወልታ ፡ የዐውደከ ። ቸልታም ፡ ሲኾን ፡ የእንዘ ፡ ወራሽ ፡ ነው ፤ ጸለየ ፡ ወሰ አለ ፡ ኀበ ፡ እግዚ ፡ በብካይ ፤ አልቅሶ ፡ ወይም ፡ እያለቀሱ ፡ ያሰኛል ። በ + በማይስማማው ፡ ግስ ፡ ገብቶ ፡ ሲገኝ ፡ በሚስማማው ፡ ግስ ፡ ይፈታል ። መጻእከሙ ፡ ተአኀዙኒ ፡ በአብ ትር ፤ በበትር ፡ መትታችኹ ፡ ትይዙኝ ፡ ዘንድ ፤ ወይም ፡ መጻእከሙ ፡ በአብትር ፤ በትር ፡ ይዛችኹ ። ከልብኑ ፡ አነ ፡ ከመ ፡ ትምጻእ ፡ ኀቤየ ፡ በአእባን ፡ ወበትር ፤ ድንጊ ያና ፡ በትር ፡ ይዘኽ ። ነሐውር ፡ በእግረ ፡ ደቂቅ + በልጆች ፡ እግር ፡ ልክ + ወይም ፡ እንደ ፡ ልጆች ፡ እግር ፡ ያሰኛል ። አምላክ ፡ ውእቱ ፡ በሥጋ ፤ በሥጋ ፡ ሳለ ። ወበቱ ፡ ፍጹም ፡ መለኮት ፡ በአርአያ ፡ ንጼትነ ፤ በነዳይ ፡ ባሕርያችን ፡ ሳለ ፤ ሳይለወጥ ፡ ማለት ፡ ነው ። ሐመ ፡ ሕማመ ፡ ሥጋ ፡ እሙነ ፡ በመለኮቱ ፤ በምላክነቱ ፡ ሳለ + ሳይታመም ። በበታ ፡ ላይ ፡ ሲወድቅ ፡ አገባብነቱን ፡ ሳይለቅ ፡ አንቀጽ ፡ ይኾናል ፤ ኤልያስ ፡ በገነት ። አፁነ ፡ ዘበሰማያት ። ሲዘረዝርም ፡ በጥሬነቱ + በ ፡ ባ ፡ እያለ ፡ በርሱ ፡ በርሷ ፡ ያሰኛል ። በበ + በየ ፡ ይኾናል ፤ ከተጸውዖ ፡ ስም ፡ በቀር ፡ በብትን ፡ ኹሉ ፡ ይገባል ፤ በበ ፡ ደወሉ +

በያውራጃው ። ከዕለት፡እስካመት፡ያሉትን፡ጊዜያት፡በዝርዝር፡ወይም፡በደጊመ፡ቃል፡ያናግራል ። ይህም፥በበ፡ዕለት፤በየለቱ፥ዕለት፡ዕለት ። በበ፡ወርኅ፤በየወሩ፥በወር፡በወር ። በበ፡ዓመት፤በያመቱ፡ባመት፡ባመት ። ይሠውዑ፡በበ፡ነግህ፡ወበበ፡ሠርክ፤ጧ.ት፡ጧ.ት፥ማታ፡ማታ ። በአኃዝም፡ገብቶ፡እንዲሁ፡ይፈታል ። በበ፡አሐዱ፤በያንዳንዱ፥አንዱም፡አንዱም፥አንዳንድ ።

፻፲፫፤ ለ ። አቀባይ፥ወይም፡በቊም፡ቀሪ፤አቀብሎ፡ሽሽ፥አዳማቂ ። የ፡ን፡ከ፡ወደ፡ላይ፡ስለ፡ጋራ፡ይኾናል ። በቊም፡ቀሪ፡ሲኾን፡ሀቡ፡ዘቄሳር፡ለቄሳር፥ወዘእግዚ፡ለእግዚ ። ኢ.ትበሉ፡ለጌሠም ። በባለቤትና፡በቅጽልም፡እንደ፡በ፡እየ ተደረበ፡ይነገራል ። ለካህናት፡ለደቂቀ፡አሮን፤ለብእሲ.ት፡ለመርዓተ፡በግዑ፤ለጋይዮስ፡ለእኁነ ። በና፡ለ፡ባማርኛም፡እንደዚሁ፡ናቸው፤ተደራርበው፡ይነገራሉ ። በሰማይ፡በላዕሉን፡ተመልከት ። አቀብሎ፡ሽሽ፡ሲኾን፥ለይኩን፡ብርሃን፤ለይትጋባእ፡ማይ፤ለትቅረብ፡ስእለትየ፡ኀቤከ፡እያሰኘ፡በትእዛዝ፡አንቀጽ፡ይገባል ። አዳማቂም፡ሲኾን፥ለኀበ፡ሰማያት፡ለመንገለ፡እግዚ፤ለእመ፡ርኅበ፡ጸላኢ.ከ፡እያለ፡በገባብ፡ይወድቃል ። የ፡ሲኾን፡ዘርፍ፡እያያዥና፡የዘርፍ፡ደፊ፡ነው፤ን፡ሲኾን፡ተጠቃሽ፡ወይም፡የግእዝ፡ወራሽ፡ይባላል፤፪ቱም፡በዘርፍና፡በባለቤት፡ክፍል፡ተነግረዋል፡(ዕር፲፯፡ቊ፭፪) ። ከ፡ሲኾን፡ተሠጠ፡ለክልኤ፤ተከፍለ፡ለአርባዕቱ፡እያለ፡በአኃዝ፡ገብቶ፡ይነገራል ። ወደ፡ሲኾን፡ተመይጠ፡ለብሔሩ፡ግብጽ፡ይላል ። ላይ፡ሲኾን፡ወአምጽአ፡ረኀበ፡ለብሔር፤በምድር፡ላይ ። ስለ፡ሲኾን፡ኢ.ትጸሊ.፡ለዝ፡ሕዝብ፡ይላል ። ፪ኛም፡ለዝ፡ያለው፡በቊም፡ቀሪ፡ሲኾን፡ያምርለታል ። ጋራ፡ሲኾን፡የምስለ፡ወራሽ፡ነው ። ትከውኑ፡ሱቱፋነ፡ለሐራ፡ሰማይ ። ለ፥ላይ፡ስለ፥መኾኑ፡መላሾች፡በላዕለና፡በበእንተ፡ፈንታ፡ስላገቡት፡ነው፤ይኸውም፡ሊ.ታወቅ፡ከዚህ፡በቀር፡በሌላ፡አይገኝም ። በዘ፡ፈንታ፡ገብቶ፡የ፡ሲኾን፡ውእቱን፤በቊም፡ቀሪ፡ሲኾን፡ደለወ፡ይደሉን፡ያመጣል ። ለእግዚ፡ምድር፡በምልኣ ። ለአብ፡ስብሐት፥ለወልድ፡ስግደት፥ወለመንፈስ፡ቅዱስ፡በርከት ። ሲ.ዘረዘርም፥ሎ፡ሎቱ፡ላ፡ላቲ፡እያለ፡ለርሱ፡ለርሷ፡ያሰኛል፤አንቀጽነቱ፡ከበ፡ጋራ፡በደቂቀ፡ርባታ፡ተነግሯል ። ለለ ። ለየ፡እየ፡ደጊመ፡ቃል፡ይኾናል ። ከተጸውዖ፡ስም፡በቀር፡በብትን፡ኹሉ፡ይገባል፤ከዕለት፡እስካመት፡ያሉትን፡እንደ፡በበ፡ይዘረዝራል ። ለለ፡ርእሱ፥ለየራሱ፡እየራሱ፡ራስ፡ራሱ ። ለለ፡አሐዱ፥ለያንዳንዱ፡እያንዳንዱ፥አንዳንዱ፤አንዱም፡አንዱም ። ለለ፡ዕለቱ፥ለየለቱ፡እየለቱ፥ዕለት፡ዕለት፡እያሰኘ፡ሌላውን፡ኹሉ፡ያሳያል ። ፪ኛም፡በኀላፊና፡በትንቢ.ት፡ሲ.ገባ፡ዐቢ.ይ፡አገባብ፡ይኾናል፤ዐቢ.ይነቱም፡አመንና፡ሰበን፡እንዘን፡ይመስላል፤ፍችውም፡ጊዜና፡የ፡ሲ.፡ስ፡ደጊመ፡ቃል፡ነው ። ወለለ፡ወለዳ፤አው፡ወለለ፡ይወልዳ፡ተባዕተ፡ቅትላሁ፤ወንድ፡ወንድ፡በወለዱ፡ጊዜ፥ሲ.ወልዱ፤ወይም፡የወለዱትን፥የሚወልዱትን፥ወንድ፡ወንዱን፡ግደሉት ። ለለ፡ተናገርኩ፡ተዘከርኩ፤በተናገርኹ፡በተናገርኹ፡ጊዜ፤የተናገርኹ፡የተናገርኹትን ። ለለ፡እትናገር፤ስናገር፡ስናገር ። በደጊመ፡ቃልም፡ፈንታ፡ቊጥር፡ይኾናል፤ምስጢሩ፡ጊዜን፡አይ

ለቅም ። ለለ፡ ወለዳ፡ በወለዱ፡ ቊጥር ፥ ለለ፡ ተናገርኩ፡ በተናገርኹ፡ ቊጥር ። ይኸ ውም፡ በቀዳማይ፡ ብቻ፡ ነው ።

፻፲፬ ፤ ምስለ ። ጋራ ፥ ከነ ። እንደ ፥ ከ ፥ ና ፥ ይኾናል ፤ ጋራ፡ በሚኾንበት፡ ኅቡረ፡ ሲጨመር፡ ዐብሮ፡ ባንድነት፡ ያሰኛል ። ንዒ፡ ኀቤየ፡ አ፡ ድንግል፡ ምስለ፡ ወል ድኪ ፤ ከልጅሽ፡ ጋራ ። ወመላእክትኒ፡ ተጋብኡ፡ ምስሌሆሙ፡ ኅቡረ ፤ ከርሳቸው፡ ጋራ፡ ዐብረው፡ ወይም፡ ባንድነት ። መጽአ፡ ብእሲ፡ ምስለ፡ ብእሲቱ ፤ ከነሚስቱ ፥ ወይም፡ ከሚስቱ፡ ጋራ ። እንደ፡ ሲኾን፡ የከመ፡ ወራሽ፡ ነው ። አበስነ፡ ምስለ፡ አበዊነ ፤ ወኢ ተቀሥፉ፡ ምስለ፡ ሰብእ ፤ እንደ፡ ሰው ። ከ፡ ሲኾን፡ የእም፡ ወራሽ፡ ነው ፤ መለያየ ትን፡ በሚያሳዩ፡ ግሶች፡ ይገባል ፤ ወብእሲትኒ፡ ኢትትኃደግ፡ ምስለ፡ ምታ ፤ ከባሏ፡ አትፋታ ። ና፡ ሲኾን፡ እንደ፡ ወ፡ አጫፋሪ፡ ነው ፤ በብዙ፡ ወንድ፡ አንቀጽ፡ ይገባል ። ከንቶ፡ ይትናገሩ፡ አሐዱ፡ ምስለ፡ ካልኡ ፤ አንዱና፡ ሌላው፡ ኹለተኛው ። ተማከ ሮሙ፡ ብእሲ፡ ምስለ፡ ብእሲቱ ፤ ባልና፡ ሚስቱ ። ምስለ ፥ በማይመስለው፡ ግስ፡ ሲገባ፡ በዝ፡ ኹኖ፡ ይፈታል ። ሰረረ፡ ንስር፡ ምስለ፡ መጽሐፍ ፤ መጽሐፍ፡ ይዞ ። ሲዘረ ዘርም፡ ምስሌሁ፡ ሃ፡ እያሰኘ፡ እንደ፡ ፈተኞቹ፡ ይፈታል ። አነ፡ ምስሌክሙ ፥ እስመ፡ እግዚአብሔር፡ ምስሌነ፡ ሲል፡ በነበር፡ በዘማች፡ ያሳስራል ።

፻፲፭ ፤ አያተ ፤ ጽላሎተ ። አያተ፡ በብትን፡ ብቻ ፥ ጽላሎተ፡ በተጸውዖ፡ ስም፡ እየገቡ፡ እንደ፡ ይኾናሉ ። ተዋሕዶ፡ ሥጋ፡ ወቃል፡ አያተ፡ ሐመልማል፡ ወነበልባል ። አስናኒከ፡ አያተ፡ አዕናቍ፡ እለ፡ ተሰክዓ ። ተሰቅለ፡ ጴጥሮስ፡ ቊልቊሊተ፡ ጽላሎተ፡ ዶርሆ ። አርእስትና፡ ሳቢ፡ ዘርም፡ እንደ፡ ይኾናሉ ፤ ተመትሩ፡ ያዕቆብ፡ ወማቴዎስ፡ ወጳውሎስኒ፡ ተመትሮተ፡ መጥምቅ፡ ምትረተ፡ መጥምቅ፡ ዮሐንስ ፤ እንደ፡ መጥምቁ፡ ዮሐንስ ።

፻፲፮ ፤ ከደቂቅ፡ አገባብ፡ የሚጨመሩ፡ የቦታና፡ የጊዜ፡ ጥሬዎች ። እነዚ ህም፡ ተናበውና፡ ተዘርዝረው ፥ ግእዝ፡ ኃምስ፡ ኹነው፡ ይነገራሉ ። ላዕል፡ ላዕሉ፡ መልዕልት፡ ላዕሊት ፤ ወደ፡ ላይ፡ ይኾናሉ ፤ ማሰሪያቸውም፡ ዐርገ፡ ርእየ፡ አንቃዕ ደወ፡ ነበረ፡ ሐወጸ፡ እነዚህን፡ የመሰለ፡ አንቀጽ፡ ነው ። ዐርገ፡ ወነበረ፡ ላዕለ፡ መል ዕልተ፡ ላዕሊተ ፤ ወደ፡ ላይ፡ ወጣ ፤ በላይ፡ ተቀመጠ ። በደጊመ፡ ቃልም፡ ይነገ ራሉ ፤ ላዕለ፡ ላዕለ፡ እንዘ፡ ያንቃዕዱ ፥ በነጽሮ፡ ተሰብረ፡ ክሣዱ ። ሖረ፡ ሮጸ፡ ርእየ፡ ኖመ ፤ እነዚህን፡ የመሰለ፡ አንቀጽ፡ ሲስባቸው፡ ሽቅብ፡ አሻቅቦ፡ ይኾናሉ ። በቀረው፡ እንደ፡ ማንም፡ ጥሬ፡ ተደራጊ፡ ተሳቢ ፥ ዘርፍና፡ ባለቤት፡ ኹነው፡ ይነገራሉ ፤ ፫ቱ፡ የቦታ፡ አገባቦች፡ ይሰማሟቸዋል ፤ ላዕለ፡ ግን፡ እየተናበበ፡ ይነገራል ። የነላዕል፡ አን ጻር ፥ ታሕት፡ ታሕቱ፡ መትሕት፡ ታሕቲት፡ ታች፡ ይኾናሉ ። ሲዘረዘሩም፡ ላዕል፡ ታሕት፡ ያለውን፡ ላዕሉ፡ ላዕልከ ፥ ታሕቱ፡ ታሕትከ፡ ያሰኛሉ ። ላዕሉና፡ ታሕቱ፡ ግን፡ የማይፈልሱና፡ የማይበዙ፡ ጕልት፡ ቀለም፡ ናቸው ፤ በቅጽል፡ ባርእስት፡ በብትን፡ በአኃዝ፡ ይገባሉ ። ክቡር፡ ውእቱ፡ ንቡረ፡ ላዕሉ፡ ወነጻሬ፡ ታሕቱ ። ያፈቅር፡ ባሕ ታዊ፡ ነጽሮተ፡ ላዕሉ፡ እምነጽሮ፡ ታሕቱ ። አንትሙሰ፡ እምታሕቱ ፤ ወአንሰ፡ እምላ ዕሉ ። ዘእምዕሥራ፡ ዓም፡ ወዘላዕሉ ፥ አው፡ ወዘታሕቱ ። የነታሕቱ፡ አንቀጾች፡ ወረደ፡

ሐወጸ፡ርእየ+እነዚህንም፡የመሰሉ፡ ኹሉ ። የቀረውም፡ አገባባቸው፡ እንደነላዕል፡ ነው ።   ትርአስ፡ትርጋፅ፤ውስጥ፡ውሳጢ፡ውሳጢት፤ ቅድም፡ፍጽም፡ገጽ፤ ድኅር፡ ከዋላ፤  የማን፡ ይምን+ፀጋም፡ ፅግም ።  የነዚህም፡ ዐዋጅ፡ እንደነላዕል፡ ነው ። ግድም+  በደጊም፡ ብቻ፡ ይነገራል፤ አንትሙ፡ ተሐውሩ፡ ግድመ፡ ግድመ ።  ድኅ ሬት፡ ግንጽሊት፡ ግፍትዒት፤ ማሰሪያቸው፡ ወድቀ፡ ተአስረ፡ ይህን፡ የመሰሉ፡ ናቸው ። ወድቀ፡ ዔሊ፡ ድኅሬተ፡ ግንጽሊተ፡ ግፍትዒተ፤ የኋሊት ። ተአስረ+ወይም፡ አሰርዎ፡ ድኅሬተ፡ ግንጽሊተ፡ ግፍትዒተ፤ የኋሊት፡ የግርንግሬት ።

፻፲፯፤  በዝርዝርነት፡ ግእዝ፡ ኃምስ፡ ኹነው፡ የሚነገሩ፡ የቦታ፡ ጥሬዎች፡ እሊህ፡ ናቸው ።   አፍአ፤ ከዋላ፤ ዝየ፡ ህየ፤ ለፌ፡ ከሃ፤ ኀለሄ ።  አፍአ+ውጭ፡ በውጭ(ጪ)፡ ይኾናል፤ ከንቀጽ፡ ጋራ፡ ይነገራል፤  በቀረው፡ እንደነላዕል፡ ነው ። ይቀውም፡ አፍአ፤ አውፅእዎ፡ አፍአ ።  ከዋላ+  ኋላ፡ በኋላ፡ ይኾናል፤ ነዐቅብ፡ ፍጽመ፡ ወከዋላ፤ የሐውሩ፡ ከዋላ፤ በኋላ፡ በስተኋላ ። ዝየ፡ የቅርብ፡ ቅርብ፡ ነው፤ በዚህ፡ ከዚህ፡ ወደዚህ፡ ይኾናል፤ ከዘማች፡ ከነባር፡ ዐብሮ፡ ይነገራል ። ዝየ፡ አኀ ድር ። ምንት፡ ብከ፡ ዝየ ። አምጽእዎን፡ ሊተ፡ ዝየ ።   ህየ+የቅርብ፡ ሩቅ፡ የዝየ፡ አንጻር፡ ነው፤ በዚያ፡ ከዚያ፡ ወደዚያ፡ ይኾናል፤ በቦታና፡ በነገር፡ ዐጸፋ፡ ይገባል ። በቦታ+ተከለ፡ ገነተ፡ ወሤሞ፡ ህየ ። በነገር+በህየኒ፡ ሰመዮ፡ ወልደ፤ ወበዝየኒ፡ ሰ መዮ፡ እኅወ ።   ለፌ፤ ወዲህ፡ ወደዚህ፡ ይኾናል፤ ትመጽእ፡ ለፌ፡ ኀበ፡ አነ፡ እቀ ውም ። በጊዜም፡ ሲገባ+እለ፡ ይብሉ፡ ከመ፡ ክርስቶስ፡ ለፌ፡ እማርያም+አው፡ ለፌ፡ እምጥምቀት፡ ይላል ። ተደጋግሞና፡ ተጫፍሮ፡ ሲነገር፡ ወዲህና፡ ወዲያ+ቀኝና፡ ግራ፡ ይኾናል ። ነጸረ፡ ለፌ፡ ወለፌ ። አንጌገየ፡ ለፌ፡ ወለፌ ። ሰቀሉ፡ ምስሌሁ፡ ክል ኤተ፡ ፈያተ፡ አሐደ፡ እምለፌ፡ ወአሐደ፡ እምለፌ ። ጽሑፋት፡ እንተ፡(በ፡ እም) ለፌኒ፡ ወእንተ፡ ለፌኒ ።

፻፲፰፤ ከሃ+ወዲያ፤ ከሃት+ወዲያዎች፡ ወዲያኞች፡ ይኾናል ።  ዝርዎ፡ ከሃ፤ ሑር፡ ከሃ ። ሲዘረዝርም፡ ከሃሁ፡ ከሃቲሁ፡ ሃ፡ ሆሙ፡ ሆን፤ ከሃከ፡ ከሃቲከ፡ እያሰኘ፡ በባዕድ፡ በራሱ፡ ያናግራል ። ከዝርዝሩ፡ በቀር፡ እንደ፡ ህየ፡ ነው፤ የቦታ፡ አገባቦች፡ ይሰማሙታል ። እምለፌሁ፡ ወእምከሃሁ ። እልክቱ፡ እምከሃ+ወእሉኒ፡ እምለፌ ። ሰበከ፡ ማርቆስ፡ በግብጽ፡ ወእምህየ፡ እስከ፡ ከሃቲሃ ።   ኀለሄ፤ ቦታ፡ ኹሉ+መ ላው፡ ጠቅላላው፡ አራቱ፡ ማእዝን ። ብቻውንም፡ ከገባብም፡ ጋራ፡ ይነገራል፤ ብቻ ውን+ሖርኩ፡ መትሕተ፡ ሰማይ፡ ኀለሄ፤ እስከ፡ ይሰማዕ፡ ኀለሄ ። ከገባብም፡ ጋራ+ም ሉእ፡ በኀለሄ ። ተጋብኡ፡ ኀቤሁ፡ እምኀለሄ፤ እለ፡ ይነብሩ፡ ውስተ፡ ኀለሄ ። ይነድ ፍዋ፡ እንተ፡ ኀለሄ፡ እያለ፡ ይገባል ።

## እየተናበቡ፡ የሚነገሩ፡ የቦታ፡ ጥሬዎች ።

፻፲፱፤ ጽንፍ፡ ክንፍ፡ ክንፈር፡ ሐይቅ፡ ድንጋግ፡ ገበዝ፡ ወሰን፤ ዳር፡ ዳርቻ + ጫፍ፡ ጠርዝ፡ ይኾናሉ ። ጽንፍ+ለባሕር፡ ለየብስ፡ ለኅብስት፡ ለልብስ፡ ይኾናል ። ጽ ንፈ፡ ባሕር፡ የብስ፤ ወጽንፈ፡ የብስኒ፡ ባሕር ። ጽንፈ፡ ኅብስት፡ ወልብስ ። ክንፍ+ለ

ኹሉ ፡ ይኾናል ፤ ክንፈ ፡ ምድር ፥ ክንፈ ፡ ቤት ። ክንፈር ፡ ሐይቅ ፥ ለባሕር ፡ ይኾናሉ ፤ ድንጋግ ፥ ለወንዝ ፡ ለባሕር ፡ ለዘመን ፡ ይኾናል ። ገበዝ ፥ ለወንዝ ፡ ብቻ ፤ ወሰን ፥ ለኹሉ ፡ ይኾናል ። ወበጽሐ ፡ ዮርዳኖስ ፡ እስከ ፡ ድንጋጊሁ ። ኖጻ ፡ ዘድንጋገ ፡ ባሕር ። ሞት ፡ ድንጋገ ፡ ዕድሜ ፡ ዘኢይበጽሖ ፡ መልአክ ። ተቀበሎ ፡ ዲበ ፡ ገበዘ ፡ ተከዚ ። ኢትትዓደዊ ፡ እምወሰንኪ ። ጽፍሕ ፥ ድልድል ፤ ስፍሕ ፥ ስፋት ፡ ወልወል ፡ ይኾናል ። ጽፍሐ ፡ መሠረቱ ፤ የመሠረቱ ፡ ድልድል ፥ ወይም ፡ የግንቡ ፡ አርመን ፡ ወርዱ ፡ ሆዱ ፡ ማለት ፡ ነው ።

፻፹ ፤ አድያም ፡ ደወል ፡ ብሔር ፤ አውራጃ ፡ ቀበሌ ፡ ግዛት ፡ አገር ፡ ይኾናሉ ። አድያመ ፡ ዮርዳኖስ ። ደወለ ፡ ጢሮስ ። ብሔረ ፡ ግብጽ ። ብሔረ ፡ አሕዛብ ። ደወል ፡ ተለይቶ ፡ ወሰን ፡ ደንበር ፡ ይኾናል ፤ ኢታፍልስ ፡ ደወለ ፡ ገራህት ። አፍአና ፡ ማእከል ፡ በየቦታቸው ፡ ተነግረዋል ። ጥቃ ፡ ኀር ፡ ሕፅን ፡ ገቦ ፡ ጕንድ ፤ አጠገብ ፡ ጐን ፡ ወገብ ፡ ይኾናሉ ፤ የቦታ ፡ አገባቦች ፡ ይሰማሟቸዋል ። ጥቃ ፥ ለቦታ ፡ ብቻ ፤ የቀሩት ፡ ለቦታም ፡ ላካልም ፡ ይኾናሉ ። ይነብር ፡ ጥቃ ፡ ፍኖት ። ወቤቱ ፡ ኀረ ፡ ምሥራብ ። ሕፅነ ፡ ደብር ፡ ገቦ ፡ ደብር ፡ ጕንደ ፡ ደብር ። ኢትጸውዕ ፡ ኀረከ ፤ ይረፍቅ ፡ ውስተ ፡ ሕፅኑ ። ይወድቁ ፡ በገቦከ ። አጻብዒከ ፡ እምጕንደ ፡ ክልኤ ፡ አእጋር ። ጽጕ ፡ ጽጕጕ ፡ ጽጕኅት ፥ ጥግ ፡ ወልወል ፡ ይኾናል ። ጽጕ ፡ ቤት ፤ ጽጕ ፡ ሀገር ፤ ወለእመ ፡ ሀለዉ ፡ ጽጕኅት ፡ ማእከለ ፡ አብያት ፥ ወልወል ። ዐውድ ፡ ዘውር ፥ ዙሪያ ፡ ይኾናሉ ፤ ክበብ ፡ ባለው ፡ ኹሉ ፡ ይገባሉ ። ፀውደ ፡ ቤት ፥ ዘውረ ፡ አክሊል ። ዐውድ ፡ ተለይቶ ፡ አደባባይ ፡ ሸንጎ ፡ ዐውድማ ፡ ይኾናል ። ነበሩ ፡ ዐውደ ፡ ለኵንኖቱ ። ዘቦቱ ፡ ያነጽሕ ፡ ዐውደ ፡ እክሉ ። ሲዘረዘሩም ፡ ዐውዱ ፡ ዳ ፥ ዘውሩ ፡ ራ ፡ እያሰኙ ፡ እንዳንቀጹ ፡ ስልት ፡ ይፈታሉ ። ይቀውሙ ፡ ዐውዶ ፤ በዙሪያው ። ንንሥት ፡ ዐውደነ ፤ ሸንጓችንን ፡ እንፍታ ።

## የጊዜ ፡ ጥሬዎች ።

፻፹፩ ፤ ቅድም ፡ መቅድም ፡ ቀዲሙ ፡ አቅዲሙ ፡ ቀዳሚ ፤ ቀድሞ ፡ አስቀድሞ ፡ ፊት ፡ መዠመሪያ ፡ ይኾናሉ ። ቅድምና ፡ መቅድም ፡ ግእዝ ፡ ኹነው ፥ የቀሩት ፡ ጕልት ፡ ኹነው ፡ ሳይፈልሱ ፡ ይነገራሉ ። ቅድም ፡ ተለይቶ ፡ በቦታም ፡ በጊዜም ፡ እንዲገባ ፡ በፊት ፡ ተነግሯል ። ፫ቱ ፡ ኹሉ ፥ ላንድና ፡ ለብዙ ፡ ለወንድና ፡ ለሴት ፡ ለሩቅና ፡ ለቅርብ ፡ እየኾኑ ፡ እንዳንቀጻቸው ፡ ስልት ፡ ይፈታሉ ። ቅድመ ፡ አሠኒ ፥ መቅድመ ፡ ኅሡ ። ቀዲሙ ፡ ዜነወነ ፤ ዘነገሩክሙ ፡ ቀዲሙ ፤ አቅዲሙ ፡ ነገረ ፡ በአሪት ። ቀዳሚ ፡ ጸሐፍኩ ፡ ለከ ። መቅድምና ፡ አቅዲሙ ፡ ሲቀሩ ፡ እምና ፡ በ ፡ ይሰማሟቸዋል ። የቅድምና ፡ የቀዳሚ ፡ አንጻሮች ፡ ድኅርና ፡ ደኃሪ ፥ ኋላ ፡ መጨረሻ ፡ ይኾናሉ ፤ አገባባቸውም ፡ እስከ ፡ ነው ። ድኅር ፡ ግእዝ ፡ እየኾነ ፥ ደኃሪ ፡ ከዋላ ፡ በነባርነት ፡ ሲነገሩ ፥ ኋላ ፡ በኋላ ፡ ወደ ፡ ኋላ ፡ ይኾናሉ ። ይነብሩ ፡ ሙታን ፡ ውስተ ፡ መቃብር ፡ እስከ ፡ ይትነሥኡ ፡ ድኅረ ፥ አው ፡ ደኃሪ ፡ ከዋላ ። ገብኡ ፡ ድኅረ ። በ ፡ ለ ፡ መንገለ ፡ እም ፡ ይሰማሟቸዋል ፤ ቅድመና ፡ ድኅረም ፡ እንደ ፡ ግድም ፡ እንደ ፡ ላዕል ፡ ተደጋግመው ፡ ይነገራሉ ። ቅድመ ፡ ቅድመ ፡ እንዘ ፡ የሐውሩ ፥ ነቢያት ፡ ድኅሬተ ፡ ነጸሩ ። ፈረሱ ፡ ለፈርዖን ፡ ይቤ ፡ ድኅረ ፡ ድኅረ ፤ እስመ ፡ እግሩ ፡ ኢለመደ ፡ ባሕረ ። መቅድም ፡ መስም ፡ ነው ፤ ቀዳሚ ፡ ደኃሪ ፡

ሣልስ፡ቅጽሎች+ቅድምና፡ድኅር፡ጥሬዎች+ቀዲሙና፡አቅዲሙ፡ በዝ፡አንቀጾች፡
ናቸው ። ኹሉም፡ በ፳፡ አርእስት፡እየገቡ+ቅድመ፡መቅድመ+ቀዲሙ፡ አቅዲሙ፡
ቀዳሚ+አው፡ ድኅረ፡ ደኃሪ፡ ጸውዐ፡ አጸውዐ+ተጻውዐ፡ ተጻውዐ፡ አስተጻውዐ፡
ያሰኛሉ ። ይኸውም፡ በምልአት፡ ለሚነገሩ፡ እንጂ፡ ለኹሉ፡ አይዶለም፤ በሳድስ፡
ቅጽልም፡ሲገቡ+ጽዉዕ፡ ቅድመ፡ ቀዳሚ፡ ወምጹእ፡ ድኅረ፡ደኃሪ፤ፊት፡የተጠራ፡
ኋላ፡የመጣ፡ያሰኛሉ ። ጊዜም፡ከነክፍሎቹ፡ከቅጽል፡ጋራ፡ይነገራል ።ቅጽሉም፡
አኃዝና፡የአኃዝ፡ጥሬ፡ነው፤የአኃዙ፡በቦታው፡ተነግሯል ። ኵሎ፡ጊዜ፡ኵሎ፡ሰ
ዓተ፡ኵሎ፡ዕለተ፡ኵሎ፡አሚረ፡ኵሎ፡ዘመነ፤ ኹል፡ጊዜ+ኹል፡ቀን፡ዘወትር፡
በዘመኑ፡ኹሉ፡ያሰኛሉ ። ተናበው፡የሚነገሩ ። ጥንት፡መሠረት፤ መዠመሪያ ።
ፍጻሜ፡ተፍጻሜት፤መጨረሻ፡ይኸናሉ ።ሲገቡም፡ጥንተ፡ሕይወት፡ጥንተ፡ዕለት+
መሠረተ፡ንጽሕ፡መሠረተ፡ቃል ። ፍጻሜ፡ዘመን+ተፍጻሜተ፡መዋዕል፡ያሰኛሉ ።
መሠረት፡ለኹሉ፡ይኸናል ። ተዘርዝረው፡የሚነገሩ ። ንእስ፡ናእስ፡ንእስና፤ልጅ
ነት፡ታናሽነት ። ውርዙት፡ውርዛዌ፡ውርዝውና፤ጕልማስነት፡ዐፍላ፡ጕብዝና ።
ርሥእ፡ርሥአን፡ርሥእና፤ እርግና፡አሮጌነት ። እም፡በ፡አመ፡እስከ፡ድኅረ፡ይሰ
ማሟቸዋል ። ዘንተ፡ኵሎ፡ዐቀብኩ፡እምንእስየ ። ሰሎሞን፡ኮነ፡ጠቢበ፡እምንእሱ፡
በንእሱ፡ አመ፡ ውርዛዌሁ፤ ወአመ፡ ርሥአኑ፡ ኮነ፡ አብደ ። አብርሃም፡እምውርዛ
ዌሁ፡እስከ፡ርሥአኑ፡ኢወለደ፤ወበልህቅናሁ፡ረከበ፡ወልደ ። ወእምድኅረ፡ርሥ
አን፡ጥሉል ።

ያከልና፡የበሕርይ፡ጥሬዎች ።

፻፳፱፤ ኵለንታ፤ ኹለንተና+ኹለመና፡ይኸናል ። ከራስ፡ጠጕር፡እስከ፡
እግር፡ጥፍር፡እንደ፡ማለት ። ጠባይዕ፤በቁሙ፡ ጠባይ፡ ባሕርይ፡ ይኸናል ።
አባል፡ሕዋስ+መንፈስ፡ነፍስ+ነፍስት፡ መሌሊት፤ አካል፡ ብልት፡ ገላ፡ ሰውነት፡
ይኸናሉ ።ቅጽሎቻቸውም፡ኵሉ፡ኵላ፡ናቸው፤አኃዝም፡ይሰማማቸዋል፤ ለእመ፡
ሐመ፡አሐዱ፡አባል ። አካል፤በቁሙ+ቁመት፡አቋቋም+ለመያዝ፡የሚበቃ፤መ
ጠን፡ግዘፍ፡ይኸናል፤ዘመጠነ፡ገዘ፡አካሉን ። ሀላዌ፤ባሕርይ፡አካል+አቋቋም፡
አናዎር ። ከዋኔ፤ አኳኋን፡ኹነታ ፤ ከዋኒ፤ ኗኝ፡ቀዋሚ፡ይኸናሉ ። በት
ምርት፡በስሎ፡የታጨደው፡ያገባበች፡ነዶና፡ክምር+ክምሉ፡በክፍሉ፡ከብዙ፡በጥ
ቂቱ፡ይህ፡ነው ።

፫ኛ፡ክፍል ።

ጸዋትወ፡ቅኔ+የሠምና፡የወርቅ፡ኵርጓኔ ።

፳፪ኛ፡ዕርከን ።

ሠምና፡ ወርቅ፡ ማለት፡ እንደ፡ ወንድማማች፡ በምስጢር፡ መንታ፡ ሲኾኑ፡
በንባብ፡ሳይጣፈሩ፡በ፮፡ነገር፡ተባብረው፡ተጣምረው፡፩፡ወጣት፡ቃል፡መስለው፡

የሚነገሩ ፡ ተመሳሳዮች ፡ ማለት ፡ ነው ። በተረትም ፥ ሠምና ፡ ወርቅ ፡ እንጀራና ፡ መረቅ ፡ ይባላል ።

፻፹፫ ፤ ሠምና ፡ ወርቅ ፡ ሲመሰሉ ፡ ሠም ፡ ተናበ ፡ እየቀደመ ፡ ወርቅ ፡ ይከተላል ፤ ወርቅም ፡ ቀድሞ ፡ ሠም ፡ ቢከተል ፡ ካልተናበበ ፡ ጸያፍ ፡ አይባልም ፤ ቢናበብ ፡ ግን ፡ ግንባር ፡ ጸያፍ ፡ ይባላል ። ፩ኛውን ፡ ዐዋጅ ፡ ለማሳየት ፥ ርኁባን ፡ አሕዛብ ፡ በልዑ ፡ ኅብስተ ፡ ሃይማኖት ፤ ወይም ፡ ኅብስተ ፡ ሃይማኖተ ፡ በል ። ፪ኛውን ፡ ለማሳየት ፥ በልዑ ፡ ሃይማኖተ ፡ ኅብስተ ፡ በል ፤ ይህ ፡ ጸያፍ ፡ አይባልም ፤ ሃይማኖተ ፡ ኅብስት ፡ ቢል ፡ ግን ፡ ግንባር ፡ ጸያፍ ፡ ነው ። ሠም ፡ ተናበ ፡ ለወርቅ ፡ ፫ ፡ ፊደላት ፡ ያተርፍለታል ፤ ፊደላቱም ፡ ግእዝ ፡ ሳብዕ ፡ ኃምስ ፡ ናቸው ። ይህም ፥ ሰሎሞን ፡ ዐማኑኤል ፡ ሐነጸ ፡ መቅደሰ ፡ ደሙ ፡ ማሕየዊ ፡ በለ ፡ ጊዜ ፡ ሳብዕና ፡ ኃምስ ፡ ማስቀረቱን ፡ ያሳያል ፤ ባይናበበው ፡ ግን ፡ ደሞ ፡ ማሕየዌ ፡ ባለ ፡ ነበረ ። ግእዝ ፡ ማስቀረቱም ፥ መቅደሰ ፡ ደም ፡ ሐነጸ ፡ በማለት ፡ ይታያል ። ሠም ፡ ለወርቅ ፡ የሚያተርፍለት ፡ ይህ ፡ ብቻ ፡ አይደለም ፤ ከዚህ ፡ ሌላ ፡ ደግሞ ፡ ፮ ፡ ነገር ፡ ያተርፍለታል ፤ እነዚሁም ፡ ማሰሪያ ፥ አንቀጽ ፥ ተናባቢ ፥ አፈታት ፥ ቅጽል ፥ ዝርዝር ፡ ናቸው ። አገባብ ፡ ያተርፋል ፡ የሚሉም ፡ አሉ ፤ አገባብ ፡ ግን ፡ በሠም ፡ ላይ ፡ ወድቆ ፡ ለወርቅ ፥ በወርቅ ፡ ላይ ፡ ወድቆ ፡ ለሠም ፡ ይኸናልና ፤ ሠም ፡ ለወርቅ ፡ አገባብ ፡ ያተርፋል ፡ ማለት ፡ ለልብ ፡ አይረዳም ። ፮ ፡ ነገር ፡ ማትረፉም ፡ እንዲህ ፡ ነው ። እመ ፡ ርኅራኄ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ትወግዕ ፡ ጥዑመ ፡ ሥጋዌ ፡ ሐሊበ ፡ እግዚእን ፡ ለደቂቃ ፡ ምእመናን ፥ በይነ ፡ ዘአእመረት ፡ ከመ ፡ ይከውኖሙ ፡ ሕይወተ ፡ ኀይለ ፡ ሥጋ ፡ ብሎ ፥ ትወግዕ ፡ በማለት ፡ ማሰሪያ ፡ ማትረፉን ፥ ጥዑመ ፡ በማለት ፡ ቅጽልን ፥ ሐሊበ ፡ እግዚእን ፡ በማለት ፡ ተናባቢን ፥ ሥጋዌ ፡ ወተትን ፡ በማለት ፡ አፈታትን ፥ በይነ ፡ ዘአእመረት ፡ በማለት ፡ አንቀጽን ፥ ለደቂቃ ፡ በማለት ፡ ዝርዝር ፡ ማትረፉን ፡ ያሳያል ።

፻፹፬ ፤ ባለቤትና ፡ ዘርፍ ፡ በሠምና ፡ በወርቅ ፡ አካኼድ ፡ ሲነገሩ ፡ ብዙ ፡ ስም ፡ አላቸው ፡ አስቀድመን ፡ በ፲፯ኛ ፡ ዕርከን ፡ እንደ ፡ ተናገርን ፡ (ቍ፹፰) ። የሠም ፡ ባለቤት ፡ ከወርቅ ፡ ዘርፍ ፡ ተናበ ፡ የወርቅን ፡ ባለቤት ፡ ሲያመጣ ፡ ውስጠ ፡ ወይራ ፡ ያሰኛል ። ይህም ፡ ነዳያን ፡ አሕዛብ ፡ በልዑ ፡ ኅብስተ ፡ ጴጥሮስ ፡ ባዕል ፡ ባለ ፡ ጊዜ ፡ ሃይማኖተ ፡ ጴጥሮስ ፡ ማለቱን ፡ ያሳያል ። ስሙም ፡ ክብ ፡ ውስጠ ፡ ወይራ ፡ ይባላል ፤ የሠሙ ፡ ዘርፍ ፡ ባዕል ፡ ሲቀር ፡ ግን ፡ ክብ ፡ አይባልም ። ፪ኛም ፡ የወርቅ ፡ ባለቤት ፡ እየቀደመ ፡ የሠም ፡ ባለቤት ፡ ተከትሎ ፡ ከወርቅ ፡ ዘርፍ ፡ ሲናበብ ፡ ዝምድ ፡ ያሰኛል ። ይህም ፡ ተበልዐ ፡ ሃይማኖት ፡ ኅብስተ ፡ ጴጥሮስ ፡ ባዕል ፡ ማለቱን ፡ ያሳያል ። ስሙም ፡ ድርብ ፡ ዝምድ ፡ ይባላል ፤ ባዕል ፡ ሲቀር ፡ ግን ፡ ነጠላ ፡ ዝምድ ፥ ወይም ፡ ቅጽል ፡ ከምሳሌ ፡ ያሰኛል ። ፫ኛም ፡ የሠም ፡ ባለቤት ፡ ከወርቅ ፡ ዘርፍ ፡ ተናበ ፡ እየቀደመ ፡ የወርቅ ፡ ባለቤት ፡ ሲከተል ፡ ፍላጻ ፡ ይባላል ። ይህም ፡ ተበልዐ ፡ ኅብስተ ፡ ጴጥሮስ ፡ ባዕል ፡ ሃይማኖት ፡ ሲል ፡ ድርብ ፡ ፍላጻ ፤ የሠሙ ፡ ዘርፍ ፡ ባዕል ፡ ሲቀር ፡ ነጠላ ፡ ፍላጻ ፡ ይባላል ። ፬ኛም ፡ የሠም ፡ ባለቤት ፡ በወርቅ ፡ ባለቤት ፡ ላይ ፡ በሚናበብበት ፡ ጊዜ ፡ በወርቅ ፡ ባለቤት ፡ ሲጠበቅ ፡ ጥምዝ ፡ ይባላል ። ይህም ፡ በልዐ ፡ ኅብስተ ፡ ዘጴጥሮስ ፡ ሃይማኖት ፡ ባለ ፡ ጊዜ ፡ ጥምዝ ነቱን ፡ ያሳያል ። ፭ኛም ፡ ዘርፍ ፡ በዘና ፡ በለ ፡ ሲደፋ ፡ ስሙ ፡ ድፋት ፡ ይባላል ። ይህም ፡

በልዐ ፡ ዘጴጥሮስ ፡ በዕል ፡ ሃይማኖተ ፡ ኅብስተ ፡ ሲል ፡ የዘ ፡ ድርብ ፡ ድፋት ፤ በዕል ፡ ሲቀር ፡ ነጠላ ፡ ድፋት ፡ መኾኑን ፡ ያሳያል ። ዳግመኛም ፡ በልዐ ፡ ለጴጥሮስ ፡ በዕል ፡ ጥዑመ ፡ ሃይማኖተ ፡ ኅብስቶ ፡ ጊዮርጊስ ፡ ርኁብ ፡ ሲል ፡ የለ ፡ ድርብ ፡ ድፋት ፤ በዕል ፡ ሲቀር ፡ ነጠላ ፡ ድፋት ፡ ይባላል ። ፯ኛም ፡ በልዐ ፡ ወይም ፡ ተበልዐ ፡ ሃይማኖተ ፡ ጴጥሮስ ፡ ኅብስተ ፡ በዕል ፡ ተብሎ ፡ በየገንዘቡ ፡ ሲነገር ፡ ተቻቻይ ፡ ይባላል ።

፻፷፰ ፤ ብሂልም ፡ በሰዋስውነቱ ፡ ዘርፍና ፡ ምሳሌ ፡ ይኾናል ፤ ከዘርፍም ፡ ሲያገዝ ፡ ለብሂል ፡ ለ ፡ የለው ፡ ለብሂሎት ፡ ዘ ፡ የለው ፡ ይባላል ። ዘርፍ ፡ ሲኾን ፡ ዝምድ ÷ ፍላጻ ÷ ድፋት ÷ ጥምዝ ÷ ክብ ፡ ውስጠ ፡ ወይራ ÷ ምፀት ÷ ሠረዝ ÷ ተራ ፡ ምሳሌ ፡ ይኾናል ። ዝምድ ፡ ሲኾን ÷ ምሕረት ፡ ወርቀ ፡ ብሂል ፡ አድኅን ፡ ነዌ ፡ ለእግዚእ ፡ ላዕለ ፡ ኵሉ ፡ ንዋዩ ። ፍላጻ ፡ ሲኾን ÷ ወይነ ፡ ብሂል ፡ ለብሰ ፡ ሥጋ ፡ ማርያም ፡ ወልደ ፡ አብ ፡ መዐዛ ፡ ሃይማኖት ፡ ሰትየ ፡ ቌርሎስ ፡ ንጉሥ ። ድፋት ፡ ሲኾን ÷ ዘብሂል ፡ ተወልደ ፡ አምላክ ፡ ወጴጥሮስ ፡ ተሰቅለ ፡ ቍልቍሊተ ፡ ምስጢረ ፡ ቤተ ፡ ሐነጽኩ ። ጥምዝ ፡ በትረ ፡ ዘብሂል ፡ አጽንዕ ፡ ሕገ ፡ አ ፡ ሰብእ ፡ ለአድኅኖ ፡ ነፍስከ ፡ ወንጌል ፡ ጳውሎስ ፡ ኖላዊ ፡ ነሥአ ፡ በእደ ፡ ጉባኤ ። ያልተከበበ ፡ ውስጠ ፡ ወይራ ፡ ሲኾን ÷ መሶበ ፡ ብሂል ፡ እትወለድ ፡ እምወለተ ፡ ወለትከ ፡ ሰፈየት ፡ ድንግል ፡ መርዓተ ፡ ሙሴ ፡ አ ፡ አዳም ። ክብ ፡ ሲኾን ÷ በግዐ ፡ ብሂል ፡ ተወልደ ፡ አምላክ ፡ እምነ ፡ ማርያም ፡ በዕል ፡ በልዐ ፡ ዕጕለ ፡ አርዌ ፡ ንስጥሮስ ። ምፀት ÷ ብሂል ፡ እድግት ፡ አውዕአት ፡ ቀርነ ÷ ብሂል ፡ ተናገረት ፡ እብን ፡ ነገረ ። ረሠዝ ÷ ብሂል ፡ ተሰቅለ ፡ እግዚእ ፡ ላዕለ ፡ ጽሒፎተ ፡ ቀይሕ ፡ ቀለም ፡ ወብሂል ፡ ተሰቅለ ፡ ጴጥሮስ ፡ ታሕተ ፡ ተርጕሞተ ፡ ሃይማኖተ ፡ አበው ፡ ይደልዎሙ ፡ ለሐዋርያት ፡ ሊቃውንት ፤ የዋዌ ፡ ሠረዝ ፡ ነው ። ተራ ፡ ምሳሌም ፡ ሲኾን ÷ ወርቀ ፡ ብሂል ፡ ሞተ ፡ እግዚእ ፡ በእንተ ፡ ፍቅረ ፡ ሰብእ ፡ ዘገበ ፡ ጊዮርጊስ ፡ በዕል ፡ ይላል ። ከዚህ ፡ የቀረው ፡ የብሂል ፡ ጓዝ ፡ አንቀጽነቱና ፡ አገባብነቱ ፡ በቦታው ፡ ተነግሯል ፡(ቍ ፫፻፫) ።

፻፷፱ ፤ የምሳሌ ፡ ዐዋጅ ። ሩቅና ፡ ቅርብ ÷ አንድና ፡ ብዙ ÷ ወንድና ፡ ሴት ፡ አይመስሉም ፤ ይኸውም ፡ በማሰሪያ ፡ በንቀጽ ፡ በቅጽል ፡ ኅብረትና ፡ አንድነት ፡ የላቸውምና ፡ ስለዚህ ፡ ነው ። ይህም ÷ ብህለ ፡ ብህልከ ÷ ተብህለ ፡ ተብህሉ ÷ አብህለት ÷ በሃሊ ፡ በሃሊት ፡ በማለት ፡ ይታያል ። ፪ኛም ፡ ወ ፡ አንድ ፡ ያደረጋቸው ፡ ኹለት ፡ ስሞች ፡ ሠም ፡ ኹነው ÷ ወርቅም ፡ ኹነው ፡ ከስም ፡ ተዛምደው ፡ አይመስሉም ። ይህም ፡ ርኁብ ፡ ወነዳይ ፡ አሕዛብ ፡ በልዑ ፡ ኅብስተ ፡ ሃይማኖት ፡ አለማለት ፡ ነው ። ፫ኛም ፡ ነባቢና ፡ ኢነባቢ ÷ የተጸውዖ ፡ ስምና ፡ ስም ÷ ስምና ፡ ግብር ፡ ኀዳሪና ፡ ማኅደር ÷ አንድና ፡ ብዙ ÷ ወንድና ፡ ሴት ÷ እነዚህ ፡ ፯ቱ ፡ ተናበው ፡ አይመሰሉም ። ቅርብና ፡ ሩቅ ፡ ግን ፡ ተናበ ፡ ሲመሰል ÷ ተበላዕከ ፡ ኅብስተ ፡ ሃይማኖት ፡ ዘረትዐ ፡ ሲል ÷ የሠሙ ፡ አቅራቢ ፡ ለወርቁ ፡ ተርፎ ፡ ቅጽሉን ፡ ዘረታዕከ ፡ ያሰኛልና ፤ ጸያፍ ፡ አይባልም ። ይህም ÷ ዘተወልደ ፡ ዘተጠምቀ ፡ ዘተንሥአ ፡ ብሎ ፡ ተሣህለነ ፡ እግዚአ ፡ በለው ፡ ይታወቃል ፤ የግልጠ ፡ ዘ ፡ ጠባይ ፡ ይህ ፡ ነው ። ውስጠ ፡ ዘም ፡ ቢኾን ፡ ከቅርብና ፡ ከሩቅ ፡ ይሰማማል ፤ ባላገባቦች ፡ ግን ፡ እንደ ፡ ላይኛው ፡ መስሏቸው ፡ በልማድ ፡ ዐዋጅ ፡ ጸያፍ ፡ ነው ፡

ይሉታል ። ነባቢና ፡ ኢነባቢ ፣ ካህን ፡ እብን ፡ ቀዳሲ ። ስምና ፡ ስም ፣ ዳዊት ፡ ሚካኤል ። ስምና ፡ ግብር ፣ ሰሎሞን ፡ ጥበብ ። ኀዳሪና ፡ ማኅደር ፣ ወርቀ ፡ መዝገብ ፣ ወይም ፡ ኅብ ስተ ፡ መሶብ ፡ ብሎ ፡ አለመመሰል ፡ ነው ። ከ፮ቱ ፡ ደግሞ ፡ ፫ቱ ፡ ፊተኞች ፡ ሲቀሩ ፡ ፫ቱ ፡ ኋለኞች ፡ በውስጠ ፡ ወይራነት ፡ ሠም ፡ ለበስ ፡ ኹነው ፡ ሲነገሩ ፡ ከውስጣቸው ፡ ጥሩ ፡ ወርቅ ፡ ይወጣል ። ኀዳሪና ፡ ማኅደር ፣ ግሩም ፡ ውእቱ ፡ አንበሳ ፡ ገዳም ፡ በኀበ ፡ አራ ዊት ፡ ሰብእ ፡ ብሎ ፣ ባሕታዊ ፡ ገዳም ። አንድና ፡ ብዙ ፣ አዋልደ ፡ ጊዮርጊስ ፡ ብሎ ፡ ሐዋሳተ ፡ ጊዮርጊስ ። ወንድና ፡ ሴት ፣ ብእሲተ ፡ ጊዮርጊስ ፡ ወለደት ፡ ሠለስተ ፡ ብሎ ፡ ክሣደ ፡ ጊዮርጊስ ፡ አውሐዘት ፡ ደመ ፡ ወማየ ፡ ወሐሊበ ፡ ማለት ፡ ነው ። ዳግመኛም ፡ ዘርፍ ፡ ከዘርፍ ፡ ሳይማሰል ፡ ወንድና ፡ ሴት ፡ አንድና ፡ ብዙ ፡ ያናግራል ። ይህም ፣ እደ ፡ ሐዋን ፡ ደሙ ፡ ለዐማኑኤል ፡ መተረ ፡ ፍዳ ፡ ኀጢአታ ፡ ለሔዋን ፡ በለሰ ፡ ገነት ። ትም ህርተ ፡ ሐዋርያት ፡ መቅደሱ ፡ ለሰሎሞን ፡ ተሐንጸት ፡ በወርቅ ፡ አርእዮተ ፡ መንክር ። ምሳሌም ፡ ከንቀጽ ፡ ወዲህ ፡ እንጂ ፡ ከንቀጽ ፡ ወዲያ ፡ የለም ፤ ዝናም ፡ መጽአ ፡ ሆሳዕና ፡ ቢል ፡ ፍርቅ ፡ ይባላል ። ከዚህ ፡ የቀረውን ፡ የሠምና ፡ የወርቅ ፡ አከኼድ ፣ የቅኔ ፡ ጐዳና ፣ የንባቡን ፡ አሰካክና ፡ መልክ ፡ ከነስሙ ፡ መጽሐፍ ፡ በሚባለው ፡ በታላቁ ፡ አገባብ ፡ ተመልከት ፡ (ገጽ ፡ ፻፶፰—፻፶፲) ።

## ፳፫ኛ ፡ ዕርከን ።

## ብትን ፡ ሰዋስው ።

### የደቂቅ ፡ አገባብ ፡ አንጻሮች ፣ ወይም ፡ ውስጠ ፡ ወይሮች ።

ብትን ፡ ሰዋስው ፡ ማለት ፣ ፯ ፡ ቅንጣት ፡ ጥሬ ፣ ወይም ፡ ፯ ፡ ዐይነት ፡ ፍሬ ፡ ማለት ፡ ነው ፤ ውጥንቅጥ ፡ እንደ ፡ ማለት ። እነዚሁም ፡ ቦታና ፡ ጊዜ ፣ ባሕርይና ፡ አካል ፣ ስምና ፡ ግብር ፣ ነገር ፡ ናቸው ። ብትን ፡ ሰዋስውም ፡ ያሰኛቸው ፣ አገባብ ፡ ሳይዙ ፡ ብቻ ፡ ብቻ ቸውን ፡ ተነግረው ፡ ባፈታታቸው ፡ አገባብ ፡ ማምጣት ፡ ነው ።

፪፳፯፤ መድረሻቸው ፡ በዝርዝርነት ፡ በነባርነት ፡ ግእዝ ፡ ራብዕ ፡ ኃምስ ፡ ሳብዕ ፡ ሲኾን ፡ በልማዳዊ ፡ ዐማርኛው ፣ በ፫ ፡ አናቅጽ ፡ ዐማርኛና ፡ በ፰ ፡ አገባብ ፡ ዐማርኛ ፡ ይ ፈታል ። ልማዳዊ ፡ ዐማርኛው ፡ ን ፡ ነው ፤ ፫ቱም ፡ አናቅጽ ፣ ገብረ ፡ መሰለ ፡ ብህለ ፡ ና ቸው ። ዐማርኛቸውም ፣ ኹኖ ፡ አድርጎ ፡ ፩ ፡ ወገን ፤ መስሎ ፡ አስመስሎ ፡ ፩ ፡ ወገን ፤ ብሎ ፡ ተብሎ ፡ አሰኝቶ ፡ ተባብሎ ፡ አባብሎ ፡ ፩ ፡ ወገን ፡ ነው ። ኹኖ ፡ መስሎ ፡ ተብሎ ፡ ተባብሎ ፡ በ፰ ፡ አርእስት ፡ ያሳስራሉ ። አድርጎ ፡ አስመስሎ ፡ ብሎ ፡ አባብሎ ፡ በ፫ ፡ አ ርእስት ፣ አሰኝቶም ፡ በራሱ ፡ ያሳስራሉ ። ያ፰ቱ ፡ አገባብ ፡ ዐማርኛ ፡ በ ፡ ከ ፡ ወደ ፡ ጋራ ፡ ለ ፡ ነው ። ን ፡ ሲኾን ፣ ጼሐ ፡ ፍኖተ ፤ ተከለ ፡ ደብተራ ፤ ቀሠመ ፡ ጽጌ ፤ አኀዘ ፡ መርኖ ፡ ይላል ። በ ፡ ሲኾን ፡ በኹሉ ፡ ይገባል ፤ ወደ ፡ ሲኾን ፡ በቦታ ፡ ብቻ ፡ ነው ። ማሰ ሪያዎቹም ፣ ቦአ ፡ ወፅአ ፣ ሖረ ፡ መጽአ ፣ ተመይጠ ፡ ገብአ ፣ ዐርገ ፡ ወረደ ፣ ተፈነወ ፡ ነ ገደ ፣ በጽሐ ፡ ተሰደ ፣ እነዚህን ፡ የመሰሉ ፡ ናቸው ፤ ሲገባም ፣ ዐርገ ፡ ሐመረ ፡ ወረደ ፡ ምድረ ፡ ጐየ ፡ ግብጸ ፡ ተመይጠ ፡ ናዝሬተ ፡ ወገሊላ ። ሰፍያ ፡ ንግሥት ፡ ነገደት ፡ ሮሜ ፣

ወበጺሓ ፡ ሮሜ ፡ ሖረት ፡ ተሰሎንቄ ፥ ወእምህየ ፡ ገብአት ፡ ደማስቆ ፡ ያሰኛል ። ባለቦታ ውንም ፡ ፈልጎ ፡ በተጸውዖ ፡ ስም ፡ ሲገባ ፥ ግእዝ ፡ ወራሽ ፡ ቀለም ፡ ይፈልጋል ፤ እነዚ ሁም ፡ ሀ ፡ ሃ ፡ ናቸው ፥ ግእዙ ፡ የወንድ ፡ ራብዑ ፡ የሴት ። ፈነወ ፡ ኪራም ፡ አግብርቲሁ ፡ ሰሎሞንሀ ። ተፈነወ ፡ ገብርኤል ፡ መልአክ ፡ ማርያምሃ ፡ እያሰኘ ፡ ኀበ ፡ በገባበት ፡ ይ ገባል ።

፻፳፰ ። ግብር ፡ ነገር ፡ በዝርዝርነት ፡ በነባርነት ፡ ግእዝ ፡ ራብዕ ፡ ኃምስ ፡ ሳብዕ ፡ ሲኾኑ ፡ በ ፡ ይኾናሉ ። በ፮ ፡ ግሶች ፡ ያሳስራሉ ፤ ግሶቹም ፡ ንእሰ ፡ ዐብየ ፡ ዐረየ ፡ ቀደመ ፡ ኀብረ ፡ ሰክረ ፡ ናቸው ። ግብር ፡ በ ፡ ሲኾን ፥ ኢትስክሩ ፡ ወይነ ፤ በወይን ። ንእሰ ፡ ክብረ ፡ ይሁዳ ፡ ዐብየ ፡ ማትያስ ፡ እምይሁዳ ፡ ክብረ ፤ በክብር ። እምከመ ፡ ዐረይነ ፡ ሕማመ ፡ ንዔሪ ፡ ክብረ ፡ ምስሌሁ ፤ በመከራ ፡ በክብር ። ቀደመ ፡ አሳሄል ፡ ሩጻተ ፡ እምአብያጺሁ ፤ በሩጫ ። ነገር ፡ በ ፡ ሲኾን ፡ ኀበሩ ፡ ቃለ ፡ ነቢያት ። ኀብሩ ፡ ምክረ ፡ ወሃይማኖተ ፥ አው ፡ አሚነ ፡ ብሎ ፡ በምክር ፡ በሃይማኖት ፡ ያሰኛል ። ቦታ ፡ ግን ፡ በ ፡ ሲኾን ፡ ሀሎ ፡ ኮነ ፡ ነበረ ፥ እነዚህን ፡ በመሰሉ ፡ ግሶች ፡ ያሳስራል ። ሀሎ ፡ ገዳመ ፡ አው ፡ ቤተ ፤ ነበረ ፡ ላዕለ ፡ አው ፡ ታሕተ ፤ በዱር ፡ በቤት ፥ በላይ ፡ በታች ።

፻፳፱ ፤ ጊዜም ፡ በ ፡ ሲኾን ፡ ለቦታ ፡ በሚስማሙ ፡ አናቅጽ ፡ ያሳስራል ። ይህም ፥ ሌሊተ ፡ ቦኡ ፡ ወሌሊተ ፡ ወፅኡ ። መዓልተ ፡ ወሌሊተ ፡ ዕቀበነ ፡ አንተ ። ተሰቅለ ፡ ቀትረ ፥ ወወረደ ፡ ሠርከ ፡ እያሰኘ ፥ በመዓልትና ፡ በሌሊት ፥ በቀትር ፡ በሠርክ ፡ ማለ ቱን ፡ ያሳያል ። አኃዝ ፡ ቅጽል ፡ ሲጨመርበት ፡ ግን ፡ በ ፡ ወይም ፡ ን ፡ ተብሎ ፡ መፈ ታት ፡ የለውም ፤ ዐማርኛው ፡ በአኃዝ ፡ ይበዘበዛል ። ይህም ፡ ነበረ ፡ ሠሉሰ ፡ መዋዕለ ፡ ወሠሉሰ ፡ ለያልየ ። ሰዱሰ ፡ ዕለተ ፡ ተገበር ፡ ግብረከ ። ጾመ ፡ አርብዓ ፡ መዓልተ ፡ ወአ ርብዓ ፡ ሌሊተ ፡ በለው ፡ ይታወቃል ።

፻፴ ፤ ግብር ፡ ነገር ፡ ባሕርይ ፡ አካል ፥ ግእዝና ፡ ራብዕ ፡ ኃምስ ፡ ሳብዕ ፡ ኹነው ፡ ሲነገሩ ፡ ከ ፡ ይኾናሉ ። የሚስቧቸውም ፡ አናቅጽ ፡ ርኅበ ፡ ጸምአ ፡ ነድየ ፥ ተዐርቀ ፡ ጾመ ፡ ዐብየ ፡ ንእሰ ፥ እነዚህን ፡ የመሰሉ ፡ ናቸው ። ግብር ፥ ከ ፡ ሲኾን ፥ ተዐርቀ ፡ ልብሰ ፤ ርኅበ ፡ ኅብስተ ፤ ጾመ ፡ መብልዐ ፡ ብሎ ፥ ከልብስ ፡ ከንጀራ ፡ ከመብል ፡ ያሰኛል ። ነገርም ፡ ከ ፡ ሲኾን ፥ ተከልአ ፡ ውዴተ ፡ ወሐሜተ ፥ ከሰብቅ ፡ ከሐሜት ። ባሕርይ ፡ ከ ፡ ሲኾን ፥ ጸምአ ፡ ማየ ፥ ነድየ ፡ ወርቀ ፥ በደረ ፡ ልሂቀ ፤ ከውሃ ፡ ከወርቅ ፡ ከልሂቅ ። አካልም ፡ ከ ፡ ሲኾን ፥ ዐብየ ፡ መልአከ ፡ በኀይል ፡ ሰብአ ፤ ንእሰ ፡ ሰብእ ፡ በኀይል ፡ መልአከ ፡ ያሰኛል ፤ ኹሉንም ፡ ከ ፡ ብለኽ ፡ ፍታ ።

፻፴፩ ፤ ብትን ፡ ሰዋስው ፡ ኹሉ ፡ በዝርዝርነት ፡ በነባርነት ፥ ግእዝ ፡ ራብዕ ፡ ኃምስ ፡ ሳብዕ ፡ ሲኾን ፡ ጋራ ፡ እንደ ፡ ይኾናል ። ጋራ ፡ ሲኾን ፡ በመደራረግ ፡ በማደራረግ ፡ ያሳስ ራል ። በመደራረግ ፡ ተማከረ ፡ ሰብአ ፡ ባለ ፡ ጊዜ ፡ ከሰው ፡ ጋራ ፡ ተማከረ ፡ ያሰኛል ። በማ ደራረግም ፡ ጊዜ ፡ አስተማከረ ፡ ሰብአ ፡ በል ። ብትን ፡ ሰዋስው ፡ እንደ ፡ ሲኾን ፡ በዘፈቀደ ፡ ግስ ፡ ያሳስራል ። ተቀሥፈ ፡ እግዚእነ ፡ ሰራቂ ፥ ወተሰቅለ ፡ እቡሰ ፤ እንደ ፡ ሌባ ፡ እንደ ፡ በደለኛ ። ኹኖም ፡ ሲኾን ፥ አምላክ ፡ ሞተ ፡ ሰብአ ፤ ሰው ፡ ኹኖ ። አድርጎም ፡ ሲኾን ፥ አስተየ ፡ ማየ ፡ ወይነ ፤ ውሃውን ፡ ወይን ፡ አድርጎ ። መስሎም ፡ ሲኾን ፥ አስተርአየ ፡

ሰይጣን ፡ ሰብአ ። አስመስሎም ፡ ሲኾን ፥ ይውህብ ፡ ሰይጣን ፡ እብነ ፡ ወርቀ ፥ አው ፡ ኅብ ስተ ፡ ይላል ። ተብሎም ፡ ሲኾን ፥ ተሰቅለ ፡ ክርስቶስ ፡ ኃጥአ ። ብሎም ፡ ሲኾን ፥ ሰቀ ልዎ ፡ አይሁድ ፡ ለክርስቶስ ፡ ኃጥአ ። አሰኝቶም ፡ ሲኾን ፥ አስቀሎሙ ፡ ሰይጣን ፡ ለአ ይሁድ ፡ ክርስቶስሀ ፡ ኃጥአ ። ተባብሎም ፡ ሲኾን ፥ ተቃጸበ ፡ ሄሮድስ ፡ ምስለ ፡ ወፀልቱ ፡ ላዕለ ፡ ክርስቶስ ፡ ዐላዌ ። አባብሎም ፡ ሲኾን ፥ መስተዋድይ ፡ ያስተፃርፍ ፡ ጻድቃነ ፡ ሐሳዌ ፡ ያሰኛል ።

፻፴፱ ፤ ብትን ፡ ሰዋስው ፡ ለ ፡ ሲኾን ፥ ተቀባይነት ፡ በሚሰማማው ፡ ጥሬ ፡ ይገ ባል ። ይህም ፥ ዘይትቀነይ ፡ ወፍረ ፡ ተኀርየ ፡ ሢመተ ፡ ብሎ ፥ ለርሻ ፡ የሚገዛ ፡ ለሹ መት ፡ ተመረጠ ። ወይምህክ ፡ ነዳየ ፡ ወምስኪነ ፡ ብሎ ፥ ለድኻ ፡ ለጦም ፡ ዐዳሪ ፡ ይራ ራል ። ኢያንእስ ፡ እንዘ ፡ ይፌትት ፡ ርእሰ ፡ ብሎ ፥ ለራሱ ፡ ሲቈርስ ፡ አያሳንስ ፡ እያሰኘ ፡ ተቀባይነቱን ፡ ያሳያል ። በተቀብዖ ፡ ስም ፡ ሲገባ ፡ ፍችው ፡ ና ፡ ነት ፡ ይኾናል ። ተሰ ይመ ፡ ጳጳሰ ፥ አው ፡ ቀሲሰ ፡ ወዲያቆነ ፤ ጵጵስና ፡ ቅስና ፡ ዲቁና ፤ ወይም ፡ ጳጳስነት ፡ ቄስ ነት ፡ ዲያቆንነት ። በግእዝም ፡ ቋንቋ ፡ የጥሬው ፡ መድረሻ ፡ ና ፡ ሲኾን ፡ እንዲሁ ፡ ይፈ ታል ፤ ንጽሕና ፡ ቅድስና ፥ ንጹሕነት ፡ ቅዱስነት ፤ የመሰለው ፡ ኹሉ ።

፻፴፲ ፤ ብትን ፡ ሰዋስው ፡ በዝርዝርነት ፡ በነባርነት ፡ ግእዝ ፡ ራብዕ ፡ ኃምስ ፡ ሳ ብዕ ፡ ኹኖ ፡ በስመ ፡ ነገድ ፡ እየገባ ፡ ኛ ፡ ሲኾን ፡ ቋንቋ ፡ ያሰማል ። ተአምርኑ ፡ ዐረበ ፡ ወዐምሐራ ፥ ዐረብኛና ፡ ዐማርኛ ፤ አው ፡ ጋላ ፡ ወሱማሌ ፥ ጋልኛና ፡ ሱማልኛ ፤ ወዓዲ ፡ ወላሞ ፡ ወላምኛም ፡ ደግሞ ። ይነቁ ፡ አብድ ፡ ዝእበ ፥ አው ፡ አድገ ፤ ዥብኛ ፡ አህይኛ ። ምስጢሩም ፡ አንጻርነት ፡ ኹኖ ፡ እንደ ፡ ከማለት ፡ ይገባል ። የብትን ፡ ሰዋስው ፡ ዐዋጅ ፡ በጭሩ ፡ ይህ ፡ ነው ።

## ፳፬ኛ ፡ ዕርከን ።

## ሙሻዘር ።

፻፴፩ ፤ ሙሻዘር ፡ ማለት ፡ በማርኛ ፡ መጣብቅ ፡ ይኾናል ፤ በሰዋስው ፡ ግን ፡ ተናበ ፡ የሚስብና ፡ ደቂቅ ፡ አገባብ ፡ የሚያመጣ ፥ ተናባቢ ፡ ዘር ፡ ማለት ፡ ነው ። ሙሻዘሮችም ፡ የሚባሉ ፡ ፬ ፡ ናቸው ፤ ሳድስ ፡ ቅጽልና ፡ ሣልስ ፡ ቅጽል ፥ አርእስትና ፡ ሳቢ ፡ ዘር ። የሳ ድስና ፡ የሣልስ ፡ ውስጠ ፡ ዘ ፡ ባዕድ ፡ ቅጽልነት ፥ ተናበውም ፡ ገቢር ፡ ተገብሮ ፡ መሳበ ቸው ፡ ከግልጠ ፡ ዘ ፡ ጋራ ፡ በበታው ፡ ተነግሯል ፡ (ምፀ ፡ ቍ፴፰) ። አኹን ፡ ግን ፡ በዚህ ፡ ክፍል ፡ ከርእስትና ፡ ከሳቢ ፡ ዘር ፡ ጋራ ፡ ሙሻዘር ፡ ያልናቸው ፥ ከብትን ፡ ሰዋስው ፡ ተ ናበው ፡ በባዕድ ፡ ግልጠ ፡ ዘ ፡ የተነገሩትን ፡ ፱ ፡ አገባቦች ፡ የሚያመጡ ፡ ስለ ፡ ኾኑ ፡ ነው ፤ ሙሻዘርም ፡ ኹነው ፡ ሲነገሩ ፡ ቅጽልነታቸው ፡ አይቀርም ።

፻፴፰ ፤ ሳድስ ፡ ቅጽል ፡ ተናበ ፡ ፱ኙን ፡ አገባብ ፡ ሲያመጣ ። ክርስቶስ ፡ ምዉተ ፡ አዳም ፡ በለ ፡ ጊዜ ፥ ለአዳም ፡ ስለ ፡ አዳም ፡ የሞተ ። ስቁለ ፡ ፈያት ፡ ሲል ፡ ከወንበዶች ፡ ጋራ ፥ እንደ ፡ ወንበዶች ፡ ማለት ፡ ነው ። ገብርኤል ፡ ፍንወ ፡ ማርያም ፡ ሲል ፥ እስከ ፡ ማ ርያም ፥ ወደ ፡ ማርያም ፡ የተላከ ። ሰሎሞን ፡ ንጉሠ ፡ ዳዊት ፡ ሲል ፥ የዳዊትን ፡ ያኽል ፤

የነገሠ ። አዳም ፡ ፍጡረ ፡ መሬት ፡ ሲል ፥ ከመሬት ፡ የተፈጠረ ። ኢየሱስ ፡ ስቁለ ፡ ዕፅ ፡ ወቅንወ ፡ ኀጺን ፤ በንጨት ፡ የተሰቀለ ፥ በብረት ፡ የተቸነከረ ። ፪ኛም ፡ ያሉታ ፡ አገባብ ፡ ኢ ፡ ወድቆበት ፡ የነዚህን ፡ አፍራሽ ፡ ሲያመጣ ፡ ፍችው ፡ አለ ፡ ያለ ፡ ይኾናል ። ክርስቶስ ፡ ኢምዉት ፡ አዳም ፥ አላዳም ፡ ያላዳም ፡ ያልሞተ ። ኢስቁለ ፡ ፈያት ፥ ያለወንበዶች ፡ ያልተሰቀለ ። ገብርኤል ፡ ኢፍንወ ፡ ማርያም ፥ ያለማርያም ፡ ያልተላከ ። ሰሎሞን ፡ ኢንጉሠ ፡ ዳዊት ፥ ያለዳዊት ፡ መጠን ፡ ያልነገሠ ። አዳም ፡ ኢፍጡረ ፡ መሬት ፥ ያለመሬት ፡ ያልተፈጠረ ። ኢየሱስ ፡ ኢስቁለ ፡ ዕፅ ፡ ወኢቅንወ ፡ ኀጺን ፤ ያለንጨት ፡ ያልተሰቀለ ፡ ያለብረት ፡ ያልተቸነከረ ። እንበለ ፡ ከኢ ፡ ተሰማምቶ ፡ የ፱ኙ ፡ ኹሉ ፡ አሉታና ፡ አፍራሽ ፡ እንደ ፡ ኾነ ፡ አስተውል ። ፱ ፡ ያልናቸውም ፡ እሊህ ፡ ናቸው ፤ ለ ፡ በእንተ ፡ ከመ ፡ ምስለ ፡ ኀበ ፡ እስከ ፡ መጠነ ፡ እም ፡ በ ።

፻፵፮ ፤ ዳግመኛም ፡ የ፮ቱ ፡ አዕማድ ፡ ሣልስ ፡ ቅጽል ፡ ከብትን ፡ ተናቦ ፡ እሊህን ፡ ፱ኙን ፡ ሲያመጣ ፡ አገባቡ ፡ እንዲህ ፡ ነው ። የገቢር ፡ ሣልስ ፡ ለንና ፡ በእንተን ፡ ሲያመጣ ፥ አብ ፡ መጣዌ ፡ ዓለም ፡ ወልዶ ፡ ከመ ፡ ይኩን ፡ ቤዛ ። ከመንና ፡ ምስለን ፡ ሲያ ፥ ጲላጦስ ፡ ቀሣፌ ፡ ሰረቅት ፡ ወሰቃሌ ፡ ፈያት ፡ ክርስቶስሀ ። ኀበንና ፡ እስከን ፡ ሲያ ፥ አብ ፡ ፈናዌ ፡ ማርያም ፡ ገብርኤልሀ ። መጠነን ፡ ሲያ ፥ ሳሙኤል ፡ ቀባዒ ፡ ሳኦል ፡ ዳዊትሀ ፡ ወአንጋሢሁ ፤ ዳዊትን ፡ በሳኦል ፡ መጠን ፡ የቀባውና ፡ ያነገሠው ። እምንና ፡ በን ፡ ሲያ ፥ ወልድ ፡ ፈናዌ ፡ ሰማይ ፡ መንፈሶ ፡ ወከዓዌ ፡ አርድእት ፡ ሞገሶ ፤ ወይም ፡ ፈጣሬ ፡ መሬት ፡ አዳምሀ ፡ ወሠያሜ ፡ ገነት ፡ ኪያሁ ፡ ያሰኛል ።

፻፵፯ ፤ የአግብሮ ፡ ሣልስ ፡ ለንና ፡ በእንተን ፡ ሲያመጣ ፥ መሐላ ፡ ውእቱ ፡ አቅታሌ ፡ አዳም ፡ ወሔዋን ፡ ክርስቶስሀ ። ከመንና ፡ ምስለን ፡ ሲያ ፥ ሕገ ፡ ሮም ፡ አቅሣፌ ፡ ሰረቅት ፡ ወአስቃሌ ፡ ፈያት ፡ ክርስቶስሀ ። ኀበንና ፡ እስከን ፡ ሲያ ፥ ምስጢረ ፡ ሥጋዌ ፡ አፈናዌ ፡ ድንግል ፡ መልአከ ፡ እምኀበ ፡ አብ ። መጠነን ፡ ሲያ ፥ መዓልት ፡ አምጻኤ ፡ ጽልመት ፡ ብርሃነ ፤ ወሌሊት ፡ አምጻኤ ፡ ብርሃን ፡ ጽልመተ ። እምንና ፡ በን ፡ ሲያ ፥ ርቱዕ ፡ ጥቀ ፡ ፍትሐ ፡ ፈጣሪ ፡ አጸዋዒ ፡ ቤቱ ፡ ለሳኦል ፡ አጋግሀ ፡ ኀበ ፡ ሳሙኤል ፡ ወአቅታሌ ፡ ኩናት ፡ ኪያሁ ፡ በእደ ፡ ነቢይ ። ለና ፡ በእንተ ፥ ከመና ፡ መጠነ ፡ ምስለ ፡ በምስጢር ፡ አንዳንድ ፡ ወገን ፡ ናቸው ።

፻፵፰ ፤ ያደራራጊ ፡ ሣልስ ፡ ለንና ፡ በእንተን ፡ ሲያመጣ ፥ አብ ፡ አስተጻባኤ ፡ አዳም ፡ ወልዶ ፡ መድኀኒ ፡ ምስለ ፡ መልአከ ፡ ሞት ፥ ኄር ፡ ውእቱ ። ከመንና ፡ መጠነን ፡ ሲያ ፥ በቀለ ፡ ዳዊት ፡ አስተቃታሌ ፡ ኢዮአብ ፡ ሰሎሞንሀ ፡ ምስለ ፡ ሳሚ ። ምስለንና ፡ በን ፡ ሲያ ፥ ወላዲተ ፡ አምላክ ፡ ይእቲ ፡ አስተዋሣኢተ ፡ ንስጥሮስ ፡ ቄርሎስሀ ፤ ወአስተጋባኢተ ፡ ኤፌሶን ፡ ካዕበተ ፡ ምእት ፡ ሊቃውንተ ። እምንና ፡ ኀበን ፡ እስከን ፡ ሲያመጣ ፥ ትንሣኤ ፡ እግዚእነ ፡ አስተራዋጺተ ፡ መቃብር ፡ አንስተ ፡ ኀበ ፡ ሐዋርያት ፤ ወዜና ፡ አንስት ፡ አስተራዋጺተ ፡ መቃብር ፡ ጴጥሮስሀ ፡ ወዮሐንስሀ ፡ ኀቡረ ። ፊተኛውን ፡ ከ ፥ ኋለኛውን ፡ ወደ ፡ እስከ ፡ ብለኽ ፡ ፍታ ።

፻፵፱ ፤ ያጕል ፡ አንቀጽና ፡ የተገብሮ ፡ ያስተጋብሮም ፡ ሣልስ ፡ አገባብ ፡ ሲያመጣ ፡ እንዲሁ ፡ ነው ። ያጕል ፡ አንቀጽና ፡ የተገብሮ ፡ ሣልስ ፡ ለንና ፡ በእንተን ፡ ምስለንና ፡

ከመን ፡ በን ፡ ሲያ ፥ ክርስቶስ ፡ ተሳታፌ ፡ አዳም ፡ ወሔዋን ፡ ጽዋዐ ፡ ሞት ፡ ምስለ ፡ ውሉዶሙ ፤ ውእቱኬ ፡ ተኀላቄ ፡ ፈያት ፡ ወተካፋሌ ፡ ሐብል ፡ ነዊኅ ፡ ተአሰሮተ ፡ ድኅሬት ፡ ርስቶሙ ። ኀበንና ፡ እስከን ፡ ሲያመጣ ፥ ገብርኤል ፡ ተፈናዌ ፡ ድንግል ። እምን ፡ ሲያ ፥ ዮሴፍ ፡ ጕያዬ ፡ ቤተ ፡ ልሔም ፡ ግብጸ ፥ ወተመያጤ ፡ ግብጽ ፡ ናዝሬተ ፡ ነሚአ ፡ ሕፃነ ፡ ወእሞ ። የተጋብሮ ፡ ሣልስ ፡ ለንና ፡ በእንተን ፡ በን ፡ ሲያመጣ ፥ ዐማኑኤል ፡ ተጻባኤ ፡ አዳም ፡ ወሔዋን ፡ ምስለ ፡ መልአከ ፡ ሞት ፡ በሞቱ ፡ ወተቃራኔ ፡ ትንሣኤሁ ፡ ምስለ ፡ ስፉሐ ፡ ከርሥ ፡ መቃብር ። ምስለንና ፡ ከመን ፡ መጠነን ፡ ሲያ ፥ ቄርሎስ ፡ ተዋሣኤ ፡ ንስጥሮስ ፡ ወታየድሬጣ ፥ ወተማላኌ ፡ ጴጥሮስ ፡ ሰይፈ ፡ ምስሌሆሙ ። እምንና ፡ ኀበን ፡ እስከን ፡ ሲያ ፥ ማርያም ፡ መግደላዊት ፡ ተራዋጺተ ፡ መቃብር ፡ ምስለ ፡ አብያጺሃ ፡ ኀበ ፡ ሐዋርያት ። ጴጥሮስ ፡ ወዮሐንስ ፡ ተባዳርያነ ፡ መቃብር ፡ ሩጸተ ፡ በጽሐ ፡ በተቃልዎ ።

፻፵ ፤ መስም ፡ ቅጽልም ፡ መድረሻው ፡ ሣልስና ፡ ሳድስ ፡ ስለ ፡ ኾነ ፡ ቍጥሩ ፡ ከውስጠ ፡ ዘ ፡ ነውና ፥ እንዲሁ ፡ ተናበ ፡ ፱ኙን ፡ አገባብ ፡ ያመጣል ። አ ፡ ዘረሰየከ ፡ እግዚአብሔር ፡ አዶናይ ፡ አምላከ ፡ ለፈርዖን ፡ ሙሴ ፡ ዕጓለ ፡ ማይ ፥ መቅተሌ ፡ ዕብራዊ ፡ ግብጻዌ ፡ ወመድፈኔ ፡ ኖጻ ፡ ኪያሁ ፡ ጽሚተ ፤ ክቡደ ፡ መዝራዕት ፡ አንተ ፡ (ለ ፡ በእንተ ፡ በ) ። በትርከሂ ፡ በትረ ፡ ጽድቅ ፡ መገሥጽተ ፡ ውሉድ ፡ ቀላየ ፥ ወመንቅዒተ ፡ ኰኵሕ ፡ ማየ ፡ (ከመ ፡ መጠነ ፡ እም) ። መርሐ ፡ ደብረ ፡ሲና ፡ እምግብጽ ፡ ስሳ ፡ እልፈ ፡ ይቡሳነ ፡ ልብ ፡ ወገጽ ፤ ወመዝለፊተ ፡ አሮን ፡ ሕዝበ ፡ ቅቡጻነ ፡ ተስፋ ፡ በዘዘ ፡ ዚአሁ ፡ ተግሣጽ ፡ ወዘዘ ፡ ዚአሁ ፡ ዘለፋ ፤ (ኀበ ፡ እስከ ፡ ምስለ) ።

፻፵፩ ፤ አርእስትና ፡ ሳቢ ፡ ዘር ። የገቢር ፡ አርእስት ፡ ፱ ፡ አገባብ ፡ ሲያመጣ ፥ ደለዎ ፡ ለክርስቶስ ፡ ለባሴ ፡ ክህነት ፥ ጸውዖተ ፡ ሐመር ፡ አርድእተ ፡ ወአንሥኦተ ፡ ደብር ፡ ስብከተ ፤ መጥዎተ ፡ አዳም ፡ ነፍሰ ፡ ወአኅስሮተ ፡ ገብር ፡ ርእሰ ፡ (እም ፡ በ ፡ ለ ፡ በእንተ ፡ ከመ ፡ መጠነ) ። መዊተ ፡ ፈያት ፡ ስቁለ ፡ ወፈንዎ ፡ ቤቱ ፡ ገነተ ፡ የማናየ ፡ ርግበ ፡ በእንተ ፡ መሐላሁ ፡ (ምስለ ፡ ኀበ ፡ እስከ) ። የቀሩትም ፡ ሳቢ ፡ ዘሮችና ፡ አርእስቶች ፡ እንዲህ ፡ ይገባሉ ። ስቅለተ ፡ አዳም ፡ ተሰቅሎተ ፡ አዳም ፡ ፈቀደ ፡ እግዚእ ፥ (ለ ፡ በእንተ) ። ልብሰተ ፡ ወይም ፡ ለቢሶተ ፡ መንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ሥጋ ፡ ማርያም ፡ ለአካለ ፡ ቃል ፡ ባሕቲቱ ፡ (በ) ። ኢዮአብ ፡ ገብረ ፡ ተቃትሎተ ፡ አቤሴሎም ፡ በትእዛዘ ፡ ዳዊት ፡ (ምስለ) ። አፍቀረ ፡ ወልድ ፡ ልደተ ፡ ማርያም ፡ ወይም ፡ ተወልዶተ ፡ ማርያም ፡ (እም) ። ተክህሎ ፡ ለንስር ፡ አብጽሖተ ፡ ኤርምያስ ፡ ጠማረ ፡ (ኀበ ፡ እስከ) ። ተውህበ ፡ ለሰሎሞን ፡ ንብረተ ፡ ዳዊት ፡ ነቢረ ፡ ዳዊት ፡ ዲበ ፡ መንበረ ፡ መንግሥት ፡ (መጠነ ፡ ከመ) ። ከንኡስ ፡ ቅጽልም ፡ ተናበው ፡ አገባብ ፡ ሲያመጡ ፥ ስቅለተ ፡ ምንት ፡ ተስቅሎተ ፡ አይ ፡ ፈቀደ ፡ እግዚእ ፤ ስቅለተ ፡ ሐብልኑ ፡ ወሚመ ፡ ተሰቅሎተ ፡ ኀጺን ፥ ዳእሙ ፡ ስቅለተ ፡ ዕፅ ። ተሰቃሌ ፡ ምንት ፡ ስቁለ ፡ ምንት ፡ አድኅነ ፡ ዓለመ ። ስቅለተ ፡ አይቴ ፡ ተሰቅሎተ ፡ ማእዜ ፡ ፈቀደ ። ተሰቃሌ ፡ አይ ፡ ሰዓት ፡ ወስቁለ ፡ ምንት ፡ ዕለት ፡ ቤዘወነ ፡ እያሰኙ ፡ በን ፡ ያመጣሉ ። ከደቂቅም ፡ ጥሬ ፡ ተናበው ፡ ነቢረ ፡ ላዕሉ ፥ ነጽሮተ ፡ ላዕሉ ፤ ርደተ ፡ መትሕት ፡ ነጻሬ ፡ ላዕል ፡ ንቡረ ፡ ታሕት ፡ እያሰኙ ፡ በንና ፡ ኀበን ፡ ያመጣሉ ። የቀሩትንም ፡ እንደዚሁ ፡ እያናበብኽ ፡ አግባ ።

፻፵፪ ፤ እንበለ ፡ ለዘጠኙ ፡ አገባብ ፡ አፍራሽና ፡ አሉታ ፡ ሲኾን ፡ በሙሻዘር ፡ ይወጣል ፤ አወጣጡንም ፡ ለማየት ፡ እንደ ፡ ቀድሞው ፡ ኢ ፡ መጨመር ፡ ነው ። ብቻ ውንም ፡ ባርእስት ፡ ገብቶ ፡ አሉታ ፡ እየኾነ ፡ ለንና ፡ በእንተን ፡ ሲያፈርስ ፥ ጥቀ ፡ ፍቁር ፡ በኀበ ፡ ወልድ ፡ ተሰቅሎተ ፡ አዳም ፡ ይላል ፤ ስትፈታም ፡ ስላዳም ፡ መሰቀል ፤ ያላዳም ፡ መሰቀል ፡ ብለኽ ፡ በጽድቅ ፡ ባሉታ ፡ በኹለቱም ፡ ፍታ ። ከኢ ፡ ተስማምቶ ፡ የበ ፡ አፍ ራሽና ፡ አሉታ ፡ ሲኾን ፥ ጻድቃን ፡ ወሰማዕት ፡ ያፈቅሩ ፡ ጥቀ ፡ ኢነሢአ ፡ ሥጋሆሙ ፡ መከራ ። በቅጽልም ፡ የከመ ፡ የምስለ ፡ አፍራሽና ፡ አሉታ ፡ ሲኾን ፥ ክርስቶስ ፡ ኢስ ቁለ ፡ ፈያት ። ለኀበ ፡ ለእስከ ፡ አሉታ ፡ ሲኾን ፥ ገብርኤል ፡ ኢተፈናዌ ፡ ማርያም ፡ ይላል ። ለእም ፡ አፍራሽ ፡ ሲኾን ፥ ወልድ ፡ ኢተፈናዌ ፡ አብ ፥ ኢፍንወ ፡ አብ ፡ ውስተ ፡ ዓለም ። ለመጠነም ፡ አፍራሽና ፡ አሉታ ፡ ሲኾን ፥ ጻድቅ ፡ ብእሲ ፡ ይፈቅድ ፡ ኢገቢረ ፡ ዐቅሙ ፡ ኢግብረተ ፡ ዐቅሙ ፡ ትሩፋተ ፡ ሥጋ ፡ ወነፍስ ፡ ይላል ።

፻፵፫ ፤ ዳግመኛም ፡ በሙሻዘር ፡ እስከኹን ፡ የተነገሩቱ ፡ ደቂቅ ፡ አገባቦች ፡ ፱ኙ ፡ ኹሉ ፡ ባንቀጽ ፡ ዝርዝር ፡ ይዘምታሉ ፤ ዘመቻውና ፡ ዝርዝሩም ፡ ይህ ፡ ነው ። ለና ፡ በእንተ ፡ ባንቀጽ ፡ ሲዘምቱ ፥ አምላክ ፡ ሞታ ፡ ለሔዋን ፡ ይላል ፤ ይህም ፡ ሞተ ፡ ላቲ ፡ ለሔዋን ፥ ወይም ፡ በእንቲአሃ ፡ ለሔዋን ፡ ማለት ፡ ነው ። አምላክ ፡ ተሰቅሎ ፡ ለመስ ቀል ፡ ሲል ፥ ቦቱ ፡ ለመስቀል ፡ በል ። ተሰቅሎሙ ፡ ለፈያት ፡ ሲል ፡ ምስሌሆሙ ፡ ከማ ሆሙ ፡ በል ። አብ ፡ ፈነዋ ፡ ለድንግል ፡ ገብርኤልሀ ፡ ሲል ፥ ኀቤሃ ፡ እስከኔሃ ፡ በል ። ሐዋርያት ፡ ተፈነውዋ ፡ ለኢየሩሳሌም ፡ ብሔረ ፡ አሕዛብ ፡ ሲል ፥ ተፈነዉ ፡ እምኔሃ ፡ ለኢየሩሳሌም ፡ በል ። እግዚአብሔር ፡ አንገሦ ፡ ለዳዊት ፡ ሰሎሞንሀ ፡ ሲል ፥ መጠኖ ፡ ለዳዊት ፡ ማለት ፡ ነው ። እንበለን ፡ ለኒሀ ፡ ለ፱ኙ ፡ አፍራሽ ፡ ስታደርግ ፡ አኹን ፡ በተናገ ርናቸው ፡ አናቅጽ ፡ በያንዳንዱ ፡ ኹሉ ፡ ኢን ፡ ጨምር ። ይህም ፡ ኢሞታ ፡ ለሔዋን ፤ ኢተሰቅሎሙ ፡ ለፈያት ፡ ማለቱን ፡ ያሳያል ። የሙሻዘር ፡ መንገድና ፡ አከኼድ ፡ ባጭሩ ፡ ይህ ፡ ነው ።

## ፳፫ኛ ፡ ዕርከን ።

## ሠረዝ ።

፻፵፬ ፤ ሠረዝ ፡ ማለት ፡ ፍጹም ፡ ቃልን ፡ ከቃል ፡ የሚለይ ፡ ማእከላዊ ፡ ነቍጥ ፡ ማለት ፡ ነው ፤ ፪ቱ ፡ ነቍጥ ፡ እንዳኃዝ ፡ ኹኖ ፡ በላይና ፡ በታች ፡ ፪ ፡ መሥመሮች ፡ ሲ ጨመሩ ፥ ስሙ ፡ ሠረዝ ፡ ይባላል ። አኹን ፡ ግን ፡ በዚህ ፡ ክፍል ፡ ሠረዝ ፡ የምንለው ፡ በሠረዝ ፡ ተከፍሎ ፡ የሚነገር ፡ ፯ ፡ መንታ ፡ ቃል ፡ ነው ፤ ኀዳሪና ፡ ማኅደር ፥ ወላጅና ፡ ተወላጅ ፥ ገንዘብና ፡ ባለገንዘብ ፥ ልዑልና ፡ ትሑት ፥ ሩቅና ፡ ቅርብ ፥ ለሚና ፡ አልሚ ፥ አጥፊና ፡ ጠፊ ። ፪ኛም ፡ ታጥፎ ፡ ተመላልሶ ፡ እየተዛወረ ፡ የሚነገር ፡ ስለ ፡ ኾነ ፡ ተዛ ዋሪ ፡ ይባላል ። ዐቢይ ፡ አገባብ ፡ የሌላቸው ፡ የፍጹማን ፡ ቃላት ፡ አነጋገር ፡ በያገባቡ ፡ ሲጠቀለል ፡ ስልቱና ፡ ዐይነቱ ፡ እንደ ፡ ሕዋሳት ፡ ፭ ፡ ነው ። ፩ኛው ፥ በአው ፡ በሚመ ፡ ማሻሻል ፡ ማማረጥ ። ፪ኛው ፥ በዋዌ ፡ መደርደር ፤ ተሠይጠ ፡ ዮሴፍ ፡ ወኮነ ፡ ገብረ ፡ ወ ሐማ ፡ እገሪሁ ፡ በመዋቅሕት ፡ እንደ ፡ ማለት ። ፫ኛው ፥ በወሂኒና ፡ በሰ ፡ በባሕቱ ፡ መክ ፈል ፡ ነው ። ፬ኛው ፥ ነጥሎ ፡ ደርበ ፡ መሠረዝ ። ፭ኛው ፥ ማነጻጸር ፡ ነው ።

፻፵፩ ፤ እነዚህም ፡ የቈጠርናቸው ፡ ፺ቱ ፡ ጥንድ ፡ ቃላት ፥ ነጠላ ፡ ወይም ፡ ሠምና ፡ ወርቅ ፡ ኹነው ፡ በክፍል ፡ በሠረዝ ፥ በድርድር ፡ በጥቅል ፡ እየገቡ ፡ ይነገራሉ ። ኀዳሪ ፡ ከማኅደር ፥ ማኅደር ፡ ከኀዳሪ ፡ አይዛመዱም ። ግብር ፡ ነገር ፡ ኀዳሪ ፥ በታ ፡ ጊዜ ፡ ማኅ ደር ፡ ይኾናሉ ፤ አካል ፡ ግን ፡ ገንዘብም ፡ ባለገንዘብም ፡ ይኾናል ። በክፍልም ፡ ኹኖ ፡ በሠረዝም ፡ ኹኖ ፡ ሲነገሩ ፡ ለኹሉም ፡ የተለየ ፡ አገባብ ፡ አላቸው ። የኀዳሪ ፡ ለ ፡ ነው ፤ የማኅደር ፡ ኀበ ፡ ዲበ ፡ ላዕለ ፡ መልዕልተ ፡ ታሕተ ፡ ቅድመ ፡ ድኅረ ፡ ውስተ ፡ ውስጠ ፡ ማእከለ ፤ በ ፡ እየተስማማቸው ፡ ኹሉም ፡ በ ፡ ናቸው ። የወላጅ ፡ እም ፥ የተወላጅ ፡ ለ ፡ ናቸው ። የገንዘብና ፡ የባለገንዘብ ፡ ለ ፡ በ ፡ ኀበ ፡ ናቸው ። የልዑልና ፡ የትሑት ፡ በ ፡ ኀበ ፡ ታሕተ ፡ ቅድም ፡ እም ፡ ናቸው ። የለሚ ፡ ለ ፡ ኀበ ፡ ቅድመ ፥ ያልሚ ፡ በ ፡ ናቸው ። የጠፌና ፡ ያጥፌ ፡ በ ፡ ኀበ ፡ ቅድመ ፡ ናቸው ። የሩቅ ፡ እም ፥ የቅርብ ፡ ኀበ ፡ መንገለ ፡ ለ ፡ ናቸው ። በተገናኝ ፡ የኹሉም ፡ ማሰሪያ ፡ ውእቱ ፡ ነው ።

፻፵፪ ፤ ኀዳሪና ፡ ማኅደር ፡ በነጠላ ፡ ገብተው ፡ በክፍል ፡ ሲነገሩ ፥ ማርያም ፡ ለዐማ ኑኤል ፡ መዝገብ ፡ ይእቲ ፤ ወዐማኑኤል ፡ በማርያም ፡ ወርቅ ፡ ውእቱ ፡ ይላል ። ስትፈታም ፡ ማርያም ፡ ለፀማኑኤል ፡ ሣጥን ፡ ናት ፤ ዐማኑኤልም ፡ በማርያም ፡ ዘንድ ፡ ወርቅ ፡ ነው ፡ በል ። በነጠላ ፡ ገብተው ፡ በሠረዝ ፡ ሲነገሩ ፥ መቃብር ፡ ወመዋቲ ፡ ለመዋቲ ፥ ወታሕተ ፡ መቃብር ፡ ገራህተ ፡ ዘርዕ ፡ ወዘርዐ ፡ ገራህት ፡ ይላል ። ስትፈታም ፡ መቃብር ፡ ለሟች ፡ የዘር ፡ ዕርሻ ፡ ናት ፤ ሟችም ፡ በመቃብር ፡ ታች ፡ የርሻ ፡ ዘር ፡ ነው ፡ በል ። ፪ኛም ፥ በሠ ምና ፡ በወርቅ ፡ ገብተው ፡ በክፍል ፡ ሲነገሩ ፥ ማርያም ፡ መዝገብ ፡ ለዐማኑኤል ፡ ወርቅ ፡ ሰማይ ፡ ሙዳይ ፡ ይእቲ ፤ ወዐማኑኤል ፡ ወርቅ ፡ በማርያም ፡ መዝገብ ፥ ወይም ፡ በው ስተ ፡ በማእከለ ፡ በኀበ ፡ በዲበ ፡ በታሕተ ፡ በቅድመ ፡ ማርያም ፡ መዝገብ ፡ መንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ብሩር ፡ ውእቱ ፡ ይላል ። ስትፈታም ፥ ማርያም ፡ ሣጥን ፡ ለዐማኑኤል ፡ ወርቅ ፡ ሰማይ ፡ ሙዳይ ፡ ናት ፤ ዐማኑኤል ፡ ወርቅም ፡ በማርያም ፡ ሣጥን ፡ መንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ብር ፡ ነው ፡ በል ። በሠረዝም ፡ ሲነገሩ ፥ ማርያም ፡ መዝገብ ፡ ወዐማኑኤል ፡ ወርቅ ፥ ለዐማኑኤል ፡ ወርቅ ፤ ወበማርያም ፡ መዝገብ ፡ ሰማይ ፡ ሙዳይ ፡ መንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ብሩር ፡ ይላል ፤ እንደ ፡ ላይኛው ፡ ፍታ ።

፻፵፫ ፤ ወላጅና ፡ ተወላጅ ፡ በነጠላ ፡ ገብተው ፡ በሠረዝ ፡ ሲነገሩ ፥ ራሔል ፡ ወዮ ሴፍ ፡ ለዮሴፍ ፥ ወእምራሔል ፡ ያዕቆብ ፡ ወብንያም ፡ ይላል ። በሠምና ፡ በወርቅ ፡ ገብ ተው ፡ በክፍል ፡ ሲነገሩ ፥ ገቦ ፡ ኢየሱስ ፡ ከርሠ ፡ ዐንበሪ ፡ ለዮናስ ፡ ደም ፥ ክሣደ ፡ ጊዮ ርጊስ ፡ እም ፤ ወዮናስ ፡ ደም ፡ እምከርሠ ፡ ዐንበሪ ፡ ገቦ ፡ ኢየሱስ ፡ ማየ ፡ ሕይወት ፡ ዓሣ ፡ ውእቱ ፡ ይላል ።

፻፵፬ ፤ ገንዘብና ፡ ባለገንዘብም ፡ በነጠላ ፡ ገብተው ፡ በክፍል ፡ ሲነገሩ ፥ ዘመነ ፡ ሊቃውንት ፡ ለትምህርተ ፡ ሃይማኖት ፡ ዘመነ ፡ ሐዋርያት ፡ ውእቱ ፥ ወትምህርተ ፡ ሃይ ማኖት ፡ ለዘመነ ፡ ሊቃውንት ፡ መሢዕተ ፡ ወንጌል ፡ ውእቱ ፡ ይላል ፤ ይህ ፡ በታና ፡ ጊዜ ፡ ሲገቡ ፡ ነው ። በነጠላ ፡ ገብተው ፡ በሠረዝ ፡ ሲነገሩም ፥ ተክለ ፡ በለስ ፡ ወገነት ፡ በገነት ፡ ወለተክለ ፡ በለስ ፡ ተክለ ፡ ወይን ፡ ወደብር ፡ ውእቱ ፡ ይላል ፤ ይህም ፡ በታና ፡ ግብር ፡ ሲገቡ ፡ ነው ። በሠምና ፡ በወርቅ ፡ ገብተው ፡ በክፍል ፡ ሲነገሩ ፥ አካልም ፡ ገንዘብና ፡

በለገንዘብ ፡ ሲኾን ፤ ዳዊት ፡ ወልድ ፡ ለሚካኤል ፡ ኢዮአብ ፡ ሰሎሞን ፡ አብ ፡ ውእቱ ፤ ወሚካኤል ፡ ኢዮአብ ፡ ለዳዊት ፡ ወልድ ፡ ገብርኤል ፡ አቢሳ ፡ ውእቱ ፡ ይላል ፤ የኹሉም ፡ አገባብ ፡ ለ ፡ ነው ፡፡ ዳግመኛም ፡ አካልና ፡ ነገር ፡ በሠምና ፡ በወርቅ ፡ ሲገቡ + ንስሓ ፡ ወርቅ ፡ ለአዳም ፡ ኪራም ፡ ብሩር ፡ ጌጋይ ፡ ውእቱ ፤ ወአዳም ፡ ኪራም ፡ ለንስሓ ፡ ወርቅ ፡ ዳዊት ፡ ነዌ ፡ ውእቱ ፡ ይላል ፡፡ የቀረውም ፡ በኅዳሪና ፡ በማኅደር ፡ እንደ ፡ ተባለው ፡ ነው ፡፡ ልውልና ፡ ትሑት ፡ በነጠላ ፡ ገብተው ፡ በክፍል ፡ ሲነገሩ + ወርቅ ፡ እምብሩር ፡ ዕንቍ ፡ በሕርይ ፡ ውእቱ ፤ ወብሩር ፡ እምወርቅ ፡ ኅጺን ፡ ውእቱ ፡ ይላል ፡፡ በሠምና ፡ በወርቅ ፡ ገብተው ፡ በሠረዝ ፡ ሲነገሩ + ጴጥሮስ ፡ ወርቅ ፡ ወይሁዳ ፡ ብሩር + እምይሁዳ ፡ ብሩር ፡ ወእምጴጥሮስ ፡ ወርቅ ፡ ክርስቶስ ፡ ዕንቍ ፡ በሕርይ ፤ ወመልአከ ፡ ዝንቱ ፡ ዓለም ፡ ኅጺን ፡ ውእቱ ፡ ይላል ፡፡

፻፹፱ ፤ ለሚና ፡ አልሚ ፡ በነጠላ ፡ ገብተው ፡ በሠረዝ ፡ ሲነገሩ + ነፋስ ፡ ወእሳት ፡ ለእሳት ፡ ወበነፋስ ፡ ሕይወት ፡ አርዝ ፡ ውእቱ ፡ ይላል ፡፡ በሠምና ፡ በወርቅ ፡ ገብተው ፡ በክፍል ፡ ሲነገሩ + ንጽሕና ፡ ነፋስ ፡ ለሥጋ ፡ ማርያም ፡ እሳት ፡ ክብረ ፡ መላእክት ፡ ሕይወት ፤ ወሥጋ ፡ ማርያም ፡ እሳት ፡ በንጽሕና ፡ ነፋስ ፡ አካለ ፡ ኪሩብ ፡ አርዝ ፡ ውእቱ ፡ ይላል ፡፡ ጠሬና ፡ አጥሬ ፡ ደግሞ ፡ በነጠላ ፡ ገብተው ፡ በሠረዝ ፡ ሲነገሩ + ቤት ፡ ወነፋስ ፡ በኀበ ፡ ነፋስ ፡ ወቤት ፡ ደመና ፡ ንስር ፡ ውእቱ ፡ ይላል ፡፡ በሠምና ፡ በወርቅ ፡ ገብተው ፡ በክፍል ፡ ሲነገሩ + አበሳ ፡ አዳም ፡ ቤት ፡ በኀበ ፡ ደመ ፡ ኢየሱስ ፡ ነፋስ ፡ አበሳ ሔዋን ፡ ደመና ፡ ውእቱ ፡፡ ወደመ ፡ ኢየሱስ ፡ ነፋስ ፡ በኀበ ፡ አበሳ ፡ አዳም ፡ ቤት ፡ መስቀል ፡ ንስር ፡ ውእቱ ፡ ይላል ፡፡ የቀረው ፡ እንደ ፡ ኅዳሪና ፡ እንደ ፡ ማኅደር ፡ ነው ፡፡ ሩቅና ፡ ቅርብ ፡ በነጠላ ፡ ሲገቡ ፡ ሩቁ + ፀሓይ ፡ እምነ ፡ ምድር ፡ ሰማይ ፡፡ ቅርቡም + ከከብ ፡ ለወርኅ ፡ ፀሓይ ፡ ይላል ፡፡ በሠምና ፡ በወርቅ ፡ ሲገቡም ፡ ሩቁ + ሥጋ ፡ ማርያም ፡ ፀሓይ ፡ እምነ ፡ ምድር ፡ አበሳ ፡ አካለ ፡ ሱራፌ ፡ ሰማይ ፡፡ ቅርቡም + ሥጋ ፡ ማርያም ፡ ከከብ ፡ ለወርኅ ፡ ንጽሕና ፡ አካለ ፡ ኪሩብ ፡ ፀሓይ ፡ ይላል ፡፡ የሠረዝ ፡ አፈታት ፡ ሲገለጥ ፡ ማርያም ፡ ለዐማኑኤል ፡ ከመ ፡ መዝገብ ፡ ይእቲ ፤ ወዐማኑኤል ፡ በማርያም ፡ ከመ ፡ ወርቅ ፡ ውእቱ ፡ ማለት ፡ ነው ፡፡ በ፲፱ኛው ፡ ዕርከን ፡ ቍ፩፫ ፡ ከመ + ሠረዝ ፡ ይኾናል ፡ ያልነው ፡ ስለዚህ ፡ ነው ፡፡

፻፺ ፤ በድርድር ፡ በጥቅል ፡ ሲነገሩም ፡ አገባባቸው ፡ እስመ ፡ ነው ፤ ባንድ ፡ አንቀጽ ፡ ታስረው ፡ ባንድ ፡ አገባብ ፡ ይጠቀለላሉ ፡፡ ሦስቱ ፡ ድርድር + ወይም ፡ ጕንጕን ፡ ሠረዝ ፤ ሦስተኛ ፡ ደግሞ ፡ በቅኔነቱ ፡ ሥላሴ ፡ የሚባል ፡፡

አስተብፅዑ ፡ ነፍስተ ፡ ዓሣ ፡
ኢየሱስ ፡ ወጴጥሮስ ፡ ወሩፋኤል ፤

በሕረ ፡ ጥብርያዶስ ፡ አኮኑ ፡ እመ ፡ ኢየሱስ ፡ ወፈረ ፡
በኅዳጥ ፡ ዓሣ ፡ አጽገበ ፡ ማኅበረ ፡፡ አባ ኃይለ ገብርኤል ደነቀ ቆሞስ
ወእምከርሠ ፡ ዓሣ ፡ አውፅአ ፡ ጸባሕተ ፡ ቄሳር ፡ ??? ፡ እስተዳዳሪ
መሠግር ፡ ጴጥሮስ ፡ አመ ፡ አሥገረ ፡፡ Abba H Gebrael Deneke Komos

ሩፋኤልኒ ፡ ሥራየ ፡ በዘአእመረ ፡
በዓሣሁ ፡ አሕየወ ፡ ዕዉረ ።

ይህም ፡ አካኼድ ፡ የተገኘ ፡ ከመጻሕፍት ፡ ነው ፤ ይኸውም ፡ ወመጺአ ፡ ውእቱ ፡ ይዘ ለፎ ፡ ለዓለም ፡ በአንተ ፡ ኀጢአት ፡ ወበአንተ ፡ ጽድቅ ፡ ወበአንተ ፡ ኵነኔ ፡ ባለው ፡ ይታወቃል ። ነጠላውንም ፡ ቃል ፡ በዘ ፡ ተርጕሞ ፡ ሲሠርዝ+ዐማኑኤል ፡ ዘበትርጓሜሁ ፡ አምላክ፡ ወሰብእ+እስመ ፡ ውእቱ፡አምላክ ፡ በመለኮቱ፡ ወሰብእ ፡ በትስብእቱ፡ ይላል ። ዳግመኛም ፡ ፪ ፡ ፍጹማን ፡ ቃላት ፡ እየብቻቸው ፡ እንደ ፡ ነዶ ፡ ታስረው ፡ በወ ፡ ሲደረደሩ ፡ በእስመ ፡ ይጠቀለላሉ ።

እምከዊነ ፡ ካህን ፡ ይኄይስ ፡ ከዊነ ፡ ኖላዊ ፤
ወኀለ ፡ እንስሳ ፡ ትትበደር ፡ እምቤተ ፡ መቅደስ ፡ ዐባይ ፤
እስመ ፡ ቤተ ፡ መቅደስ ፡ ኮነት ፡ ቤተ ፡ ፈያታይ ፤
ወበላዕለ ፡ ኖሎት ፡ ኢሀለወ ፡
ላዕለ ፡ ካህናት ፡ ዘሀሎ ፡ እከይ ።
ትእምርተ ፡ ዝኒ ፡ ከመ ፡ ንርይ ፡
በኀለ ፡ እንስሳ ፡ ሠረቀ ፡ ዘኢየዐርብ ፡ ፀሓይ ፤
ወኖሎት ፡ ተዛውዑ ፡ ምስለ ፡ ሐራ ፡ ልዑል ፡ ሰማይ ።
ዓዲ ፡ እምቅድመ ፡ ዝኒ ፡ በመከነ ፡ ኖሎት ፡ ወመራዕይ ፡
ከመ ፡ ተጸውዑ ፡ ደምፀ ፡ እግረ ፡ ቃለ ፡ ዜና ፡ ሠናይ ፡
ወልደ ፡ እንበረም ፡ ለምስፍና ፡ ወለቅብዐ ፡ መንግሥት ፡ ወልደ ፡ እሴይ ፡

ብሎ ፡ በዠመረበት ፡ ይጨርሳል ። የሠረዝ ፡ ዐዋጅና ፡ አካኼድ ፡ ባጭሩ ፡ ይህ ፡ ነው ።

## ፳፯ኛ ፡ ዕርከን ።

## አንጻር ።

፻፶፩ ፤ አንጻር ፡ ማለት ፡ ትይዩ ፡ አፋዛዥ ፡ አኳያ ፡ ማለት ፡ ነው ። አኹን ፡ ግን ፡ በዚህ ፡ ክፍል ፡ አንጻር ፡ የምንለው ፡ ፊት ፡ የተነገረው ፡ ፍጹም ፡ ቃል ፡ በደቂቅ ፡ ቅጽል ፡ ሲታጠፍ ፡ ፊተኛውን ፡ ለመግለጥና ፡ ለማስረዳት ፡ ከጸፉ ፡ በኋላ ፡ የሚጨመር ፡ ቃል ፡ ነው ። አስተማጠፉም+ትእምርተ ፡ ዝኒ ፡ ከመ ፡ ንርአይ ፡ እንዳለው ፡ ነው ።

፻፶፪ ፤ የአንጻር ፡ ጥሬዎች ። ንባብ ፡ ዜና+ነገር ፤ ጽድቅ ፡ አማን+እውነት ፤ አምሳል ፡ ምሳሌ ፡ ጽላሎት+አምሳያ ፤ አርአያ+አብነት ፤ ተአምር ፡ ትእምርት+ምልክት ፡ ሲኾኑ ፡ እነዚህንም ፡ የመሰሉ ፡ ተውላጥና ፡ ፍዳ ፡ ጥንት ፡ መሠረት ፡ ፍጻሜ ፡ ተፍጻሜት ፡ ተጨምረው ፡ ከደቂቅ ፡ ቅጽል ፡ እየተናበቡ ፡ በጥሬነታቸው ፡ ያጸፉ ፡ ባለቤት ፡ ሲኾኑ ፤ ወይም ፡ ከመ ፡ በኀላፊና ፡ በትንቢት ፡ በነገር ፡ ገብቶ ፡ ሲጫናቸው ፡ ኋለኛውን ፡ ቃል ፡ ከፊተኛው ፡ ያነጻጽራሉ ። ማሰሪያቸውም ፡ ከነ ፡ ረሰየ ፡ ጸድቀ ፡ ተሐሰወ ፡ ተከሥተ ፡ ነጸረ ፡ ሰአለ ፡ ለበወ ፡ ፆቀ ፡ ጠየቀ ፡ ጽሕቀ ፡ ተዘከረ ፡ ሐተተ ፡ ተርፈ+እነዚህን ፡ የመሰለ ፡ ነው ።

፻፵፫ ፤ ሲገቡም ፡ ኵሉ ፡ ሰብእ ፡ ከነ ፡ ጻድቀ ፡ ወረሰየ ፡ ርእሰ ፡ ጻድቀ ፤ ወይም ፡ ኵሉ ፡ ሰአለ ፡ ወለበወ ፡ ፆቀ ፡ ወሐተተ ፡ ሃይማኖተ ፥ ወጽሕቀ ፡ ወተዘከረ ፡ ይኩን ፡ ፍጹመ ፡ በዘመነ ፡ ስብከቱ ፡ ለእግዚእነ ፤ ወዜና ፡ ዝንቱ ፡ ወጽድቀ ፡ ዝንቱ ፡ ወከመ ፡ አማን ፡ ዝንቱ ፡ ይትዐወቅ ፡ በፍድፋዴ ፡ ምእመናን ። ወምሳሌ ፡ ዝንቱ ፡ ወጽላሎተ ፡ ዝንቱ ፡ ወአርአያ ፡ ዝንቱ ፡ ተከሥተ ፡ በስብከተ ፡ ሐዋርያት ። እስፍንተ ፡ ጥበበ ፡ ፆቀ ፡ ሰሎሞን ፤ በሕቱ ፡ ተውላጠ ፡ ዝንቱ ፡ ፍዳ ፡ ዝንቱ ፡ ምስብዒተ ፡ አብደ ። በሕቱ ፡ ፍጻሜ ፡ ዝንቱ ፡ ተፍጻሜተ ፡ ዝንቱ ፡ ረሰየ ፡ እበደ ። ጽሕቀ ፡ ኢዮስያስ ፡ ለዐቂበ ፡ ሥርዐት ፤ ወጥንተ ፡ ዝንቱ ፥ ወመሠረተ ፡ ዝንቱ ፡ ይትዐወቅ ፡ በተሰእሎቱ ፡ ክህናተ ። ኵሉን ፡ ወ ፡ ሂ ፡ ኒ ፡ ጥቀ ፡ ሲከተሉት ፥ አከ ፡ አልበ ፡ ኢ ፡ የነዚህ ፡ መነሻ ፡ ይኾኑለታል ፤ ሲገባም ፡ ኵሉ ፡ ዐለወ ፥ አልበ ፡ ዘይገብራ ፡ ለሠናይት ፡ ወኢአሐዱ ፤ ይትርፍሰ ፡ ገቢሮታ ፡ ኀልዮታሂ ፡ ኀልዮታኒ ፡ ኀልዮታ ፡ ጥቀ ፡ ወኀልዮታ ፡ አልበ ፡ ኀቤሁ ፡ ይላል ። ዳግመኛም ፡ ኵሉ ፡ በንድ ፡ ተነሥቶ ፡ በብዙ ፥ በብዙም ፡ ተነሥቶ ፡ በንድ ፡ ያነጽራል ። በንድ ፡ ተነሥቶ ፡ በብዙ ፡ ሲያነጽር ፥ ዘማች ፡ አንቀጽ ፡ እንጂ ፡ ነባር ፡ አይመቸውም ። ይህም ፡ በመዋዕሊሁ ፡ ለኖኅ ፡ ነበረ ፡ አሐዱ ፡ ዕልው ፥ ወአከ ፡ አሐዱ ፡ በሕቲቱ ፥ አላ ፡ ኵሎሙ ፡ ማለቱን ፡ ያሳያል ። በብዙም ፡ ተነሥቶ ፡ በንድ ፡ ሲያነጽር ፥ ነባር ፡ አንቀጽ ፡ እንጂ ፡ ዘማች ፡ አይመቸውም ። የሠምና ፡ የወርቅ ፡ ንዝ ፡ ፯ኛው ፡ ክፍል ፡ ተፈጸመ ።

## ፰ኛ ፡ ዕርከን ።

## የርባ ፡ ቅምርና ፡ የጸዋትወ ፡ ርባ ፡ ተረፍ ፡ በለ፬ ፡ ረድፍ ።

፻፵፬ ፤ ረድፍ ፡ ማለት ፡ ተከታታይ ፡ ክፍል ፡ ማለት ፡ ነው ፥ ዕርከን ፡ እንደ ፡ ማለት ፤ እነዚሁም ፡ የዋሀ ፡ ርባታና ፡ መሠሪ ፡ ርባታ ፥ ጽንዕ ፡ አንቀጽና ፡ አሉታ ፡ አንቀጽ ፡ ናቸው ። አንዱን ፡ ጽድቅ ፡ አንቀጽ ፡ በየዋሀና ፡ በመሠሪ ፡ በጽንዕ ፡ ባሉታ ፡ ሲያረቡት ፡ ብዙ ፡ ጠባይ ፡ ልዩ ፡ ልዩነት ፡ አለውና ፤ ባላ፬ ፡ ረድፍ ፡ ማለት ፡ ስለዚህ ፡ ነው ። የርባታም ፡ ትምርት ፡ የሚዠመር ፡ በብትን ፡ ባርእስትና ፡ በደቂቅ ፡ ርባታ ፡ ነው ፡ እንጂ ፤ በዐቢይ ፡ አንቀጽ ፡ አይዶለም ። ከደቂቅ ፡ ርባታም ፡ አስቀድሞ ፡ መራሕያን ፡ የሚባሉትን ፡ ያሥሩን ፡ ሰራዊት ፡ ስምና ፡ ተራ ፥ ውእቱ ፡ አንተ ፥ ውእቶሙ ፡ አንትሙ ፥ ይእቲ ፡ አንቲ ፥ ውእቶን ፡ አንትን ፥ አነ ፡ ንሕነ ፡ እያሉ ፡ ማጥናት ፡ ይገባል ። ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ከራስ ፡ ጠጕር ፡ እስከ ፡ እግር ፡ ጥፍር ፡ ያሉትን ፡ ሕዋሳት ፡ በመልክየስ ፡ ተራ ፡ አንዳንዱን ፡ በየስማቸው ፡ ማርባት ፡ ነው ። ይህም ፡ ሥዕርት ፡ ብሎ ፡ ሥዕርቱ ፡ ሥዕርትከ ፤ ርእስ ፡ ብሎ ፡ ርእሱ ፡ ርእስከ ፤ አርእስት ፡ ብሎ ፡ አርእስቲሁ ፡ ከ ፡ ሆሙ ፡ ክሙ ፡ እያሰኙ ፡ ከናፈታቱ ፡ ሲነገር ፥ ላቢይ ፡ ርባታ ፡ በር ፡ ከፋች ፡ መቅድም ፥ ለዘማች ፡ አንቀጽ ፡ መሪ ፡ ፈታውራሪ ፡ መኾኑን ፡ ያሳያል ። ምሳሌውም ፥ ርካብ ፡ ተረግጦ ፡ ወደ ፡ ኮር ፥ ድንክ ፡ ተረግጦ ፡ ወደ ፡ ዙፋን ፡ እንደ ፡ መውጣት ፡ ነው ።

፻፵፭ ፤ ዐቢይ ፡ ርባታም ፡ የሚዠመር ፡ ገቢርነት ፡ ባለው ፡ በ፫ ፡ ፊደል ፡ ግስ ፡ በቀተለ ፡ ቤት ፡ ነው ፤ ያውም ፡ በምልአት ፡ የሚረባ ፥ በድራጊነቱ ፡ ላይ ፡ አስደራጊና ፡

ተደራጊ፥ተደራራጊና፡አደራራጊ፡የሚደርብ፥ላልቶ፡የሚነገር፡መደበኛ፡አንቀጽ፡ ነው ። በዋቆችና፡በጠንቃቆች፡ዐዋጅ፡እንደ፡አአመረ፡የማስደረግ፡ልማድ፡አ፡ ያለበት፡ያራት፡ፊደል፡ግስ፡አስደራጊ፡አንቀጽ፤ እንደነተዝኅረም፡የመደረግ፡ ልማድ፡ተ፡ያለበት፡ተደራጊ፡አንቀጽ፡የርባታ፡መሠረት፡አይኾንም ። ይኹና ልም፡ብሎ፡ቢያደርጉት፡ሲፈተሽና፡ሲመረመር፡ማሳፈሩና፡ማስነወሩ፡አይቀርም ። በአና፡በሀ፡የሚነሣ፡የ፫፡ፊደል፡ግስ፡እንደ፡ቀተለ፡ላልቶ፡ሲነገር፥ሥርወ፡ትን ቢቱን፡በካልአይ፡ኹሉ፡ግእዝ፡ያደርጋል፤ ዖረ፡የዐውር፤ ሖረ፡የሐውር ። እንደ፡ ቀደሰም፡ጠብቆ፡ሲነገር፡በካልአዩ፡ሳድስ፥በቀሩት፡ግእዝ፡ያደርጋል፤ አመረ፡ ይኤምር፡የአምር ። ሐወጸ፡ይሔውጽ፡የሐውጽ ።

፻፶፯፤ ያቢይ፡አንቀጽ፡ርባ፡በዘሩና፡በሥረ፡ነገሩ፡ንኡስ፡አንቀጽ፡ኹኖ፡ በንኡስ፡ርባታ፡ሲዠመር፥ግሱም፡የ፫፡ፊደል፡ኹኖ፡በጥንተ፡ፊደሉ፡በአልፍ፡ ሲነሣ፥አነሣሡ፡ይህ፡ነው ።

## አርእስት፡ወይም፡ንኡስ፡አንቀጽ ።

አሚር፡አሚሮት፤ ማወቅ፥ዐዋቂነት ።

### ንኡስ፡ርባታ ።

አሚርሁ፡አሚሮቱ፡ ማወቁ፡የርሱ፡ማወቅ ።
አሚርከ፡አሚሮትከ፡ ማወቅኽ ።
አሚርሆሙ፡አሚሮቶሙ፡
አሚርከሙ፡አሚሮትከሙ፡
አሚርሃ፡አሚሮታ፡
አሚርኪ፡አሚሮትኪ፡
አሚርሆን፡አሚሮቶን፡
አሚርከን፡አሚሮትከን፡
አሚርየ፡አሚሮትየ፡
አሚርነ፡አሚሮትነ፡ ማወቃችን ።

የገቢር፡ተሳቢም፡ሲኾኑ፡አሚርሁ፡ባለው፡ይከታሉ፤ በአሚሮት፡ግን፡ሙታንየ፡ ብቻ፡(ትሙ፡ታ፡ቶን፡ትየ)፡እነዚህ፡፬ቱ፡ሲቀሩ፡ካዕቡን፡ሳብዕ፥ሳድሱን፡ግእዝ፡ ይወርሰዋል ።

ይህም፡ አሚሮቶ፡ ማወቁን፡
አሚሮተከ፡ተከሙ፤ ተኪ፡ተክን፡ተነ፤ ማወቃችንን፡ማለቱን፡ያሳያል ።
አርእስትን፡ኹሉ፡እንዲህ፡እያልኽ፡አርባ ።

፩ኛ፡ ረድፍ ።

ዐቢይና፡ መደብ፡ የዋህ፡ ርባታ ።

መደበኛ፡ አንቀጽ ።

፻፶፯፤ አመረ፤ ዐወቀ ።
የአምር፡ ያውቅ፡
ይእምር፡ ያውቅ፡ ዘንድ፡ እንዲያውቅ፡ ሊያውቅ፡
ይእምር፤ ይወቅ ። ዘንድ፡ አንቀጽን፡ ኹሉ፡ እንደዚህ፡ ፍታ፤ በትንቢቱም፡ አልን፡ አትጨምር፤ ዐውቋል፡ ያውቃል፡ ማለት፡ የጽንዕ፡ አንቀጽ፡ ፍች፡ ነውና፥ ኋላ፡ ይመጣል ።

አመርከ፤ ተአምር፡ ትእምር፡ እምር ።
አመሩ፤ የአምሩ፡ ይእምሩ፡ ይእምሩ ።
አመርክሙ፤ ተአምሩ፡ ትእምሩ፡ እምሩ ።
አመረት፤ ተአምር፡ ትእምር፡ ትእምር ።
አመርኪ፤ ተአምሪ፡ ትእምሪ፡ እምሪ ።
አመራ፤ የአምራ፡ ይእምራ፡ ይእምራ ።
አመርክን፤ ተአምራ፡ ትእምራ፡ እምራ ።
አመርኩ፤ አአምር፡ እእምር፡ እእምር ።
አመርነ፤ ነአምር፡ ንእምር፡ ንእምር ።

በዝ፡ አንቀጽ ።

አሚሮ፡ ዐውቆ ።
አሚረከ፡ ዐውቀኽ ።
አሚሮሙ፡ አሚረክሙ ። አሚራ፡ አሚረኪ ።
አሚሮን፡ አሚረክን ። አሚርየ፡ አሚረነ ።

ሣልስ፡ ቅጽል ።

አማሪ፡ አማርያን፤ አማሪት፡ አማርያት ።

መድበል፡ ቅጽል ።

አመርት፤ ያወቁ፡ የሚያውቁ፡ ዐዋቆች ።

፪ኛ፡ ረድፍ ።

፻፶፰፤ ያሥሩ፡ መደብ፡ ዝርዝር፥ መሠሪ፡ ርባታ ።

ካሥሩ፡ ሰራዊት፡ ፩ቱ፡ ሩቆች፡ በ፲፡ በ፲፥ ፩ቱ፡ ቅርቦች፡ በ፯፡ በ፯፥ አነና፡ ንሕነ፡ በ፰፡ በ፰፡ ሲዘረዘሩ፡ ድምራቸውና፡ መደባቸው፡ ፹፡ ይኾናል ። አንቀጻቸውም፡

ያሥሩ፡መደብ፡፴፡እንደ፡ኾነ፡የ፹ውም፡፪፻፵፡ይኾናል። መራሕያኑም፡አንቀጽ፡ተቀባዮች፡እየኾኑ፡በየመደቡ፡ራስ፡ተጥፈዋል። ዝርዝራቸውን፡በ፺ኛ፡ዕርከን፡ተመልከት።

(ውእቱ)፡

አመሮ፤ ዐወቀው፤ዐወቀለት፤ዐወቀበት።
የአምሮ፡ ያውቀው፡ያውቅለት፡ያውቅበት፡
ይእምሮ፡ ያውቀው፡ያውቅለት፡ያውቅበት፡ዘንድ፡እንዲያውቀው፡እንዲያውቅለት፡በት፤ሊያውቀው፡ሊያውቅለት፡በት። ኹሉን፡እንዲህ፡ፍታ።
ይእምሮ፤ ይወቀው፤ይወቅለት፤ይወቅበት።

አመረከ፤የአምረከ፡ይእምርከ፡ይእምርከ።
አመሮሙ፤የአምሮሙ፡ይእምሮሙ፡ይእምሮሙ።
አመረከሙ፤የአምረከሙ፡ይእምርከሙ፡ይእምርከሙ።
አመራ፤የአምራ፡ይእምራ፡ይእምራ።
አመረኪ፤የአምረኪ፡ይእምርኪ፡ይእምርኪ።
አመሮን፤የአምሮን፡ይእምሮን፡ይእምሮን።
አመረክን፤የአምረክን፡ይእምርክን፡ይእምርክን።
አመረኒ፤የአምረኒ፡ይእምረኒ፡ይእምረኒ።
አመረነ፤የአምረነ፡ይእምረነ፡ይእምረነ።

(አንተ)፡

አመርከ፤ተአምሮ፡ትእምሮ፡እምሮ።
አመርከሙ፤ተአምሮሙ፡ትእምሮሙ፡እምሮሙ።
አመርከ፤ተአምራ፡ትእምራ፡እምራ።
አመርከን፤ተአምሮን፡ትእምሮን፡እምሮን።
አመርከኒ፤ተአምረኒ፡ትእምረኒ፡እምረኒ።
አመርከነ፤ተአምረነ፡ትእምረነ፡እምረነ።

(ውእቶሙ+አው፡እሙንቱ)፡

፻፶፱፤አመርዎ፤የአምርዎ፡ይእምርዎ፡ይእምርዎ።
አመሩከ፤የአምሩከ፡ይእምሩከ፡ይእምሩከ።
አመርዎሙ፤የአምርዎሙ፡ይእምርዎሙ፡ይእምርዎሙ።
አመሩከሙ፤የአምሩከሙ፡ይእምሩከሙ፡ይእምሩከሙ።
አመርዋ፤የአምርዋ፡ይእምርዋ፡ይእምርዋ።
አመሩኪ፤የአምሩኪ፡ይእምሩኪ፡ይእምሩኪ።

አመርዎን ፤ የአምርዎን ፡ ይእምርዎን ፡ ይእምርዎን ።
አመሩክን ፤ የአምሩክን ፡ ይእምሩክን ፡ ይእምሩክን ።
አመሩኒ ፤ የአምሩኒ ፡ ይእምሩኒ ፡ ይእምሩኒ ።
አመሩነ ፤ የአምሩነ ፡ ይእምሩነ ፡ ይእምሩነ ።

(አንትሙ) ፡

አመርክምዎ ፤ ተአምርዎ ፡ ትእምርዎ ፡ እምርዎ ።
አመርክምዎሙ ፤ ተአምርዎሙ ፡ ትእምርዎሙ ፡ እምርዎሙ ።
አመርክምዋ ፤ ተአምርዋ ፡ ትእምርዋ ፡ እምርዋ ።
አመርክምዎን ፤ ተአምርዎን ፡ ትእምርዎን ፡ እምርዎን ።
አመርክሙኒ ፤ ተአምሩኒ ፡ ትእምሩኒ ፡ እምሩኒ ።
አመርክሙነ ፤ ተአምሩነ ፡ ትእምሩነ ፡ እምሩነ ።

(ይእቲ) ፡

፻፰ ፤ አመረቶ ፤ ተአምሮ ፡ ትእምሮ ፡ ትእምሮ ።
አመረተከ ፤ ተአምረከ ፡ ትእምርከ ፡ ትእምርከ ።
አመረቶሙ ፤ ተአምሮሙ ፡ ትእምሮሙ ፡ ትእምሮሙ ።
አመረተክሙ ፤ ተአምረክሙ ፡ ትእምርክሙ ፡ ትእምርክሙ ።
አመረታ ፤ ተአምራ ፡ ትእምራ ፡ ትእምራ ።
አመረተኪ ፤ ተአምረኪ ፡ ትእምርኪ ፡ ትእምርኪ ።
አመረቶን ፤ ተአምሮን ፡ ትእምሮን ፡ ትእምሮን ።
አመረተክን ፤ ተአምረክን ፡ ትእምርክን ፡ ትእምርክን ።
አመረተኒ ፤ ተአምረኒ ፡ ትእምረኒ ፡ ትእምረኒ ።
አመረተነ ፤ ተአምረነ ፡ ትእምረነ ፡ ትእምረነ ።

(አንቲ) ፡

አመርኪዮ ፤ ተአምሪዮ ፡ ትእምሪዮ ፡ እምሪዮ ።
አመርኪዮሙ ፤ ተአምሪዮሙ ፡ ትእምሪዮሙ ፡ እምሪዮሙ ።
አመርኪያ ፤ ተአምሪያ ፡ ትእምሪያ ፡ እምሪያ ።
አመርኪዮን ፤ ተአምሪዮን ፡ ትእምሪዮን ፡ እምሪዮን ።
አመርክኒ ፤ ተአምርኒ ፡ ትእምርኒ ፡ እምርኒ ።
አመርክነ ፤ ተአምርነ ፡ ትእምርነ ፡ እምርነ ።

(ውእቶን ፥ አው ፡ እማንቱ) ፡

፻፰፩ ፤ አመራሁ ፤ የአምራሁ ፡ ይእምራሁ ፡ ይእምራሁ ።
አመራከ ፤ የአምራከ ፡ ይእምራከ ፡ ይእምራከ ።
አመራሆሙ ፤ የአምራሆሙ ፡ ይእምራሆሙ ፡ ይእምራሆሙ ።

አመራክሙ ፤ የአምራክሙ ፡ ይእምራክሙ ፡ ይእምራክሙ ።
አመራሃ ፤ የአምራሃ ፡ ይእምራሃ ፡ ይእምራሃ ።
አመራኪ ፤ የአምራኪ ፡ ይእምራኪ ፡ ይእምራኪ ።
አመራሆን ፤ የአምራሆን ፡ ይእምራሆን ፡ ይእምራሆን ።
አመራክን ፤ የአምራክን ፡ ይእምራክን ፡ ይእምራክን ።
አመራኒ ፤ የአምራኒ ፡ ይእምራኒ ፡ ይእምራኒ ።
አመራነ ፤ የአምራነ ፡ ይእምራነ ፡ ይእምራነ ።

(አንትን) ፡

አመርክናሁ ፤ ተአምራሁ ፡ ትእምራሁ ፡ እምራሁ ።
አመርክናሆሙ ፤ ተአምራሆሙ ፡ ትእምራሆሙ ፡ እምራሆሙ ።
አመርክናሃ ፤ ተአምራሃ ፡ ትእምራሃ ፡ እምራሃ ።
አመርክናሆን ፤ ተአምራሆን ፡ ትእምራሆን ፡ እምራሆን ።
አመርክናኒ ፤ ተአምራኒ ፡ ትእምራኒ ፡ እምራኒ ።
አመርክናነ ፤ ተአምራነ ፡ ትእምራነ ፡ እምራነ ።

(አነ) ፡

፻፹፱ ፤ አመርክዎ ፤ አአምሮ ፡ እእምሮ ፡ እእምሮ ።
አመርኩከ ፤ አአምረከ ፡ እእምርከ ፡ እእምርከ ።
አመርክዎሙ ፤ አአምሮሙ ፡ እእምሮሙ ፡ እእምሮሙ ።
አመርኩክሙ ፤ አአምረክሙ ፡ እእምርክሙ ፡ እእምርክሙ ።
አመርክዋ ፤ አአምራ ፡ እእምራ ፡ እእምራ ።
አመርኩኪ ፤ አአምረኪ ፡ እእምርኪ ፡ እእምርኪ ።
አመርክዎን ፤ አአምሮን ፡ እእምሮን ፡ እእምሮን ።
አመርኩክን ፤ አአምረክን ፡ እእምርክን ፡ እእምርክን ።

(ንሕነ) ፡

አመርናሁ ፤ ነአምሮ ፡ ንእምሮ ፡ ንእምሮ ።
አመርናከ ፤ ነአምረከ ፡ ንእምርከ ፡ ንእምርከ ።
አመርናሆሙ ፤ ነአምሮሙ ፡ ንእምሮሙ ፡ ንእምሮሙ ።
አመርናክሙ ፤ ነአምረክሙ ፡ ንእምርክሙ ፡ ንእምርክሙ ።
አመርናሃ ፤ ነአምራ ፡ ንእምራ ፡ ንእምራ ።
አመርናኪ ፤ ነአምረኪ ፡ ንእምርኪ ፡ ንእምርኪ ።
አመርናሆን ፤ ነአምሮን ፡ ንእምሮን ፡ ንእምሮን ።
አመርናክን ፤ ነአምረክን ፡ ንእምርክን ፡ ንእምርክን ።

የበዝ ፡ አንቀጽ ፡ ዝርዝር ፡ እስከ ፡ ፲ ፡፡

(ውእቱ) ፡

፻፺፫ ፤ አሚሮሁ ፡ ዐውቆት ፡ ለት ፡ በት ፡፡
አሚሮከ ፡ አሚሮሆሙ ፡ ክሙ ፡፡ አሚሮሃ ፡ ኪ ፡ ሆን ፡ ክን ፡ የ ፡ ነ ፡፡
(አንተ) ፡ አሚረከሁ ፡ ሆሙ ፤ አሚረከሃ ፡ ሆን ፡ ክኒ ፡ ክነ ፡፡
(እሙንቱ) ፡ አሚሮሙሁ ፡ ከ ፡ አሚሮሙሆሙ ፡ ክሙ ፡፡
አሚሮሙሃ ፡ ኪ ፡ አሚሮሙሆን ፡ ክን ፡ ሙኒ ፡ ነ ፡፡
(አንትሙ) ፡ አሚረክሙሁ ፡ ሆሙ ፤ አሚረክሙሃ ፡ ሆን ፡ ኒ ፡ ነ ፡፡
(ይእቲ) አሚራሁ ፡ ከ ፡ አሚራሆሙ ፡ ክሙ ፡ አሚራሃ ፡ ኪ ፡
አሚራሆን ፡ ክን ፡ አሚራኒ ፡ አሚራነ ፡ ዐውቃን ፡፡
(አንቲ) ፡ አሚረኪሁ ፡ ሆሙ ፡ አሚረኪሃ ፡ ሆን ፡ ክኒ ፡ ነ ፡፡
(እማንቱ) ፡ አሚሮንሁ ፡ ከ ፡ ሆሙ ፡ ክሙ ፡ አሚሮንሃ ፡ ኪ ፡
አሚሮንሆን ፡ ክን ፡ አሚሮንኒ ፡ ንነ ፡ ዐውቀውን ፡፡
(አንትን) ፡ አሚረክንሁ ፡ ሆሙ ፡ አሚረክንሃ ፡ ሆን ፡ ናኒ ፡ ናነ ፡፡
(አነ) ፡ አሚርየሁ ፡ ከ ፡ ሆሙ ፡ ክሙ ፤ አሚርየሃ ፡ ኪ ፡ ሆን ፡ ክን ፡፡
(ንሕነ) ፡ አሚረነሁ ፡ ከ ፡ ሆሙ ፡ ክሙ ፤ አሚረነሃ ፡ ኪ ፡ ሆን ፡ ክን ፡፡

፪ኛ ፡ ዐምድ ፤ አስደራጊ ፡ አንቀጽ ፡፡

፻፺፬ ፤ አእመረ ፤ አሳወቀ ፡፡
ያአምር ፡ ያሳውቅ ፡
ያእምር ፡ ያሳውቅ ፡ ዘንድ ፡ ያሳውቅ ፡ እያልኽ ፡ እስከ ሥር ፡ አርባ ፡፡
ዝርዝሩንም ፡ አእመሮ ፤ አሳወቀው ፤ ለት ፤ በት ፡፡
ያአምሮ ፡ ያሳውቀው ፡ ያሳውቅለት ፡ በት ፡ እያልኽ ፡ እስከ ፡ ፲ ፡
አዝምት ፡፡ ከጥንት ፡ ልማዱ ፡ የተለወጠበት ፡ ፪ ፡ ነገር ፡ ነው ፡ ሥርወ ፡ ትንቢትና ፡ አፈ
ታት ፤ ሥረወ ፡ ትንቢት ፡ ግእዝ ፡ የነበረውን ፡ የተአነ ፡ በራብዕ ፡ ያቃአና ፡ ማለት ፤ አፈ
ታት ፡ አድራጊ ፡ የነበረውን ፡ ዐወቀን ፡ ትቶ ፡ ባስደራጊ ፡ አሳወቀ ፡ ማለት ፡፡ ዐወቀ ፡ አሳ
ወቀ ፡ ብለውም ፡ በ፪ ፡ ጾታ ፡ ለሚፈቱት ፡ እወና ፡ አልቦ ፡ ይኽንባቸዋል ፡፡

፫ኛ ፡ ዐምድ ፤ ተደራጊ ፡ አንቀጽ ፡፡

፻፺፭ ፤ ተአምረ ፤ ታወቀ ፡፡
ይትአመር ፡ ይታወቅ ፡
ይትአምር ፡ እያልኽ ፡ እስከ፲ ፡፡
ዝርዝሩንም ፡ ተአምሮ ፤ ታወቀው ፤ ለት ፤ በት ፡፡
ይትአመሮ ፡ ይታወቀው ፡
ይትአመሮ ፡ እያልኽ ፡ እስከ ፡ ፲ ፡ አርባ ፡፡

## ፬ኛ ፡ ዐምድ ፤ ተደራራጊ ፡ አንቀጽ ።

፻፷፮ ፤ ተኣመረ ፤ ተዋወቀ ።
ይትኣመር ፡ ይተዋወቅ ፡
ይትኣመር ፡ እያልኽ ፡ እስከ ሥር ።

ዝርዝሩንም ፡ ተኣመሮ ፡ ይትኣመሮ ፡ ይትኣመሮ ፡ እያልኽ ፡ እስከ ፡ ፹ ፡ አርባ ። ሥርወ ፡ ትንቢቱ ፡ እንዳለፈው ፡ ሳድስ ፡ መኾኑን ፥ ሥርወ ፡ ቀለሙ ፡ ግን ፡ ተለይቶ ፡ ራብዕ ፡ መኾኑን ፡ አስተውል ፤ የሚመጣውም ፡ እንዲሁ ፡ ነው ።

## ፭ኛ ፡ ዐምድ ፤ አደራራጊ ፡ አንቀጽ ።

፻፷፯ ፤ አስተኣመረ ፥ አስተዋወቀ ፤ ያስተኣምር ፡ ያስተኣምር ፡ እያልኽ ፥ መሠሪውንም ፡ አስተኣመሮ ፡ ያስተኣምሮ ፡ እያልኽ ፡ አርባ ። ካ፭ቱ ፡ አዕማድ ፡ የሚገኙ ፡ ዐበይት ፡ አናቅጽ ፡ በየዋህ ፡ ርባታ ፡ ፻፶ ። በመሠሪ ፡ ርባታ ፡ ሺሕ ፡ ከ፪፻ ፡ ናቸው ። አርእስቶቻቸው ፥ ሣልስና ፡ ሳድስ ፡ ቅጽሎቻቸው ፤ ሳቢ ፡ ዘሮቻቸው ፡ ሳይቀሩ ፡ ንኡሳን ፡ አናቅጽ ፡ ተብለው ፡ በንኡስ ፡ ርባታ ፡ ተነግረዋል ፡ (፲፩ኛ ፡ ዕርከን) ። በምልአት ፡ የሚነገር ፡ ግስ ፡ ልኩና ፡ መልኩ ፡ ይህ ፡ ነው ።

## ፫ኛ ፡ ረድፍ ።

## ጽንዕ ፡ አንቀጽ ።

፻፷፰ ፤ የጽንዕ ፡ አንቀጾች ፡ ከነና ፡ ሀሎ ፡ ውእቱና ፡ በ ፡ ሎ ፡ እንደ ፡ ኾኑ ፡ ከናዋጃቸው ፡ ከናገባባቸው ፡ በ፰ኛ ፡ ዕርከን ፤ የመደበኛውም ፡ የሀሎ ፡ ርባታ ፡ በ፱ኛ ፡ ዕርከን ፡ ተነግሯል ። ጽንዕ ፡ የሚባል ፡ በኀላፊና ፡ በትንቢት ፡ የኾነውን ፡ እንዳልኾነና ፡ እንደማይኾን ፤ ያልኾነውን ፡ እንደ ፡ ኾነና ፡ እንደሚኾን ፡ አድርጎ ፡ የሚያሳይ ፡ የጸጸት ፡ የምኞት ፡ የፍርድና ፡ የትች ፡ አነጋገር ፡ ነው ። ይህም ፡ በንኡስ ፡ አገባብ ፡ ከእም ፡ ጋራ ፡ ገብቶ ፡ ተነግሯል ። ጽንዕም ፡ ያሰኘው ፡ አንቀጹ ፡ ዕጥፍ ፡ ድርብ ፡ ኹኖ ፡ ሲነገር ፡ የነገሩን ፡ ጥናትና ፡ ብርታት ፡ ማሳየት ፡ ነው ። አንቀጹና ፡ ርባታው ፡ ፍችውም ፡ ይህ ፡ ነው ።

### የዋህ ፡ ጽንዕ ።

አሚሮ ፡ ሀለወ ፤ ዐውቋል ፤ ዐውቆ ፡ ነበር ።
የአምር ፡ ሀሎ ፤ ያውቃል ፤ ያውቅ ፡ ነበር ።
አሚሮ ፡ የሀሉ ፡ ዐውቆ ፡ ይኖር ፡ ዘንድ ፡ እንዲኖር ፡ ሊኖር ፡
አሚሮ ፡ የሀሉ ፤ ዐውቆ ፡ ይኑር ። ኹሉን ፡ እንዲህ ፡ ፍታ ።
አሚረከ ፡ ሀሎከ ፤ ተአምር ፡ ሀሎከ ፤ አሚረከ ፡ ተሀሉ ፡ አሚረከ ፡ ሀሉ ።
አሚሮሙ ፡ ሀለዉ ፤ የአምሩ ፡ ሀለዉ ፤ አሚሮሙ ፡ የሀልዉ ።
አሚረክሙ ፡ ሀሎክሙ ፤ ተአምሩ ፡ ሀሎክሙ ።

አሚረክሙ ፡ ተሀልዉ ፡ አሚረክሙ ፡ ሀልዉ ።
አሚራ ፡ ሀለወት ፤ ተአምር ፡ ሀለወት ፤ አሚራ ፡ ተሀሉ ።
አሚረኪ ፡ ሀሎኪ ፤ ተአምሪ ፡ ሀሎኪ ፤ አሚረኪ ፡ ተሀልዊ ፡ ሀልዊ ።
አሚሮን ፡ ሀለዋ ፤ የአምራ ፡ ሀለዋ ፤ አሚሮን ፡ የሀልዋ ።
አሚረክን ፡ ሀሎክን ፤ ተአምራ ፡ ሀሎክን ፤
አሚረክን ፡ ተሀልዋ ፡ አሚረክን ፡ ሀልዋ ።
አሚርየ ፡ ሀሎኩ ፤ አአምር ፡ ሀሎኩ ፤
አሚርየ ፡ አሀሉ ፡ አሚርየ ፡ አሀሉ ።
አሚረነ ፡ ሀሎነ ፤ ነአምር ፡ ሀሎነ ፤ አሚረነ ፡ ነሀሉ ።

መሠሪ ፡ ጽንዐ ።

፻፷፱ ፤ አሚሮሁ ፡ ሀለወ ፤　　ዐውቆታል ፤ ዐውቆለታል ፤ ዐውቆበታል ፤ ዐውቆት ፡ ዐውቆለት ፡ ዐውቆበት ፡ ነበር ።

የአምሮ ፡ ሀሎ ፤　　ያውቀዋል ፤ ያውቅለታል ፤ ያውቅበታል ፤ ያውቀው ፡ ያውቅለት ፡ ያውቅበት ፡ ነበር ።

አሚሮሁ ፡ የሀሉ ፡　　ዐውቆት ፡ ዐውቆለት ፡ ዐውቆበት ፡ ይኖር ፡ ዘንድ ፡ እንዲያውቀው ፡ ሊያውቀው ፡ ሊያውቅለት ፡ በት ፡

አሚሮሁ ፡ የሀሉ ፤　　ዐውቆት ፡ ዐውቆለት ፡ በት ፡ ይኑር ።

አሚሮከ ፡ ሀለወ ፤ የአምረከ ፡ ሀሎ ፤ አሚሮከ ፡ የሀሉ ።

አሚሮሆሙ ፡ ሀሎ ፤ የአምሮሙ ፡ ሀሎ ፤ አሚሮሆሙ ፡ የሀሉ ።

አሚሮክሙ ፡ ሀለወ ፤　ኹሉን ፡ እንዲህ ፡ እያልኽ ፡ እስከ ፡ ፲ ፡ አርባ ። በቀሩትም ፡ ባራቱ ፡ አዕማድ ፡ በያንዳንዱ ፡ ኹሉ ፡ እስከ ፡ ፲ ፡ እንዲሁ ፡ ይዘምታል ። ውእቱም ፡ ጽንዐ ፡ እየኾነ ፡ ሀሎ ፡ በገባበት ፡ ሲገባ ፡ በኀላፊና ፡ በትንቢት ፡ ብቻ ፡ ይነገራል ፤ አንቀጽነቱ ፡ ነባር ፡ ስለ ፡ ኾነ ፡ እንደ ፡ ሀሎ ፡ ዘንድና ፡ ትእዛዝ ፡ የለውም ። ይህም ፡ ዐዊቆ ፡ ውእቱ ፡ የዐውቀ ፡ ውእቱ ። ዐዊቀከ ፡ አንተ ፡ ተዐውቀ ፡ አንተ ፡ እያሰኘ ፡ ዐውቀኻል ፡ ዐውቀኽ ፡ ነበር ፡ ታውቃለኽ ፡ ማለቱን ፡ ያሳያል ።

፩ኛ ፡ ረድፍ ።

አሉታ ፡ አንቀጽ ።

፻፸ ፤ ኢአመረ ፤　　አላወቀም ።
ኢየአምር ፤　　አያውቅም ።
ኢይእምር ፡　　እንዳያውቅ ፡ ላያውቅ ፡ ሳያውቅ ፡
ኢይእምር ፤　　አይወቅ ። ኹሉን ፡ እንዲህ ፡ ፍታ ።　በጽድቅ ፡ አንቀጽ ፡ አ ፡ የነበረውን ፡ የአነን ፡ ሥርወ ፡ ትንቢት ፡ ብቻ ፡ ኢ ፡ ስትወድቅበት ፡ የ ፡ ይወርሰዋል ። ይህም ፡ ኢአመርኩ ፡ ብሎ ፡ ኢየአምር ፡ ኢይእምር ፡ ኢይእምር ፡ እያለ ፡

እንደ፡ሩቁ፡ወንድ፡መኼዱን፡ያሳያል ። ዳግመኛም፡የ፪ኛና፡ያ፫ኛ፡ዐምድ፡ልማዳቸው፡አ፡በኢ፡ምክንያት፡ያ፡ይኸናል ። ይህም፡ኢያእመረ፡ኢያአምር፡ኢያእምር፥ኢያእምር ። ኢያስተአመረ፡ኢያስተአምር፡ኢያስተአምር፡እያለ፡ሌላውን፡ኹሉ፡ያሳያል ። ቦዝ፡አንቀጹንም፤ኢአሚሮ፡ኢአሚረከ፡ብሎ፥ሳያውቅ፡ሳታውቅ፡ያሰኛል ። የቀረውን፡ዐዋጅ፡ተመልሰኽ፡በርባ፡ቅምርና፡በጸዋትወ፡ርባ፡ተመልከት ።

፪፻፩፤ የአኃዝም፡ጥሬ፡ካንድ፡እስከሥር፡ያለው፡ኹሉም፡እያንዳንዱ፡ባ፲፡ባ፲፡መደብ፡ሲረባ፡ወይም፡ሲዘረዘር፥ርባታውና፡ዝርዝሩ፡ባጭር፡ቃል፡ይህ፡ነው ።

## ጅምላ፡ቍጥር ።

አሐድ፡አሐዱ፡አሐዳ፡አሐዶሙ፡አሐዶን፤አሐድከ፡አሐድኪ፡አሐድክሙ፡ክን፡የ፡ነ ። ክልኤ፤ክልኤሁ፡ሃ፡ሆሙ፡ሆን፤ክልኤከ፡ኪ፡ክሙ፡ክን፡የ፡ነ ። ክልኤት፤ክልኤቱ፡ታ፡ቶሙ፡ቶን፤ክልኤትከ፡ኪ፡ክሙ፡ክን፡የ፡ነ ። ኹሉን፡እስከ፡ዐሥርት፡እንዲሁ፡አርባ፤ስትፈታም፡አንዱ፥የርሱ፡አንድ፤ኹለቱ፥የርሱ፡ኹለት፡እያልኽ፡እስከ፡ንሕነ፡ፍታ ። ዐይነ፡ምስጢሩም፡ሲገለጥ፥ቍጥሩ፡ገንዘብን፥ዝርዝሩ፡ባለገንዘብን፡ያሳያል ። በተራ፡ቍጥር፡ግን፥መነሻውን፡ራብዕ፡አድርጎ፥ኣሐድ፡ዱ፤ካልእ፡ኡ፤ዓሥር፡ሩ፡እያለ፥አንደኛው፥ኹለተኛው፥ዐሥረኛው፡ያሰኛል ። ከዚህ፡የቀረውን፡በአኃዝ፡ቅጽል፡ተመልከት ።



መዐዛ ፡ ሰዋስው ፡ ዕጣን ፡ ወጼና ፡ ትምህርት ፡ ከርቤ ፥
ለእለ ፡ ያጼንዉ ፡ ምክረ ፤ ወይሰምዑ ፡ ዘይቤ ፤
የግጥም ፡ ስብከት ፥ ወይም ፡ ይባቤ ።

በዶሮ ፡ ሥጋ ፡ አምሳል ፡ ምስጢሩ ፡ እንዲጥም ፡
ዐጽሬ ፡ ረኀሚ ፡ ይባላል ፡ ግጥም ፤
ዐጽሬው ፡ ሰዋስው ፡ ረኀሚው ፡ ግስ ፡
የሦስት ፡ ፊደል ፡ ሥጋ ፡ የርባ ፡ ቅምር ፡ ነፍስ ፤
ለልጆች ፡ እንዲተርፍ ፡ ያዋቆች ፡ መብል ፡
ያቡን ፡ ወጥ ፡ በሚሉት ፡ በተማቲም ፡ ቃል ፡
ሠርቶ ፡ ያቀረበው ፡ የግእዝ ፡ ወጥ ፡ ቤት ፡
ላስነባቢው ፡ ምሳ ፡ ላንባቢው ፡ እራት ።

ለወጣቶች ፡ ኹሉ ፡ ከታች ፡ ወደ ፡ ላይ ፡
ሰዋስው ፡ እንጂ ፡ ነው ፡ መንገደ ፡ ሰማይ ፡
ያዕቆብና ፡ ዕዝራ ፡ የግዜር ፡ ጉበኞች ፡
ቀድሞ ፡ የሰለሉት ፡ ከላይ ፡ እስከ ፡ ታች ።

የሰዋስው ፡ ትምርት ፡ ሥጋውና ፡ ዐጥንቱ ፡
ባጽሬው ፡ ተከቷል ፡ ረኀሚነቱ ።
ላንቀጹ ፡ ፍልሰታ ፡ ለርባታው ፡ ሐዳጼ ፡
የተለቀመውን ፡ ጥሩ ፡ ፊደል ፡ ስንጼ ፡
አስተውል ፡ ተመልከት ፡ ጸሓፊና ፡ አንባቢ ፡
ያማርኛ ፡ ገበዝ ፡ የግእዝ ፡ ዐቃቢ ።

የግእዝን ፡ ትምርት ፡ አባይን ፡ በጽልፉ ፡
ቀድቶ ፡ የሚጨርስ ፡ ማነው ፡ ባለተስፉ ፤
ቀድቶም ፡ ባይጨርሰው ፡ ከርሱ ፡ ለሚጠጣ ፡
ለሚሻገረውም ፡ እየተቀናጣ ፡
ካዋቆች ፡ ራስ ፡ ቅል ፡ የተከፈለው ፡
ፋጋውና ፡ ሚጼው ፡ እንሆ ፡ ይኸው ።
ዐዘውም ፡ ስንፍና ፡ ተማሪ ፡ እንዳይነጥቅ ፡
ዋነተኛው ፡ መምህር ፡ ተግቶ ፡ ይጠብቅ ።
በቀለም ፡ ገበያም ፡ ጣፊው ፡ ብር ፡ ሲቀርጥ ፡
ፊደሉ ፡ እንዳይሸጥ ፡ እንዳይለወጥ ።

ነቢያት ፡ የዘሩት ፡ የፊደላት ፡ ገብስ ፡
ስሙ ፡ ልጅ ፡ አልቅሶ ፡ ቶሎ ፡ የሚደርስ ፤

ገብሱም ፡ ደረቅ ፡ ትንቢት ፡ ገበሬው ፡ ዘመን ፡
ዐጭዶና ፡ ከምሮ ፡ ያሳየን ፡ አኹን ።

ነዶውም ፡ ክምሩም ፡ የጎግ ፡ ማጎግ ፡ ሥጋ ፡
ለአዕዋፍ ፡ መርዔት ፡ ለአራዊት ፡ መንጋ ፡
እግዜር ፡ የወሰነው ፡ በሕዝቅኤል ፡ አፍ ፡
ሰባት ፡ ዓመት ፡ ብሎ ፡ መንፈቅ ፡ ሳያተርፍ ።

ይህም ፡ ሰባት ፡ ዓመት ፡ ዘመነ ፡ ማእረር ፡
ከበጉ ፡ ዐይንና ፡ ቀንድ ፡ የሚተባበር ፤
የግእዝም ፡ ፊደል ፡ በሰባትነቱ ፡
ከትንቢት ፡ ከራእይ ፡ ወየው ፡ መስማማቱ ።

ጊዜ ፡ በስረገጠው ፡ በትምርት ፡ ዐውድማ ፡
ተንጣሎ ፡ ነበረ ፡ የግእዝ ፡ ምርትማ ፤
ፈልገን ፡ ስላጣን ፡ ዐፋሽ ፡ አጕንባሽ ፡
ድካማችን ፡ ኹሉ ፡ እንዳይቀር ፡ ብላሽ ፡
ከምርቱ ፡ ቈንጥረን ፡ ይህን ፡ ሰዋስው ፡
ስሙን ፡ ለኋላ ፡ ልጅ ፡ ዘር ፡ ይኹን ፡ አልነው ።

የዛሬማ ፡ ልጆች ፡ ብስሉን ፡ ግእዝ ፡ ቋንቋ ፡
ባለመማራቸው ፡ አስመሰሉት ፡ ጨርቋ ፤
ጠጅ ፡ ነውም ፡ ብለን ፡ ብንሰጣቸው ፡ ቅሉ ፡
እንደ ፡ ጌታ ፡ ቀምሰው ፡ መጠጣት ፡ እንቢ ፡ አሉ ።
አጥብቆ ፡ ጠያቂም ፡ ሲመረምራቸው ፡
ስለ ፡ ግእዝ ፡ ቋንቋ ፡ ይህ ፡ ነው ፡ ምላሻቸው ፤

ምንም ፡ ቢንደረከክ ፡ የሴም ፡ ቋንቋ ፡ ፍሕም ፡
እንደ ፡ ያፌት ፡ ከኛክ ፡ ሆድ ፡ አያሞቅም ፤
ስለ ፡ ሥጋ ፡ ጥበብ ፡ ስለ ፡ ደመወዝ ፡
ከኛኩ ፡ ይሻላል ፡ ከጠጁ ፡ ግእዝ ።

አብዝቶም ፡ ሲጠጡት ፡ በሽልም ፡ ፊደል ፡
ሆድ ፡ ስላላሞቀ ፡ ጠላ ፡ ነው ፡ ብንል ፡
አያስነቅፈንም ፡ በዛሬው ፡ ክረምት ፤
መስከረም ፡ ሲጠባ ፡ እንጃ ፡ ምናልባት ።

የመለኪያውም ፡ ስም ፡ አፈ ፡ ድስቱ ፡ ግብጥ ፡
ማብረጃ ፡ ይባላል ፡ ሙቀት ፡ እንዳይሰጥ ፤
ከማኽልም ፡ ገብቶ ፡ እንደ ፡ ሰው ፡ ቢቆም ፡
ዐላፊ ፡ አሳላፊ ፡ መኾን ፡ አልቻለም ።

ዐላፊም ፡ ከሌለው ፡ ለቋንቋ ፡ ትምርት ፡
ራስ ፡ የነበረው ፡ ይኾናል ፡ ዥራት ።

ብርሃኑ ፡ ጠፍ ፡ ኹኖ ፡ የግብጥ ፡ ጨረቃ ፡
ስንኳን ፡ ለኛ ፡ ይተርፍ ፡ ለራሱም ፡ አልበቃ ፤
እስላሞች ፡ ሳይቀሩ ፡ የሚሰዮን ፡ ዦግና ፡
ሕዝቡን ፡ እንደ ፡ ምርከ ፡ ተከፍሎታልና ።

የውጭ ፡ አገር ፡ ጳጳስ ፡ ርባታው ፡ ሕጹጽ ፥
የገንዘብ ፡ ሳቢ ፡ ዘር ፡ ወይም ፡ በዝ ፡ አንቀጽ ፤
ዘርፉና ፡ ቅጽሉም ፡ ባዕድ ፡ አታላይ ፡ ስም ፡
የማይስማማ ፡ ከግእዝ ፡ ቀለም ።

ስለ ፡ ቋንቋ ፡ ትምርት ፡ መንገድና ፡ አካኼድ ፤ ስለ ፡ ተማሮችም ፡ አረማመድ ።

ዐጭሬ ፡ ግጥም ፡ ቁመተ ፡ ዶሮ ፡ — የሚንጠራራ ፡ ወደ ፡ ሰው ፡ ዦሮ ፡
ቸብቸቦው ፡ ዜማም ፡ ሳይቈረጥ ፡ — በየመሥመሩ ፡ የሚያስረግጥ ፤
ባልተኛ ፡ አዝማሪም ፡ መስሎ ፡ ሲያሥቅ ፡ እንዳቤሴሎም ፡ ልብ ፡ የሚሰርቅ ።

ክቡደ ፡ መዝራዕት ፡ ኀይለ ፡ ሥላሴ ፡ አባት ፡ ኹኗቸው ፡ እንደነሙሴ ፡
ከተረገዙት ፡ በመንግሥት ፡ ሆድ ፡ — ከታዘሉትም ፡ በባንዲራ ፡ ለምድ ፡
ሞግዚታቸውም ፡ ዐዲሳበበ ፡ — ካቀፈቻቸው ፡ በክንዷ ፡ ስባ ፡
አንድ ፡ እንኳ ፡ ሳይቀር ፡ ኹሉን ፡ ሰብስቤ ፡ ዐጥናቸዋለሁ ፡ የምክር ፡ ክርቤ ።

ባንድነት ፡ ደንጊያ ፡ በኅብረት ፡ ዕፅ ፡ መቅደስ ፡ ልባቸው ፡ እንዲታነጽ ፤
ኋላም ፡ እንዳይፈርስ ፡ በጠላት ፡ በንብ ፡ ሃይማኖታቸው ፡ የወንጌል ፡ ግንብ ።
እንደ ፡ ፫ ፡ አካል ፡ የተካከሉ ፡ — ስለ ፡ ኅብረትም ፡ አንድ ፡ የሚባሉ ፡
፫ቱን ፡ ጉባኤ ፡ ምሰሶ ፡ አቁሞ ፡ — እግዜር ፡ የሠራው ፡ ከኛ ፡ አስቀድሞ ።

የምክሩም ፡ ክርቤ ፡ ኹለት ፡ ቈቀር ፡ በመቀነት ፡ ልብ ፡ የሚቋጠር ፥
ቍጥሩም ፡ ተገልጦ ፡ ሲታይ ፡ ሲፈታ ፡ ሽታው ፡ የሚነድፍ ፡ ልብ ፡ የሚመታ ፤
ገንዘብነቱም ፡ የቤተ ፡ ክሲያን ፡ — የሚቀበለው ፡ ገበዝ ፡ ሕፃን ፤
ስጭውም ፡ ለጋስ ፡ አቶ ፡ መንግሥቱ ፥ ርሱ ፡ ነውና ፡ በለስለቱ ።

፩ኛ ፡ ቈቀር ፡ ዕጣነ ፡ ሞገር ፥ ልጅ ፡ ዐዋቂውን ፡ ከግእዝ ፡
እንደ ፡ ድጕስና ፡ እንደ ፡ ጥራዝ ፡ የሚያጣብቅና ፡ የሚያያይዝ ።
ዘገሰሰ ፡ ፒሳ ፡ ይትአኀዝ ፡ ቦቱ ፡ (ሢራ ፲፫ ፡ ፩) ።

ስሕ ፡ ጣይቱ ፡ የግእዝ ፡ ቋንቋ ፡ — ዐማርኛዋም ፡ ኮከብ ፡ ጨረቃ ፤
ፊደሏ ፡ ብርሃን ፡ ዘእምብርሃን ፡ — ሰባት ፡ ቍልጭልጭ ፡ የግዜር ፡ በግ ፡ ዐይን ።
ግእዝ ፡ ግእዙ ፡ ወርቅ ፡ ቀለም ፡ — ባለ፯ ፡ ዐጽቅ ፡ ጕንደ ፡ ተቋም ፤
ስድስቱም ፡ ዐጽቆች ፡ ግራና ፡ ቀኙ ፡ — ከሱራፌል ፡ ክንፍ ፡ የተሰናኙ ።

ከኪሩቤልም፡ካራቱ፡ኹሉ፡ — በራብዕ፡ትውልድ፡ይዛመዳሉ÷
በሣልሱማ፡ኀይለ፡ሥላሴ፡ — ኹሉን፡ያገባል፡ወደ፡ቅዳሴ፤
ከ፼፡ቍጥር፡አንዱ፡ቢጐድል፡ — ቅዳሴው፡እሳት፡ይዳፈናል ።

የመላእክትም፡ጥንተ፡ልሳን፡ — ያጠራጥራል፡ርሷ፡እንዳትኾን፤
የፊደሏ፡ምንጭ፡ዐይነ፡ውሃው፡ — ከላይ፡ነውና፡የፈለቀው ።

ከሣር፡ከቅጠል፡በዝቶ፡ጊዜዋ፡ — አሮጊት፡ስትኾን፡በተፈጥሮዋ፡
እንደ፡ሔኖክ፡ንስር፡ሕዋሳቶች፡ — በተሐድሶ፡ስለ፡ኖረች፡
ዐይንና፡ጥርሷ፡ብሉይ፡ሐዲስ፡ — ነጭና፡ጥቍር፡የሚያጣቅስ ።

ዠርባዋም፡ንባብ፡እንደ፡ሰሎሜ፡ — ጌታን፡ያዘለው፡በሰው፡ትርጓሜ፤
ጡቷም፡ደረቷም፡ባለሳንቃው፡ — እንደ፡ማርያም፡የታቀፈው፡
ለመምህራንም፡ላረገዙት፡ — መወልዲት፡ናት፡መወልዲት ።

ጌታም፡ለሄኖስ፡ሲድራት፡በርኮ፡ ስላረገዘች፡የርሱን፡አምልኮ፡
ከአልፍ፡እስከ፡ታው፡መልኳ፡ፊደል፡ የሥነ፡ፍጥረት፡ጠቅላይ፡መድበል፤
የመልኳም፡ድርሰት፡በማሕልይ፡ — ተጥፎለታል፡ደግሞ፡ለሚያይ ።
እንደ፡ወጌሻ፡ገላ፡እንደሚያሽ፡ — እንደ፡ሐኪምም፡እንደ፡ፈታሽ፡
ኹለንተናዋን፡ቀምለን፡አይተን፡ — ስላጣንበት፡ነውር፡እንከን፡
መስለናታል፡በጥሩ፡ዐይናማ፡ — ከወጣቶች፡ልብ፡እንድትስማማ፤
ዐይናማነቷም፡ከገጸ፡ንስር፡ — የወረደ፡ነው፡በፊደል፡ዘር ።

ዐይኗን፡ስትገልጠው፡ከጥርሷ፡ጋራ፡ አስተያየቷ፡በቀኝ፡በግራ÷
ስትናገርም፡በፊት፡በኋላ፡ — ከኈ፡ይፈሳል፡የማር፡ወለላ፤
ልሳኗም፡ጥዑም፡የወይን፡እሸት፡ — እየተሻሙ፡የሚበሉት ።

ከአዳም፡ከኖኅ፡ካባት፡ከናቷ፡ — ለሴም፡የታጨች፡ስለ፡ውበቷ፡
ከንጉሡም፡ከግዜር፡ከባለቤቱ፡ — ስለ፡ተሰጣት፡እቴጌነቱ፡
ምንም፡ቢያጅቧት፡መኳንንቶች፡ — ዐይኗና፡ልቧ፡ከተማሮች ።

እኔም፡ልጨፍር፡ቃሌን፡ላንሣው፡ ተማሪን፡ኹሉ፡ደስ፡እንዲለው፤
የተጌ፡አሽከሮች፡የንጉሡም፡ጭፍራ፡ ወንድሞቼ፡ሆይ፡ትግሬና፡ዐማራ፡
እንዲህ፡ብታይዋት፡ድኻ፡መስላችኹ፡ ባለጸጋ፡ናት፡ግእዝ፡ቋንቋችኹ ።

የግምጃ፡ቤቷ፡ባሕር፡መዝገብ፡ — ዕብራይስጥና፡ሱርስት፡ዐረብ÷
በዥርወንዶቿም፡ነገደ፡ሴም፡ — የተሠራጨት፡በምድረ፡ካም፤
ታሪኳም፡ቈንዦ፡ስሙ፡ብርሃነ፡ — በምሥራቅ፡ቋንቋ፡የሠለጠነ ።

ማነው፡የሚላት፡ድኻ፡ምስኪን፡ ካላዩት፡በቀር፡ገብተው፡ውስጧን፤
ማእዷም፡ትምርት፡እንዲህ፡መስፋቱ፡ ልትበሉለት፡ነው፡መቼ፡ለከንቱ ።

ባዕዶቹ፡ነጮች፡ሲሻሙባት፡ — ምነው፡እናንተ፡የማትደፍሯት÷
ደፈሩኝ፡ብላም፡እንዳትከሳችኹ፡ — እኔ፡ስለ፡ርሷ፡ልማልላችኹ፤
ከምትገዛቸው፡ባስበ፡ተፈሪ፡ — እኔ፡ነኝና፡አንዱ፡አቃጣሪ ።

ደፍሮ ፡ አለመቅመስ ፡ እየከጀሉ ፡ — የጐደሎ ፡ ነው ፡ መቼ ፡ የሙሉ ።
ደፋር ፡ ወንድ ፡ እንጂ ፡ ልቧን ፡ የሚያግም ፡ የከንፈር ፡ ወዳጅ ፡ አላጣችም ።

በውበት ፡ በመልክ ፡ ግእዝ ፡ ሙሽራ ፡ ልዩ ፡ ስትኾን ፡ ከጋላ ፡ ዱብራ ፡
በፉ ፡ ሊሸኛት ፡ ከንፈሯን ፡ ለክፎ ፡ — አይገበውም ፡ ለጦቢያው ፡ ለፎ ።

በለፈው ፡ ዘመን ፡ ከቀን ፡ ጨለማ ፡ — ዐይናማነቷ ፡ ስላልተስማማ ፡
የሌበው ፡ አከን ፡ ልሳነ ፡ ወርቅ ፡ — ሰው ፡ እንዳስፈጀች ፡ በመደበቅ ፡
የደፈሯትን ፡ ለንጉሡ ፡ ነግሯ ፡ — ታስቄርጥ ፡ ነበር ፡ ምላስ ፡ በከራ ፤
ያልተቈረጠው ፡ ከገር ፡ ተሰዶ ፡ — እስኪንከራተት ፡ በፍሪቃ ፡ ማዶ ።

እንደ ፡ ሙሴ ፡ ፊት ፡ እንደ ፡ ምዠራብ ፡ እንደ ፡ ቱርክም ፡ ሴት ፡ እንደ ፡ ዐረብ ፡
አብነት ፡ ነሥታ ፡ ከበር ፡ ማሸላ ፡ — ባቡን ፡ በጨጌ ፡ ድርብ ፡ ቀጻላ ፡
ትወድ ፡ ነበር ፡ መሸፋፈን ፡ — ልቧ ፡ ሳይጠላው ፡ መገለጡን ።

እንዳትታይም ፡ በመሸፈኗ ፡ — አልተጠቀመም ፡ ቀዳዳው ፡ ዐይኗ ÷
ከርሷ ፡ የታማው ፡ አንዳንዱ ፡ ዠግና ፡ ታስሮ ፡ ሲገረፍ ፡ ታይ ፡ ነበረና ፤
ዳግመኛ ፡ እንዳያይ ፡ ዐይኗን ፡ መጽሐፍ ፡ እስኪከልሉት ፡ በጃቸው ፡ ሰይፍ ÷
ለከተማውም ፡ ላይነ ፡ ስውሩ ፡ — ብርሃን ፡ እስኪታይ ፡ በመቃብሩ ።
ብርሃንም ፡ ታይቶ ፡ ስላሳፈረ ፡ — ከማሰር ፡ በቀር ፡ መሰየፍ ፡ ቀረ ፤
በፖዝያንም ፡ በባለሰይፉ ፡ — ለምጽ ፡ ኾነበት ፡ ማሰር ፡ መግረፉ ፤
በተራራ ፡ ላይ ፡ የሠሩት ፡ ግፍ ፡ — አይሰወርም ፡ ከታሪክ ፡ አፍ ።

ስለ ፡ ሃይማኖት ፡ በመሞት ፡ ፈንታ ፡ መግደል ፡ መሰየፍ ፡ የቍርአን ፡ ዛንታ ÷
ረቂቁማ ፡ የወንጌል ፡ ፍርድ ፡ — መታረድ ፡ ነበር ፡ መቼ ፡ ማረድ ፤
ቀኑ ፡ ጨልሞ ፡ በደባበይ ፡ — ያያት ፡ ሰው ፡ የለም ፡ ርሷ ፡ ስታይ ።

ዛሬ ፡ ግን ፡ ዐፍራ ፡ እንደ ፡ ነጮች ፡ የቀድሞ ፡ ግብሯን ፡ ስለ ፡ ተወች ፡
መጋረጃዋም ፡ በታምራት ፡ — ከላይ ፡ እስከ ፡ ታች ፡ ተቀዶላት ፡
ወደ ፡ ነጻነት ፡ ዐይኗን ፡ አሻግራ ፡ — ኹሉን ፡ ታያለች ፡ እንደ ፡ ዲበራ ።

ቅዱስ ፡ መጽሐፍም ፡ በርሷ ፡ ዐማርኛ ፡ ከግዜር ፡ ተልኮ ፡ መጣ ፡ ዳግመኛ ÷
የትምርቷን ፡ ወንዝ ፡ አለወረፉ ፡ — ኹሉ ፡ እንዲቀዳ ፡ እየተስፋፋ ፤
ርሷም ፡ ጣይቱ ፡ መሐንድስ ፡ ኹና ፡ — እየቀየሰች ፡ የሰው ፡ ልቡና ፡
ወጣት ፡ ወጣቱን ፡ ለመቀበል ፡ — አዘጋጅታለች ፡ ቤቷን ፡ ፊደል ።

የግእዝን ፡ ጣዕም ፡ ብትቀምሱትማ ፡ አትቷዙም ፡ ነበር ፡ ሌላ ፡ ውሽማ ፤
ለንግዴሁ ፡ ግን ፡ ውሽማ ፡ አታብዙ ፡ ርሷን ፡ ዐቅፋችኹ ፡ ቀድሞ ፡ ሳትቷዙ ።

ብትጨምሩ ፡ ግን ፡ በርሷ ፡ ላይ ፡ ደግሞ ፡ ዕዳው ፡ ገብስ ፡ ነው ፡ መች ፡ ዐረማሞ ፤
በዚህስ ፡ ነገር ፡ ሐሜት ፡ ሳትፈሩ ፡ — እንደ ፡ ያዕቆብ ፡ ብትጨማምሩ ፡
ስንኳን ፡ ነቢያት ፡ እነዳዊት ፡ — አይነቅፏችኹም ፡ ሐዋርያት ።

## አሥረ ፡ ንጉሥ ፡ ጠቢብ ፡

### ኋላፍያትን ፡ የሚያዘክር ፡ መጻእያትን ፡ የሚያሳስብ ።

ዓሣ ፡ ጕርጓሪ ፡ ዘንዶ ፡ ሲያወጣ ፡ — የሰው ፡ ፈላጊም ፡ የራሱን ፡ ሲያጣ ፡
ከኹለቱ ፡ ዛፍ ፡ ለወደቀው ፡ — አላገር ፡ ቋንቋ ፡ ማነው ፡ አንሺው ።

የሀገር ፡ ቋንቋም ፡ ያላማ ፡ ቀኝ ፡ — ኹሉን ፡ ሰብስቦ ፡ አንድ ፡ የሚያሰኝ ፥
ጋላና ፡ ዐማራ ፡ እስላም ፡ ሳይል ፡ — የፈረስ ፡ ስሙ ፡ አባ ፡ ጠቅል ፤
አባ ፡ ቀስቅስም ፡ የሚሉት ፡ አሉ ፡ — ስላነቃቸው ፡ ጠርቶ ፡ ፊደሉ ።

እኛም ፡ ተኝተን ፡ ሕልም ፡ እንዳናልም ፡ አባ ፡ ነጋ ፡ ነው ፡ የጊዜው ፡ ስም ፤
የፀሓይ ፡ መቅድም ፡ አጥቢያ ፡ ኮከብ ፡ — የሚታይበት ፡ ላፍሪቃ ፡ ሕዝብ ፥
የጠቢያውም ፡ ልጅ ፡ የሴም ፡ ቡችላ ፡ — የሚከፍትበት ፡ ያይኖቹን ፡ ግላ ፤
አፍሪቃን ፡ ያይ ፡ ዘንድ ፡ ባይኑ ፡ ማሚቶ ፡ እየቀመለ ፡ እንደ ፡ ድሪቶ ።
አንዳንድ ፡ ጊዜ ፡ እኮ ፡ የትንቢት ፡ ቃል ፡ ሳይታወቅ ፡ ነው ፡ በጥለቅ ፡ የሚል ።

ቋንቆቻችንም ፡ ባልና ፡ ሚስት ፡ — ርስ ፡ በርሳቸው ፡ የሚፋቱት ፥
ላይለያዩ ፡ ተለያይተው ፡ — ያሻማቱናል ፡ ኹለት ፡ መስለው ፤
ከቶ ፡ እኛ ፡ አንችልም ፡ ልንለያቸው ፡ — እግዜር ፡ ነውና ፡ ያጣመራቸው ።
ነፍስና ፡ ሥጋ ፡ ከተለያዩ ፡ — ሕያው ፡ እንዳይኾን ፡ የሰው ፡ ባሕርዩ ፡
ያማርኛም ፡ ቃል ፡ የግእዝ ፡ ሥጋ ፡ — አለግእዝ ፡ ነፍስ ፡ ሬሳ ፡ ባልጋ ፤
ሬሳውን ፡ ቃል ፡ የሚሸከሙ ፡ — በግእዝ ፡ ቋንቋ ፡ ሲፈታ ፡ ይስሙ ።

ሥረ ፡ ነገሩ ፡ ግእዝ ፡ ሳይጸድቅ ፡ — ፍሬ ፡ አያፈራም ፡ ዐማርኛ ፡ ዐጽቅ ።
ነገር ፡ ከሥሩ ፡ ውሃ ፡ ከጥሩ ፡ — የተባለውን ፡ እስኪ ፡ መርምሩ ፤
እነማናቸው ፡ ዛፉን ፡ ሳያውቁ ፡ — ፍሬውን ፡ በልተው ፡ የሚጨነቁ ፥
ዛፉንም ፡ ዐውቀው ፡ ሳይገላልጡ ፡ — ሾላ ፡ በድፍን ፡ የሚያላምጡ ፤
አለበትና ፡ ብዙ ፡ ቍጫጭ ፡ — ሆድ ፡ የሚያሳምም ፡ የሚያበሳጭ ፤
ቄስ ፡ ኹኜ ፡ ቢኾን ፡ ወይም ፡ ዲያቆን ፡ — አጠራው ፡ ነበር ፡ ስማቸውን ።

ዳቦ ፡ የሚልስ ፡ ካልገመጠው ፡ — መላሱ ፡ ብቻ ፡ ምን ፡ ሊያጠግበው ፤
አፍ ፡ አለዠሮ ፡ ቢያዜም ፡ ቢያነብ ፡ — አይታነጽም ፡ ሸካራው ፡ ልብ ፥
መርጌታ ፡ ኹኖ ፡ አቡን ፡ ሲቃኝ ፡ — እንዲህ ፡ እንዳለ ፡ አምጃር ፡ ዘፉኝ ፤

የጠቢያው ፡ ሰው ፡ እንዲያው ፡ ላይ ፡ ላዩን ፥ ውስጡን ፡ ለምን ፥
ውስጡን ፡ ለቄስ ፡ ለሚናዝዝ ፥ ቄሱም ፡ ግእዝ ፤
ስሙ ፡ ፋና ፡ ወይም ፡ መብራት ፡ የነፍስ ፡ አባት ።

እንዶድ ፡ ሳይዙ ፡ ወይም ፡ ሳሙና ፡ — አጥርቶ ፡ ማጠብ ፡ ዘበት ፡ ነውና ፡
አለሰዋስው ፡ አለጥፈት ፡ — ትምርት ፡ አይጠሬም ፡ ምንም ፡ ቢያጥቡት ፡

የትምርት ፡ ዕንቅርት ፡ አለመጣፍ ፥ — አለመስማትም ፡ ዠሮ ፡ ደግፍ ፤
ዐንገት ፡ ላለው ፡ ሰው ፡ ዙሮ ፡ ለሚያይ ፡ ከበድ ፡ ሸክም ፡ ነው ፡ እንደ ፡ ድንጋይ ።

ያኖሩት ፡ ዕንቅርት ፡ ስሙ ፡ አገልግል ፡ ቢከፍቱ ፡ ተልባ ፡ ፍሬ ፡ ቢስ ፡ ቅል ፤
ያለፈው ፡ ዐልፏል ፡ ለወደ ፡ ፊቱ ፡ — በትምርት ፡ ይራቅ ፡ ግብዝነቱ ፡፡

ካፍሪቃ ፡ ወንዞች ፡ ወርቅና ፡ አልማዝ ፡ እንደሚያስገኘው ፡ እንዳባይ ፡ ወንዝ ፡
ተርፎን ፡ እንዲፈስ ፡ ትምርቱ ፡ ንግድ ፡ — በዚህ ፡ ሰዋስው ፡ ጥርጊያ ፡ መንገድ ፡
ይልቅ ፡ ኑ ፡ እንውጣ ፡ ወደ ፡ ገበያ ÷ — ገበያችንም ፡ ኢትዮጵያ ፡፡

መደብሮቿ ፡ የተዘጉቱ ፡ — ባራቱ ፡ ማእዘን ፡ እንዲከፈቱ ፡
ልጆቿን ፡ በውቀት ፡ እያሳደገ ፡ — መንገዶቿንም ፡ እያስጠረገ ፡
እግዜር ፡ ያቆማት ፡ ከማኸል ፡ በታ ፡ — በውጭ ፡ አገር ፡ ሰው ፡ እንዳትፈታ ፡፡

ያፍሪቃ ፡ ደንደስ ፡ ሻኛና ፡ ጫንቃ ፡ — ጦቢያው ፡ እንጂ ፡ ናት ፡ ምሥራቅ ፡ አፍሪቃ ፤
የሰማይ ፡ ምድር ፡ የምድር ፡ ሰማይ ፡ — የተከበበች ፡ በነጭ ፡ አባይ ፡፡

ዐይኗም ፡ ሲመሰል ፡ በገነት ፡ ዐይን ፡ ነጩ ፡ አባይ ፡ መደብ ፡ ጥቍሩ ፡ ብሌን ፤
ባስተያየትም ፡ ሲመረመሩ ፡ — ማየት ፡ አይችልም ፡ ነጩ ፡ አለጥቍሩ ፡፡
ነጩ ፡ ሲፈተሽ ፡ ውስጠ ፡ ጥቍር ፡ — ጥቍሩም ፡ ሲፈተሽ ፡ ውስጠ ፡ ነጭ ፡ ዘር ፤
ሕብረ ፡ ሰማይ ፡ ነው ፡ ጥቍሩ ፡ አባይማ ፡ በቂጥኛም ፡ አፍ ፡ የማይታማ ፡፡

ነጭና ፡ ጥቍር ፡ የዓለም ፡ ዐይን ፡ — ኹሉም ፡ ተገልጦ ፡ የሚከድን ፤
መከደኛውም ፡ ሞት ፡ ወዝ ፡ ከንባይ ፡ ነው ÷ ያዳም ፡ ሌባ ፡ ጣት ፡ የሰሩችው ፡፡

## ዓዲ ፡ ቃለ ፡ ዐዋዲ ፡

### መስቌረ ፡ ጥይዕት ፡ እዝን ፡ ወመክሥተ ፡ ክድንት ፡ ዐይን ፡፡

የማናውቀውን ፡ ፊደል ፡ ሩዝ ፡ — ከሚስዮን ፡ ቤት ፡ ስንጋበዝ ፡
በትምርት ፡ ወጭት ፡ በጥፈት ፡ ዳካ ፡ — በምላስ ፡ በብርዕ ፡ በቀለም ፡ መንካ ፡
የውጭ ፡ ቋንቋ ፡ ብንፈተፍት ፡ — ከምሳ ፡ በቀር ፡ የለም ፡ እራት ፤
ያጠግባል ፡ እንጂ ፡ ለጊዜው ፡ ብቻ ፡ — ሥንቅ ፡ አይኾነንም ፡ ለሩቅ ፡ ዘመቻ ፡፡

ለዘመቻውስ ፡ ሥንቅ ፡ የሚኾን ፡ — የዳበ ፡ ቈሎ ፡ ግእዛችን ፡
በኑን ፡ ዘመን ፡ በቀን ፡ ብዛት ፡ — የማይነቅዝና ፡ የማይሻግት ፤
ዐማርኛውም ፡ የንብ ፡ እንጀራ ፡ — በላስቶች ፡ ቀፎ ፡ ቀድሞ ፡ ሲሠራ ፡
ካረብ ፡ ከሱርስት ፡ ከዕብራይስጥ ፡ — የተቀመመ ፡ እጅግ ፡ ጥፍጥ ፡፡

ከውጭም ፡ ቋንቋ ፡ የሚገኝ ፡ ጥቅም ፡ ወደኛው ፡ ቋንቋ ፡ በመተርጐም ÷
ሊጥም ፡ እንዳይኾን ፡ ትርጓሜው ፡ ኹሉ ፡ ትምርቱን ፡ ማብሰል ፡ በየፊደሉ ፤
ቋንቋም ፡ ካልጠራ ፡ በሰዋስው ፡ — አነጋገሩ ፡ የለት ፡ ጕሽ ፡ ነው ፡፡

ስሙ ፡ ፕራቲክ ፡ የድምጫ ፡ ቋንቋ ፡ የኰረፌ ፡ ዐይነት ፡ ወይም ፡ የድቋ ፤
ዠሮ ፡ ሲቀምሰው ፡ ከዋንጫው ፡ አፍ ፡ ያሰኛልና ፡ እንትፍ ፡ እንትፍ ፡፡

በጥሩው ፡ መጠጥ ፡ በሀገር ፡ ፍቅር ፡ ራሴ ፡ ዞሮ ፡ ስቀባጥር ፡
ስላገር ፡ ቋንቋ ፡ ምንም ፡ ብተች ፡ — አትፍረዱብኝ ፡ ያገር ፡ ዳኞች ፡፡

ከባቶች ፡ ይልቅ ፡ በሽንገ ፡ ካሉ ፡ — ወደ ፡ ልጆች ፡ ነው ፡ ነገሬ ፡ ኹሉ ፤
የቋንቋን ፡ ፀዋጅ ፡ ለልጅ ፡ መልፈፍ ፡ በደንጊያ ፡ ጽላት ፡ እንደ ፡ መጣፍ ፤
ገና ፡ የሚያድገው ፡ ጨቅላው ፡ ወጣቱ ፡ ይሻላልና ፡ ካባት ፡ ከናቱ ፤
ዠሮው ፡ አእምሮው ፡ የላሸውማ ፡ — የነገሩትን ፡ መቼ ፡ ሊሰማ ።

የቅዱስ ፡ መጽሐፍ ፡ ማርና ፡ ኮሶ ፡ — በዓለም ፡ ቋንቋ ፡ ስሙ ፡ ተፋልሶ ፡
መራራው ፡ ጥዑም ፡ ስለ ፡ ተባለ ፡ — ማር ፡ የማይጥመው ፡ ብዙ ፡ ሰው ፡ አለ ።
ቢጥመውማ ፡ የማር ፡ ወለላ ፡ — አይጠጣም ፡ ነበር ፡ ኮሶ ፡ ባንኮላ ፤
ኮሶውም ፡ አስፌስ ፡ እንዲያ ፡ ሲመር ፡ መላልሶ ፡ አስቀምጦ ፡ የማያሽር፥
ተስፋውም ፡ ከንቱ ፡ የበጥባጭ ፡ ወሬ ፡ በዶሮ ፡ ፈንታ ፡ ቃሪያ ፡ በርበሬ ።
ትምርትና ፡ ዕውቀት ፡ ቶሎ ፡ እንዲሰፋ ፡ ይህ ፡ ነው ፡ መንገዱ ፡ የባለተስፋ ።

ምክር ፡ ሠናይት ፡ ለኵሉ ፡ ዘይገብራ ፡ ወለዘያስተጋብእ ፡ ማእረራ ።

እምአርቶዶክሳዊ ፡ ኪ ፡ ወ ፡ ክ ፡ ዘልሳነ ፡ ግእዝ ፡ ላእክ ።



## ፫ኛ ፡ ምዕራፍ ።

## ጸዋትወ ፡ ግስ ፥ የዘርና ፡ የነባር ፡ መቅደስ ፡ ባለ፷፮ ፡ ክፍልና ፡ ራስ ፡ ከአ ፡ እስከ ፡ ፐ ፡ ድረስ ።

### የቍራኛና ፡ የጥቅስ ፡ ምልክት ።

የብሉይ ፡ ጥቅስና ፡ የሐዲስ ፡ ምልክታቸው ፡ ባማርኛው ፡ ቅዱስ ፡ መጽሐፍ ፡ ውስጥ ፡ በሐዲስ ፡ ኪዳን ፡ መዠመሪያ ፡ በ፩ኛውና ፡ በ፮ኛው ፡ ገጽ ፡ በከፊል ፡ ስም ፡ ተወስኖና ፡ ተተርጕሞ ፡ እንደ ፡ ተጣፈው ፡ ነው ።

የብሉይ ፡ የሐዲስ ፡ አዋልድና ፡ የሊቃውንት ፡ ጥቅስ ፡ ምልክት ።

| | | |
|---|---|---|
| አቡሻ ፡ | ማለት ፡ | አቡሻህር ። |
| አዋል ፡ | » | አዋልድ ። |
| አፈ ፡ | » | አፈ ፡ ወርቅ ። |
| ድ ፡ | » | ድርሳን ። |
| ተ ፡ | » | ተግሣጽ ። |
| አረ ፡ መን ፡ | » | አረጋዊ ፡ መንፈሳዊ ። |
| አርጋ ፡ | » | አርጋኖን ። |
| ገድ ፡ አዳ ፡ | » | ገድለ ፡ አዳም ። |
| ገድ ፡ ዳን ፡ | » | ገድለ ፡ ዳንኤል ። |
| ገድ ፡ ኪሮ ፡ | » | ገድለ ፡ ኪሮስ ። |
| ገድ ፡ ላሊ ፡ | » | ገድለ ፡ ላሊበላ ። |
| ገድ ፡ ፊቅ ፡ | » | ገድለ ፡ ፊቅጦር ። |
| ገድ ፡ ሲኖ ፡ | » | ገድለ ፡ ሲኖዳ ። |
| ገድ ፡ ተክ ፡ | » | ገድለ ፡ ተክለ ፡ ሃይማኖት ። |
| ጊ ፡ ወ ፡ ሐ ፡ | » | ጊዮርጊስ ፡ ወልደ ፡ ሐሚድ ። |
| ግንዘ ፡ | » | መጽሐፈ ፡ ግንዘት ። |
| ዲድ ፡ | » | ዲድስቅልያ ። |
| ድር ፡ መድ ፡ | » | ድርሳነ ፡ መድኀኔ ፡ ዓለም ። |
| ድር ፡ ሚካ ፡ | » | ድርሳነ ፡ ሚካኤል ። |
| ደራሲ ፡ | » | ድርሰት ፡ ደራሽ ። |
| ሃይ ፡ አበ ፡ | » | ሃይማኖት ፡ አበው ። |
| ሄርማ ፡ | » | ተረፈ ፡ ጳውሎስ ። |
| ውዳ ፡ ማር ፡ | » | ውዳሴ ፡ ማርያም ። |
| ዜና ፡ እስ ፡ | » | ዜና ፡ እስክንድር ። |
| ሔኖ ፡ | » | ሔኖክ ። |

| | | |
|---|---|---|
| ጥበ፡ጠቢ፡ | ማለት፡ | ጥበበ፡ጠቢባን ። |
| ጦቢ፡ | » | ጦቢት ። |
| ጥሬ፡ሰዋ፡ | » | ጥሬ፡ሰዋስው ። |
| ዮዲ፡ | » | ዮዲት ። |
| ዮሐ፡መደ፡ | » | ዮሐንስ፡መደብር ። |
| ያዕ፡ዘእል፡ | » | ያዕቆብ፡ዘእልበረዳኢ ። |
| ዮሴፍ፡ | » | ዮሴፍ፡ወልደ፡ኮርዮን ። |
| ኪዳ፡ | » | መጽሐፈ፡ኪዳን ። |
| ኩፋ፡ | » | ኩፋሌ ። |
| መዋሥ፡ | » | መዋሥዕት ። |
| መ፡ፊ፡ | » | መጽሐፈ፡ፊውስ ። |
| መጽ፡ባሕ፡ | » | መጽሐፈ፡ባሕርይ ። |
| መጽ፡ባሮ፡ | » | መጽሐፈ፡ባሮክ ። |
| መጽ፡ኑዛ፡ | » | መጽሐፈ፡ኑዛዜ ። |
| መጽ፡ምስ፡ | » | መጽሐፈ፡ምስጢር ። |
| መጽ፡ቄድ፡ | » | መጽሐፈ፡ቄድር ። |
| መቃ፡ | » | መቃብያን ። |
| መቅ፡ወን፡ | » | መቅድመ፡ወንጌል ። |
| ማር፡ይሥ፡ | » | ማር፡ይሥሐቅ ። |
| ሥር፡ጳኵ፡ | » | ሥርዐተ፡ጳኵሚስ ። |
| ዕር፡ኢሳ፡ | » | ዕርገተ፡ኢሳይያስ ። |
| ፊ፡መ፡ | » | ፊውስ፡መንፈሳዊ ። |
| ፊልክ፡ | » | ፊልክስዩስ ። |
| ፊላስ፡ | » | ፊላስፋ ። |
| ፍ፡ነ፡ | » | ፍትሐ፡ነገሥት ። |
| ቅዳ፡ | » | ቅዳሴ ። |
| ቀሌ፡ | » | ቀሌምንጦስ ። |
| ቄር፡ | » | ቄርሎስ ። |
| እስት፡ | » | እስትጉቡእ ። |
| ጳላ፡ | » | ጳላድዮስ ። |
| ራእ፡ኤል፡ | » | ራእየ፡ኤልያስ ። |
| ሲኖዶ፡ | » | ሲኖዶስ ። |
| ስንክ፡ | » | ስንክሳር ። |
| ሱቱ፡ዕዝ፡ | » | ሱቱኤል፡ዕዝራ ። |
| ተረ፡ኤር፡ | » | ተረፈ፡ኤርምያስ ። |
| ተረ፡ቄር፡ | » | ተረፈ፡ቄርሎስ ። |

| | | |
|---|---|---|
| ታሪ ፡ አክ ፡ | ማለት ፡ | ታሪክ ፡ አክስም ። |
| ታሪ ፡ ነገ ፡ | » | ታሪክ ፡ ነገሥት ። |
| ትር ፡ ወን ፡ | » | ትርጓሜ ፡ ወንጌል ። |

ግእዝን ፡ ከሴምና ፡ ከያፌት ፡ ቋንቋ ፡ ለመግጠምና ፡ ለማመሬር ፡
በቀርን ፡ እየተከበበ ፡ የሚጣፍ ፡ ምልክት ።

| | | |
|---|---|---|
| ዕብ ፡ | ማለት ፡ | ዕብራይስጥ ። |
| ሱር ፡ | » | ሱርስት ፡ የአራም ፡ ቋንቋ ። |
| ዐረ ፡ | » | ዐረብ ። |
| ጽር ፡ | » | ጽርእ ፥ ዮናኒ ። |
| ሮማይ ፡ | » | ሮማይስጥ ፥ ላቲን ። |

የሰዋስው ፡ ጥቅስ ፡ ምልክት ።

| | | |
|---|---|---|
| ዕር ፡ | ማለት ፡ | ዕርከን ። |
| ቍ ፡ | » | ቍጥር ። |
| እግዚ ፡ | » | እግዚአብሔር ። |

የሚጠብቅና ፡ የሚላላ ፡ ምልክቱ ፥ ጥ ፡ ላ ፡ ናቸው ።

(ጥ) አምሮ ፡ አመረ ። ሰብሖ ፡ ሰብሐ ። ጠፊር ፡ ጠፈረ ፡ ይጠፍር ።

(ላ) አሚር ፡ አመረ ፡ የአምር ፡ ይእምር ። ሠቢሕ ፡ ሠብሐ ፡ ይሠብሕ ፡ ይሥበሕ ።

የብዙ ፡ ምልክት ፡ ብ ፡ ነው ።

ደብር ፤ (ብ ፡ አድባር ፡ ራት) ፤ ተራራ ። ያንዱ ፡ ፍች ፡ ውጥን ፡ ጨራሽ ፡ ኹኖ ፡ የብዙውን ፡ ተራሮች ፡ እንዲያሰኝ ፡ አስተውል ። ፪ኛም ፡ በግስ ፡ አርእስት ፡ ቀቲል ፡ ብሎ ፡ ቀቲሎት ፡ በማለት ፡ ፈንታ ፡ ቀቲን ፡ ጕርዶ ፡ ሎት ፡ ይላልና ፤ በሣልስና ፡ በሳድስ ፡ ቅጽልም ፡ ቀታሊ ፡ ብሎ ፡ (ሊት ፡ ልያን ፡ ያት ፥ ቀተልት) ፤ ቅቱል ፡ ብሎ ፡ (ላን ፡ ላት ፡ ትልት) ፡ እያለ ፡ ባንዱ ፡ የኹሉ ፡ የሚታወቅለት ፡ ስለ ፡ ኾነ ፥ አንዳንዱን ፡ ብቻ ፡ ይፈ ታል ። ንባቡም ፡ ፍችውም ፡ በከፊል ፡ በውጥን ፡ መጣፉ ፡ ነገር ፡ ለማሳጠር ፡ ነውና ፥ እንዳትሳሳት ፡ ተጠንቀቅ ።

የፊደላትና ፡ የቃላት ፡ ሞክሼ ፡ በያንዳንዱ ፡ መሥመር ፡ ተከታትሎ ፡ መሪና ፡ ተመሪ ፡ እየኾነ ፥ መሪው ፡ አለገንዘቡ ፡ ተመሪው ፡ በየገንዘቡ ፡ ተጥፎ ፡ ልዩ ፡ ልዩነ ቱን ፡ ያስረዳል ።





**አ** ፤ (**ፊደልና ፡ አኃዝ**) ፤ አንደኛ ፡ መገርመሪያ ፡ ፊደል ፤ የፊደል ፡ ኹሉ ፡ ራስ ፤ በቍር ፡ ቀዳማይ ፡ ባለም ፡ ቋንቋ ፡ ኹሉ ፤ ይልቁንም ፡ በጥንታዊው ፡ ተራ ፡ በግእዝ ፡ አልፍ ፡ ቤት ፡ በአበገደ ። ስሙ ፡ አልፍ ፡ ቍጥሩ ፡ አንድ ፤ አኃዝ ፡ ሲኾን ፡ አ ፡ አሐድ ፡ አሐዱ ፡ ይባላል ። ምስጢሩ ፡ እሑድንና ፡ የእሑድን ፡ ፍጥረት ፡ መደብ ፡ አድርጎ ፡ ፈጣሪን ፡ ያሳያል ። (ዘፍ፩ ፡ ፩—፭ ። ራእ፩ ፡ ፰ ፡ ፲) ። ዳግመኛም ፡ በዕብራይስጥ ፡ ዐዋጅ ፡ አለንቍጣ ፡ አሐዱ ፡ ይባል ፡ የነበረው ፡ ያው ፡ አንዱ ፡ አሌፍ ፡ አ ፡ በራሱ ፡ ላይ ፡ ነቍጣ ፡ ሲኾንበት ፡ በነቍጣው ፡ ምክንያት ፡ እልፍ ፡ እንዲባል ፤ በግእዝም ፡ ሥርዐት ፡ እ ፡ እልፍ ፡ ይባላል ፤ እልፍ ፡ ያስኘውም ፡ የራሱ ፡ ነቍጣ ፡ ነው ፤ አለፈን ፡ ተመልከት ።

**አ** ፤ የማብዛት ፡ ልማድ ፡ አብገር ፤ ፍችው ፡ ዎች ። **ደብር ፡ አድባር ÷ ወግር ፡ አውግር ÷ ፈለግ ፡ አፍላግ** ፤ ተራሮች ፡ ኰረብቶች ፡ ወንዞች ። አንዳንድ ፡ ጊዜም ፡ ት ፡ ምእላድ ፡ እየኾነለት ፡ ከት ፡ ጋራ ፡ ያበዛል ፤ **ጥብ ፡ አጥባት ÷ ነቅዕ ፡ አንቅዕት ÷ ባሕር ፡ አብሕርት** ። ዳግመኛም ፡ በአ ፡ ብቻ ፡ የሚበዛ ፡ ቃል ፡ ት ፡ ሲጨመርበት ፡ የብዙ ፡ ብዙ ፡ ይኾናል ፤ **አድባር ፡ ራት ÷ አውግር ፡ ራት ÷ አፍላግ ፡ ጋት** ። በአና ፡ በት ፡ የሚበዛም ፡ የብዙ ፡ ብዙ ፡ ለመኾን ፡ ኹለተኛ ፡ ት ፡ ይፈልጋል ፤ **ነቅዕ ፡ ባሕር ፡ ርእስ** ፡ ብሎ ፡ **አንቅዕት ፡ አንቅዕታት ፤ አብሕርት ፡ አብሕርታት ፤ አርእስት ፡ አርእስታት** ። የተን ፡ አፈታት ፡ እይ ።

**አ** ፤ የማስደረግ ፡ ልማድ ፤ አስደራጊ ፤ ፍችው ፡ አስ ። **ቀተለ ፡ አቅተለ ፤ ክህለ ፡ አክህለ ፤ ገብረ ፡ አግበረ** ። ዳግመኛም ፡ **ቆመ ፡ቦአ ፡ ወፅአ ፡ መጽአ** ፡ ይህን ፡ በመሰለ ፡ በሐውልትና ፡ ባንጐል ፡ ግስ ፡ ላይ ፡ ሲጨመር ፡ የማድረግና ፡ የማስደረግ ፡ ልማድ ፡ እየኾነ ፡ አንዱን ፡ አንቀጽ ፡ በ፪ ፡ ጾታ ፡ ያስፈታል ። **አቀመ** ፤ አቆመ ፡ አስቆመ ። **አብአ** ፤ አገባ ፡ አስገባ ። **አውፅአ** ፤ አወጣ ፡ አሶጣ ። **አምጽአ** ፤ አመጣ ፡ አስመጣ ። ባለቅኔዎች ፡ ግን ፡ አ ፡ ከወደቀበት ፡ ማናቸውም ፡ ግስ ፡ በ፪ ፡ ጾታ ፡ ይፈታል ፡ ብለው ፡ ያውጁና ፡ አእመረን ፡ ዐወቀ ፡ አሳወቀ ፡ ብለው ፡ ይፈታሉ ፤ የተሳሳተ ፡ ነው ፤ አሳወቀ ፡ እንጂ ፡ ዐወቀ ፡ አያሰኝም ፤ አመረን ፡ ተመልከት ። ሦስተኛም ፡ በክልኣይና ፡ በሣልሳይ ፡ ራሱን ፡ እየጐረደ ፡ የትንቢት ፡ መነሾች ፡ አሥራውን ፡ ኹሉ ፡ ራብዕ ፡ ያደርጋል ። **አቅተለ ፡ ያቀትል ፡ ያቅትል** ። **አግበረ ፡ ያገብር ፡ ያግብር** ። **አእመረ ፡ ያአምር ፡ ያእምር** ። ቀዳማዩን ፡ አመረ ፡ አኰተ ፡ ዐረፈ ፡ በማለት ፡ ፈንታ ፡ አእመረ ፡ አእኰተ ፡ አዕረፈ ፡ ብሎ ፤ ክልኣዩን ፡ ደግሞ ፡ የአምር ፡ የአኵት ፡ የዐርፍ ፡ ማለት ፡ ዕጥፍ ፡ ድርብ ፡ ስሕተት ፡ ይባላል ፤ በነዚህ ፡ በሦስቱ ፡ ሌላውን ፡ ኹሉ ፡ ማየት ፡ ነው ።

**አ** ፤ የትንቢት ፡ መነሻ ፤ የክልኣይ ፡ ሥር ፤ አነ ፡ ለሚል ፡ ብቻ ፡ ላንድ ፡ አካል ። ግእዙ ፡ ብቻ ፡ ስለ ፡ ተነገረ ፡ ሳድሱ ፡ አይቀርም ። **ሖርኩ ፡ አሐውር ÷ ዐረጉ ፡ አዐርግ ÷ ወረድኩ ፡ እወርድ** ። በማስደረግ ፡ ጊዜ ፡ ፪ኛ ፡ አ ፡ ስላለበት ፡ ራብዕ ፡ ይኾናል ። **አሖርኩ ፡ ኣሐውር ፤ አዕረጉ ፡ ኣዐርግ ፤ አውረድኩ ፡ ኣወርድ** ። **አእመርኩ ፡ ኣአምር** ።

**አ** ፤ የግስ ፡ ልማድ ፤ ጠባይና ፡ አካኼድ ፡ የሚለውጥ ። በ፫ ፡ ፊደል ፡ ግስ ፤ ከዚያውም ፡ በቀተለ ፡ ቤት ፤ መነሻ ፡ መድረሻ ፡ ማእከል ፡ ሲኾን ፤ ሳድስ ፡ ይኾን ፡ የነበረውን ፡ ግእዝና ፡ ራብዕ ፤ ግእዝ ፡ ይኾን ፡ የነበረውን ፡ ሳድስ ፡ ያደርጋልና ፤ አደራረጉና ፡ አገባቡ ፡ እንዴት ፡ እንደ ፡ ኾነ ፡ በርባ ፡ ቅምር ፡ ክፍል ፡ ተመልከት ፡ (ዕር፪ ፡ ቍ፲፭) ።

**አ** ፤ (**ንኡስ ፡ አገባብ**) ፤ እንደ ፡ ሶና ፡ እንደ ፡ ኬ ፡ እንደ ፡ መ ፡ ትራስ ፡ ኹኖ ፡ በመጨረሻ ፡ ቃል ፡ እየገባ ፡ ቃለ ፡ መልእክት ፤ አጋኖ ፤ አስተብቍዖ ፤ ተጋንዮ ፡ ይኾናል ፤ ምስጢሩም ፡ ቍልምጫና ፡ ከበሬታ ፡ ነው ። አፈታቱንና ፡ ምስክሩን ፡ በንኡስ ፡ አገባብ ፡ ተመልከት ፡ (ዕር፳ ፡ ቍ፯፬) ።

**ኡ** ፤ ኡኡ ፤ (ዐማርኛ) ፡ ኡኡታ ፤ ኦ ፡ ኦኦ ።

**ኢ** ፤ አሉታ ፤ ነባር ፡ አንቀጽና ፡ ንኡስ ፡ አገባብ ፤ ነባር ፡ አንቀጽ ፡ ሲኾን ፡ ፍችው ፡ እንደ ፡ አኮና ፡ እንደ ፡ ሐሰ ፡ እንደ ፡ አልቦ ፡ ነው ፡ (ዕር፲፩ ፡ ቍ፯፮) ። ንኡስ ፡ አገባብ ፡ ሲኾን ፤ አል ፡ አ ፡ እንዳ ፡ ላ ፡ ሳ ፡ ያል ፡ የማ ፡ ይኾናል ። ኢጸሐፈ ፤ አል ፤ ኢይጽሕፍ ፡ አ ፤ ኢይጽሐፍ ፤ እንዳ ፡ ላ ፡ ሳ ። ኢጽሒፎ ፤ ሳ ፤ ኢጸሓፊ ፡ ያልጣፈ ፡ የማይጥፍ ። ትራስ ፡ እየኾነም ፡ በእፎ ፡ ሲገባ ፡ ኤ ፡ ይኾናል ፤ እፎኢ ፤ ምስጢሩም ፡ ያሉታ ፡ አንክሮ ፡ ነው ። ደቂቅ ፡ አገባብም ፡ ሲኾን ፡ እንደ ፡ እንበለ ፡ ነው ፤ አለ ፡ ያለ ፡ ይኾናል ። ኢ ፡ ወኢ ፡ እያለ ፡ ሲጫፈርና ፡ ሲደጋገም ፡ ኹኖ ፤ ቢኾን ፡ ያሰኛል ። ፍችው ፡ አለ ፡ ሲኾን ፡ ከይቤ ፡ ዐማርኛ ፡ ይስማማል ፤ (ግጥም) ፤ ትስሙ ፡ እንደኾን ፡ የወንጌል ፡ ቃል ፡ አለ—መስጠት ፡ ያጸድቃል ። ባማርኛም ፡ ኢ ፡ አዪ ፤ አዬ ፡ ተብሎ ፡ ሲነገር ፡ ቃለ ፡ አኅስሮ ፡ ሐዘንና ፡ አንክሮ ፡ ይኾናል ። ምስጢሩ ፡ አሉታና ፡ አፍራሽ ፡ ሲኾን ፡ ያማርኛው ፡ ስልት ፡ በዝቷልና ፤ ኹሉንም ፡ በንኡስ ፡ አገባብ ፡ ተመልከት ፡ (ዕር፳ ፡ ቍ፱) ።

**ኣ** ፤ (**የቅጽል ፡ በር ፡ ከፋች**) ፤ በዝርዝር ፡ ጊዜ ፤ ቅጽሎቹም ፡ ዘ ፡ እንተ ፡ እለ ፡ ናቸው ። **ዚኣሁ** ፡

እንቲኣሁ ፡ እሊኣሁ ፤ ሃ ፡ ሆሙ ፡ ሆን ፤ ዚኣከ ፡ እንቲኣከ ፡ እሊኣከ ፡ ኪ ፡ ክሙ ፡ ክን ፡ የ ፡ ነ ።

**ኤ** ፤—ስመ ፡ ፊደል ፤—ዐ ፡ ፯ ።

**አ** ፤ አልፍ ፡ ፩ ፡ ሺሕ ፤ መቶ ፡ ጊዜ ፡ መቶ ።

**አ** ፤—ስመ ፡ አምላክ ፤—ዖ ፡ አልፋ ፡ ወዖ ።

**አ** ፤ (ንኡስ ፡ አገባብ) ፤ ሆይ ፤ ወዮ ፡ ወየው ፤ ምን ፤ ይብላኝ ። በምስጢር ፡ ቃለ ፡ ጽዋዔ ፡ ወአንክሮ ፤ ቃለ ፡ አክብሮ ፡ ወአፍቅሮ ፤ ቃለ ፡ ብካይ ፡ ወሰቈቃው ፤ ቃለ ፡ አኅስሮ ፡ ወአፍርሆ ፤ ቃለ ፡ አፉኅርኆ ፡ ይኾናል ። ፍችውንና ፡ ምስክሩን ፡ በቦታው ፡ ተመልከት ፡ (ዕርጀ ፡ ቍ፺፬) ።

**አአ** ፤ (ጽር ፡ ዖዖ ። ዕብ ፡ ሆይ ፡ ሆይ ። ዐረ ፡ ያያ) ፤ የጩኸት ፡ የቡታ ፡ የሪታ ፡ ቃል ፤ በቁሙ ፡ ወይም ፡ ኡኡ ፡ ዎዎ ፡ ወዮ ፡ ወዮ ፤ ሆይ ፡ ሆይ ። አአ ፡ ጕዩ ፡ እምብሔረ ፡ ሰሜን ፡ (ዘካ፪ ፡ ፮) ። አንዳንድ ፡ መጣፍ ፡ ግን ፡ ከጣፊ ፡ ስሕተት ፡ የተነሣ ፡ አአ ፤ ኦአ ፡ ወይም ፡ ኹሉን ፡ ትቶ ፡ ጕዩ ፡ ይላል ። በኦኦ ፡ ፈንታ ፡ አአ ፡ ወይም ፡ ኦአ ፡ ማለት ፡ ስሕተት ፤ ኹሉን ፡ መተው ፡ ግድፈት ፡ ይባላል ።

**አእይ** ፤ ዮት ፤ (አአየ ፡ የአኢ ፡ የአኢ) ፤ ወደ ፡ ወጡበት ፡ መመለስ ፤ መግባት ። መስማት ፤ እህ ፡ ማለት ።

**አኢ** ፤ (አአይክ ፡ ተአኢ ፡ ተአኢ ፡ አኢ) ፤ ትእዛዝ ፡ አንቀጽ ፤ ግባእ ፡ ተመየጥ ። አኢ ፡ ወሑር ፡ ብሔረ ፡ ግብጽ ፡ (ዘፀ፬ ፡ ፲፱) ።

**አኢ** ፤ ያዋጅ ፡ ቃል ፤ ስማ ፡ ስማ ። በጽሐ ፡ ጊዜ ፡ ዘይትበሀል ፡ አኢ ፡ ዘውእቱ ፡ ስማዕ ፡ ብሂል ፡ (ገድ ፡ ተክ) ።

**አኤል** ፤ (ዕብ ፡ ኤል ፡ ኤላው) ፤ የግንብ ፡ ዐምድ ፤ ውስጡ ፡ ግንብ ፡ ኹኖ ፡ አፍኣው ፡ በሉሕ ፡ የተጌጠ ፡ በልዝብ ፡ ጠርብ ፡ የተለበጠ ። ኤልንና ፡ ኤላውን ፡ ተመልከት ፤ ከዚህ ፡ ጋራ ፡ አንድ ፡ ነው ። ወአኤል ፡ ዘኖኖት ፡ (ሕዝ፵ ፡ ፱) ።

**አኤናዖን** ፤ (ጽር ። ዕብ ፡ ዖላም) ፤ ለዓለም ፤ ዘለዓለም ፡ (ዘዳ፴፫ ፡ ፲፭ ፡ ፳፯) ።

**አአትሪክን** ፤ (ጽር ፡ ቱሎጉ) ፤ ዝርው ፡ ቃል ፤ ድምፅ ፡ ሰብኣዊ ፤ ፍሬ ፡ ነገር ፡ የሚሰማበት ። አአትሪክን ፡ ውእቱ ፡ ቃልነ ፡ ዘይትከዐው ፡ ውስተ ፡ አየር ፡ ወእምኔሁ ፡ ይትፌኖ ፡ ንባብ ፡ (ሃይ ፡ አበ ፡ ጎር ፡ ገባ) ።

(ጥ) **አብ** ፤ (ዕብራ) ፤ የዕብራውያን ፡ ወር ፡ ነሐሴ ፡ የሚያዝያ ፡ ፭ኛ ። በ፲ኛው ፡ ቀን ፡ ያውም ፡ በጨረቃ ፡ ቍጥር ፤ ፊተኛውና ፡ ኋለኛው ፡ ፪ቱ ፡ መቅደሶች ፡ በዘመን ፡ ሩቅ ፡ ተከታትለው ፡ የፈረሱበት ፡ የተቃጠሉበት ፡ ስለ ፡ ኾነ ፤ ዕለቱን ፡ ፳፬ ፡ ሰዓት ፡ ይጾሙታል ፤ ወርኁንም ፡ ወርኀ ፡ ምዝባሬ ፡ ይሉታል ። መጥበቁም ፡ ስለ ፡ ደጊመ ፡ ቃል ፡ ነውና ፤ የደጊሙ ፡ ምስጢር ፡ ፪ቱን ፡ ምዝባሬ ፡ ያሳያል ። *ኦብ ፡ ዘውእቱ ፡ ወርኅ ፡ ኃምስ* ፡ (ዮሴፍ) ።

**እባብ** ፤ (ዐማርኛ ። ዐረ ፡ ኡባብ ፤ ማዕበል) ፤ በቁሙ ፡ ውሀኛ ፡ ማዕበልኛ ፡ የሚኼድ ፡ የሚዘል ፡ የሚወረወር ፤ በልቡ ፡ የሚሳብ ፡ የሚጕተት ፡ መርዛም ፡ ምላስ ፡ መንታ ፡ የሰይጣን ፡ አርኣያ ፡ የክፉ ፡ ሰው ፡ አምሳል ፤ እንገሌ ፡ እባብ ፡ ነው ፡ እንዲሉ ። (ተረት) ፤ እባብ ፡ ግደል ፤ ከንበትሩ ፡ ገደል ።

**አቢብ** ፤ (ዐረብ ። ቅብጥ ፡ ኤፒፕ) ፤ የግብጻውያን ፡ ወር ፡ ሐምሌ ፡ የመስከረም ፡ ፲፩ኛ ፡ (አቡሻ) ።

**አቢብ** ፤ (ዕብራ) ፤ መፀው ፤ ዘመነ ፡ መፀው ፡ ከክረምት ፡ ቀጥሎ ፡ የሚብት ፤ የጽጌ ፡ የፍሬ ፡ የልምላሜ ፡ ወራት ፤ በዓለ ፡ ፋሲካ ፡ የሚውልበት ፡ ወርኀ ፡ ትፍሥሕት ፡ ወርኀ ፡ ተሐድሶ ። ይኸውም ፡ ሚያዝያ ፡ ነው ፡ (ዘፀ፳፫ ፡ ፲፭) ።

**አቢብ** ፤ የሰው ፡ ስም ፤ በትንቢትና ፡ በምሳሌ ፡ ቡላ ፡ ለሚባል ፡ መነኵሴ ፡ ከግዜር ፡ የተሰጠ ፤ ብዙኅ ፡ ዐጽቅ ፡ መፍርየ ፡ ጽድቅ ። ተዘኪረከ ፡ ክርስቶስ ፡ ሥቃየተ ፡ አቢብ ፡ ገብርከ ፡ (ንግሥ ። ሰንክ ፡ ጥቅ፳፭) ።

**አቢብ** ፤ ቦት ፤ (ጥ ፡ አበ ፡ የአብብ ፡ ይአብብ) ፤ ማበብ ፡ ማፍራት ፤ የዕፀዋት ። አበባ ፡ መልበስ ፡ መቀዳጀት ፤ የመርዓዊና ፡ የመርዓት ። አባት ፡ መኾን ፡ ዘር ፡ መስጠት ፤ ወልደ ፡ ማዕለድ ፤ የወንድ ፡ የተባት ።

(ጥላ) **አባ** ፤ **አብ** ፤ (ብ ፡ አበው) ፤ ወላጅ ፡ አባት ፤ ወንድ ፡ ተባት ፡ በዘር ፡ በሩካቤ ፡ የሚወልድና ፡ የሚያዕልድ ። አክብር ፡ አባከ ፡ ወእመከ ፡ እስመ ፡ እሙንቱ ፡ ምክንያተ ፡ ፍጥረትከ ፡ (ዲድ) ።

**አባ** ፤ **አብ** ፤ የግብርና ፡ የክብር ፡ የማዕርግ ፡ ስም ። አባት ፡ መባል ፡ በብዙ ፡ ወገን ፡ ስለ ፡ ኾነ ፤ ከግዜር ፡ ዠምሮ ፡ ያባትነት ፡ ሥራ ፡ ለሚሠሩ ፡ ለመንፈሳውያን ፡ አባቶች ፤ ለቄስ ፡ ለመነኵሴ ፡ ለአእሩግና ፡ ለሊቃውንት ፡ ለመምህራን ፡ ኹሉ ፡ ይነገራል ። አቡነ ፡ ዘበሰማያት ፡ ኢታብአነ ፡ ውስተ ፡ መንሱት ። ትእዛዘ ፡ አበዊነ ፡ ሐዋርያት ። ብፁዕ ፡ አባ ፡ አቡነ ፡ ተክለ ፡ ሃይማኖት ፤ የመሰለው ፡ ኹሉ ፡ (ቅዳ ፡ ድጓ) ።

**አባት** ፤ (ዕብ ፡ አበት) ፤ አባቶች ። አብ ፡ ሲበዛ ፡ አበው ፡ እንዳሰኘ ፤ አባም ፡ ሲበዛ ፡ በግድ ፡ አባት ፡ ያሰኛል ፤ ባማርኛ ፡ ግን ፡ ውስጠ ፡ ብዙኅነቱ ፡ ሳይታወቅ ፤ ፩ ፡ መስሎ ፡ ፩ ፡ ተብሎ ፡ ስላንድ ፡ አካል ፡ ብቻ ፡ ይነገራል ። አምላክ ፡ የመለክ ፡ ብዢ ፡ ሲኾን ፡ ስላንድ ፡ እንዲነገር ፤ ይህም ፡ እንደዚያ ፡ ነው ፤ መለክን ፡ ተመልከት ። (ሐተታ) ፤ አብ ፡ በጥሬነቱ ፡ ዘርፍ ፡ ይዞ ፡ ሲቀጸል ፡ ወይም ፡ ብቻ ፡ ኹኖ ፡ እንደ ፡ ዘርፉ ፡ ስልት ፡ ሲፈታ ፤ ምስጢሩ ፡ ከባትነትና ፡ ከጌትነት ፡ ከባለቤትነት ፡ አይወጣም ።

አባም ፣ ባማርኛ ፣ ለሥጋዊ ፣ ሐርበኛ ፣ የፈረስ ፣ ስም ፣ ኹኖ ፣ ሲነገር ፣ እንደዚሁ ፣ ነው ። አባ ፣ ጠቅል ፣ ብሎ ፣ የጠቅል ፣ ጌታ ፣ ወይም ፣ ባለቤት ፣ ያሰኛል ። አብ ፣ የግ እዝ ፣ የዐረብ ፣ የዕብራይስጥ ፤ አባ ፣ የሱርስት ፣ ነው ። አባ ፣ ገቢር ፣ ተገብሮ ፣ ይከታል ፣ ጕልት ፣ ቀለም ፣ ነው ፤ አብዎ ፣ በገቢር ፣ ጊዜ ፣ አባ ፣ ይባላል ። አክብር ፡ አባከ ።

**አበ ፡ ጉንባሕ ፤ (ትግሬኛ ፡ አባ ፡ ጉን ባሕ) ፤** ርኩም ፤ ጕንባሳ ፤ የጨኽት ፣ ባለቤት ። ጉንባ ሕን ፣ እይ ። አበ ፡ ጉንባሕ ፡ ወከራ ድዮን ፡ (ዘዳ፲፱ ፣ ፲፰) ።

**አበ ፡ ደም ፤** ደመኛ ፣ ባለደም ፣ ደም ፣ አፍ ሳሽ ፣ ወይም ፣ የሜች ፣ ወገን ፣ ደም ፣ ፈላጊ ። አድኅ ንኒ ፡ እምአበ ፡ ደም ፡ (ደራሲ) ።

**አበ ፡ ላሕም ፤** አቢ ፣ ላም ፣ ዘላን ፣ ባለብዙ ፣ ላም ፤ የላሞች ፣ ሐፃኒ ፣ መጋቢ ። ወይም ፣ የላም ፣ ጌታ ፣ የከብት ፣ በሽታ ።

**አቤሜሌክ ፤ (ዕብ ፡ አቢሜሌኽ) ፤** አበ ፣ ንጉሥ ፤ የንጉሥ ፣ አባት ።

**አበ ፡ ምኔት ፤** የገዳም ፣ አባት ፤ ባለገዳም ።

**አቡ ፡ ፈረጅ ፤ (ዐረብ) ፤** የመጽሐፍ ፣ ስም ፤ ባለጸጋ ፣ ሀብታም ፣ ዕድላም ፤ በተገናኝ ፣ ፀቱን ፣ ፈርጅ ፣ ወንጌል ፣ እንደ ፣ ኩታ ፣ ገጥሞና ፣ አያይዞ ፣ የሚፈታ ፣ ዘርፍና ፣ ቅጽሉን ፣ የሚቋጭ ፣ ዐይን ፣ ምስጢሩን ፣ የሚ ገልጥ ፣ የሚያቀለጨልጭ ፣ ሊቅ ፣ መተርጕም ።

**አቢሳ ፤ (ዕብ ፡ አቢሻይ) ፤** አበ ፣ ጋዳ ፣ በዓለ ፣ ጋዳ ፣ እጅ ፣ መንሻ ፣ የሚሰጥ ፣ ወይም ፣ የሚቀበል ።

**አቡ ፡ ሻህር ፡ (ዐረብ) ፤** ታላቅ ፣ ስመ ፣ ጥር ፣ የቍጥር ፣ መጽሐፍ ፣ ብዙ ፣ ወግ ፣ ታሪክ ፣ ያለበት ። አበ ፣ ወርኅ ፣ በዓለ ፣ ወርኅ ፤ የጨረቃ ፣ ቍጥር ፣ ባለቤት ። መ ጽሐፉ ፣ የጸሓፊውን ፣ ቃል ፣ ስለ ፣ ያዘ ፣ በጸሓፊው ፣ ስም ፣ ይጠራል ።

**አቤሴሎም ፤ (ዕብ ፡ አብ ፡ ሻሎም) ፤** አበ ፣ ሰላም ፤ በዓለ ፣ ሰላም ፤ ሰላማዊ ።

**አበወ ፤ (ገቢር) ፤** ቃለ ፣ መሐላ ፤ ምጥንታም ፣ ይኾናል ። አበውን ፣ አበውና ፣ መሐላ ፤ በአበው ፣ ምጥ ንታ ። ሌላውም ፣ ስም ፣ ኹሉ ፣ በመሐላ ፣ ጊዜ ፣ መድረ ሻው ፣ ግእዝ ፣ ሲኾንለት ፣ ወይም ፣ የግእዝ ፣ ወራሽ ፣ ሀ ፣ ሲጋባበት ፣ እንደዚህ ፣ ይፈታል ። ጊዮርጊስሀ ፡ ማር ያምሃ ፤ የመሰለው ፣ ኹሉ ።

(ላ) **አበዊ ፤ አበዋዊ ፤ (ዊት ፡ ውያን ፡ ያት) ፤** ወገን ፣ ቅጽል ፣ ወይም ፣ ሙሻዘር ፣ ውስጠ ፣ ዘ ፤ ዘአበው ፣ እንተ ፣ አበው ። በጽሐ ፡ ጊዜ ፡ ተራኅርኆ ፡ ማህል ፡ አባዊት ፡ ላዕለ ፡ ልሕሡት ፡ አዳማዊት ፡ (ያዕ ፣ ዘእል ። ገድ ፣ አዳ) ። ተዓድዎ ፡ አበዋዊት ፡ (ማር ፣ ይሥሐ፪ ።

(ጥ) **አባዊ ፤** ስመ ፣ ፈለግ ፤ ንዌ ፣ አባይና ፣ ጥቍር ፣ አባይ ፤ ታላቅ ፣ ፈሳሽ ፣ ጕርፍ ፣ ማዕበል ፣ ማለት ፣ ነው ። ተለይቶ ፣ ግን ፣ ለጥቍሩ ፣ አባይ ፣ ብቻ ፣ ሲነገር ፤ አበ ፣ አፍላግ ፤ በኵረ ፣ አፍላግ ፤ ቀዳማይ ፣ ፈለግ ፣ ማለት ፣ ነው ፤ አብ ፣ ከርሱ ፣ ለሚገቡ ፣ ለታናናሾቹ ፤ በኵር ፣ ቀዳማይ ፣ ለወንድሞቹ ፣ ለሦስቱ ፣ ዐበይት ፣ አፍላጋት ። ኤፌሶንንና ፣ ግዮንን ፣ ተመልከት ። ፈለገ ፡ አባዊ ፡ (ታሪ ፣ ነገ) ።

**አባዊ ፤** የመንኵሴ ፣ ወገን ፣ ረድ ፣ አመክሪ ፣ ጥ ቍር ፣ ራስ ፤ ወንጌል ፣ በምናኔ ፣ ወተት ፣ ሳሳደጋት ፣ ለወ ለተ ፣ እንጦንስ ፣ ለምንኵስና ፣ የታጨ ።

**አብና ፤** አብነት ፤ አባትነት ፤ አባት ፣ መኾን ። እስመ ፡ አብ ፡ ይሰመይ ፡ አበ ፡ በእንተ ፡ አብናሁ ። ለአብ ፡ ቦቱ ፡ ስብሐት ፡ አብና ፡ (አፈ ፣ ድ፪ ። ሃይ ፣ አበ) ።

**አበውና ፤** ዝኒ ፣ ከማሁ ፤ አባቶችነት ፣ ከዊነ ፣ አበው ። ኢይኩን ፡ ሎሙ ፡ ላዕሌሁ ፡ ማዕርገ ፡ አበ ውና ፡ (ፍ ፣ ነ ፣ ፲ ፣ ፮) ።

**አቡን ፤ (ዐማርኛ) ፤** የቤተ ፣ ክሲያን ፣ አባት ፣ ጳጳስ ፣ ኤጲስቆጶስ ፤ ምእመናን ፣ አባታችን ፣ ብለው ፣ የሚጠሩትና ፣ የሚያከብሩት ፣ አቦ ፣ አቦ ፣ የሚሉት ። (ተ ረት) ፤ ያቡን ፣ የጨጌ ፣ ከብት ፣ በየወገኑ ፣ ይከተት ። ከመ ፡ ዝ ፡ ይቤሉ ፡ አቡን ፡ (ታሪክ ፣ ጕንደር) ።

**አቡን ፤** የድጓ ፣ መዝሙር ፣ ሰንበት ፣ ነክ ፣ ያይ ደለ ፣ ሌጣ ፣ የዘወትር ። መሪውን ፣ ባምጃር ፣ ተመሪውን ፣ ባቡን ፣ ሲመስሉት ፣ መተባበሩ ፣ እንደ ፣ ጌሾና ፣ እንደ ፣ ብቅል ፣ ኹኖ ፣ ሺሕ ፣ ፮፻ ፣ ዓመት ፣ ሆድ ፣ ያባውን ፣ የግ ብጦችን ፣ ምስጢር ፣ ያወጣዋል ። (ታሪከኛ ፣ ግጥም) ፤ በከሣቴ ፣ ብርሃን ፣ ሰላማ ፣ አንጻር ፣ ብርሃን ፣ አዜብ ፣ ከተ ባለው ፣ ክክልእ ፣ ሰላማ ፣ ዠምሮ ፣ በሰላማና ፣ በሰላማ ፣ በ፪ቱ ፣ የቀናች ፣ ሃይማኖት ፤ ኋላ ፣ በሣልስ ፣ ሰላማ ፣ በ ቀን ፣ ጨለማ ፣ ትጠፋለች ፣ ትለወጣለች ፣ ተብሎ ፣ ቃል ፣ በቃል ፣ ሲነገር ፣ የመጣውን ፣ ነግርና ፣ ትንቢት ፣ ለመፈ ጸም ፤ ፫ኛው ፣ ሰላማ ፣ ደጃች ፣ ውቤንና ፣ ራስ ፣ ዐሊን ፣ ካዋጋ ፣ በኋላ ፣ ሣልሳይነቱን ፣ ቀዳማይ ፣ ትንቢት ፣ እየ መራው ፣ ከፋሲል ፣ ከተማ ፣ ጕንደር ፣ ገብቶ ፣ በተንቤ ኖች ፣ ቋንቋ ፣ አፉን ፣ ባልፈታ ፣ አምጃር ፣ ባስተርጓሚ ፣ የመናፍቃንን ፣ ትፋትና ፣ ቅርሻት ፣ ማር ፣ እያስመሰለ ፣ መንፈስ ፣ ቅዱስን ፣ ዐሎ ፣ ብሎ ፣ ፩ ፣ ባሕርይ ፣ ወልድ ፣ ቅብ ፣ በሰውነቱ ፣ አምላክ ፣ እያለ ፣ ለውጦ ፣ ገልብጦ ፣ ስለ ፣ ሰበከ ፣ ወደ ፣ ሺዋም ፣ የግዝት ፣ ወረቀት ፣ ስለ ላከ ፣ በዚህ ፣ ምክንያት ፣ የሺዎች ፣ አፈ ፣ ጉባኤ ፣ አለቃ ፣ ዐሥራት ፣ ከሣህለ ፣ ሥላሴ ፣ ተልከው ፣ ፱፻ ፣ ሰው ፣ አስ ከትለው ፣ እስከ ፣ ጕንደር ፣ ወርደው ፣ በሃይማኖት ፣ ዜማ ፣ በሥግው ፣ ቃል ፣ ትምርት ፣ አምላክ ፣ ወሰብእ ፣ መንፈስ ፣ ቅዱስ ፣ ቅብዕ ፣ በማለት ፣ ከጕንደር ፣ ሊቃው ንት ፣ ተስማምተው ፣ አቡኑንም ፣ ድርስ ፣ ቍርጥ ፣ ባለው ፣ አነጋገር ፣ በክርክር ፣ ቃኝተው ፣ ወደ ፣ ትግሬ ፣ መርተው ፣ ሲመለሱ ፣ ያንኮበሩ ፣ ደብተራ ፣ ጕልቴ ፣ የገጠመው ። እን ዳሥራት ፣ ማን ፣ አለ ፣ የሚያውቀው ፣ ድጓውን ፤ ትግሬ ፣ መርቶት ፣ መጣ ፣ ያን ፣ ረዥም ፣ አቡን ።

(ጥ) **አበ ፤ (ጋልኛ) ፤** አባቶ ፣ አባት ፣ ሆይ ፣ አንተ ። ትግሮች ፣ አባ ፣ ጋብር ፣ ዐማሮች ፣ አቡየ ፣ የሚሏቸውን ፣

ጻድቅና ፡ ቅዱስ ፡ ጋሎች ፡ አበ ፡ ይሏቸዋል ። (ግጥም ፤ አበን ፡ የምትዘክር ፡ ያምሳ ፡ ዓመት ፡ ሴት ፡ በመከንንቷ ፡ እንደነኤልሳቤጥ ፡ በሳዘንች) ፤ ልጅ ፡ ታስጡኝ ፡ እንደኹ ፡ ልምጣ ፡ በመጋቢት ፤ የዝቋላው ፡ አበ ፡ የምድረ ፡ ከብዱ ፡ አባት ። ኋላም ፡ ልጅ ፡ አግኝታ ፡ ደስፈቅ ፡ ስላላት ፤ ያበን ፡ ገድል ፡ ፀዝለው ፡ እሸርር ፡ ከሚሉ ፡ ከቶ ፡ እንማናቸው ፡ ወልደው ፡ ያሳዘሉ ።

**አበገደ** ፤ (ዐረ ፡ አብጀድ) ፤ የፊደላት ፡ ሴም ፡ የጀመሩ ፡ እሌፋት ፡ ስምና ፡ አርእስት ፡ የግእዝና ፡ የዕብራይስጥ ፡ የሱርስት ፡ የዐረብ ፡ ሥርና ፡ ምንጭ ፡ ዘሩን ፡ እንደዚህ ፡ መጽሐፍ ፡ አካኼድ ፡ በአልፍ ፡ ዠምሮ ፡ በታው ፡ የሚጨርስ ። ፪ኛም ፡ የግእዙ ፡ ተራ ፡ ሳይፋለስ ፡ ከከዕብ ፡ እስከ ፡ ሳብዕ ፡ ያሉት ፡ ፯ ፡ ጸቱ ፡ እየተዘነቁ ፡ ሲጣፉ ፡ ስሙ ፡ አቡጊዳ ፡ ይባላል ። (ተረት) ፤ አቡጊዳ ፡ የተማሪ ፡ ዕዳ ።

**አብድ** ፤—በሪያ ፤—ዐብድ ።

**አቢድ** ፤ ዶት ፤ (አብደ ፡ የአብድ ፡ ይእበድ ። ዕብ ፡ አባድ) ፤ ማበድ ፤ መቈጣት ፤ አእምሮ ፡ ማጣት ፡ መወግሸት ፡ መነሣሣት ፡ አፈፍ ፡ አፈፍ ፡ ወፈፍ ፡ ወፈፍ ፡ ማለት ፡ መስነፍ ፤ ሞኝ ፡ አላዋቂ ፡ መኾን ፤ መጥፋት ፡ መበላሸት ፡ የልብ ፡ የናላ ። ተአብዱኑ ። ተአብድኑ ፡ ጳውሎስ ። ወአብደ ፡ መራዕይ ። የአብዱ ፡ ዘሎሙ ፡ እለ ፡ ነበከሙ ፡ ኅቡረ ፡ ምስሌሁ ፤ በቁሙ ፡ (ግብ፲፪ ፡ ፲፭ ። ጀ፮ ፡ ጀ፱ ። ማርሽ ፡ ፲፫ ። ዲድ ፡ ፯) ። ወእንዘ ፡ ይፈቅዱ ፡ ይጥብቡ ፡ አብዱ ። እስመ ፡ አብዱ ፡ ኖሎት ። ኢየአብድ ፡ እምኔክሙ ፤ ስንፈ ፡ (ሮሜ፩ ፡ ጀ፪ ። ኤር ፲ ፡ ጀ፩ ። ኢዮ፲፫ ፡ ፪) ።

**አባዲ** ፤ (ዲት ፡ ድያን ፡ ያት) ፤ የሚያብድ ፡ የሚሰንፍ ፤ ሰናፊ ፡ ሰነፍ ፤ አላዋቂ ። ማርደም ፡ መጥበቢት ፡ ዓለም ፡ አባዲ ። ልቡ ፡ አባዲ ፡ (ደራሲ ። ስንክ ፡ ታኅ፯) ።

**አብድ** ፤ (ዳን ፡ ዳት ፡ በድ) ፤ ዝኒ ፡ ከማሁ ፤ እብድ ፤ ቊጡ ፤ ሰነፍ ፡ ሞኝ ፡ አላዋቂ ። እመኒ ፡ በምክንያተ ፡ ጋኔን ፡ ዘየጌብሮ ፡ ዝንቱ ፡ አብድ ፡ ውእቱ ። አብድ ፡ ከልብ ፡ ዘነሰከ ። ከመ ፡ አብድ ፡ ሐራውያ ። አብዳን ፡ አጥብብ ። ኅምስ ፡ አብዳት ፡ ወኅምስ ፡ ጠበባት ፡ (ፍ ፡ ነ ፡ ፴፪ ። መ ፡ ፈ ። ስንክ ፡ ነሐሴ፳፫ ። ኪዳ ። ማቴ፳፭ ፡ ፪) ።

**እቡድ** ፤ (ዳን ፡ ዳት ፡ ብድ) ፤ ያበደ ፡ የለከረ ፡ የወገሸ ፤ እብድ ፡ ቍጡ ፡ ብስጩ ፡ ጨኺ ፤ ደረቅ ። ከልብ ፡ እቡድ ። ከነ ፡ እቡደ ፡ ከመ ፡ ሐራውያ ፤ እቡድ ፡ ወእሱር ፡ በሰናስል ። ሞገዳተ ፡ ባሕር ፡ እቡዳት ፡ (የሚጮኹ ፡ የሚተሙ) ። ወለት ፡ እቡድ ። ብእሲት ፡ እቡድ ፡ (ዲድ ፡ ፯ ። ገድ ፡ ተክ ። ይሁ ፡ ፲፫ ። ሚራ፳፪ ፡ ፫ ። ምሳ፱ ፡ ፲፫) ። በእብድ ፡ ፈንታ ፡ እቡድ ፡ ይላል ፡ አያስኝም ። እምንጉሥ ፡ እቡድ ፡ ይኄይስ ፡ ገብር ፡ ጠቢብ ፡ (አዋል) ። ጠባቢና ፡ ጠቢብ ፡ ፩ ፡ እንደ ፡ ኾኑ ፤ እብዳና ፡ እብድም ፡ ፩ ፡ ናቸው ።

**እበድ** ፤ (ዳት) ፤ ማበድ ፡ እብደት ፤ እብድነት ፤ ቍጣ ፤ ስንፍና ፡ ድንቍርና ፤ ሞኝነት ፤ አለውቀት ፡ አላዋቂነት ፤ ልጅነት ፡ ጅልነት ። እበድከ ፡ አደንገፀኒ ። እበድስ ፡ አልብየ ። ዝንቱ ፡ አሚን ፡ እበድ ፡ ውእቱ ፤ እበደ ፡ ደቂቅ ። በመዋዕለ ፡ እበድ ። ፈድፈደት ፡ እበደሙ ፡ (ሚራ፵፩ ፡ ፲፭ ። ግብ፳፯ ፡ ጀ፱ ። ቄር ፡ እስት ። አቡሻ ፡ ፪ ። ፪ጢሞ ፡ ፫ ፡ ፱) ።

**አእበደ** ፤ አሳበደ ፤ እብድ ፡ አደረገ ። አሰነፈ ፤ አሞኘ ፡ አታለለ ፡ ሸንገለ ፤ ናቀ ፡ አቃለለ ። ለምንት ፡ ታእብድ ፡ ሰብአ ፡ ኦ ፡ ሰይጣን ። ያእብድዎሙ ፡ አጋንንት ፤ በቊሙ ፡ (ገድ ፡ ተክ ። ኩፋ ፡ ፲) ። ኢታእብደኒ ። አከኑ ፡ አእበዳ ፡ እግዚ ፡ ለጥበበ ፡ ዝ ፡ ዓለም ። አእበዳ ፡ ለነፍስከ ፡ (ጦቢ፲ ፡ ፯ ። ፩ቆሮ ፡ ፩ ፡ ፯ ። ማር ፡ ይሥ፪ ፡ ፲፩) ። በአእበደ ፡ ፈንታ ፡ አስተእበደ ፡ እንደ ፡ ማለት ፡ አስተአበደ ፡ ይላል ። ትክልኑ ፡ ታስተአብዶ ፡ ለእግዚ ። አልቦ ፡ ዘያስተአብዳ ፡ ለውርዙትከ ። ኢያስተአብዱ ፡ ወኢያስተአክዩ ፡ ትእዛዘ ፡ እግዚ ፡ (ሮሜ፪ ፡ ፬ ። ፩ጢሞ ፡ ፬ ፡ ፲፪ ። ቀሌ) ።

**አእባዲ** ፤ ማእበዲ ፤ መስተአብድ ፤ የሚያሳብድ ፤ የሚያሰንፍ ፤ አስናፊ ፤ አጥፊ ። ቀታሌ ፡ ሰብአ ፡ ማእበዲ ፡ (ኪዳ ፡ ፩) ።

**አስተአበደ** ፤ (አደፈራረጊ) ፤ አሳነፈ አስናነፈ ፤ አቋጣ ፡ አቈጣጣ ፡ አናናቀ ።

**መስተአብድ** ፤ (ድት ፡ ዳን ፡ ዳት) ፤ ሰንፎ ፡ የሚያሰንፍ ፤ የሚያሳንፍ ፡ አሳናፊ ፤ ዋዘኛ ፤ ፌዘኛ ፤ ሕጹጸ ፡ አእምሮ ። መስተአብዳን ፡ ለአስተአብዶ ። ዕደው ፡ መስተአብዳን ፡ (፪ጴጥ ፡ ፫ ፡ ፫ ። ሶፎ፫ ፡ ፬) ።

**አበድቢድ** ፤ (ድት ፡ ዳን ፡ ዳት) ፤ እብድ ፡ ሞኝ ፤ ሰነፍ ፡ አላዋቂ ፤ ዕውቀቱ ፡ ትምርቱ ፡ ያጠረ ፤ ወደ ፡ ስንፍና ፡ የሚያደላ ፤ ጥበብና ፡ ምስጢር ፡ የማይገባው ፡ የማይስማማው ።

—፤ ከስንፍ ፡ ሰው ፡ አፍ ፡ የሚወጣ ፡ ተርታ ፡ ነገር ፡ ዐልማ ፡ ቃል ፡ ጣዕምና ፡ ምስጢር ፡ የሌለው ። ወበአበድቢዳት ፡ ቃላት ፡ ይትቃሐዉ ፡ (ቄር ፡ ጳላ፩) ። መምህራን ፡ ግን ፡ የበድበደ ፡ ዘር ፡ አድርገው ፡ ፍችውን ፡ የሚያዝግ ፡ ይሉታል ፤ ስሕተት ፡ ነው ።

**አብዶን** ፤ (ዕብ ፡ አበዶን) ፤ ፍጹም ፡ ጥፋት ፤ መፍረስ ፡ መደምሰስ ፡ ባዶ ፡ ባድማ ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ መኾን ፤ ሲኦል ፡ መቃብር ። ወስሙ ፡ በዕብራይስጥ ፡ አብዶን ፡ (ራእ፱ ፡ ፲፩) ። ባለብሉዮች ፡ በኤርምያስ ፡ (ምጀ ፡ ፯) ። ሂሮድያኖስን ፡ ሽመላ ፡ እንደ ፡ ማለት ፡ የፈ ፡ ፈንክስ ፡ ብለው ፡ ሲተርጉ ፤ አብዱ ፡ የዲን ፡ ጭቃ ፡ የሚሉት ፡ ከዚህ ፡ የወጣ ፡ ነው ።

**አብደረ** ፤—አስቀደመ ፤—በዲር ፡ በደረ ።

**አብደሬናን** ፡ ቱቂኢ.ም ፤ (ጽር ፡ አቤዲሬን ፡ አቱኪዩም) ፤ ቃሉ ፡ የዕብራይስጥ ፡ ነው ፤ ዕብ

ራይስጡ ፡ ወሀድባሪም ፡ አቲቂም ፡ ያለውን ፤ ጽርኡ ፡ እን ዳለ ፡ በጥሬው ፡ ወስደታል ። ወእሉ ፡ ዜናት ፡ ቀደምት ፤ ነገራት ፡ ቀደምት ፡ ማለት ፡ ነው ፤ አንቲካ ፡ ወሬ ፡ እንደ ፡ ማለት ፡ (፩ዜና ፡ ፬ ፡ ፳፪) ። ዜናት ፡ ያላቸውም ፡ በአሪት ፡ ዘኍልቍ ፡ ይገኛሉ ፡ (ም፳፩ ፡ ፩--፱) ።

**አበው ፤—የአብ ፡ ብዙ ፡ አበዎች ፤—አብ ፡ አበ ።**

**አብሐ ፤—አሠለጠነ ፤—በዊሕ ፡ ቦሐ ።**

**አበጠ ፤—ሳበ ፡ ጐተተ ፤—ዐበጠ ።**

**አብጥሊስ ፤ (ሳት ። ዐረ ፡ እተጥላሳት) ፤** የመጽሐፍ ፡ ስም ፤ ሦስተኛው ፡ የሐዋርያት ፡ ሲኖዶስ ። ፍችው ፡ ቀኖና ፡ ማለት ፡ ነው ፤ ተጥላስን ፡ እይ ። ግጽው ፡ ወሥርዐት ፡ ወአብጥሊስ ። ረስጠ፳ ፡ ዘውእቱ ፡ ቀሌምንጦስ ፡ ሣልስ ። ከመ ፡ ዝ ፡ መሀሩነ ፡ ሐዋርያት ፡ በአብጥሊሶሙ ፡ (ፍ ፡ ነ ፡ መቅ ። ቅዳ) ።

**አብይ ፤ ዮት ፤ (አበየ ፡ የአቢ ፡ ይእበይ ። ዐረ ፡ አበይ) ፤** እንቢ ፡ ማለት ፤ አበያ ፡ እንቢተኛ ፡ መ ኾን ፡ መኳደድ ፤ የሰጡትንና ፡ ያዘዙትን ፡ የለመኑትን ፡ አለመቀበል ፤ አለመስማት ፡ አለማድረግ ፡ ዕሺ ፡ በጎ ፡ ይ ኹን ፡ አለማለት ። እንብየን ፡ ተመልከት ፤ የዚህ ፡ ዘር ፡ ነው ፤ ን ፡ ስፎጽ ፡ ኹኖ ፡ ስለ ፡ ገባበት ፡ ወደዚያ ፡ ኺዷል ። ተአብዩ ፡ ትእዛዝየ ፡ ሰሚዐ ፡ ወሕግየ ። አበየት ፡ ሰሚ ዖቶ ። አበዩ ፡ ኵሎሙ ፡ ትእዛዘ ፡ ንጉሥ ። ኢየአቢ ፡ ስ እለተኪ ። አበየ ፡ ዝናም ፡ ተውህቦ ፡ ለምድር ። ኢይ እቢይ ፡ ባዕል ፡ ከመ ፡ ኢይጠመቅ ፡ ምስለ ፡ ነዳይ ። እመ ፡ ጸውዐከ ፡ ኢትእበዮ ፡ (ዘፀ፲፯ ፡ ፳፫ ። አስቴ፩ ፡ ፲፪ ። ዮዲ፩ ፡ ፲፩ ። ኩፋ ፡ ፴፭ ። ፵፱ ። ፍ ፡ ነ ፡ ፫ ። ሚራ ፲፫ ፡ ፱) ።

**አባዪ ፤ (ዪት ፡ ይያን ፡ ያት) ፤** እንቢ ፡ ባይ ፤ እንቢተኛ ፤ ተኳዳጅ ፤ አበያ ።

**እበይ ፤ (ያት) ፤** እንቢታ ፤ እንቢተኝነት ።

**አእበየ ፤** እንቢ ፡ አሰኘ ፡ እንቢታ ፡ አስተማረ ፤ እንቢ ፡ በል ፡ አለ ።

**ተአብየ ፤** እንቢ ፡ ተባለ ፤ ተጠላ ፤ ተሰለቸ ፡ ተ ጠገበ ፤ ፍቅሩ ፡ ለእግዚእነ ፡ ኢይትአበይ ፡ (አዋል) ።

**ተአበየ ፤** እንቢ ፡ ተባባለ ፤ በፈቃድ ፡ በግብር ፡ ተለያየ ፤ ተጣላ ፤ ተፈራቀቀ ፡ አንድነት ፡ ስምምነት ፡ ዐጣ ። እስመ ፡ ሥጋኒ ፡ ይፈቱ ፡ ዘኢይፈቱ ፡ መንፈስ ፤ ወመ ንፈስኒ ፡ ይፈቱ ፡ ዘኢይፈቱ ፡ ሥጋ ፡ ወይትኣበዩ ፡ በበ ይናቲሆሙ ፡ ከመ ፡ ኢትግበሩ ፡ ዘትፈቅዱ ፡ (ገላ፭ ፡ ፲፯) ።

**አብየ ፤—ወፈረ ፡ ላቀ ፤—ዐብየ ።**

**አቢል ፤ ሎት ፤ (አበለ ፡ የአብል ፡ ይእ ብል ። ዕብ ፡ አቤር ፤ አጸና) ፤** መጽናት ፡ መበር ታት ፤ ማደግ ፡ እየጨመሩ ፡ መኼድ ።

**አባል ፤ (ላት ። ዕብ ፡ ኤቤር ፤ ኤበር ፤ ብ ፡ ኤበሪም) ፤** ብልት ፡ የገላ ፡ ክፍል ፤ በየስሙና ፡ በያ ንጻሩ ፡ እኩያ ፡ አምሳያ ፡ ያለው ፤ ከራስ ፡ ጠጕር ፡ እስከ ፡ እግር ፡ ጥፍር ፡ በየክፍሉና ፡ በያንዳንዱ ፡ በየማውዱ ፡ ያለ ፡ ሥጋ ፤ ሕዋስ ፡ አካል ፡ ገላ ። አከለንና ፡ ሌለየን ፡ ተመልከት ፤ የዚህ ፡ ጎር ፡ ነው ። ከመ ፡ አባል ፡ ውስተ ፡ መቅፀት ። መተሮ ፡ ለበግዐ ፡ በበ ፡ አባላቲሁ ። እንዘ ፡ ንስቲት ፡ አባል ፡ አንቲ ። ወተዐጽፈ ፡ አባለ ፡ መንፈስ ፡ ረቂቅ ። ለእመ ፡ ሐመ ፡ አሐዱ ፡ አባል ፡ የሐምም ፡ ምስሌሁ ፡ ኵሉ ፡ ነፍስትነ ። ዘፈወሰ ፡ አባለ ፡ ሙሱነ ። አባለ ፡ ዘርዐ ። ኢይኩን ፡ ዕሩቀ ፡ አባል ፡ ቅድመ ፡ መ ኑፒ ። ብእሲት ፡ አባሉ ፡ ለብእሲ ፡ (ሚክ፫ ፡ ፫ ። ዘሌ፰ ፡ ፳ ። ቅዳ ፡ ሕር ። ዮሐ ። ፩ቆሮ ፡ ፲፪ ፡ ፳፯ ። ዲድ ፡ ፳፩ ። ፊልክ ፡ ፯ ። ፈ ፡ መ ፡ ፴፱ ፡ ፫ ። ዲድ ፡ ፲) ። አባሎ ፡ የሚሉት ፡ ብርቱ ፡ የቁላ ፡ ዕንጨት ፡ ስሙ ፡ ከዚህ ፡ የወጣ ፡ ነው ።

(ጥ) **አበለ ፤—አሰኘ ፤—ብህለ ፡ አብህለ ።**

**አበለ ፤—በቁሙ ፡ ዐማርኛ ፤—ሐቢል ፡ ሐብለ ።**

**አቤል ፤ (ዕብ ፡ ሀቤል) ፤** የሰው ፡ ስም ፤ ወልደ ፡ አዳም ፡ (ዘፍ፬ ፡ ፪) ። አቤል ፡ መስክ ፡ ጨፌ ፤ አል ቃሽ ። ሀቤል ፡ ከንቱ ፡ ብላሽ ፡ ማለት ፡ ነው ።

**አቦሊ ፤ (ጽር ፡ አቦሎስ) ፤** የገንዘብ ፡ ስም ፤ ታናሽ ፡ ገንዘብ ፡ ፩ ፡ ሳንቲም ፤ የዲድርክም ፡ ኻያኛ ፡ በዕብራይስጥ ፡ ጌራ ፡ ይባላል ፤ ኻያው ፡ ጌራ ፡ ፩ ፡ ሰቅል ፡ እንዲኾን ፤ ኻያው ፡ አቦሊ ፡ አንድ ፡ ዲድርክም ፡ ነው ። ዕሥራ ፡ አቦሊ ፡ ለአሐቲ ፡ ዲድርክም ፡ (ዘሌ፳፯ ፡ ፳፭ ። ዘኍ፫ ፡ ፵፯ ። ዘፀ፴ ፡ ፲፫ ። ፩ነገ ፡ ፪ ፡ ፴፯) ።

**ኡባል ፤ (ዕብራ) ፤** ታናሽ ፡ ወንዝ ፤ ፈፋ ፡ በ ዱር ፡ በዛፍ ፡ ውስጥ ፡ ያለ ። የግንብ ፡ ደጃፍ ፡ የድልድይ ፡ በር ። ወሀሎኩ ፡ አነ ፡ በኡባል ፡ ኡላይ ፡ (ዳን፰ ፡ ፪) ። ኡላይ ፡ የወንዙ ፡ ስም ፡ ነው ።

**እብላ ፤** ጨረቃ ፤ የጨረቃ ፡ ስም ። ወቦቱ ፡ ለወርኅ ፡ አርባዕቱ ፡ አስማት ፤ አሶንያ ፡ እብላ ፡ ብ ናሴ ፡ ኤራስ ፡ (ሔኖ፸፰ ፡ ፪ ። ስንክ ፡ ነሐ፲፯) ።

**አብላሊት ፤—አለብላቢት ፤—በሊል ፡ በለ ።**

**አበሞ ፤ አበሜ ፤ (ጽር ፡ አሞሞን ። ዕብ ፡ ቂዳ) ፤** ሽቱ ፤ የሽቱ ፡ ስም ፤ ቅመም ፤ ቀረፋ ፤ የጢስ ፡ ዕንጨት ፡ ቅጠላም ፡ ያይደለ ። ቀረፋ ፡ ኹለት ፡ ዐይነት ፡ ነው ፤ ቅመምና ፡ ሽቱ ፡ የሚኾን ፡ (ራእ፲፰ ፡ ፲፫ ። ዘፀ፴ ፡ ፳፬ ። ሕዝ፳፯ ፡ ፲፱) ። ቀንሞስን ፡ እይ ፤ ከዚህ ፡ ጋራ ፡ አንድ ፡ ነው ።

**አቡን ፤—ጳጳስ ፤—አብ ።**

**እብን ፤ (ዐረ ፡ ኢብን ። ዕብ ፡ ቤን) ፤** ወንድ ፡ ልጅ ፡ ተባት ፤ ሲያበዛ ፡ አብናእ ፡ ይላል ። እብን ፡ እልሐኪም ፡ (ከብ ፡ ነገ) ።

**እብን ፤ (ዕብ ፡ ኤቤን ። ሱር ፡ አብናእ) ፤** ደንጊያ ፤ ድንጋይ ፡ በአፍኣ ፡ በውስጥ ፡ ከምድር ፡ የሚገኝ ፤ የምድር ፡ ዐጥንት ፤ ዕንቍ ። ለዕንጨት ፡ ብዙ ፡ ዐይነት ፡ እንዳለው ፡ ለደንጊያም ፡ ብዙ ፡ ዐይነት ፡ አለው ፤ ክቡርና ፡ ኀሡር ፡ ግብዝና ፡ ብርቱ ። **እብን ፡ ዐቢይ ። ጽላት ፡ ዘእብን ። ንሕንጽ ፡ በእብን ፡** (፩ነገ ፡ ፮ ፡ ፲፬ ። ዘፀ፴፪ ፡ ፲፭ ። ኢሳ፱ ፡ ፲) ።

**እበን ፤ አእባን ፤ (ናት) ፤** ደንጎች ፤ ደንጊያዎች ፤ ድንጋዮች ፤ አዕናቍ ። **እስመ ፡ ሠምሩ ፡ አበኒሃ ። አእባን ፡ ዐበይት ። አእባናት ። አእባነ ፡ ወርቅ ። አእባነ ፡ ህንደኬ ። አእባን ፡ ክቡራት ፡ በበ ፡ ሕበሪሆሙ ፡** (መዝ ፡ ፻፩ ። ኤር፶ ፡ ፱ ። ስንክ ፡ የካ፱ ፡ ግንቦ ። መቃ ፡ ፲፴፭ ። ፩ዜና ፡ ፳፱ ፡ ፪) ። እበን ፡ ኹለት ፡ ወይም ፡ ጥቂት ፤ አእባን ፡ ብዙ ፤ አእባናት ፡ የብዙ ፡ ብዙ ፡ ይባላል ፤ ባለቅኔዎች ፡ ግን ፡ እበንን ፡ የብዙ ፡ ብዙ ፡ ይሉታል ፤ አያሰኝም ፤ እደውንና ፡ እገርን ፡ ተመልከት ።

**አቤኔዜር ፤ (ዕብ ፡ ኤቤን ፡ ሃዔዜር) ፤** እብነ ፡ ረድኤት ፤ የረድኤት ፡ ደንጊያ ። (፩ነገ ፡ ፯ ፡ ፲፪) ።

**እብነ ፡ አድማስ ፤** ርሳስ ፤ ገንቢዎች ፡ ሕንጻ ፡ የሚለኩበት ፤ ብረትና ፡ ደንጊያም ፡ ይኾናል ፡ (ቅዳ ፡ ሕር) ።

**እብነ ፡ እዝኅ ፤** ብልጭት ፡ ደንጊያ ፤ በለታም ፡ (ኢያ፳ ፡ ፪) ።

**እብነ ፡ አስሐትያ ፤** የውርጭ ፡ ደንጊያ ፤ የረጋው ፡ ግግሩ ። ወይም ፡ ውርጭ ፡ የሚመስል ፡ ጽሩይ ፡ የብርሌ ፡ ጠብ ፤ ብርሌ ፡ ዐይነት ፡ ደንጊያ ፡ (ሔኖ፳፩ ፡ ፭) ።

**እብነ ፡ በረድ ፤** በቊሙ ፡ የበረደ ፡ ደንጊያ ፡ እንዳረር ፡ እንደ ፡ ጠጠር ፡ ያለ ፡ ከዚያም ፡ የሚበልጥ ፤ ራስ ፡ የሚሰብር ፡ የሚቀጠቅጥ ፡ (ኢያ፲ ፡ ፲፩ ። ሢራ፵፫ ፡ ፲፯ ። ጥ፮ ፡ ፳ ። ሕዝ፴፰ ፡ ፳፪ ። ሔኖ፲፬ ፡ ፱) ።

**እብነ ፡ በረድ ፤** ነጭ ፡ ደንጊያ ፤ በረድ ፡ የሚመስል ፤ የበረደ ፡ ዐይነት ፡ (ዐማርኛ) ።

**እብነ ፡ ክቡር ፤** ዕንቍ ፡ የዕንቍ ፡ ወገን ፤ ሕብርና ፡ መልክእ ፡ ያለው ።

**እብነ ፡ ኰኵሕ ፤** ጥኑ ፡ ጠንካራ ፡ ኀይለኛ ፡ ደንጊያ ፤ የማይሰበር ፡ የማይፈነከት ፤ አልማስ ፤ አለት ፡ (ዘዳ፰ ፡ ፲፭ ። ሮሜ፱ ፡ ፴፫ ። ኢዮ፵፩ ፡ ፲፱ ። ሕዝ፫ ፡ ፱) ።

**እብነ ፡ ማእዘንት ፤** የማእዝን ፡ ደንጊያ ፡ ማጠፊያውና ፡ መቀነፊያው ፡ ኹለቱን ፡ ማእዘን ፡ የሚይዝና ፡ የሚያያይዝ ፤ ኹለት ፡ ክንፍ ፡ ያለው ፡ (፩ጴጥ ፡ ፪ ፡ ፮) ።

**እብነ ፡ መዳልው ፤** የሚዛን ፡ ደንጊያ ፤ ልክነት ፡ ያለው ፤ ሌላውን ፡ በርሱ ፡ መመዘኛ ፡ ማስተካከያ ፡ (ሕዝ፵ ፡ ፩) ።

**እብነ ፡ መከራ ፤** የፈተና ፡ ደንጊያ ፤ ታላቅ ፡ ከባድ ፤ ክብ ፡ እንክብል ፡ ድንቡልቡል ፤ ጕበዛዝት ፡ ርሱን ፡ በማንሣት ፡ በመሸከም ፡ ጕልበታቸውን ፡ የሚፈትኑበት ፡ (ሢራ፮ ፡ ፳፪) ።

**እብነ ፡ ሞፀፍ ፤** የወንጭፍ ፡ ደንጊያ ፤ ታናናሽ ፡ ኵረት ፤ እንደ ፡ ፍላጻና ፡ እንደ ፡ ጥይት ፡ ርቆ ፡ የሚኼድ ፡ የሚወረወር ፡ (ዘካ፱ ፡ ፲) ።

**እብነ ፡ ቈናማት ፤** የሚዛን ፡ ደንጊያ ፤ ታላቁም ፡ ታናሹም ፡ በየስሙና ፡ በያይነቱ ፡ ተሰብስቦ ፡ በኪስ ፡ በከረጢት ፡ የሚከተት ፡ (ምሳ፲፮ ፡ ፲፩) ።

**እብነ ፡ ሰንፔር ፤** ሰንፔር ፡ የሚባል ፡ ዕንቍ ፤ ክቡር ፡ ደንጊያ ፡ (ኢዮ፳፰ ፡ ፮ ። ፩ቆሮ ፡ ፫ ፡ ፲፪) ።

**አበነ ፤** ደነገየ ፤ ደንጊያ ፡ ኾነ ፤ ወደ ፡ ደንጊያነት ፡ ተለወጠ ፤ ደረቀ ፡ ከረረ ፡ ፈዘዘ ።

**አእበነ ፤** አደነገየ ፤ ደንጊያ ፡ አደረገ ። **እግዚ ፡ አእበና ፡ ወሜጠ ፡ ህላዌሃ ፡ ለከዊነ ፡ ሐውልት ፡** (መጽ ፡ ምስ ። ዘፍ፲፱ ፡ ፳፮) ።

**ኢብን ፡ (ጽር ፡ ይቢስ) ፤** የወንዝ ፡ አሞራ ፡ በወንዝ ፡ ዳር ፡ በባሕር ፡ ጠረፍ ፡ የሚኖር ፤ ነጭ ፡ አሞራ ፤ ረኸም ፤ ትሎችን ፡ ተሐዋስያንን ፡ የሚለቅም ፤ ከዚህ ፡ የተነሣ ፡ ግብጻውያን ፡ ያመልኩት ፡ ነበረ ፡ ይባላል ፡ (ዘሌ ፲፩ ፡ ፲፯ ። ዘዳ፲፬ ፡ ፲፮) ። ዕብራስጡ ፡ ግን ፡ ያንሹፍ ፡ ይላል ፤ ጕጕት ፡ ማለት ፡ ነው ።

**አብኖስ ፡ (ዐረ ፡ አብኑስ ። ጽር ፡ ሄቤኖስ) ፤** ዘጺ ፤ ጥሩ ፡ ጠንካራ ፡ ዕንጨት ፤ መልኩ ፡ ጥቍር ፡ ዋጋው ፡ ክቡር ፤ በህንድና ፡ በሱዳን ፡ አገር ፡ በኢትዮጵያ ፡ የሚገኝ ፤ ከክቡርነቱም ፡ የተነሣ ፡ በሚዛን ፡ የሚሼጥ ። **ወገብረ ፡ መጥቅዐ ፡ እምዕፀወ ፡ አብኖስ ፡** (ቀሌ ። ገድ ፡ አዳ) ። ዘጺን ፡ ተመልከት ።

**አብሠረ ፤—አበሠረ ፤—በሠረ ።**

**አበቅ ፡ (ዕብ ፡ አባቅ) ፤** በቁሙ ፤ ጸበል ፡ ትቢያ ፡ ዐቧራ ፤ ቅንቅን ፤ በነፋስ ፡ የሚበን ፡ ደቃቅ ፡ ነገር ፡ ኹሉ ።

**አበቅ ፡ (ዕብ ፡ ሻሐፍ ። ጽር ፡ እብሶራን) ፤** ደዌ ፡ ሥጋ ፤ ዕከክ ፤ ፈረሳቤት ፡ እንዳበቅ ፡ የሚያለብስ ፡ አበቅ ፡ የሚመስል ፤ ሰውነት ፡ የሚፍቅ ፡ የሚያሰለስል ። **አበቅ ፡ እኩይ ። ደዌ ፡ ቢሕ ፡ ወአበቅ ። ኢዮብ ፡ አመ ፡ አንዘ ፡ አበቅ ። አ ፡ ፈታኔ ፡ ኢዮብ ፡ በደዌ ፡ ወአበቅ ።** (ዘዳ፳፰ ፡ ፳፯ ። መቃ ። ስንክ ፡ መስ፩ ። ጥበ ፡ ጠቢ) ።

**አበቀ ፤** ታመመ ፡ ተደወየ ፤ ዐከከ ፤ ነጣ ፡ ገረጣ ፤ ቈሸሸ ፡ ተበላሸ ። አበቅ ፡ ለበሰ ፤ አበቅ ፡ መሰለ ፤ ኾነ ።

**እቡቅ ፤ (ቃን ፡ ቃት ፡ ብቅት) ፤** ያከከ ፤ ዕከካም ፤ ቈሻሻ ፡ ቋቍሻም ፡ ድውይ ፡ (ዘሌ፳፩ ፡ ፳ ። ፳፪ ፡ ፳፪) ።

**አብቀወ ፤—ከፈተ ፤—በቂው ፡ በቀወ ።**

**አቡቀለምሲስ ፤ (ጽር ፡ አፖካሊፕሲስ) ፤** መጽሐፍ ፡ የመጽሐፍ ፡ ስም ። ቃሉ ፡ ኹለት ፡ ነው ፤ ቅጽልና ፡ ባለቤት ። አፖ ፡ ሩቅ ፡ ረቂቅ ፡ ስውር ፡ ድብቅ ፡ ኅቡእ ፡ ክቡት ፤ ካሊፕሲስ ፡ ራእይ ፡ ትንቢት ። **ራእየ ፡ ዮሐንስ ፡ አቡቀለምሲስ ። ዮሐንስ ፡ ጸሐፈ ፡**

ወንጌለ ፡ ወአቡቀለምሲስ ፡ ዘርእየ ፡ ውስተ ፡ ደሴተ ፡ ፍጥሞ ፡ (ስንክ ፡ ታኅ፭ ። ጥር፲፬) ። እንዳረቡ ፡ ቃል ፡ በአብ ፡ ዘይቤ ፡ ሲፈታ ፡ ግን ፡ ለባለመጽሐፉ ፡ ስምና ፡ ቅጽል ፡ ይኾናል ።

**አቡቀለምሲስ** ፤ አበ ፡ ራእይ ፤ አበ ፡ ትን ቢት ፤ የሕልም ፡ ጌታ ፡ የራእይ ፡ ባለቤት ፤ በዓለ ፡ ራእይ ። ዮሐንስ ፡ ቴዎሎጎስ ፡ ዮሐንስ ፡ አቡቀለምሲስ ፡ ዮሐ ንስ ፡ ዘረፈቀ ፡ ውስተ ፡ ሕፅኑ ፡ ለኢየሱስ ። ወንጌለ ፡ መለኮት ፡ ሰበከ ፡ ስምዐ ፡ ጽድቅ ፡ ኮንከ ፡ ወበእንተ ፡ ዝ ፡ አቡቀለምሲስ ፡ ተሰመይከ ፡ (ድጓ) ።

**አበቅቴ** ፤ (ትያት ። ጽር ፡ ሄፓክቴ) ፤ ጭማሪ ፡ ተውሳክ ፤ የቍጥር ፡ ማማያ ፡ ማስተካከያ ። ተረፈ ፡ ዓመት ፡ የቀመር ፡ ትራፊ ፤ ትርፍ ፡ ፍድፋጅ ። አበቅቴ ፡ ፀሓይ ። አበቅቴ ፡ ወርኅ ። አበቅትያት ። ሠርዐ ፡ ሐሳበ ፡ አበቅቴ ፤ (አቡሻ ፡ ፳፫ ። ፳፭ ። ፴፩ ። ስንክ ፡ ጥቅ፲፪) ።

**አብር ፤ (ብ ፡ አባር ። ዐረ ፡ ኢብረት ፤ ብ ፡ ኢባር)** ፤ እሾኽ ፡ ቀጭን ፡ ሹል ፤ መርፌ ፡ የሚ መስል ። ዕፀ ፡ ግረት ፡ እንዘ ፡ ቈጽለ ፡ ዕፁ ፡ ኢይትነ ገፍ ፡ ወአባሪሁኒ ፡ ኢይጸድፉ ፡ (መጽ ፡ ምስ) ።

**አባር ፤—ድርቅ ፤—ዐቢር ፡ ዐበረ ።**

**እቤር ፤—ባልቴት ፤—ዐቢር ፡ ዐበረ ።**

**አበርባሬ ፤—ዶቢ ፤—በሪር ፡ በረ ፥—በ ርበረ ።**

**አበርጊላ** ፤ ገበጣ ፤ የገበጣ ፡ ጨዎት ፡ (ፍ ፡ ነ ፡ ፵፫ ፡ ፲፪) ።

**አብሮጥስ ፤ (ጽር ፡ ፔሪዎዴፍቲስ)** ፤ ታላቅ ፡ ቆሞስ ፡ የኤጲስቆጶስ ፡ ተከታይ ፡ (ፍ ፡ ነ ፡ ፭) ።

**አብረክሲስ ፤ (ዐረ ፡ አብርክሲስ ። ጽር ፡ ፕራክሲስ)** ፤ መጽሐፍ ፤ የመጽሐፍ ፡ ስም ፤ ግብረ ፡ ሐዋርያት ፤ የሐዋርያት ፡ ሥራ ፤ ዜና ፤ ታሪክ ። መጽሐፈ ፡ አብረክሲስ ፡ (ፍ ፡ ነ ፡ ፪) ።

**አብሬክ ፤ (ዕብ ፡ አብሬኽ ። ጽር ፡ ኪሪ ክስ)** ፤ ትእዛዝ ፡ አንቀጽ ፤ ብርክ ፡ አስተብርክ ፤ ስግድ ፡ አምኅ ፤ ግነይ ፡ ባርክ ። ዮሴፍ ፡ በተሾመ ፡ ጊዜ ፡ ለሰብእ ፡ ግብጽ ፡ የተነገረ ፡ የፈርዖን ፡ ዐዋጅ ፡ ነው ፡ (ዘፍ፵፩ ፡ ፵፫) ። ዳግመኛም ፡ ረበናት ፡ አብሬኽን ፡ አብ ፡ ራኽ ፡ ብ ለው ፡ ፪ ፡ ቃል ፡ አድርገው ፡ ይፈቱታል ፤ አብ ፡ በቁሙ ፤ ራኽ ፡ ለጋ ፡ ቀንበጥ ፡ ጮጠና ፡ ወጣት ። አብ ፡ የተባለ ፡ ዮሴፍ ፡ ነው ፤ ራኽ ፡ በተሾመ ፡ ጊዜ ፡ የ፴ ፡ ዓመት ፡ ልጅ ፡ ነበረና ፡ የድሜውን ፡ ማነስ ፤ አብ ፡ የአእምሮውን ፡ መጕ ልመስ ፡ የሰውነቱን ፡ መሾምና ፡ መንገሥ ፤ ለነፈርዖን ፡ እንዳባት ፡ መኾኑን ፡ ያሳያል ፤ ለወንድሞቹም ፡ ለነሮ ቤል ፡ በመጋቢነቱ ፡ እንደ ፡ ያዕቆብ ፡ አባት ፡ ይባላል ። ረሰየኒ ፡ አበ ፡ ለፈርዖን ። ለደቂቀ ፡ ያዕቆብ ፡ ወዮሴፍ ፡ (ዘፍ፵፭ ፡ ፰ ። መዝ ፡ ፸፯) ። የግእዝ ፡ ኦሪት ፡ ግን ፡ ወልደ ፡ ይላል ። አብሬኽንም ፡ ኤር ፡ አብሬር ፤ ኤል ፡ አብሬል ፡ ይላል ። ባለብሉዮችም ፡ ፍችውን ፡ ዐዋጅ ፡ ዐዋጅ ፡ ገ ብር ፡ ኮን ፡ እግዚአ ፤ ባላገባቦችም ፡ ይደልዎ ፤ ይበጅ ፡ ያድርግ ፡ ይሉታል ፤ ኹሉም ፡ ስሕተት ፡ ነው ።

**አብሪል ፤ (ሮማይ ፡ አፕሪል)** ፤ የወር ፡ ስም ፤ ሚያዝያ ።

**አቢስ ፤ (አቢሲን ፥ አቢሲኔ ፥ አቢሲንያ)** ፤ ስመ ፡ ነገድ ፤ የኵሽ ፡ ልጅ ፡ የሳባ ፡ ሳብዓይ ፡ የናምሩድ ፡ ተከታይ ። ፪ኛ ፡ ስሙ ፡ ከለው ፡ ይባላል ፤ ፪ቱም ፡ በታሪክ ፡ እንጂ ፡ በቅዱስ ፡ መጽሐፍ ፡ አይገኙም ። የሳባ ፡ ክፍል ፡ ሳባ ፡ እንደ ፡ ተባለች ፡ የአቢስም ፡ ክፍል ፡ አቢሲንያ ፡ ተብ ላለች ። አቢሲን ፤ አቢሳውያን ፤ አቢሲኔ ፤ አቢሳዊ ፤ አቢሲ ንያ ፤ ሀገረ ፡ አቢስ ፡ ማለት ፡ ነው ፤ እስክንድርያ ፡ እንደ ፡ ማለት ። ስምነቱም ፡ ከዛፍና ፡ ከተክል ፡ የወጣ ፡ ገንታዊ ፡ ስም ፡ ነው ። ቢሲን ፡ ቢሲና ፡ የሚባል ፡ ፍሬው ፡ የወይን ፡ ፍሬ ፡ የሚያክል ፡ ጥሩ ፡ ተክል ፡ አለ ፤ ሕብሩ ፡ እጅግ ፡ ፍጹም ፡ ቍጥር ፡ እጅግም ፡ ፍጹም ፡ ቀይ ፡ ሳይኾን ፡ ደበብ ፡ ያለ ፡ ማእከላዊ ፡ ነው ፤ ጣዕሙና ፡ መልኩ ፡ ደም ፡ ግባቱ ፡ ከመዐዛው ፡ ጋራ ፡ ደስ ፡ ያሰኛል ። አቢሲንም ፡ ማለት ፡ እንደ ፡ ቢሲን ፡ ፍሬ ፡ የሚያምር ፡ የቢሲና ፡ ፍሬ ፡ የሚመስል ፡ ማእከላዊ ፡ ሕብር ፡ ያለው ፡ ጥሩ ፡ ደመ ፡ ግቡ ፡ ማለት ፡ ነው ። ስኒጋል ፡ የሚባለው ፡ ነገድ ፡ የሱ ዳን ፡ ቍራጭ ፡ እንደ ፡ ኾነ ፤ መደገዝክርም ፡ የአቢስ ፡ ቍራጭ ፡ ነው ፡ ይባላል ፤ ይኸውም ፡ በቅርጹና ፡ በመል ክአ ፡ ገጹ ፡ ይታወቃል ፡ (ጽርኣዊ ፡ ታሪክ) ።

(ጥ) **አብሶ ፤ ሶት ፤ (አበሰ ፡ ይኤብስ ፡ የአ ብስ ። ዕብ ፡ አባስ)** ፤ ማብላት ፡ ማጥገብ ፤ መቀለብ ፡ መመገብ ፤ ማሥባት ፡ ማወፈር ፤ ከብትን ፡ ሰውነትን ። ወይም ፡ በቁሙ ፡ ማበስ ፡ መጥረግ ፤ አብዝቶ ፡ መብላት ፡ መጋፈፍ ፤ እንደ ፡ እንስሳ ፡ መቀለብ ፤ መሥባት ፡ መወ ፈር ። ከዚህ ፡ የተነሣ ፡ ማበስ ፡ መበደል ፤ ኀጢአት ፡ መሥ ራት ፤ ዐውቆ ፡ ደፍሮ ፡ ኾነ ፡ ብሎ ። አብሶ ፡ አበሰት ። ኢይደግሙ ፡ አብሶ ። ዘይገብር ፡ ኃጢአተ ፡ ይኤ ብስ ፡ ላዕለ ፡ ነፍሱ ። ኢተአብስ ፡ በቃልከ ። መላ እክት ፡ አበሱ ፡ ምስለ ፡ አዋልደ ፡ ሰብእ ። ዳዊት ፡ አመ ፡ አበሰ ፡ በብእሲተ ፡ ኦርዮ ፡ (ሰቈ፩ ፡ ፰ ። ሔኖ፩ ፡ ፰ ። ሢራ፲፱ ፡ ፬ ። ፴፭ ፡ ፲፪ ። ኩፉ ፡ ፬ ። ዲድ ፡ ፲) ።

**አባሲ ፤ (ሲት ፡ ስያን ፡ ያት)** ፤ የሚያበስ ፡ የሚበድል ፤ በዳይ ፡ በደለኛ ፤ ያዋቂ ፡ አጥፊ ፤ ደፋር ፤ ጥጋ በኛ ። ኃጥእ ፡ ወአባሲ ። አባሲ ፡ ዝንቱ ፡ ሕዝብ ፡ አ በሳ ፡ ዐቢየ ፡ (አርጋ ። ዘፀ፴፪ ፡ ፴፩) ።

**መአብስ ፤ (ስት ፡ ሳን ፡ ሳት)** ፤ ዝኒ ፡ ከ ማሁ ፤ በደለኛ ። ዘይስሕት ፡ በአሐቲ ፡ ኮነ ፡ መአብሰ ፡ በኵሉ ። መአብስ ፡ ውእቱ ፡ ላዕለ ፡ እግዚእነ ፡ (ያዕ፪ ፡ ፲ ። ፍ ፡ ነ ፡ ፲፫) ።

**እቡስ ፤ (ሳን ፡ ሳት ፡ ብስት)** ፤ ያበሰ ፡ የበ ደለ ፤ አበሰኛ ፤ ኃጥእ ፡ ወንጀለኛ ። እቡሰ ፡ ትሬስዮሙ ። እቡሳነ ፡ ልብ ። ተሰቅለ ፡ ከመ ፡ እቡስ ፡ (ምሳ፲፫ ፡ ፮ ። መጽ ፡ ምስ ። ስንክ ፡ መጋ፳፯) ።

**እብሰት ፤** ማበስ ፤ መበደል ፡ አበዳደል ፤ በደላ ፡ በደል ፤ ኀጢአት ፡ ክሕደት ። ወእምዝ ፡ በርሕቀት ፡ መዋዕል ፡ ተእኅዘ ፡ ልማደ ፡ እብሰት ፡ ወርስዐት ፡ (ጥበ፲፱ ፡ ፲፯) ።

**አበሳ ፤ (ሳት) ፤** በቁሙ ፤ ዕዳ ፡ በደል ፤ ኀጢአት ፤ ክሕደት ። አልብየ ፡ አበሳ ። አበሳ ፡ ዘኢኮነ ፡ ለሞት ፤ እስመ ፡ ቦ ፤ አበሳ ፡ ዘለሞት ። ኅድግ ፡ ለነ ፡ አበሳነ ። ወዘይመስሎ ፡ ለዝንቱ ፡ እምአበሳት ። ገባር ያነ ፡ አበሳት ፡ (ኢዮ፴፬ ፡ ፮ ። ፩ዮሐ ፡ ፭ ፡ ፲፯ ። ፈ ፡ መ ፡ ፮ ፡ ፩ ። ፍ ፡ ነ ፡ መቅ) ።

**አአበሰ ፤** አሳበሰ ፤ አስበደለ ፤ ኀጢአት ፡ አሠራ ። እንተ ፡ ታኤብስ ፡ ምድረ ፡ (ኩፋ ፡ ፳፻) ።

**አአባሲ ፤ መአብስ ፤** የሚያሳብስ ፤ የሚያስበድል ፤ አገባሪ ፡ ኀጢአት ፡ አሠሪ ።

(ጥ) **አባስ ፤ (ሱርስት) ፤** መምህር ፤ አበ ፡ ማኅበር ፤ አበ ፡ ምኔት ፡ የገዳም ፡ አባት ፡ (ሥር ፡ ጳሖ) ። አባስ ፡ ካህን ፡ ሮሜ ፡ (ታምረ ፡ ማር) ።

**አቡሻህር ፤—መጽሐፍ ፤—አብ፥አቡ፡ ሻህር ።**

**አብስሊዲስ ፤ (ጽር ፡ እብሳልቲስ) ፤** መዘምር ፡ ዘማሪ ፤ አወዳሽ ፡ ደብተራ ፡ (ፍ ፡ ነ ፡ ፱) ።

**አብስልዋጥስ ፤ (ሮማይ፡ አብሶሉቲዮኒስ) ፤** የፍታት ፡ ቃል ፡ የፍታት ፡ ሥርዐት ፡ ናዛዥ ፡ ለተናዛዥ ፡ የሚያሰማው ፡ ቃል ፤ እፈትሐከ ፤ ኩን ፡ ፍቱሐ ፤ ፍትሐት ፡ ዘወልድ ፡ ይህን ፡ የመሰለ ። የፍታት ፡ ዜማ ፤ ለሙታን ፡ የሚጸለይ ፡ ጸሎት ፤ በግንዘት ፡ ያለ ፡ ቃል ፤ ፍትሕተ ፡ ወንጽሕተ ፡ ረስየ ፤ የመሰለው ፡ ኹሉ ። አብስልዋጥስ ፡ ይትበሀል ፡ በዜማ ፡ ግንዘት ፡ (ግንዘ) ።

**አቢሳ ፤—በዓለ፡ ጋዳ ፤—አቢብ፡ አብ ።**

**አብሲማዳክስ ፤ (ጽርእ) ፤** ከኹለት ፡ አንድ ፡ የኾነ ፡ አምላክና ፡ ሰው ፡ ፩ ፡ አካል ።

**አብሰረ ፤—አበሠረ ፤—በሠረ ።**

**አቢት ፤ ቶት ፤ (አበተ ፡ የአብት ፡ ይእብት) ፤** ማበት ፡ ሸብ ፡ ማድረግ ፤ ወይም ፡ መማገር ፡ አጥብቆ ፡ ማሰር ፤ አብታረግ ፡ እንዲሉ ፤ ኹሉም ፡ ዐማርኛ ፡ ነው ።

**አጊድ ፤ ዶት ፤ (አገደ ፡ የአግድ ፡ ይእግድ ። ዕብ ፡ አጋድ ፤ አሰረ ፡ የነዶ ፡ የችቦ) ፤** በቁሙ ፡ ማገድ ፡ መከልከል ፡ መግታት ። መስበር ፡ መቀልጠም ፤ መክፈል ፡ መለየት ፤ የሥጋና ፡ ያጥንት ።

**አገዳ ፤ (ዳት) ፤** እግር ፡ ዛል ፤ ጭን ፡ ማኽል ፡ አገዳ ፡ ቅልጥም ፡ የእጅና ፡ የእግር ፤ መደበኛ ፡ ዐጥንት ። ዘቦ ፡ አገዳ ፡ መልዕልተ ፡ እገሪሁ ። አገዳሁ ፡ ዘየማን ። ያነጕዕ ፡ አገዳሆን ። ተሰብረት ፡ አሐቲ ፡ አገዳ ፡ እግሩ ። ሌዊ ፡ እኅወ ፡ ይሁዳ ፡ ዘሀብተ ፡ ክህነቱ ፡ አገዳ ፡ (ዘሌ፲፩ ፡ ፳፩ ። ፯ ፡ ፴፪ ። ዘካ፲፩ ፡ ፲፯ ። ገድ ፡ ተክ ። ደራሲ) ።

—፤ ዐጥቅ ፡ አንጓ ፡ ክፍል ፤ የሽመልና ፡ የቀርከሐ ፡ የመቃ ፡ የሸንበቆ ፡ የሸንኰር ፤ የጥንቅሽ ፡ ያገዳ ፡ እኽል ፡ ኹሉ ። (ቅኔ ፡ ራስ ፡ መኰንን ፡ ዐደ ፡ ሳሉ) ፤ ጣሊያንንሂ ፡ የማሽላ ፡ እሸት ፡ እንድታበላው ፡ ጠብሰኽ ፤ ምኒልክ ፡ ያ ፡ ደገኛ ፡ ይመጣልና ፡ ወደ ፡ ቤትኽ ፤ አምጥተኽ ፡ ቈየው ፡ በፊት ፡ ራስ ፡ ራሱን ፡ ቈርጠኽ ፤ አገዳውንስ ፡ ይመጡታል ፡ እየሰባበሩ ፡ አሽከሮችኽ ።

**አግዋል ፤—ዘለላ ፤—ዐግዋል ።**

**እግዚእ ፤—ጌታ ፤—ግዚእ ፡ ገዝአ ፤ አግዝአ ።**

**አጋዘን ፤ አጋዜን ፤** በቁሙ ፤ የዱር ፡ የበረሓ ፡ ላም ፤ ቀንዳም ፡ ቀንደ ፡ ረዥም ፡ (አዋል) ።



አጋዘን ፡

**አግዮስ ፤ (ጽር ፡ አጊዎስ) ፤** ቅዱስ ፤ ክቡር ፡ ምስጉን ፡ (ቅዳ ። ግንዘ) ።

**አግያ ፤ (አጊያ) ፤** ቅድስት ። አግያ ፡ ሶፍያ ። እልመስጦ ፡ አግያ ፡ (አዋል ። ሃይ ፡ አበ) ።

**አግያስማንጦን ፤ (ጽር ፡ አጊዮ ፡ ፕኔፍማቶስ) ፤** ቅዱስ ፡ መንፈስ ፡ (ቅዳ) ።

**አጕል ፤—በቁሙ ፤ ክብ ፡ እንክብል ፤—ዐጕል ።**

**አግል ፤—ዝኒ ፡ ከማሁ ፤—ዐግል ።**

**እጓል ፤—ልጅ ፤—ዕጓል ።**

(ጥ) **አገለ ፤ ተአገለ ፤—ቀማ ፤—ዐግሎ ፡ ዐገለ ።**

**እገሌ ፤—በቁሙ ፤—ገልይ ፡ ገለየ ፤ አግለየ ።**

**አጋም ፤ (ዕብራ ፤ የውሃ ፡ ቦታ ፤ ወንዝ ፡ ኩሬ) ፤** በቁሙ ፡ አጋም ፤ ያጋም ፡ ፍሬ ፡ ጣዕሙና ፡ መልኩ ፡ ከማንሱ ፡ በቀር ፡ የጥቍር ፡ ወይን ፡ እሸት ፡ የሚመስል ፡ ጥፍጥ ፤ ዕንጨቱ ፡ እሾኻም ፡ ዐጥር ፡ የሚኾን ።

**አግመረ፤** (አስደራጊ)፤ ገሚር፡ ገመረ፤ ግሙራ ።

**አግሙስ፤** (ብዙ)፤ ገሚስ፡ ገመሰ፤ ገመስ፡ ገሙስ ።

**አጊን፤ ኖት፤** (አገነ፡ የአግን፡ ይእግን ። ዐረ፡ ዐጀነ፤ አበከ)፤ መቈረጥ፡ መክፈል፡ ማሥመር፤ የሊጥ ። መገመት፡ ይህን፡ ያኽል፡ ማለት፡ የዋጋ ። አገና፤ ዋጋ፡ ገኙና፡ ሸያጭ፡ የሚስማሙበት፡ (ዐማርኛ) ።

**አግን፤** ቡሖ፡ ሊጥ ።

**አገን፤** ንፍጥ፡ ያፍንጫ፡ እድፍ፡ (ሐባብ) ።

**ኤጎንጤ፤** (ጽር፡ ጎኒኤ)፤ ውስጥ፤ ውሳጢት፡ (ሕዝ፵፩፡ ፲፭) ።

**እጕሥታር፤—ሬት፤—ፅጕሥታር ። ፅጕትሣር + ዐገተ ።**

(ጥ) **አግሮ፤ ሮት፤** (አገረ፡ ይኤግር፡ የአግር ። ትግ፡ ሐባብ፡ አግረ ። ዐረ፡ ጀራሀ ። ዕብ፡ አጋር፤ ሰበሰበ)፤ ሞኼድ፡ መራመድ፤ መሮጥ፡ መፈርጠጥ፤ እግራም፡ እግረኛ፡ መኾን ። በቁሙ፤ ማገር፡ መገርገር፡ ማወክ፡ መክልከል፤ ከመንገድ፡ ከሥራ፡ ማስተጓጐል ።

**አጋር፤** (ራን፡ ራት ። አጋሬ፡ ሬት፡ ርያን፡ ያት)፤ እግረኛ፡ ሯጭ፡ ገሥጋሽ፤ ኻያጅ፡ ተራማጅ፤ ዕድሜው፡ ኻያ፡ ዓመት፡ የመላ፤ ከዚያም፡ በላይ፡ እስከርባ፡ ዓመት፡ ያለ፡ ጐበዝ፡ ጐልማሳ፤ ወታደር፡ ሰልፈኛ፡ ዘማች፤ ባዋጅ፡ በቱልቱላ፡ የተጠራ፡ የተሰበሰበ ። ስሳ፡ እልፍ፡ አጋር ። አጋሮሙ ። አጋርያን ። ዐሠርቱ፡ ምእት፡ አጋር፡ ብእሲ፤ (ዘፀ፲፪፡ ፴፯ ። ዘኍ፲፩፡ ፳፩ ። ዮዲ፯፡ ፳ ። ፪፡ ፲፱ ። ፪ነገ፡ ፲፫፡ ፯) ።

**መአግር፤** (ርት፡ ራን፡ ራት)፤ ዝኒ፡ ዓዲ፡ ከማሁ፡ ለአጋር፡ ወአጋሬ ።

**አጋር፤** (ዕብ፡ ሀጋር)፤ ስመ፡ ብእሲት፤ የፈርዖን፡ ዲቃላ፡ ከገረድ፡ የተወለደች፤ ኋላም፡ ለአብርሃም፡ ሚስት፡ ለሳራ፡ ገረድ፡ ትኹንሽ፡ ብሎ፡ የሰጣት፤ የይስማኤል፡ እናት ። ፍችው፤ ግይርት፡ ፈላሲት፡ ኰብላይ፡ ማለት፡ ነው፤ የመኼድና፡ የመራመድ፡ የሩጫ፡ የግሥገሣ፡ ምስጢር፡ አለበት፡ (ዘፍ፲፯፡ ፩—፲፯) ።

**አጋራዊ፤** (ዊት፡ ውያን፡ ያት)፤ ያርበኛ፡ ወገን፡ ዐርበኛ፤ የጦር፡ ሰው ። የአጋር፡ ልጅ፡ የይስማኤል፡ ዘር ። ወሰብአ፡ ኢትዮጵያ፡ ጸሊማን፡ ወአጋራውያን፤ ዐርበኛ ። ሞአብ፡ ወአጋራውን፤ ይስማኤላዊ፡ (ገድ፡ ፊቅ ። መዝ፡ ፹፪) ።

(ላ) **አግሬ፤** በቁሙ፤ አላባሽ፡ ጋሻ፡ (ዐማርኛ) ።

**እግር፤** (ዕብ፡ ሬጌል ። ሱር፡ ሬግላ ። ዐረ፡ ሪግል)፤ በቁሙ፤ መቆሚያ፡ መርገጫ፤ መኼጃ፡ መራመጃ፤ ከጭን፡ እስከ፡ ሰኰና፤ እንደ፡ እጅ፡ ፫፡ ክፍል፡ ያለው ። ኪደተ፡ እግረ፡ ብእሲ ። ከመ፡ እግር፡ ሙቁሕ ። እግር፡ ቦሙ፡ ወኢየሐውሩ ። እግረ፡ ሰብእ፡ ወእንስሳ ። ክልኤ፡ እግር ። ዘአርባእቱ፡ እግሩ፡ (ሉቃ፡ ዕዝ፭፡ ፯ ። ሚራ፳፭፡ ፲፱ ። መዝ፡ ፻፲፫ ። ሕዝ ፳፱፡ ፲፩ ። ዓሞ፫፡ ፲፪ ። ዘፀ፱፡ ፱) ።

እግር፡

**እግር፤** እግሮች፡ ለብዙም፡ ለጥቂትም፡ ባንድ፡ ገላ፡ ላሉ፡ ላራትም፡ ለኹለትም፡ ብቻ፡ ከዚያም፡ ለሚበዙ፡ ላምሳና፡ ለሺሕ፡ ይነገራል ። ሺ፡ እግር፤ ዐምሳ፡ እግር፡ እንዲሉ ። ወይቀውማ፡ እገሪሁ ። እገሪሆሙ፡ ይረውጻ ። ወድቀ፡ ውስተ፡ እገሪሃ፡ ለዮዲት ። ርቱዕ፡ እገሪሆሙ ። ዘብዙኅ፡ እገሪሁ፡ (ዘካ፲፬፡ ፬ ። ምሳ፩፡ ፲፮ ። ዮዲ፲፬፡ ፯ ። ሕዝ፩፡ ፯ ። ዘሌ፲፩፡ ፵፪) ።

**አእጋር፤** (ራት)፤ ዝኒ፡ ከማሁ፤ እግሮች ። አእጋራት፤ የብዙ፡ ብዙ ። ኦ፡ አእጋር፡ እለ፡ አንሶሰዋ፡ ውስተ፡ ገነት፡ ተቀነዋ፡ በቅንዋት ። ሰላም፡ ለአእጋሪከ፡ እለ፡ ጠብዓ፡ ለቀዊም፡ (ቅዳ፡ አፈ ። ደራሲ) ።

**እግር፤** ታች፡ ታችኛ፤ ሥር ። ታሰከቦ፡ ለኀጕዝ፡ ኀበ፡ እግረ፡ ታቦት፡ (ግንዘ) ።

**እግር፤** ጫማ፤ ውስጥ፡ እግር፤ የጥላ፡ መስፈሪያ፤ ከተረከዝ፡ እስካውራ፡ ጣት፡ ጫፍ ። ጽላሎት፡ በግንቦት፡ ዕሥራ፡ ወአሐዱ፡ እግር፡ ወመንፈቀ፡ እግር፡ (አዋል ። ቁር) ። ግልያን፡ ተመልከት ።

**እግር፤** ጮራ፤ ጨረር፤ ቀርን፡ ምዕዛር ። እግረ፡ አሚር ። እገሪሃ፡ ለፀሓይ ። በረቀ፡ ሥጋሆሙ፡ ከመ፡ እግረ፡ ፀሓይ፡ (ጥበ፪፡ ፬ ። ሔኖ፸፩፡ ፬ ። መቃ፡ ገ፪) ።

**እግረ፡ ደቂቅ፤** የሕፃናት፡ መንገድ፤ የልጆች፡ አካኼድ፡ አረማመድ፤ አቱ፡ ሥግራ፡ ታቱ፡ ሥግራ፡ ማለት፤ ምስጢሩ፡ ጕዞና፡ ማዝገም፡ ነው፡ (ዘፍ፴፫፡ ፲፬) ።

**እግረ፡ ማጣ፤** (ዕብ፡ ሬጌል፡ ሚጣ)፤ የኪሩቤል፡ ስም፤ ያራቱ፡ ኹሉ ። ዘይቤው፡ ያልጋ፡ ሸንኰር፡ የዙፋን፡ እግር፤ ምስጢሩ፡ ጸወርተ፡ መንበር፡ (ድጓ ። መዋሥ) ። ቅዱስ፡ ያሬድ፡ እንዲህ፡ ማለቱ፤ ጌታን፡ በንጉሥ፤ መንበረ፡ መንግሥትን፡ በኮር፡ በግላስ፤ ሰማይ፡ ውዱድን፡ ባልጋ፡ በፈረስ፤ ኪሩቤልን፡ ባራት፡ እግሮቹ፡ መስሎ፡ ነው ። (ሕዝ፩፡ ፳፮ ። መዝ ፲፯፡ ፲፩) ።

**እግረ፡ መራጕት፤** የመክፈቻች፡ እግር፡ መያገርቸው፡ መንጠልጠያቸው፡ ቀለበቱ፤ ወይም፡ ሳንቆች፡

የሚቆሙበት ፣ መድረክ ፤ የመዝጊያ ፣ ቍላ ፤ ወንደው ፣ (አዋል) ።

**እግራዊ ፤** እግራም ፣ እግረኛ ፤ ዘዋሪ ፤ እግሯ ፣ ብዙ ፤ ሺ ፣ እግር ፣ ዐምሳ ፣ እግር ፣ የሚሉት ፣ ጥቍር ፣ ትል ።



እግራዊ ፣

**አግሬም ፤ (ዕብ ፡ ሀግሬም ፤ ሀግሪኢም) ፤** አጋራውያን ፣ የይስማኤል ፣ ልጆች ፣ በዮርዳኖስ ፣ ማደ ፣ ያሉት ። ፈለገ ፡ አግሬም ፡ (፩ዜና ፣ ፭ ፣ ፲፱ ። ፪ዜና ፣ ፳፭ ፣ ፲፭) ። ጽርኡና ፣ ዕብራይስጡ ፣ ግን ፣ ፈለገ ፣ ጴው ፣ ይላል ፤ የባሕረ ፣ ጴው ፣ ዱሓ ፤ ሸለቆ ፤ ወደ ፣ ባሕረ ፣ ጴው ፣ የሚፈስ ፣ ወንዝ ፣ ማለት ፣ ነው ።

**አግሬም ፤ (ዕብ ፡ ጊር ፤ ኖራ) ፤** መገይራን ፤ ኖራ ፣ አውጮች ፤ ሸያጮች ፣ ቀቦች ፣ ለቅላቆች ። እሊሁም ፣ ስብአ ፣ ስደም ፣ ናቸው ፤ የጊርንና ፣ የስደምን ፣ ፍቺ ፣ ተመልከት ።

**አግሬጳስ ፤** ፬ ፣ እግር ፣ ያለው ፣ አሞራ ። ወሀሎ ፡ ዖፍ ፡ ዘይሰመይ ፡ አግሬጳስ ፡ በሀገረ ፡ ቃራት ፡ ወቦ ፡ አርባዕቱ ፡ አእጋር ፤ ይመሥጥ ፡ ሶረ ፡ ወይሰርር ፡ መልዕልተ ፡ አየር ፡ እንበይነ ፡ ጽንዑ ፡ (ጊ ፣ ወ ፣ ሐ ፣ ገ፳፱) ። ፪ኛም ፣ የሰው ፣ ስም ፣ ይኾናል ፣ (ግብ፳፭ ፣ ፲፫) ።

**አገተ ፤—ከበበ ፤—ዐጊት ፣ ዐገተ ።**

**እድ ፤—እጅ ፡ እጀታ ፤—አዲው ፣ አደወ ።**

**አዲግ ፤ ጎት ፤ (አደገ ፣ የአድግ ፣ ይእድግ ። ዐረ ፣ ሐደጀ) ፤** መሸከም ፤ መጫን ፤ ማንገት ፣ ማዘል ፣ መደብለል ፤ ተሸካሚ ፣ መኾን ፤ በገርባ ። በቁሙ ፤ ማደግ ፣ መመንደግ ፤ ቁመትና ፣ ጕን ፣ መጨመር ፤ ለሸክም ፣ ለጭነት ፣ መብቃት ፤ የሰው ፣ የከብት ።

**አድግ ፤ (ብ ፡ አእዱግ ፤ ጋት) ፤** ተሸካሚ ፤ የጭን ፣ የጭነት ፣ የኮርቻ ፣ ከብት ፤ አህያ ፣ አጋሰስ ፣ በቅሎ ፣ ፈረስ ፣ ገመል ፣ ዝኆን ። ስምንቱ ፣ የግብር ፣ ነውና ፤ ለኹ



አድግ ፣

ሉም ፣ ይኾናል ፤ ልማዱ ፣ ግን ፣ ላህያ ፣ ብቻ ፣ ነው ። አድግ ፡ ወላሕም ። አድገ ፡ ጸላኢከ ። ወተገድፉ ፡ አእዱጊሁ ፡ ለቂስ ። አእዱግ ፡ ፍኖቶሙ ፡ (ቅዳ ። ዘፀ ፳፫ ፣ ፭ ። ፩ነገ ፣ ፱ ፣ ፫ ። ቅኔ) ።

**አድግት ፤ እድግት ፤ (ብ ፡ አእድግት ፤ እድግታት) ፤** እንስት ፣ አህያ ፤ አህዩት ፤ አህዪት ፤ ወላድ ፣ እመጫት ። ይጼዐን ፡ ዲበ ፡ እድግቱ ። ዲበ ፡ እድግት ፡ ወዲበ ፡ ዕዋል ፡ ዕጓለ ፡ እድግት ፡ (ዘኍ፳፪ ፣ ፳፱ ። ማቴ፳፩ ፣ ፭) ። እድግታት ፣ በማለት ፣ ፈንቃ ፣ አእዱግ ፣ አእኑስ ፣ ይላል ፤ አያሰኝም ፣ (ኢዮ፩ ፣ ፫) ። ፈረስን ፣ ተመልከት ።

**አድገ ፡ ገዳም ፤** የዱር ፣ የበዳ ፣ አህያ ፣ ሠጋር ፣ ጠጕረ ፣ መልካም ፤ ነብርማ ፣ ሽልምልም ፤ ሽመልመሌ ፣ ዐይነት ። ሐለስትዮን ፣ እይ ። ወኮንኩ ፡ ከመ ፡ አድገ ፡ ገዳም ። በበዓሎሙ ፡ ለአእዱገ ፡ ገዳም ፡ (ኢዮ፳፱ ፣ ፭ ። ኢሳ፴፪ ፣ ፲፬ ። ሔኖ፹፱ ፣ ፲፩) ።



አድገ ፣ ገዳም ፣

**አድገ ፡ መረብ ፤ (ዕብ ፡ ቃአት ፣ ሚድባር ። ጽር ፡ ፔሊካን) ፤** ያፈ ፣ መረብ ፤ የበዳ ፣ ርኩም ፤ ቀቀኖ ፤ ወይም ፣ የርኩም ፣ ዐይነት ፣ መረብ ፤ ጋጋኖ ፣ የባሕር ፣ ደሮ ። እሊህ ፣ ኹሉ ፣ አንድ ፣ ወገን ፣ ናቸው ፤ ይመሳሰላሉ ፤ ቀቀኖንና ፣ መረብን ፣ ተመልከት ፤ አድግ ፣ ማለት ፣ ግን ፣ የመላሽ ፣ ስሕተት ፣ ነው ፣ (መዝ፻፩ ፣ ፮ ። ዘሌ፲፩ ፣ ፲፰) ። ማሕረጸ ፣ አድግ ፣ ቢል ፤ የወፍጮ ፣ ግልገል ፣ ማለት ፣ ነው ፤ አድግ ፣ ታችኛው ፣ እናቱ ፣ ተሸካሚው ፤ ማሕረጽ ፣ ላይኛው ፣ ልጁ ፣ መጁ ። ባለሐዲሶች ፣ ግን ፣ አህያ ፣ የሚያዞረው ፣ የመዘውር ፣ ወፍጮ ፣ ይሉታል ፣ (ማቴ፲፰ ፣ ፮) ።

**አድው ፤—ደመኛ ፣ ባለጋራ ፤—ዐደወ ።**

**አዲው ፤ ዎት ፤ (አደወ ፣ የአዱ ፣ ይእዱ ። ዕብ ፣ ያዳህ) ፤** መዋረግ ፣ መጋፍ ፤ መግፋት ፣ ማስገለል ፤ መኰስተር ፣ መሰብሰብ ፣ ዐፍሦ ፣ መጣል ፤ መወርወር ፣ ማሽቀንጠር ፤ የጕድፍ ። ወነሥአ ፡ ደናግል ፡ ማእድወ ፡ ወአደዋ ፡ ወአውፅኣ ፡ ሾሎ ፡ መሬት ፡ እምዐውደ ፡ ማኅፈድ ፡ (ሄርማ) ።

**አዲው ፤** እጃም ፣ ባለእጅ ፣ መኾን ፤ እጀ ፣ ሥራ ፣ ማወቅ ፤ በተግባረ ፣ እድ ፣ መሠልጠን ፣ መራቀቅ ። መያዝ ፣ መጨበጥ ፤ እጅ ፣ ማድረግ ፤ ከእጅ ፣ ማግባት ።

**አዳዊ ፤ (ዊት ፣ ውያን ፣ ያት ፤ አደውት) ፤** የሚጠርግ ፣ ጠራጊ ፤ ባለወግ ፤ የከተማ ፣ የቤት ፣ ከሲያን ።

**ማእድው፤ (ብ፡ መአድው፡ ዎት)፤** መጥረጊያ፤ የጕድፍ፡ መማሪያ፡ ማስገለያ ።

**ተአደወ፤** ተጠረገ፤ ተኰሰተረ፤ ተከወነ፤ ቤቱ፡ ጕድፉ ።

**እድው፤ (ዋን፡ ዋት፡ ዱት)፤** የተጠረገ፤ የተኰሰተረ፤ ጕድፍ፡ የሌለበት ። ይረክቦ፡ ዕሩቀ፡ ወእድወ፡ ወስርግወ፡ (ማቴ፲፪፡ ፵፬ ። ሉቃ፲፩፡ ፳፭ ። ሄርማ) ።

(ጥ) **እዳው፤ (ዋት)፤** ጕድፍ፤ ጥራጊ፤ ሐመድ፤ ርካሽ፡ ሣር፡ ገለባ፤ ፍግ፡ ዐዘባ ። ገደፍኩ፡ ኵሎ፡ ወረሰይክዎ፡ ከመ፡ እዳው ። ይከውን፡ ኵሉ፡ ዓለም፡ በንቤሁ፡ ከመ፡ እዳዋት፡ ወከመ፡ ኈስሕ ። ኢይገኑ፡ እዳዋተ፡ (ፊልጵ፫፡ ፰ ። አፈ፡ ተ፲፰ ። ፍ፡ ነ፡ ፴፮ ። ኢሳ፵፡ ፳፪) ።

**እድ፤ (ዕብ፤ ሱር፤ ያድ ። ዐረ፡ የድ)፤** እጅ፤ የገላ፡ ክንፍ፤ መሥሪያው፡ መማሪያው፤ ከመቶ ክፍት፡ እስከ፡ አጽባዕት፤ እንደ፡ እግር፡ ፫፡ ክፍል፡ ያለው፤ ጡንቻ፡ ክንድ፡ መዳፍ ። እዴየ፡ ከ፡ ኪ፡ ሁ፡ ሃ፤ እዴነ፤ ክሙ፡ ክን፡ ሆሙ፡ ሆን፡ እያለ፡ እንደ፡ ኀበ፡ በኃምስ፡ ይዘረዝራል ። ምስጢሩ፡ ሥራን፡ መደብ፡ አድርጎ፡ ኀይልና፡ ሥልጣንን፡ ያሳያል ። እትሕቲ፡ ርእሰኪ፡ ታሕተ፡ እዴሃ ። በእድ፡ ጽንዐት ። እድ፡ ፀቡስ ። ኵሉ፡ እድ፡ ይደክም ። እድ፡ በሙ፡ ወኢይገቡ ። ደይ፡ እዴከ፡ ላዐለ፡ እዴየ ። መጥወኒ፡ እዴከ፤ ወመጠዎ፡ እዴሁ ። ከለባት፡ ይበልዕዋ፡ ለለትረ፡ እዴነ፡ ኤልዛቤል፡ (ዘፍ፲፯፡ ፱ ። ዘፀ፮፡ ፩ ። ሚራ፳፩፡ ፳፫ ። ኢሳ፲፫፡ ፯ ። መዝ፡ ፻፲፫ ። ዘፍ፳፱፡ ፪ ። ፬ነገ፡ ፲፡ ፲፩ ። ቅኔ) ።



እድ፡

**እደው፤ እእዳው፤ (ዋት)፤** እጆች፤ የገላ፡ ቅጥዮች፤ ፀጽቆችና፡ ክንዶች ። እደው፡ ኹለት፡ እእዳው፡ ብዙ፡ እእዳዋት፡ የብዙ፡ ብዙ ። እበን፡ ዕፀው፡ ቍየጽ፡ እገር፡ ዕየን፡ እዘን፤ እንደዚህ፡ ያለ፡ ይሆን፡ የመሰለ፡ ስም፡ ኹሉ፡ መንሻው፡ መድረሻው፡ ሳድስ፡ ኹኖ፡ መከከሉ፡ ግእዝ፤ ዘውግ፡ ይባላል ። ኹለትም፡ አራትም፡ ቢኾኑ፡ ከዚያም፡ ቢበዙ፡ ተባብረው፡ ተጣፍረው፡ ተነጻጽረው፡ ባንድ፡ በታና፡ ባንድ፡ ገላ፡ ብቻ፡ ያሉትን፡ ያሳያል ። ቀነዉኒ፡ እደውየ፡ ወእገርየ ። ሰፍሐ፡ እደዊሁ፡ ለሕማም ። ኦ፡ እእዳው፡ እለ፡ ለሐኳሁ፡ ለአዳም፡ ተቀነዋ፡ በቅንዋት፡ (መዝ፡ ፳፩ ። ቅዳ፡ ዲዮ ። አፈ) ።

**እድ፤** ቃል፤ አፍ፤ እንደበት ። ወገብረ፡ እግዚ፡ ላዕሌከ፡ በከመ፡ ነበበ፡ በእዴየ ። ዘነበበ፡ በእደ፡ ኤርምያስ፡ ነቢይ ። ወኮነ፡ ቃለ፡ እግዚ፡ በእደ፡ ሐጌ፡ ነቢይ ። አምኑ፡ በእደዊሆሙ፡ (፩ነገ፡ ፳፰፡ ፲፯ ። ኤርሚ፱፡ ፱ ። ሐጌ፩፡ ፩ ። ስንክ፡ መስ፳፯) ። እድ፡ ቃል፡ መባሉ፡ አፍ፡ ሲናገር፡ እጅም፡ እንደ፡ ምላስ፡ ይሠራልና፡ ከቃል፡ ጋራ፡ ተባባሪነት፡ ስላለው፡ ነው ። አንሥአ፡ እዴሁ፡ ጳውሎስ፡ (ግብ፳፮፡ ፩) ።

**እድ፤** ወርች፤ የፊት፡ እግር፤ የእንስሳትና፡ የአራዊት ። (ተረት)፤ ወርች፡ የረገጠው፡ እግር፡ አይስተው ። ዘየሐውር፡ በእደዊሁ ። ላጽቂት፡ ዘበእደዊሁ፡ የሐውር፡ (ዘሌ፲፩፡ ፳፯ ። ምሳ፳፱፡ ፳፫) ።

**እደ፡ አቤሴሎም፤** ታላቅ፡ ሐውልት፤ አቤሴሎም፡ ለስሙ፡ ማስጠሪያ፡ ያቆመው፤ ኋላም፡ የተቀበረበት ። ምስጢሩ፡ በታ፡ ማለት፡ ነው፡ (፪ነገ፡ ፲፰፡ ፲፰) ።

**እደ፡ አትሮንስ፤** ድጋፍ፡ መከዳ፤ የመንበረ፡ መንግሥት፡ ጌጥ፤ የንጉሡ፡ እጆች፡ የሚረከዙት፡ የሚመረኰዙት ። ለመጽሐፍ፡ ሲኾን፡ ግን፡ መልሕቅ፡ ያሰኛል፤ አትሮንስን፡ እይ፡ (፫ነገ፡ ፲፡ ፲፱) ።

**እደ፡ ኀጺን፤** የብረት፡ እጅ ። በሰው፡ እጅ፡ አምሳል፡ የተሠራ፡ ብረት፤ የሰማዕታት፡ መማቀያ ። ገብሩ፡ አምሳለ፡ እድ፡ ወአጻብዕ፡ ዘኀጺን ። በእደው፡ ኀጺን፡ እንዘ፡ ይጸፍዕ፡ ገጾ፡ (ስንክ፡ ሐም፳ ። ግን፳፩) ።

**እደ፡ ኀጺን፤** የሐኪም፡ መማሪያ፤ መመርመሪያ ። የሻርት፡ የጥንቁላ፡ ብረት፡ መሰግላን፡ የሚያሻርቱበት ። እድ፡ ዘኀጺን፡ ዘየሐትት፡ ዘውስተ፡ ከርሥ፡ (ስንክ፡ ጥር፲፭ ።

**እደ፡ የማን፤** የቀኝ፡ እጅ፤ የቀኝ፡ ወርች፡ በግራ፡ አንጻር፡ ያለ፡ (ሚራ፳፩፡ ፳፩) ።

**እደ፡ ኵናት፤** የጦር፡ እንደበት፤ ቀጠሉ፡ ጫፉ፡ ሹሉ፡ ውልብልቢቱ፤ ወይም፡ ዘቢያው፡ ሶማያው ። (ተረት)፤ በጋሻው፡ ዕንብርት፡ በጦሩ፡ እንደበት፡ በፈረሱ፡ ፀንገት፡ (ኤር፲፰፡ ፳፩) ።

**እደ፡ መንሠግ፤** የመዝጊያ፡ እጀታ፤ ወይም፡ የመወርወሪያው፤ ለመክፈት፡ ለመዝጋት፡ የሚያዘው፡ (ማሕ፭፡ ፭) ።

**እደ፡ ሰይፍ፤** አፈ፡ ሰይፍ፤ ስለት፡ እንደበት፤ ወይም፡ ውላጋ፡ እጀታ፡ መክድ፡ (መዝ፡ ፳፪) ።

**እደ፡ ሰናስል፤** ፍንጅ፤ የሰንሰለት፡ እጅ፤ እስርና፡ ቍራኛ፡ በየክንዳቸው፡ የሚያገቡት፡ (መዝ፡ ፻፵፱) ።

**እድ፤** ጐን፡ ሕፅን፤ ቅርብ፡ አጠገብ፡ የቦታ፡ አዋሳኝ፡ ጎረ፡ ቤት፡ ድንበረተኛ፤ ቀበሌ፡ አውራጃ፡ ግድም፡ ገደማ ። ኀበ፡ እደ፡ ኤማት ። መንገለ፡ እደ፡ ማየ፡ ባሕር ። በእደ፡ ባሕር፡ (ሕዝ፵፰፡ ፩ ። ኩፋ፡ ፳ና፡ ፲ ።) ።

**እድ፤** ክፍል፤ የክፍል፡ ስም ። የኀልቅ፡ ክልኤ፡ እድ፤ ወይትርፍ፡ ሣልስተ፡ እዴሃ ። ራብዐተ፡ እዴሃ፡

ለምድር ። ትሰቲ ፡ ሳድስተ ፡ እዴሃ ፡ ለኢን ። ብር
ሃነ ፡ ዚኣሁ ፡ ሰብዐተ ፡ እደ ፡ ያበርሀ ፡ እምዘወርኀ ።
ለዝኩ ፡ ሳብዕተ ፡ እድ ፡ (ዘካ፲፫ ፡ ፰ ፡ ፱ ። ራእ፮ ፡ ፰ ።
ሕዝ፱ ፡ ፲፩ ። ሔኖ፸፱ ፡ ፴፯ ። ሱቱ ፡ ዕዝ፵፱ ፡ ፶፰) ።

**እድ ፡ ወእድ ፤** ዐቢይና ፡ ደቂቅ ፡ አገባብ ።
ፍችውን ፡ በወእድ ፡ ተራ ፡ ተመልከት ፤ ሊጣፍ ፡ የሚገ
ባው ፡ ከዚህ ፡ ነበረ ፤ ወ ፡ በዋዌንት ፡ ገብቶ ፡ ማርኮ ፡
ስለ ፡ ወሰደው ፡ የወ ፡ ጭፍራ ፡ ኹኗል ።

**አደየ ፤—ከፈለ ፤—ዐድይ ፡ ዐደየ ፤
ዕዳ ።**

**አድያማ ፤** ስመ ፡ ሀገር ፤ ክምስቱ ፡ አህጉረ ፡
ስደም ፡ አንዲቱ ።

**አድያም ፤ (ማት) ፤** ደወል ፡ ዙሪያ ፡ አውራጃ ፤
ሰበካ ፡ ገጠር ፡ ታናናሽ ፡ አገር ፤ ጕልት ፡ ግዛት ። **አህ
ጕር ፡ ወአድያሚሆን ። በዙሉ ፡ አድያሚነ ። አድ
ያማተ ፡ ትግሬ ፡** (ዘኍ፴፩ ፡ ፱ ። ዳን፱ ፡ ፲፯ ። ገድ ፡
ተክ) ። አድያም ፡ የአዲም ፡ ብዝር ፡ ውስጠ ፡ ብዙ ፡ ነው ።
አድያማም ፡ የወጣው ፡ አዲም ፡ አዲሞት ፡ አዳማ ፡ አ
ዳሞት ፡ ከማለት ፡ ነው ።

(ሳ) **አዲም ፤ ሞት ፤ (አደመ ፡ የአድም ፡ ይ
እድም ። ዕብ ፡ አዳም ። ዐረ ፡ አዲመ) ፤** መቅ
ላት ፡ ቀይ ፡ መኾን ፡ ደም ፡ መምሰል ፡ ዐለላ ፡ እንሶስላ ፡
መግባት ፡ በቀይ ፡ ስባቅ ፡ መነከር ፡ መታሰል ፤ የንት ፡
የልብስ ።

**አዲም ፤ (ብ ፡ አድያም) ፤** ቅጽልና ፡ ጥሬ ።
ቀይሕ ፡ ቀይሓዊ ፤ ደምማ ፤ ዐረብ ፡ አንቀልባ ፤ ንት ፡ የገባ ፡
ቈርበት ። **ማእስ ፡ በግዕ ፡ ግቡረ ፡ አዲም ። ቅናት ፡ ዘአ
ዲም ። ቅናታቲሆሙ ፡ አዲም ፡** (ዘፀ፴፱ ፡ ፳፩ ። ፱ነገ ፡
፩ ፡ ፰ ። ማቴ፫ ፡ ፱ ። ማርሸ ፡ ፯ ። ሥር ፡ ጳዥ) ።

**ኤዶም ፤ ኤዶምያስ ፤** የዔሳው ፡ ስምና ፡ ሀ
ገር ፤ ቀይሕ ፡ ማለት ፡ ነው ፡ (ዘፍ፳፭ ፡ ፴ ። ኢሳ፷፫ ፡ ፩ ።
መዝ ፡ ፶፱) ።

**ኤዶማዊ ፤** የዔሳው ፡ ዘር ፡ የኤዶምያስ ፡ ሰው ።
ዔዲንን ፡ እይ ።

**አዳማ ፤ (ዕብራ) ፤** ምድር ፡ የብስ ፡ ገራህት ፤
ቀይ ፡ መሬት ፤ መረሬ ፤ ቅላቱ ፡ ሸክላ ፡ ሕኍሬ ፤ ብስል ፡
በርበሬ ፡ የሚመስል ፤ ያፈር ፡ ወይዘሮ ። አዳማ ፡ በሴት ፡
አንቀጽ ፡ ነው ፤ ሲያበዛ ፡ አዳሞት ፡ ይላል ። ጋላም ፡ ቀይ ፡
ሲል ፡ ዲማ ፡ ዳማ ፡ ይላል ።

**እድሞ ፤ (ዐማርኛ) ፤** ያፈር ፡ ቤት ፤ ግድግ
ዳው ፡ የግንብ ፤ ጣራው ፡ የንጨት ፡ ኹኖ ፡ ክዳኑ ፡ ዐፈር ፡
መሬት ፤ እንደ ፡ ትግሬና ፡ እንዳደሬ ፡ ሥራ ። የግንብ ፡
ዐጥር ፡ ቅጥር ፡ መካበቢያ ፤ ወይም ፡ ዐፈር ፡ ቃም ፡ ካብ ።

(ጥዳ) **አዳም ፤** በቁሙ ፤ መዠመሪያ ፡ ሰው ፡ የሰው ፡
ኹሉ ፡ አባት ፤ ጕበዝ ፡ ጕልማሳ ፡ ወንድ ፡ ተባት ። የሥ
ጋው ፡ ተፈጥሮ ፡ ካፈር ፡ ከመሬት ፡ ስለ ፡ ኾነ ፡ አዳም ፡
መባልን ፡ ከአዳማ ፡ ወስዷል ። ሥጋው ፡ እምድር ፡ ዘተ
ሠገወ ፡ እመሬት ፤ ጽቡር ፡ ልሕኵት ፤ ቀይሐ ፡ ሥን ፡
ብሑሐ ፡ አምጣን ፡ ማለት ፡ ነው ፡ (ዘፍ፱ ፡ ፲፯ ፡ ፲፱—፳፫) ።
ኹለተኛም ፡ እንስሳዊና ፡ መልአካዊ ፡ ፱ ፡ ባሕርያት ፡
ስላሉት ፤ በሥጋው ፡ መዋቲ ፡ ድኩም ፡ ፈራሽ ፡ በስባሽ ፤
በነፍሱ ፡ ነባቢ ፡ ለባዊ ፡ ሕያው ፡ ባለአእምሮ ፡ ይባላል ፡
(ዘፍ፱ ፡ ፯) ። አዳም ፡ በ፮ኛ ፡ ቀን ፡ መዠመሪያ ፡ ከ
ምድር ፡ የፈለቀ ፡ የሰው ፡ ኹሉ ፡ ምንጭ ፡ ስለ ፡ ኾነ ፡
በዘር ፡ በሩካቤ ፡ ከርሱ ፡ እየተቀዳ ፡ ሞትና ፡ መቃብር ፡
የሚጠጡት ፡ ምድራዊ ፡ ሰው ፡ ኹሉ ፡ በርሱ ፡ በምንጩ ፡
ስም ፡ አዳም ፡ ይባላል ፡ (ዘፍ፫ ፡ ፲፱) ። ግእዝ ፡ ግን ፡
ዕብራይስጥና ፡ ዐረብ ፡ ትግሬና ፡ ዐማርኛም ፡ ሳይቀሩ ፡
አዳም ፡ የሚሉትን ፡ ለውጦ ፡ ዕጓለ ፡ መሕያው ፡ ይላል ፤
ፍችውን ፡ በበታው ፡ ተመልከት ።

**አዳማዊ ፤** የአዳም ፡ ዘር ፡ ሰው ፤ ወይም ፡ ባሕ
ርዩና ፡ ግብሩ ፡ ተፈጥሮው ። **ልሕዙት ፡ አዳማዊት ፡**
(ያዕ ፡ ዘእል) ።

(ፐ) **አድሞ ፤ ሞት ፤ (አደመ ፡ ይኤድም ፡ የአ
ድም) ፤** ማማር ፡ መዋብ ፤ ደማም ፡ ደመ ፡ ግቡ ፡ መኾን ፡
ማስጕምዠት ፡ ደስ ፡ ማሰኘት ፤ በባሕርይ ፡ በመልክ ፡
አዳምን ፡ መምሰል ፤ ከርሱ ፡ መተካከል ። **ሥን ፡ ወላ
ሕይ ፡ ይኤድማ ፡ ለዐይን ። እንተ ፡ አደመቶ ፡ እም
ኔሆን ፡ ብእሲት ። ሰበ ፡ ተፈሥሐ ፡ በአድሞ ፡ ሥነ ፡
ላሕዩሙ ። ቍርባንክሙ ፡ ኢይኤድመኒ ። አደሞ ፡
ቃላ ፡ በቅድሜሁ ። በከመ ፡ ይኤድመከ ፡ ግበር ፡ ም
ስሌየ ። ዙሎ ፡ ዘነሰየ ፡ ወአደሞ ፡ ለሰሎሞን ፡ በነፍሱ ፡
ከመ ፡ ይግበር ፡** (ሢራ፵ ፡ ፳፪ ። አስቴ፪ ፡ ፱ ። ጥበ፲፫ ፡ ፫ ። ኤ
ኤር፮ ፡ ፳ ። ዮዲ፲፩ ፡ ፳ ። ጠቢ፫ ፡ ፯ ። ፱ዜና ፡ ፯ ፡ ፲፩) ።
በአደመ ፡ ፈንታ ፡ አስተአደመ ፡ ይላል ፤ ስሕተት ፡ ነው ።
**ኢያስተኤድሞ ፡ ሀጕሎሙ ፡ ለሕያዋን ፡** (ጥበ፩ ፡ ፲፫) ።

**አዳም ፤** የሚያምር ፤ ደስ ፡ የሚያሰኝ ፤ ውብ ፡
ደግ ፡ መልካም ፤ መልክ ፡ መልካም ። እንደዚህ ፡ ያለው ፡
ውስጠ ፡ ዘ ፤ ነቋር ፡ ጸጓር ፡ ፀዋግ ፡ ጸያፍ ፤ የዋህ ፡ መ
ካሕ ፤ ሀካይ ፡ ይህን ፡ የመሰለ ፡ ዐጓጕል ፡ ቃል ፡ ኹሉ ፡
ቅጽልነቱ ፡ ፈናፍንታም ፡ ነው ፤ ለወንድም ፡ ለሴትም ፡
ይኾናል ። **ወራዙት ፡ ዘአዳም ፡ አርአያሆሙ ። አዳም ፡
አጥባትኪ ፡ እምወይን ። ከመ ፡ ማይ ፡ ቊዕር ፡ አዳም ፡
ለነፍስ ፡ ጽምእት ። አዳም ፡ ወሠናይት ። አዳመ ፡
ዝክር ፡ ወዜና ። ወከነ ፡ አዳመ ፡ ዝንቱ ፡ ነገር ፡ በቅ
ድመ ፡ ንጉሥ ፡** (ዮሴፍ ። ማሕ፩ ፡ ፱ ። ምሳ፳፭ ፡ ፳፭ ።
ድጓ ። ስንክ ፡ ሐም፲፱ ። ፱ዜና ፡ ፴ ፡ ፬) ።

**መአድም ፤ (ምት ፡ ማን ፡ ማት) ፤** ዝኒ ፡
ከማሁ ፤ የሚያምር ። **እስ ፡ ሠናይ ፡ ራእዮሙ ፡ ወመ
አድም ፡ ሥዕሙ ። ብእሲ ፡ ቀይሕ ፡ መአድም ፡ ገጹ ፤
መአድምት ፡ ብእሲት ። መዐርዒር ፡ ነገር ፡ ወመአ
ድም ፡ ንባብ ፡** (አፈ ፡ ተ፲፯ ። ገድ ፡ ተክ ። ስንክ ፡ ኅዳ፳፯) ።

**እዱም ፤ (ማን ፡ ማት ፡ ድምት) ፤** ያማረ ፡
ያጌጠ ፡ የተዋበ ፡ ውብ ፤ መልካም ፤ ደመ ፡ ግቡ ። ሰበ ፡

ሎረ ፡ በፍኖት ፡ ርእየ ፡ እዱመ ፡ ብእሴ ፡ ለቢሶ ፡ አልባሰ ፡ ጸዐዳ ። እዱመ ፡ ዜና ። እድምት ፡ ሥን ፡ (ዮሴፍ ። አዋል) ።

**አአደመ ፤ (ያኤድም ፡ ያአድም) ፤ አው ፡ አስተአደመ ፤ ያስተኤድም ፡ ያስተአድም ፤** አሳመረ ፤ አስማመረ ፤ አደነቀ ፤ አመሰገነ ፤ አጣጣመ ፤ ደስ ፡ ብሎት ፡ ሠራ ፡ አዘጋጀ ። ንፍረት ፡ አስተአድሞ ፡ ብእሲት ፡ ባዕድ ። አየ ፡ እምክልኤቱ ፡ ግብራት ፡ ትዌድስ ፡ ወታስተኤድም ። ኢያስተአደምኩ ፡ ስቴሁ ፡ ለንጉሥ ። ወባዕድኒ ፡ ዘአስተአደሙ ፡ በሕይወቶሙ ፡ (ሚራጓ፩ ፡ ፳ ። አፈ ፡ ድ፳፯ ። አስቴ፱ ። ፪ዕዝ ፡ ፩ ፡ ፮) ።

**እድሜ ፤—ቀጠሮ ፤—ዐደመ ።**

**አድማስ ፤ (ጽር ፡ አዳማስ ። ዕብ ፡ አናኽ ። ዐረ ፡ ዚጅ) ፤** ናእክ ፤ ርሳስ ፤ ወይም ፡ ብረት ፤ የሐዲስ ፡ ሕንጻና ፡ የማእዝን ፡ ልክ ፤ መመዘኛ ፡ ማስተካከያ ፤ ነደቅት ፡ በቀጭን ፡ ገመድ ፡ ጫፍ ፡ አስረው ፡ እንደ ፡ መልሕቅ ፡ ከላይ ፡ ወደ ፡ ታች ፡ የሚሰዱት ። የደንጊያው ፡ ተራ ፡ የማእዝኑ ፡ ሥራ ፡ አለአድማስ ፡ አይቃናም ፤ ማእዝኑ ፡ ደግሞ ፡ ከርሱ ፡ ስም ፡ ንሥቶ ፡ አድማስ ፡ ይባላል ። ወናሁ ፡ ብእሲ ፡ ይቀውም ፡ ዲበ ፡ አረፍት ፡ አድማስ ፤ ወውስተ ፡ እዴሁ ፡ አድማስ ። ከመ ፡ ቅጽረ ፡ አድማስ ፡ (ዓሞ፯ ፡ ፯ ፡ ፰ ። ራእ ፡ ባሮ) ። አድማስ ፡ የልክ ፡ የሚዛን ፡ የማእዝን ፡ ስም ፡ ስለ ፡ ኾነ ፡ ባለቅኔዎች ፡ የምድር ፡ ዳር ፡ ዙሪያዋ ፡ ከበቧ ፡ ቅጥሯ ፡ ዳር ፡ ድንበሯ ፡ ይሉታል ። ወተሀውከት ፡ ዙላ ፡ ሀገር ፡ ኢየሩሳሌም ፤ ፍኖት ፡ አድማስ ፡ መከራሃ ፡ አኮኑ ፡ ኢይትፌጸም ። ወእንዘ ፡ ዳዊት ፡ ያስቁቁ ፡ በተፈልጦ ፡ አምኖን ፡ ነፍስ ፡ ካዕበ ፡ አደንገፆ ፡ ርሒቀት ፡ አቤሴሎም ፡ አድማስ ፡ (ቅኔ) ።

አድማስ ፤

**አድማስ ፤ (ዐረ ፡ አልማስ ። ዕብ ፡ ሐላሚሽ) ፤** የደንጊያ ፡ ንጉሥ ፤ አልማዝ ፡ ፅንቍ ፡ ፈርጥ ። ጥኑ ፡ ጠንካራ ፡ ደንጊያ ፤ ኩሖሕ ፡ እሳት ፡ የማይሰበር ፡ የማይፈነክት ። የነጠረ ፡ ብረት ፤ ደንጊያ ፡ የሚጠርብ ፡ ኩሖሕ ፡ የሚነድል ፤ የሚበሳ ፡ የሚሰረስር ። እብነ ፡ አድማስ ፡ ሠራዊ ፡ ወደምሳሴ ፡ ዙሉ ። ጽኑዕ ፡ ውእቱ ፡ ዘኢይትሔየክ ፤ ዘውእቱ ፡ እብነ ፡ አድማስ ፡ ኀያል ። መላዩ ፡ ኅዳውንት ፡ አድማስ ፡ (መቃ ፡ ገጽ፩ ። ቅዳ ፡ ሕር ። ስንክ ፡ ኅዳ፲፪) ።

**አደነ ፤—በቁሙ ፤ ሻ ፡ ፈለገ ፤—ዐደነ ።**

**አዶናይ ፤ (ዕብ ፡ አዶን ፤ ጌታ ። አዶኒ ፤ ጌታዬ ። አዶኒም ፡ ጌቶች) ፤** ስመ ፡ አምላክ ፤ ይዝርዝር ፡ ነው ፤ እግዚእየ ፡ አጋዕዝትየ ፤ ወይም ፡ ጌታዬ ፡ ጌቶቼ ። ላንድም ፡ ለብዙም ፡ ይኾናል ፤ ዐዋጁ ፡ ግን ፡ የብዙ ፡ ወንዶች ፡ ነው ፡ (ሕዝ፪ ፡ ፬) ። ከመ ፡ ዝ ፡ ይቤ ፡ አዶናይ ፡ እግዚአብሔር ፡ ተብሎ ፡ ለአምላክ ፡ ሲቀጠልና ፡ የአምላክ ፡ ስም ፡ ሲኾን ፡ ምስጢሩ ፡ ምስጢረ ፡ ሥላሴ ፡ ነውና ፤ አንድነትን ፡ መደብ ፡ አድርጎ ፡ ሦስትነትን ፡ ያሳያል ፤ ዘይቤውም ፡ ጌቶቼ ፡ እግዚአብሔር ፡ እንዲህ ፡ አለ ፡ ያሰኛል ። ይቤ ፡ አንድነቱን ፤ እግዚአብሔር ፡ ባሕርዩን ፡ መለኮቱን ፤ አዶናይ ፡ አካላቱን ፡ ያመለክታል ። ይኸውም ፡ ሊታወቅ ፡ ኢሳይያስ ፡ የሱራፌልን ፡ ምስጋና ፡ ፫ ፡ ቅዱስ ፡ ከተናገረ ፡ በኋላ ፤ ወሰማዕኩ ፡ ቃሎ ፡ ለአዶናይ ፡ እንዘ ፡ ይብል ፡ መኑ ፡ እፌኑ ፡ ወመኑ ፡ የሐውር ፡ ለነ ፡ ኀበ ፡ ዝ ፡ ሕዝብ ። ወእቤ ፡ ናሁ ፡ አነ ፡ ፈንወኒ ፡ ይላል ። ለነ ፡ ዝርዝሩ ፡ ለአዶናይ ፡ ነው ፤ ንግበር ፡ ሰብእ ፡ በአርአያነ ፤ ንዑ ፡ ንረድ ፡ ያለውን ፡ ይመስላል ። አይሁድ ፡ ግን ፡ አንድ ፡ ገጽ ፡ ባዮች ፡ ስለ ፡ ኾኑ ፡ ራሱን ፡ ከሱራፌል ፡ አግብቶ ፡ ይላሉ ። በኦሪትና ፡ በነቢያት ፡ ይህን ፡ የመሰለ ፡ ብዙ ፡ አለ ፤ ኤሎሄን ፡ ተመልከት ። አዶናይ ፡ በቋንቋ ፡ ኹሉ ፡ ለአምላክ ፡ ሲቀጸል ፡ እግዚእ ፤ ለሰው ፡ ሲቀጸል ፡ አጋዕዝት ፡ ይባላል ፤ ያውም ፡ ቢኾን ፡ ለብዙዎች ፡ ብቻ ፡ እንጂ ፡ ላንድ ፡ ሰው ፡ ብቻ ፡ አይቀጸልም ። ዕብራይስጡ ፡ አዶናይ ፡ ሱኑና ፡ ኤል ፡ ቤት ፡ ዐብዴኼም ፡ ባለው ፡ ግእዙና ፡ ዐረቡ ፡ ሌላውም ፡ ኹሉ ። አጋዕዝትየ ፡ ገሐሡ ፡ ቤተ ፡ ገብርክሙ ፡ እንዲል ፡ (ዘፍ ፲፱ ፡ ፪) ። እግዚእ ፡ አጋዕዝት ፡ የሚያሰኘው ፡ አንቀጹ ፡ እንደ ፡ ኾነ ፡ አስተውል ፤ ይቤ ፡ አዶናይ ፤ ገሐሡ ፡ አዶናይ ።

**አዶናዊ ፤ አዶናይ ፤ (አዶናውያን ፡ አዶናይያን) ፤** እግዚኣዊ ፤ ወልደ ፡ እግዚእ ፤ ዘቦቱ ፡ እግዚእና ። ዓለመኛ ፡ ባላዱኛ ፤ ዘመናይ ። ንትቀበል ፡ መርዓዌ ፡ አዶናዌ ፡ (ድጓ) ። አዱኛ ፡ አዱኛ ፡ ማለት ፡ ቅሉ ፡ አዶን ፡ ከማለት ፡ የወጣ ፡ ነው ።

**አዲፍ ፤ ፎት ፤ (አደፈ ፡ የአድፍ ፡ ይእድፍ) ፤** ማደፍ ፡ መኾለፍለፍ ፤ እድፋም ፡ ጕድፋም ፡ መኾን ።

**አደፍ ፤ (ብ ፡ አእዳፍ) ፤** በቁሙ ፡ እድፍ ፡ ጕድፍ ፤ ርስሐት ፡ እዳው ። ግብ ፡ ዘምሉእ ፡ አደፈ ፡ ወዕፄ ፡ (ስንክ ፡ ሐም፩) ።

**አደፍ ፤** የሴቶች ፡ ግዳጅ ፡ ትክቶ ። ተርታ ፡ መናኛ ፡ እኽል ፡ ንፋሽ ፡ ገለባ ፡ ሐሠር ፡ ያለው ። ጥሩና ፡ አደፍ ፡ እንዲሉ ፡ (ዐማርኛ) ።

**አደፋዊ ፤ (ዊት ፡ ውያን ፡ ያት) ፤** እድፋም ፡ ጕድፋም ፡ ጭቅቅታም ።

**አዳር ፤ (ራት ። ዕብራ) ፤** የዕብራውያን ፡ ወር ፡ መጋቢት ፡ የጥቅምት ፡ ፮ኛ ፡ የሚያዝያ ፡ ፲፪ኛ ፤ በሠግር ፡ ጊዜ ፡ ፲፫ኛ ፡ (አስቴ፫ ፡ ፯ ። ዕዝ፮ ፡ ፲፭) ። ፍችው ፡ ዕበይ ፡ ርሒብ ፡ ልዕልና ፡ ማለት ፡ ነው ፤ ኅዳርን ፡ ተመልከት ። (ታሪክ) ፤ በ፫ ፡ በ፫ ፡ ዓመት ፡ አንዳንድ ፡ ወር ፡

ሠግር ፡ እየጨመረ ፡ ዓመታቸው ፡ ፲፫ ፡ ወር ፡ ይኾናል ፤ ስለዚህ ፡ መጋቢት ፡ ካለቀ ፡ በኋላ ፡ እንደ ፡ ገና ፡ መጋቢት ፡ ይላሉ ። ይኸውም ፡ ፀሐይ ፡ ከጨረቃ ፡ የምታተርፈው ፡ ፲ ፡ ፲ ፡ ቀን ፡ አለና ፡ ያ ፡ ተሰብስቦ ፡ ነው ። ወሰሰ ፡ ሠለስቱ ፡ ዓመት ፡ ያሠግሩ ፡ አሐደ ፡ ወርኀ ፡ ወይከውኑ ፡ አዳራት ፡ ክልኤተ ፡ (አቡሻ ፡ ፳) ።

**አደር** ፤ እሾኽም ፡ ዕንጨት ፡ ጋሬጣ ፤ እሾኹ ፡ እንደ ፡ ችንካር ፡ ያለ ፤ መርዛም ።

**አዴራ** ፤ አደርማ ፤ ቀኖት ፡ የቀኖት ፡ ስም ፤ አራተኛ ፡ ቀኖት ፡ የቀኝ ፡ እግሩ ። ሳዶር ፡ አላዶር ፡ ዳናት ፡ አዴራ ፡ ሮዳስ ፤ ኀምስቱ ፡ ቅንዋተ ፡ መስቀል ፡ (አዋልድ ፡ የጸሎት ፡ መጽሐፍ) ። ቀኖት ፡ ማለትም ፡ ችንካሩን ፡ ብቻ ፡ አያሳይም ፡ ስቍረቱንም ፡ እንጂ ፤ ዐምስተኛው ፡ ቀኖት ፡ ኵናት ፡ ነው ።

**አዲር** ፤ (ብ ፡ አዲሪም ፡ ዕብራ) ፤ ክቡር ፡ ምስጉን ፡ ታላቅ ፡ ገናና ። ጥቀ ፡ ተሰብሐ ፡ ባለው ፤ ማህ ፡ አዲር ፡ ሽምኻ ፡ እንዲል ፡ (መዝ ፡ ፰) ።

**አድሮሄም** ፤ (ዕብ ፡ አዲሬሄም ። ጽር ፡ አዶሪም) ፤ ዐበይቶሙ ፤ ጽኑዓኒሆሙ ፤ ክቡራኒሆሙ ፤ መላእክ(ህቅ)ቲሆሙ ፡ ማለት ፡ ነው ። ባለብሉዮች ፡ ግን ፡ ገባሮች ፡ ይሉታል ፡ (ነሐ፫ ፡ ፭) ።

**አድርያ ፤ አድርያቲክ** ፤ የባሕር ፡ ስም ፤ በኢጣልያና ፡ በግሪክ ፡ መካከል ፡ ያለች ፡ (ግብ፳፯ ፡ ፳፯) ።

**አዴሮት** ፤ (ዕብ ፡ አዴሬት ፤ ብ ፡ አዳሮት) ፤ የላይ ፡ ልብስ ፡ ታላቅ ፡ ሰፊ ፤ ጀባ ፡ ካባ ፡ መጐናጠፊያ ፤ ኀይል ፡ ጽንዕ ። ባለቅኔዎች ፡ ግን ፡ ሥርጥ ፡ መንገድ ፡ ዕዳሪ ፡ ሸንት ፡ ይሉታል ፡ (ጥሬ ፡ ስዋ) ።

**አደስ** ፤ (ዕብ ፡ ወሱር ፡ ሀዳስ) ፤ በቁሙ ፤ የሽቱ ፡ ዕንጨት ፤ ሽነት ፡ ባርሰነት ። ምርስኔን ፡ ተመልከት ፤ ከዚህ ፡ ጋራ ፡ አንድ ፡ ነው ።

**አደሳን** ፤ (ሳት ። ሱር ፡ ሀዳሲን ። ዕብ ፡ ሀዳሲም) ፤ አደሶች ፡ የሽነት ፡ የባርሰነት ፡ ዛፎች ። ማእከለ ፡ አዕዋም ፡ ዘአደሳን ፡ (ዘካ፩ ፡ ፰) ። አንዳንድ ፡ መጣፍ ፡ ዘአደሼም ፡ ይላል ፤ አንዳንዱም ፡ አደሼምን ፡ ትቶ ፤ በአዕዋም ፡ ፈንታ ፡ ማእከለ ፡ ክልኤ ፡ አድባር ፡ ይላል ፤ ኹሉም ፡ ስሕተት ፡ ነው ።

**አህ** ፤ (ዕብ ፡ አሀህ) ፤ ንኡስ ፡ አገባብ ። የሐዘን ፡ የጭንቅ ፡ ያሉታ ፡ የነቀፌታ ፡ ቃል ፤ መታመም ፡ መጐስም ። አይ ፡ አዬ ፤ ዋይ ፡ ወዮ ፤ ወዲያልኝ ፡ ወዲያ ፤ እህ ፡ እህህ ፤ ሐሰ ፡ ኀድግ ፤ ይኾናል ። (ግጥም) ፤ ሰው ፡ ኹሉ ፡ ገብቶ ፡ አገሩን ፤ እህናኔ ፡ (እኔ) ፡ ቀረን ። አህ ፡ አህ ፡ እምዛቲ ፡ ኀፍረት ። አህ ፡ እምዛቲ ፡ ሕሠም ፡ (አፈ ፡ ተ፲፩ ። ፲፭ ። ሕዝ፱ ፡ ፲፱) ። ኹለተኛም ፡ አንክሮና ፡ ብፅዓን ፡ የደስታ ፡ ቃል ፡ ይኾናል ፤ ሐሰ ፡ ኀድግ ፡ ከማለት ፡ በቀር ፡ ዐማርኛው ፡ አይለወጥም ። አህ ፡ አህ ፡ ሊድምፀ ፡ ቅኔሆሙ ። አህ ፡ አህ ፡ ሚ ፡ መንክር ፡ ወመድምም ። አህ ፡ አህ ፡ አንደደኒ ፡ ፍቅርከ ፡ (ግንዘ ። አረጋ) ።

**አሆ** ፤ ነባር ፡ አንቀጽ ፤ የትሕትና ፡ የተአዝዞ ፡ ቃል ። ዕሺ ፡ በጎ ፤ በጄ ፤ ይኹን ፤ አደርጋለኹ ፤ ምስጢሩ ፡ እንደ ፡ መሐላ ፡ ነው ። ወይቤሉ ፡ አሆ ፡ ናገብእ ፡ ሎሙ ፡ በከመ ፡ አዘዝከነ ፡ ከማሁ ፡ ንገብር ። ኢትበልዎ ፡ አሆ ፡ ለፍትወቱ ። አሆ ፡ ብሂልየ ፡ ለመማክርትየ ። አሆ ፡ በሃሊት ። አሆ ፡ በልነ ። በእንተ ፡ አሆ ፡ ብሂሎቱ ፡ ወትሕትናሁ ፡ (ነሐ፭ ፡ ፲፪ ። ሮሜ፮ ፡ ፲፪ ። አስቴ ፡ ፫ ። ዳን፩ ፡ ፳ ። ያዕ፫ ፡ ፲፯ ። ፊልክ ፡ ፺፰፱) ።

(ጥያ) **አህያ** ፤ (ቅብጥ ፡ ሄያ ፤ ሄሄያ) ፤ በቁሙ ፤ አድግ ፤ ሲጮኽ ፡ ሀሀሀ ፡ የሚል ። (ተረት) ፤ ዳኛ ፡ ቢያጋድል ፡ በዳኛ ፤ አህያ ፡ ቢያጋድል ፡ በመጫኛ ። አህያ ፡ ሠባ ፤ ካልተበላ ፡ ምን ፡ ረባ ።

(ላ) **አህያ ፡ ሸራህያ** ፤ (ዕብ ፡ ኤሀዬ ፡ አሼር ፡ ኤሀዬ) ፤ ስመ ፡ አምላክ ፤ እሄሉ ፡ ዘእሄሉ ፡ ወይም ፡ እከውን ፡ ዘእከውን ፡ (ዘፀ፫ ፡ ፲፬) ። ሦስተኛም ፡ በዚሁ ፡ ቍጥር ፡ ከዚሁ ፡ ኢየይዘ ፡ ኤሀዬ ፡ ሽላሐኒ ፡ ይላል ፤ እሄሉ ፡ ፈነወኒ ፡ ማለት ፡ ነው ፤ አንቀጹን ፡ ስም ፡ አድርጎታል ። ዘይቤው ፡ ላባቶቻችኹ ፡ ለሦስቱ ፡ ኹሉ ፡ በጭንቃቸው ፡ ጊዜ ፡ እሄሉ ፡ ምስሌክ ፡ ያላቸው ፡ አምላክ ፡ ያሰኛል ፤ ምስጢሩ ፡ ግን ፡ እንደ ፡ አደናይ ፡ ምስጢረ ፡ ሥላሴ ፡ አለበት ፤ ባ፲፱ ፡ ቍጥር ፡ ያነበበውን ፡ ከዚያው ፡ ባ፲፭ኛው ፡ ተርጕሞታል ፤ ባለብሉዮች ፡ ግን ፡ ዘይቤውን ፡ ሳይሹ ፡ ዘሀሎ ፡ ወይሄሉ ፡ ብለው ፡ የምስጢር ፡ አፈታት ፡ ይፈቱታል ። ያህና ፡ ይሆዋን ፡ ተመልከት ፤ ከዚህ ፡ ጋራ ፡ አንድ ፡ ነው ።

**አሄል** ፤ (ዕብራ) ፤ ድንኳን ፤ የድንኳን ፡ ስም ።

**አሆላ** ፤ ድንኳኗ ፤ ድንኳንነቷ ።

**አሆሊባ** ፤ ድንኳኔ ፡ በርሷ ፤ ድንኳኔ ። አንትቶ ፡ ሀላ ፡ ወሀሊባ ፡ ይላል ፤ ግድፈት ፡ ነው ። አሆላ ፡ ሰማርያ ፤ አሆሊባ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ (ሕዝ፳፫ ፡ ፩—፬) ።

**አውግሥጠስ** ፤ የሮማውያን ፡ ወር ፡ ነሐሴ ፡ አውግሥቱስ ፡ የነገሠበት ፡ (ገድ ፡ ተክ) ።

**አዊው ፤ ዎት ፤ (አወ ፤ አወወ ፡ የአውው ፡ ይእ(ው)ወው)** ፤ ማወው ፡ ኸብኛ ፡ መጮኽ ፤ አዉ ፡ አዉ ፡ ማለት ። ማያያዝ ፡ ማጫፈር ፡ ማከታተል ፤ ያንኑ ፡ ደግሞ ፡ ማሻሻል ፡ ማማረጥ ፡ ማበላለጥ ። እውዋ ፡ ዋዌ ፡ ዋው ፡ ማለት ፡ ከዚህ ፡ የወጣ ፡ ነው ፤ እውዋ ፡ የሕፃናት ፡ ንዋየ ፡ ተውኔት ፤ ዋዌንና ፡ ዋውን ፡ በቦታው ፡ ተመልከት ።

(ላ) **አው** ፤ (ዕብ ፡ አ ። ሱር ፡ ወዐረ ፡ አው) ፤ ንኡስ ፡ አገባብ ። አጫፋሪ ፡ አንጻጻሪ ፡ ቃል ፤ ዋዌ ፤ ወይ ፡ ወይም ፤ በጥያቄ ፡ ጊዜ ፡ ወይስ ። አንዳንድ ፡ ጊዜ ፡ ከሚመ ፡ ጋራ ፤ አው ፡ ውእቱ ፡ ወሚመ ፡ አንተ ፡ ንዑ ፡ ሊተ ፡ እያለ ፤ አንዳንድ ፡ ጊዜም ፡ ዋዌ ፡ ስለ ፡ ኾነ ፡ ብቻውን ፡ በመከታተል ፡ ይገባል ። ለእመ ፡ አበስነ ፡ ለከ ፡ በአእምሮ ፡ አው ፡ በኢያእምሮ ፡ አው ፡ በጽልሑት ፡ አው ፡ በእከየ ፡ ልብ ፡ አው ፡ በገቢር ፡ አው ፡ በተናግሮ ፡

አው ፡ በናእስ ፡ ልብ ። ዕሥራ ፡ ወኀምስቱ ፡ አው ፡ ሠላሳ ። አው ፡ ሠምዕ ፡ አው ፡ ዘይት ። ቦኑ ፡ አው ፡ አልቦ ። ንግሩኒ ፤ አው ፡ ትሠውዑ ፡ አው ፡ ኣነሥእ ፡ ላዕሌክሙ ፡ ጥብጣቤ ፡ ሐብል ፡ (ቅዳ ። ዮሐ፯ ፡ ፲፱ ። ፊ ፡ መ ፡ ፲፯ ፡ ፯ ። መቃ ፡ ገ፪) ። ዋዌነት ፡ ስላለው ፡ አው ፡ ወአው ፡ አይልም ፤ ምስጢሩ ፡ ማማረጥና ፡ ማሻሻል ፡ ነው ።

**እወ ፤ (ዐረ ፡ ኢ.ይ ፤ ነዐም ። ዕብ ፡ ሄን) ፤** ነባር ፡ አንቀጽና ፡ ንኡስ ፡ አገባብ ። ያምንታ ፡ ቃል ፤ ፍችው ፡ አወን ፤ እውነት ፤ በውነት ። ቦኑ ፡ ቃል ፡ እም እግዚአብሔር ፤ ወይቤሎ ፡ እወ ፡ ቦ ። እወ ፡ እኍየ ። እወ ፡ እግዚኦ ፡ ፍትሖሙ ። እወ ፡ እግዚኦ ፡ አምላከ ፡ ኵሉ ፡ እወ ፡ እግዚኦ ፡ አኃዜ ፡ ኵሉ ፡ እወ ፡ እግዚኦ ፡ ፈጣሬ ፡ ኵሉ ። ወይኩን ፡ ነገርክሙ ፡ እመኒ ፡ እወ ፡ እወ ፤ ወእመኒ ፡ አልቦ ፡ አልቦ ፡ (ኤር፴፱ ፡ ፲፯ ። ፊልሞ ፡ ፳ ። ግንዘ ። ቅዳ ። ማቴ፭ ፡ ፴፯) ። የቀረውን ፡ በደቂቅ ፡ ርባታ ፡ ተመልከት ፡ (ዕር፲፮ ፡ ቍ፵፱) ።

**አውያት ፤—ጩኸት ፡ ቡታ ፤—ዐወየ ፡ ዐውየወ ።**

**አውከከ ፤ — አወከ ፡ አስፈራ ፤ — ወኪክ ፡ ወከ ፤ ወከከ ።**

**አውክሞዲስ ፤ (ጽር ፡ አውክሞዱስ ። ዕብ ፡ ጊብዓት) ፤** ታናሽ ፡ ተራራ ፡ ጕብ ፡ ባማ ፤ የሳኦል ፡ ከተማ ፡ (፩ነገ ፡ ፲፩ ፡ ፬ ። ፳፯ ፡ ፩) ። ጽኑ ፡ በረሐ ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ ተራራ ፡ ኰረብታ ፡ ዋሻ ፡ ፍርኵታ ፡ ያለበት ፤ ድኵላ ፡ ሠሣ ፡ አጋዘን ፡ ድፋሳ ፡ ሌላውም ፡ ኹሉ ፡ አውሬና ፡ እንስሳ ፡ የሚታደንበት ፡ (፩ነገ ፡ ፳፫ ፡ ፲፬ና ፡ ፲፭ ፡ ፲፱) ።

**አውክዐ ፤—አደከመ ፡ አሰለቸ ፤—ወኪዕ ፡ ወክዐ ።**

**አውል ፤ (ዐረ ፡ አል) ፤** ጊሜ ፡ የምድር ፡ ላቦት ፡ እንፋለት ፤ የጉም ፡ ሽንት ፡ እንደ ፡ ጤፍ ፡ ቅንጣት ፡ ያለ ፤ ባለቅኔዎች ፡ ግን ፡ ጤዛ ፡ ይሉታል ። ይባርክዎ ፡ ጠል ፡ ወአውል ። ወትተርፍ ፡ ምድር ፡ ባሕቲታ ፡ ዘእንበለ ፡ ጠል ፡ ወአውል ። ኮነኒ ፡ አውለ ፡ (ዳን፫ ፡ ፵፭ ። ቀሌ ። አዋል) ።

**አውሎ ፤—ጥቅል ፡ ነፋስ ፤—ዐዊል ፡ ዖለ ፤ ዐውሎ ።**

**አውሎግያ ፤ (ጽር ፡ ኤፍሎጊአ) ፤** ቡሩክ ፡ ኅብስት ፤ ተረፈ ፡ መሥዋዕት ፡ ከቍርባን ፡ በኋላ ፡ በቡራኬ ፡ ጊዜ ፡ የሚሰጥ ። እንዘ ፡ ይሜጡ ፡ አውሎግያ ። ኅብስተ ፡ አውሎግያ ፡ (ቅዳ ። ኪዳ) ።

**አውሎግዮስ ፡ ጌርዮስ ፤ (ጽር ፡ ኤፍሎጊቶስ ፡ ኪሪዮስ) ፤** ቡሩክ ፡ እግዚአብሔር ፡ (ቅዳ) ።

**አውሎግሶን ፤ (ጽር ፡ ኤፍሎጊሶን) ፤** ትእዛዝ ፡ አንቀጽ ፤ ባርክ ። መነኮሳት ፡ ግን ፡ ቃለ ፡ ጽዋዔ ፡ ይሉታል ፤ ቤቶች ፡ ባለቤቶች ፡ እገሌ ፡ እንተኔ ፡ በማለት ፡ ፈንታ ፡ አውሎግሶን ፡ ብለው ፡ ይጠራሉ ፤ ፍችውንም ፡ ከፈት ፡ ማለት ፡ ነው ፡ ይላሉ ፤ አንዳንዶች ፡ ደግሞ ፡ አረጋዊ ፡ ዘይደልዎ ፡ ክብር ፡ ይሉታል ፡ (ገድ ዮሐ) ።

**ኤውላጦን ፤ (ጽር ፡ ሄዊላት ። ዕብ ፡ ሐዊላ) ፤** ስመ ፡ ነገድ ፤ የሰው ፡ ስም ፤ የካም ፡ የልጅ ፡ ልጅ ፤ የኵሽ ፡ ኹለተኛ ፡ ልጁ ፡ የሳባ ፡ ታናሽ ። ኖዳ ፡ ኖዳዊ ፡ ማለት ፡ ነው ፡ (ዘፍ፲ ፡ ፯) ። ምድረ ፡ ኤውላጦን ፤ (ዕብ ፡ ኤሬጽ ፡ ሐዊላ) ፤ የሐዊላ ፡ መሬት ፡ የወርቅ ፡ አሸዋ ፡ ድቡሽት ፤ ወርቅ ፡ እንዳሸዋ ፡ የሚታፈሥበት ፡ ካባይ ፡ በመለስ ፡ ያለ ፡ ቈላ ፤ ዳንግላ ፡ ምድረ ፡ ሻንቅላ ፤ ወዲያ ፡ ማደም ፡ ባባይና ፡ ባባይ ፡ መካከል ፡ ከላይ ፡ እስከ ፡ ታች ፡ እስከ ፡ ከርቱም ፡ ያለው ፡ ሸናጣ ፡ ሾጣጣ ፡ ዠላላ ፡ ሞላላ ፡ ሾገሌ ፡ የሱዳን ፡ ቀበሌ ፡ ሳይቀር ፡ (ዘፍ፪ ፡ ፲፩ ፡ ፲፪) ። ሙሴ ፡ ፵ ፡ ዘመን ፡ በሱዳን ፡ አገር ፡ ስለ ፡ ኖረ ፡ የሐዊላን ፡ ብዕል ፡ ወርቋን ፡ ወርቃምነቷን ፡ የወርቋን ፡ ጥራትና ፡ ብዛት ፡ ባየው ፡ ባወቀው ፡ ተናግሯል ፡ (ዮሴፍ) ። ባገራችንም ፡ አፈ ፡ ታሪክ ፤ ሙሴ ፡ በትግሬ ፡ እስከኵስም ፡ እስከ ፡ ሽሚዛና ፤ በጐንደርም ፡ እስከ ፡ ደንቢያና ፡ እስከ ፡ ጣና ፡ መጥቶ ፡ ነበረ ፡ ይባላል ። ርሱም ፡ ራሱ ፡ ሱዳናዊት ፡ ሴት ፡ እንዳገባ ፡ በኦሪቱ ፡ ያመለክታል ፡ (ዘኍ፲፪ ፡ ፩) ። ጊዮርጊስ ፡ ጽሩይ ፡ ወርቀ ፡ ኤውላጦን ፡ (ደራሲ) ።

**አውሎኒ ፤ ን ፤ ና ፤ (ጽር ፡ አፍሎኒ) ፤** ዘብጥ ፡ ቈላ ፤ ሜዳ ፡ ረባዳ ፡ (ዮዲ፯ ፡ ፫ ፡ ፲፯ ፡ ፲ ፡ ፲) ።

**አውልዕ ፤ (ዕብ ፡ ኤሎን ፡ አሎን) ፤** ጥኑ ፡ ጠንካራ ፡ ዕንጨት ፤ ብርቱ ፡ ዛፍ ፡ በሉጥ ፡ (ዘፍ፲፰ ፡ ፩) ።

**አውልዕ ፤ (ዐረ ፡ ወለዐ ፤ አበራ ፡ ለኰሰ) ፤** የበረሐ ፡ ዘይት ፡ ወይራ ፤ መራራ ፡ ጠንካራ ፤ ጥንካሬው ፡ እንደ ፡ በሉጥ ፡ ያለ ። አውልዐ ፡ ገዳም ። ወጽንዐ ፡ ከመ ፡ ጽንዐ ፡ አውልዕ ። ዕፀ ፡ አውልዕ ፡ (ሮሜ፲፩ ፡ ፲፯ ፡ ፳፬ ። ዓሞ፪ ፡ ፱ ። መጽ ፡ ምስ) ።

**አውናን ፤ (ጽር ፡ አፍናን ። ዕብ ፡ አናን) ።** የሰው ፡ ስም ፤ ፪ኛው ፡ የይሁዳ ፡ ልጅ ፡ (ዘፍ፴፰ ፡ ፱) ። አውስቦ ፡ አውናን ፤ የአውናን ፡ ፅምረት ፡ ሩካቤ ፤ አውናናዊ ፡ ሥራ ፤ ፈቃድን ፡ ፈጽሞ ፡ ዘር ፡ አለመስጠት ፡ ከውጭ ፡ ማፍሰስ ፡ (አንቀጸ ፡ ንስሓ ፤ ወይም ፡ መጽሐፈ ፡ ኑዛዜ ፡ (ፍ ፡ ነ ፡ ፳፱ ፡ ፭) ።

**አውሥአ ፤ — አስደራጊ ፤ — ወሢእ ፡ ወሥአ ።**

**አፍ ፤ — በቁሙ ፤ — ዐዊፍ ፡ ዖፈ ።**

**አውቃፍ ፤—አንበሮች ፤—ወቀፈ ።**

**አውርዮን ፤ (ጽር ፡ አውሪዮን) ፤** ጌሰም ፤ ሳኒታ ፡ (ዘኍ፲፱ ፡ ፳፩) ።

**አርያሬስ ፤ (ዕብ ፡ አር ፡ ሔሬስ) ፤** ፀሓይ ፤ ስመ ፡ ፀሓይ ፤ ሥዕለ ፡ ፀሓይ ፤ አር ፡ ጸዳሉ ፡ ብርሃኑ ፡

ቀርኑ ፡ ምዕዛሩ ፤ ያሬስ ፡ ሰሌዳው ፡ ክበቡ ። ቶማስን ፡ ተመልከት ፡ (ሔኖ፹፰ ፡ ፩) ። ኦርያሬስ ፡ ሰማይ ፡ ልብስኪ ፡ ወአሣእንኪ ፡ እብላ ። ሰላም ፡ ለአንጣዎስ ፡ ለሃይማኖቱ ፡ ዘአጽደላ ፡ እምኦርያሬስ ፡ ወእብላ ። እምታስግዱ ፡ ብርከ ፡ ለኦርያሬስ ፡ (ደራሲ ። ስንክ ፡ ነሐ፲፯ ። ኅዳ፱) ።

**አውራቂስ ፤ (ጽር ፡ ሄውሮክሊዶን) ፤** ብርቱ ፡ ነፋስ ፡ ባሕር ፡ የሚደርጥ ፡ የሚያናውጥ ፤ መርከብ ፡ የሚነጥ ፡ የሚገለብጥ ። ጥፉንቂስን ፡ እይ ፤ ከዚህ ፡ ጋራ ፡ አንድ ፡ ነው ፡ (ግብ፳፯ ፡ ፲፬) ።

**አውራስ ፤ (ጽርእ) ፤** ጸዳል ፡ ብርሃን ፤ ነጸብራቅ ፡ ውጋጋን ፡ (ሕዝ፰ ፡ ፪) ።

**አውስት ፤ (ጽር ፡ ጊብስ) ፤** ነስር ፡ የጥንብ ፡ አሞራ ፤ አስቀድሞ ፡ ዐይን ፡ የሚያንቍር ፡ ፊት ፡ የሚሐጭር ፡ የሚጐፈጭር ፤ ዐይን ፡ ሳያወጣ ፡ የማይበላ ። (ሙሾ) ፤ ዘምዶ ፡ የሞተ ፡ ሰው ፡ ያዝንለት ፡ አያጣ ፤ አሞራ ፡ እንኳ ፡ ወርዶ ፡ ፊቱን ፡ ነጭቶ ፡ ወጣ ። አውስትኒ ፡ ሐቂፎ ፡ ዕጕሊሁ ፡ ይበይት ፡ (ኢዮ፴፱ ፡ ፳፮ ። ሔኖ፹፱ ፡ ፲ ። ፲፫ ፡ ፪ ፡ ፲፭ ፡ ፲፫ ፡ ፲፮) ።



አውስት ፡

**አዊት ፤ (ዕብ ፡ አት) ፤** ምልክት ፡ ፊደል ፤ ታምራት ፡ ገቢረ ፡ ኀይል ። የዮሐንስ ፡ መጥምቅ ፡ ስምና ፡ በዓል ፤ ምልክታም ፡ ባለምልክት ፡ ማለት ፡ ነው ። ባለቅኔዎች ፡ ግን ፡ ያገር ፡ ስም ፡ የወይን ፡ እሸት ፡ ጊዜ ፡ ይሉታል ። በዓል ፡ ዘስሙ ፡ ይ ፡ ውእቱ ፡ ዮሐንስ ፡ አዊት ። ዘአዊት ፡ ዮሐንስ ፡ (አብጥሊ ። አዋል) ።

**አወተ ፤ (ሐባብ) ፤** ተለቃ ፡ ተበደረ ፤ ታደለ ፡ ተቀበለ ።

**አወት ፤** ልቃሕ ፤ ጸጋ ፡ ዕድል ።

**አውታይ ፤ ን ፤ (ዐረ ፡ አውታን) ፤** ታላቅ ፡ ሰፊ ፡ ቤት ፤ ወይም ፡ ድንኳን ፡ (አቡሻ ፡ ፯) ።

**አውቴ ፤ (ጽር ፡ ናዎት ። ዕብ ፡ ናዮት) ፤** የቦታ ፡ ስም ፤ የጸሎት ፡ የትምርት ፡ ቤት ፤ መጋቢያ ፡ መሰብሰቢያ ፤ መካን ፡ ጉባኤ ። አውቴ ፡ ዘራማ ፡ (፩ነገ ፡ ፲፱ ፡ ፲፱ ፡ ፳፫) ።

**አውተረ ፤ —አስደራጊ ፤ —ወቴር ፡ ወተረ ።**

**አዚብ ፤ ቦት ፤ (አዘበ ። ዐረ ፡ ወሱር ፡ ዛብ ። ዕብ ፡ ዡብ) ፤** መፍሰስ ፡ መንገርገር ፡ መንፎክ ፤ ፊር ፡ ፊር ፡ ጭርቅ ፡ ጭርቅ ፡ ጠብ ፡ ጠብ ፡ ማለት ፤ የሽንት ፡ የዘር ፡ የወተት ፡ የደም ፡ የፈሳሽ ፡ ኹሉ ።

**አአዘበ ፤ አስተአዘበ ፤** ሸነ ፡ ሸና ፤ አጨረቀ ፤ ረጨ ፡ ፈነጠቀ ። ባለብሉዮች ፡ ግን ፡ ሰለለ ፡ ጕበኘ ፡ ይሉታል ። ዘያስተአዝብ ፡ ኀበ ፡ አረፍት ። ቅጥር ፡ ተጠግቶ ፡ የሚሸን ፡ ውሻ ፤ ወንድ ፡ ልጅ ፡ ቤት ፡ ሰብ ፡ (፩ነገ ፡ ፳፭ ፡ ፳፪ ፡ ፴፬ ። ፫ነገ ፡ ፳፩ ፡ ፳፩ ። ፬ነገ ፡ ፱ ፡ ፰) ።

**ሚዘብ ፤ (ሐባብ) ፤** ቦይ ፤ መትረብ ፤ አሸንዳ ።

(ጥ) **ዝብ ፤ (ዐረ ። ዕብ ፡ ዘብ) ፤** አባለ ፡ ዘርዕ ፤ እስኪት ፤ ትእምርተ ፡ ተባዕት ።

(ጥዝ) **አዛብ ፤ (ዕብ ፡ ኤዘብ ። ጽር ፡ ሒሶፖስ) ፤** መርጫ ፡ የቀንበጥ ፡ ችቦ ፤ ታናናሽ ፡ ቀጫጭን ፡ ቀንበጥ ፡ ሐረግ ፡ መልካም ፡ ሽታ ፡ ያለው ፡ ላይን ፡ ላፍንጫ ፡ ደስ ፡ የሚያሰኝ ፤ ናዕናዕ ፡ አዩባን ፡ ነጭ ፡ ሽቱ ፡ ፊሓን ፤ ዐጡንባር ፡ የጠጅ ፡ ሣር ፡ ይህን ፡ የመሰለ ። ቅጥይ ፡ የገቦ ፡ በጕን ፡ የሚወጣ ፡ የሚያፈጠፍጥ ፤ በቤት ፡ በግንብ ፡ ላይ ፡ ሳይዘሩት ፡ የሚበቅል ፡ ሣር ፡ ቅጠል ፤ እንዳሸክትና ፡ እንደ ፡ ሙጃ ፡ ያለ ። ሁስጱን ፡ ተመልከት ፤ ከዚህ ፡ ጋራ ፡ አንድ ፡ ነው ። ባለመጽሐፎች ፡ ግን ፡ ያንንም ፡ ይኽንም ፤ የተጐነጐነ ፡ ሐር ፡ አዩባን ፡ ስምዛ ፡ አሸክት ፡ ይሉታል ፡ (ዘፀ፲፪ ፡ ፳፪ ። መዝ ፡ ፶) ። አንዳንድ ፡ ጊዜም ፡ ለናዕናዕ ፡ ብቻ ፡ ይነገራል ፤ መደበኛው ፡ ርሱ ፡ ስለ ፡ ኾነ ፡ (ማቴ፳፫ ፡ ፳፫ ። ሉቃ፲፩ ፡ ፵፪) ።

**አዜብ ፤ —ደቡብ ፡ በረሓ ፤ —አዝየብ ።**

(ጥ) **አዝዘ ፤ ዘት ፤ (አዘዘ ። ዕብ ፡ ጸዌህ) ፤** ማዘዝ ፤ መናዘዝ ፤ (ጥና) መናዘዝ ፤ በሥራ ፡ ላይ ፡ ወይም ፡ በገንዘብ ፡ በርስት ፡ ቍርጥ ፡ ቃል ፡ መስጠት ፤ አድርግ ፡ አታድርግ ፡ ይኹን ፡ አይኹን ፡ ማለት ፤ በቃል ፡ በጥፈት ፤ የሹም ፡ የቄስ ፡ ያባት ፡ የባለቤት ። (ተረት) ፤ ያልተሾመ ፡ አያዝ ፤ ያልቀሰሰ ፡ አይናዝዝ ። ላይሞቱ ፡ መናዘዝ ፤ ላይመቱ ፡ መጋበዝ ። አዝዘ ፡ ይኩን ፡ በጽሒፍ ፡ ወዘእንበለ ፡ ጽሒፍ ፡ ፈታሒ ፡ የአዝዝ ፡ ለላእካኒሁ ፡ በፈፅሀ ፡ እግዚ ። አዘዘ ፡ ያብእዋ ። አንተ ፡ ውእቱ ፡ ዘትኤዝዝ ፡ ለበዊእ ፡ ወለወፂእ ። መኑ ፡ አዘዘክሙ ፡ ትሕንጹ ። አዘዘ ፡ በእንተ ፡ ቤቱ ፡ ወሞተ ። የአዝዝ ፡ እምቅድመ ፡ ምንዙስናሁ ፡ በእንተ ፡ ንዋዩ ፡ ዘከመ ፡ ፈቀደ ፡ (ፍ ፡ ነ ፡ ፵፩ ፡ ፩ ። ፵፫ ፡ ፫ ። ዮዲ፲፪ ፡ ፩ ። ፩ዜና ፡ ፲፭ ፡ ፪ ። ዕዝ፭ ፡ ፫ ። ፪ነገ ፡ ፲፯ ፡ ፳፫ ። ፍ ፡ ነ ፡ ፲) ።

**አዛዚ ፤ (ዚት ፡ ዝያን ፡ ያት) ፤** የሚያዝ ፡ የሚናዝዝ ፤ አዛዥ ፡ ናዛዥ ፤ ሠራዒ ፡ መጋቢ ። እለ ፡ አልቦሙ ፡ አብ ፡ ወኢእም ፡ ወኢአዛዚ ። ረሰየከ ፡ እግዚአብሔር ፡ አዛዜ ፡ ለሖኔየ ፡ (ፍ ፡ ነ ፡ ፳፱ ፡ ፫ ። ዮሴፍ) ።

**አአዘዘ ፤ አስተአዘዘ ፤** አሳዘዘ ፤ እዘዝ ፡ ናዝ ፡ አለ ፤ አዛዥነት ፡ ሾመ ፤ ወከለ ።

**መአዝዝ ፤ መስተአዝዝ ፤ (ዝት ፡ ዛን ፡ ዛት) ፤** የሚያዝ ፤ የሚያሳዝዝ ፤ አዛዥ ፡ አሳዛዥ ።

**ትእዘዘ** ፤ ታዘዘ ፤ ሰማ ፡ ተቀበለ ፤ ዐሺ ፡ በን ፡ አለ ፤ ተገዛ ፡ አገለገለ ። ወተአዘዘ ፡ ውእቱ ፡ ዐንበሪ ፡ የኅጦ ፡ ለዮናስ ። ኅሊ ፡ ዳእሙ ፡ ዘተአዘዝከ ። አልቦ ፡ ዘይትኤዘዝ ፡ ለቃልከ ። ልህቀ ፡ እንዘ ፡ ይትኤዘዝ ፡ ለአዝማዲሁ ። ተአዘዛ ፡ ለአምታቲክን ፡ (ዮና፪ ፡ ፲፩ ። ሚሬ ፡ ፳፪ ። ዮዲ፲፮ ፡ ፲፬ ። ድጓ ። ዲድ ፡ ፫) ።

**ተአዛዚ** ፤ የሚታዘዝ ፡ ታዛዥ ፤ ተለኣኪ ፡ አገል ጋይ ፤ ዐሺ ፡ ባይ ፡ ፈቃደኛ ። ተአዛዚ ፡ ዲበ ፡ ሰብእ ። ተአዛዚ ፡ ለትፍሥሕት ፡ ወለኑዛዜ ። ረድኦ ፡ ወተአዛዚሁ ። ወትከውን ፡ ለከ ፡ ተአዛዚተ ፡ (ሔኖ፳ ፡ ፩ ። ስንክ ፡ የካ፲፪ ። ጥቅ፲፱ ። ፊላስ) ።

**እዙዝ** ፤ (ዛን ፡ ዛት ፡ ዝዛት) ፤ በቁሙ ፤ የታዘዘ ፤ የተገባ ፤ የተሠራ ፡ የተወሰነ ፤ የተጣፈ ፡ የተነገረ ። እዙዝ ፡ ውእቱ ፡ ከመ ፡ ያጥፍእ ። ሀቦ ፡ ክፍሎ ፡ ዘእዙዝ ፡ ለከ ። በከመ ፡ እዙዝ ፡ በእንቲኣሆሙ ፤ ወዓዲ ፡ እዙዝ ፡ ውስተ ፡ ሕግ ። ዘኢእዙዝ ፡ በውስተ ፡ ሕግ ፡ (ዮዲ፫ ፡ ፰ ። ሚሬ፯ ፡ ፴፩ ። ኩፋ ፡ ፩ ። ዲድ ፡ ፲ ። ቀሌ) ።

**ትእዛዝ** ፤ (ዛት) ፤ በቁሙ ፤ እግዚኣዊ ፡ አምላካዊ ፡ ቃል ፤ ከሥራ ፡ አስቀድሞ ፡ የሚሰጥ ፡ የሚጣፍ ፡ የሚነገር ፤ ሕግ ፡ ሥርዐት ፡ አድርግ ፡ አድርግ ፡ የሚል ፤ ፈቃድ ፡ ደንብ ፡ ዕድር ፤ የሚገባ ፡ ነገር ። እስመ ፡ በትእዛዝ ፡ ውእቱ ፡ ቃሉ ። ወፅአ ፡ ትእዛዝ ፡ እምኀበ ፡ ንጉሥ ። ይወፅኡ ፡ እምትእዛዝነ ። በእንተ ፡ ትእዛዝ ፡ ወጽሕፈቱ ። ታቦት ፡ እንተ ፡ ትእዛዝ ። ዐቂበ ፡ ትእዛዚሁ ፡ ለእግዚ ። ትእዛዛተ ፡ ሰብእ ። ትእዛዘ ፡ አበዊነ ፡ ሐዋርያት ፡ (ሉቃ፪ ፡ ፴፪ ። ዳን፪ ፡ ፲፫ ። ዮሴፍ ። ፍ ፡ ነ ፡ ፵፩ ፡ ፩ ። ዘፀ፴፱ ፡ ፲፭ ። ሚሬ፳፫ ፡ ፳፯ ። ኢሳ፳፱ ፡ ፲፫ ። ቅዳ) ። ትእዛዝ ፡ አንቀጽ ፡ ትእዛዝ ፡ መባሉ ፡ ከላይ ፡ ወደ ፡ ታች ፡ ሲመጣ ፡ ነው ፤ ከታች ፡ ወደ ፡ ላይ ፡ ሲወጣ ፡ ግን ፡ ልመና ፡ ጸሎት ፡ ይባላል ።

**ተአዘዘ** ፤ ተዛዘዘ ፤ ተደራረገ ።

**አስተአዘዘ** ፤ አስተዛዘዘ ፤ ተዛዘዙ ፡ አለ ፤ አደራረገ ።

**መስተአዝዝ** ፤ የሚያስተዛዝዝ ፡ አስተዛዛኝ ።

**እዘዝ** ፤—ጽንዕ ፡ ኀይል ፤—ዕዘዝ ፡ ዐዘዘ ።

**አዚኅ** ፤ ኆት ፤ (አዝኀ ፡ የአዝኅ ፡ ይእዛኅ ። ዐረ ፡ አዘ ፤ ዐዘ) ፤ መብጣት ፡ መቍረጥ ፡ መሰንዘር ፡ መሠንበጥ ፡ በቅዛዝ ፡ በጠርሙዝ ፡ በሱፋጭ ፡ በምላጭ ። ማገርት ፡ ማፍሰስ ፤ ማንዛት ፡ መወርዛት ። ጸወበን ፡ ተመልከት ።

**እዝኅ** ፤ (ኃት) ፤ ሻሮ ፡ ብልጭት ፡ ደንጊያ ፤ ቦረቦጭ ፤ ሲሰብሩት ፡ ስለታም ፡ ሱፋጭ ፡ ራስ ፡ የሚላጭ ። እብነ ፡ እዝኅ ። መጣብሕ ፡ ዘእዝኅ ። አንሥአ ፡ እደሁ ፡ በእዝኅ ። ኵሠሐ ፡ እዝኅ ። ለኵሠሐ ፡ ወለእዝኅ ፡ (ኢያ፭ ፡ ፪ ። ፳፩ ፡ ፵ ። ኢዮ፳፰ ፡ ፱ ። ጥበ፲፩ ፡ ፬ ። መዝ ፡ ፻፲፫) ።

**እዝኅ** ፤ (ኃት) ፤ በቁሙ ፤ እኹ ፤ የደም ፡ ውሃ ፡ ቅራሪ ፡ ጥንፋፊ ፤ የመግል ፡ ትራፊ ፡ ከተበጣ ፡ ወይም ፡ እሳት ፡ ከፈጀው ፡ ከበጠ ፡ ከቈሰለ ፡ ገላ ፤ ከሐዲስና ፡ ከስባራ ፡ ሸክላ ፡ የሚፈስ ።

**አዜብ** ፤ አዝያብ ፡ (ዐረ ፡ አዝየብ) ፤ የማእዝን ፡ ስም ፤ ንኡስ ፡ ማእዝን ፤ የአፍሪቃ ፡ ወገን ፤ በምዕራብና ፡ በደቡብ ፡ መካከል ፡ ያለ ፡ የደቡብ ፡ ግራ ፡ ምዕራብ ፤ የመስዕ ፡ ትይዩና ፡ አንጻር ፡ ፊት ፡ ለፊት ። ባለብሉዮች ፡ ቈላ ፡ በረሓ ፡ ይሉታል ። ባርኽ ፡ መስዐ ፡ ወአዜበ ። ነፋስ ፡ አዜብ ። ንግሥተ ፡ አዜብ ። ከመ ፡ ውሒዝ ፡ ውስተ ፡ አዜብ ፡ (ቅዳ ። ሉቃ፲፪ ፡ ፶፭ ። ማቴ፲፪ ፡ ፵፪ ። መዝ ፡ ፻፳፭) ። ጽባሕ ፡ ምሥራቅ ፡ በማለት ፡ ፈንታ ፡ አዜብ ፡ ይላል ፡ የመላሽና ፡ የጣፊ ፡ ስሕተት ፡ ነው ። ነፋስ ፡ አዜብ ። አንሥአ ፡ አዜበ ፡ (ዘፀ፲ ፡ ፲፫ ። ኢዮ፴፰ ፡ ፳፱ ። መዝ ፡ ፸፯ ። ሔኖ፴፯ ፡ ፩) ።

(ጥ) **አዝሎ** ፤ ሎት ፤ (አዘለ ፡ ይኤዝል ፡ የአዝል ። ዐረ ፡ አዘረ ። ዕብ ፡ አዛር ፤ ቀነተ) ፤ ማደግ ፡ መጐልመስ ፡ ለጌጥ ፡ ለመሣሪያ ፡ መድረስ ፤ መጐልበት ፡ መግነን ፤ ኀይለኛ ፡ መኾን ።

**አዛል** ፤ ጐበዝ ፡ ጐልማሳ ፤ ብርቱ ፡ ጠንካራ ። በሓ ፡ ኦ ፡ አዛል ፡ ዘኢይፈርህ ፡ ሞተ ፡ በቅድመ ፡ ቀታልያን ። አበ ፡ ኖብ ፡ ድንግል ፡ ወአዛል ፡ መስተጋድል ፡ (ስንክ ፡ ሐም፰ ። ቅዳ) ።

**አዘለ** ፤ (ዐረ ። ዕብ ፡ አዛል) ፤ ኼደ ፡ ነቀለ ፤ ጓዙን ፡ ዕቃውን ፡ አነሣ ፡ ወሰደ ፤ የነጋዴ ፡ የባለከራይ ።

**መአዝል** ፤ (ዕብ ፡ ምኡዛል) ፤ የሚኼድ ፡ ኻያጅ ፤ ገሥጋሽ ፡ ተመላላሽ ፡ (ሕዝ፳፯ ፡ ፲፱) ።

**እዝል** ፤—የዜማ ፡ ስም ፤—ዕዝል ፤

**አዝመር** ፤—ደባባ ፡ ደባሳ ፤—ዘመረ ።

**አዚን** ፤ ኖት ፤ (አዘነ ፡ የአዝን ፡ ይእዝን ። ዕብ ፡ አዜን) ፤ መቀቀር ፡ መቀፈር ፤ ዡሮ ፡ መስጠት ፡ ማቅረብ ፡ ለመስማት ።

**አዛኒ** ፤ መአዝን ፤ ቀቃሪ ፡ ቀፋሪ ፤ ሸምጣጭ ፤ አድማጭ ።

**እዝን** ፤ (ብ ፡ እዘን ፤ አእዛን ። ዕብ ፡ አዜን ። ሱር ፡ አዝና ፤ ኤዝና ። ዐረ ፡ ኡዝን) ፤ ዡሮ ፤ መስሚያ ፡ ማድመጫ ፤ መያዡ ፡ መጨበጫ ፡ የመ



እዝን ፡

ሣሪያ ። (ተረት) ፤ የነገር ፡ ጣዕም ፡ በዡሮ ፡ የእኽል ፡

ራን ፡ እድምተ ፡ ሥን ፤ ሠናይት ፡ ሠራሬ ፡ ይሉታል ፡ (ግብ፫ ፡ ፱) ።

**አርይ ፤ ዮት ፡ (አረየ ፡ የአሪ ፡ ይእሪ ። ዕብ ፡ አራህ) ፤** መልቀም ፤ መቃረም ፤ መሰብሰብ ፤ መምረጥ ፤ ማረም ፡ መንቀል ፤ መለየት ፡ መጣል ፡ (ዘሌ፲፱ ፡ ፱ ። ፳፫ ፡ ፳፱) ። እሑርኑ ፡ ውስተ ፡ ገራህት ፡ እእሪ ፡ እክለ ። ወሖረት ፡ ወአረየት ። ንሑር ፡ ወንእርዮን ። እንዘ ፡ ተአርዩ ፡ ከርዳደ ። ወነቢሮሙ ፡ አረዩ ፡ ሠናዮ ፡ (ሩት፪ ፡ ፪ ፡ ፫ ። ማቴ፲፫ ፡ ፳፰ ፡ ፳፱ ፡ ፵፰) ። አረረንና ፡ ኀረየን ፡ ተመልከት ።

**አራዪ ፤ (ዪት ፡ ይያን ፡ ያት ፤ አረይት) ፤** የሚለቅም ፡ የሚቃርም ፤ ቃራሚ ፡ መራጭ ።

**ተአርየ ፤** ተለቀመ ፡ ተቃረመ ፤ ታረመ ፡ ተመረጠ ።

**እሩይ ፤** የተለቀመ ፡ ልቅም ፤ ምርጥ ፤ ዕርም ።

**አረየ ፤—ተከከለ ፤—ዐርይ ፡ ዐረየ ።**

**አርዮብ ፤ (ጽር ፡ አሬዎን ። ዕብ ፡ ከሲል) ።** ጉቡኣን ፡ ከዋክብት ፤ ዘወትር ፡ ባንድነት ፡ ኹነው ፡ ችፍግ ፡ ብለው ፡ የሚታዩ ፤ እንደነሥስቶ ፡ እንደንስድስቶ ፡ ያሉ ፡ (ኢሳ፲፫ ፡ ፲) ። ጸዳሎሙ ፡ ለአብያዝ ፡ ወለአርዮብ ፡ (አርጋ ፡ ፯) ።

**አርዮብ ፤** ታላቅ ፡ ኮከብ ፡ እንደ ፡ ፀሐይ ፡ ያለ ፤ ካራቱ ፡ ፀበይት ፡ ከዋክብት ፡ አንዱ ። ጽዱል ፡ ኮከብ ፡ በጣም ፡ የሚያበራ ፡ የሚያሸበርቅ ። እስመ ፡ ይቤ ፡ አነ ፡ ብር ፡ መንበርየ ፡ መልዕልተ ፡ አርዮብ ፡ ወአዐርግ ፡ ውስተ ፡ ምጽንዓት ። ትጸድል ፡ እምሥነ ፡ አርዮብ ፡ (መጽ ፡ ምስ ። ኢሳ፲፬ ፡ ፲፫ ። አርጋ ፡ ፬) ።

**አርያል ፤—ምሧዋዕ ፤—አሪኤል ።**

**አርያም ፤—ልዕልና ፤—ረይም ፡ ሬመ ፡ ረየመ ።**

**አርያሬስ ፤—ፀሐይ ፤—አወር ፡ አር ።**

**አርዮስ ፤ (ጽር ፡ አሪዉስ) ፤** የሰው ፡ ስም ፤ ጽርኣዊ ፡ መናፍቅ ፤ ወልድን ፡ ከአብ ፡ የሚለይ ፡ የሚከፍል ፤ በመለኮቱ ፡ ፍጡር ፡ የሚል ፤ የሰውነቱን ፡ ለአምላክነቱ ፡ የሚናገር ፤ ከዚህ ፡ የተነሣ ፡ ጉባኤ ፡ ኒቅያ ፤ አምላክ ፡ ጽድቅ ፡ ዘእምአምላክ ፡ ጽድቅ ፡ ዘተወልደ ፡ ወአኮ ፡ ዘተገብረ ፤ ኅቡረ ፡ ህላዌ ፡ ምስለ ፡ አብ ፡ ብላ ፤ ረግማ ፡ አውግዛ ፡ የለየችው ። ወሶበ ፡ ሰምዑ ፡ ቃሎ ፡ ርኩሰ ፡ ለአርዮስ ፡ ደንገፁ ፡ ሰራዊተ ፡ ሰማያት ፡ (ሃይ ፡ አበ) ።

**አርዮሳዊ ፤ (ዊት ፤ ውያን ፡ ያት) ፤** የአርዮስ ፡ ወገን ፤ በአርዮስ ፡ ሃይማኖት ፡ የሚያምን ። አርዮሳዌ ፡ አውገዘ ። አርዮሳውያን ፡ (ዝማሬ ። ሃይ ፡ አበ ፡ ብንያሚ) ።

**አርዮስፋጎስ ፤ (ጽር ፡ አሪዎስ ፡ ፓጎስ) ፤** የፈላስፎች ፡ ሸንጎ ፤ የጥበበኞች ፡ አደባባይ ፤ የፍየሎች ፡ ምሳግ ፤ የሕፃናት ፡ መራወጫ ፡ መፈንደቂያ ፤ የአእሩግ ፡ ፀሐይ ፡ መሞቂያ ። ቤተ ፡ ምሑናን ፡ ዘስሙ ፡ አርዮስፋጎስ ፡ (ግብ፲፯ ፡ ፲፱) ።

**አሪት ፤ (ሱር ፡ አራይታ ። ዕብ ፡ ቶራ ። ዐረ ፡ ናሙስ ። ጽር ፡ ኖሞስ) ፤** በቁሙ ፤ ሕግ ፤ ፍትሕ ፤ ትእዛዝ ፤ ዐሠርቱ ፡ ቃላት ። ፍትሕ ፡ የወል ፡ የመከከል ። ሕግ ፡ አታድርግ ፡ አታድርግ ። ትእዛዝ ፡ አድርግ ፡ አድርግ ፡ የሚለው ። ባለብሉዮች ፡ ግን ፡ ዜና ፡ ብርሃን ፡ ስምዕ ፡ ደብር ፡ መደብር ፡ ብለው ፡ ይጠምሩበታል ። እስመ ፡ አሪት ፡ በሙሴ ፡ ተውህበት ፡ ለነ ። አሪትነኑ ፡ ትኴንኖ ፡ ለሰብእ ። ታቦት ፡ እንተ ፡ ውስቴታ ፡ አሪት ፡ (ዮሐ፩ ፡ ፲፯ ። ፯ ፡ ፶፩ ። ዕብ ፡ ፱ ፡ ፬) ።

—፤ መጽሐፍ ፤ የመጽሐፍ ፡ ስም ፤ ሙሴ ፡ የጻፈው ፡ ዐምስቱ ፡ ክፍል ፡ ወይም ፡ ዐምስቱ ፡ ብሔር ። አሪት ፡ ወነቢያት ፡ ሰበኩ ፡ በክርስቶስ ። መምህረ ፡ አሪት ። ብሔረ ፡ አሪት ፡ (ሃይ ፡ አበ ። ግብ፩ ፡ ፴፱ ። አብጥ) ። ከአሪት ፡ ጋራ ፡ ዐብረው ፡ የሚጣፉ ፡ ኢያሱ ፡ መሳፍንት ፡ ሩት ፡ እሊህ ፡ ሦስቱ ፡ መጽሐፍ ፡ እንጂ ፡ አሪት ፡ አይባሉም ፤ በግእዝ ፡ ልማድ ፡ ግን ፡ አለስማቸው ፡ አሪት ፡ ይባላሉ ። ሰመንቱ ፡ በሓውርተ ፡ አሪት ። አሪት ፡ ዘኢያሱ ። አሪት ፡ ዘመሳፍንት ። አሪት ፡ ዘሩት ።

**አሪታዊ ፤** የአሪት ፤ አሪታም ፤ ባለአሪት ፤ ይሁዲ ፡ ፈላሻ ። አሪታዊት ፡ ጠረጴዛ ፡ (መጽ ፡ ምስ) ።

**አርዮጳጌጤስ ፤ (ጽር ፡ አሬዎፓጊቲስ) ፤** አርዮስፋጎስ ፡ ካለው ፡ ጋራ ፡ አንድ ፡ ነው ፡ (ግብ፲፯ ፡ ፴፬) ።

**አርክ ፤—ወዳጅ ፤—ዐሪክ ፡ ዐረከ ፤ ዐርክ ።**

**አራም ፤** ስመ ፡ ነገድ ፤ ስመ ፡ ሀገር ፤ ላይኛው ፡ ሶርያ ፤ ደማስቆ ፡ (ዘፍ፲ ፡ ፳፪ ። ኢሳ፯ ፡ ፩ ፡ ፰) ።

**አረሚ ፤ (ሚት ፡ ማያን ፡ ያት) ፤** የአራም ፡ ወገን ፤ የአራም ፡ ቋንቋ ፡ ሱርስት ። አራማዊ ፡ ሶርያዊ ፡ ሕዝብ ፤ አሪታውያንን ፡ እንደ ፡ ጋላ ፡ ኹኖ ፡ ይወርና ፡ ይዘርፍ ፡ ይማርክ ፡ የነበረ ፡ የእስራኤል ፡ ጠላት ።

**አረሚ ፤** አረመኔ ፤ አሕዛብ ፤ በአሪት ፡ በወንጌል ፡ የማያምን ። አሕዛብ ፡ ሥርዐት ፡ ያለው ፤ አረመኔ ፡ ሥርዐት ፡ የሌለው ። አእምንዎ ፡ ለአረሚ ። አረሚ ፡ እለ ፡ ኢየአምርዎ ፡ ለእግዚ ፡ (ቀሌ ። ፩ተሰ ፡ ፬ ፡ ፭ ። ሮሜ፱ ፡ ፳፱ ፡ ፴) ።

**አረሚ ፤** ጽርኣዊ ፤ ግሪክ ፤ ዮናን ። ብሔረ ፡ አረሚኑ ፡ የሐውር ፡ ወይሜህሮሙ ፡ ለአረሚ ። እለ ፡ እምአረሚ ፡ (ዮሐ፯ ፡ ፴፭ ። ፲፪ ፡ ፳ ። ሮሜ፩ ፡ ፲፬ ። ፩ቆሮ ፡ ፩ ፡ ፳፪—፳፱) ።

**አረማዊ ፡ ዪ ፤ (ዊት ፡ ዪት ፡ ውያን ፡ ያት) ፤** የአራም ፡ የግሪክ ፡ ወገን ፤ አሕዛብ ፤ አረመኔ ፤ ክፉ ፡ ጨካኝ ፤ እምነት ፡ ርኅራኄ ፡ የሌለው ። ለአይሁዳዊ ፡ ወለአረማዊ ። ብእሲት ፡ ተንባላታዊት ፡ አው ፡

አረማዊት ። ኢትትመሀሩ ፡ ፍኖተ ፡ አረማውያን ፡ (ሮሜ፩ ፡ ፲፮ ። ሲኖዶ ። ኤር፲ ፡ ፪) ።

**አርማጌዶን ፤ (ዕብ ፡ ሀር ፡ ምጊዶን) ፤** የሀገር ፡ የቦታ ፡ ስም ፤ የንፍታሌም ፡ ዕፃ ፡ (ራእ፲፮ ፡ ፲፮) ።

**አርመመ ፤—አስረመመ ፤—ረሚም ፡ ረመ ፤ ረመመ ።**

**አርሞን ፤ ኤርሞን ፤ (ዕብ ፡ ሔርሞን) ፤** የተራራ ፡ ስም ፤ ጕማም ፡ በረዷም ፤ የዮርዳኖስ ፡ ራስ ። ፍችው ፡ ልዑል ፡ ነዋኅ ፤ ቅዱስ ። የግእዝ ፡ መጽሐፍ ፡ ከጽርእ ፡ ስለ ፡ ተቀዳና ፡ ባጽርእ ፡ ፊደል ፡ ሀ ፡ ሐ ፡ ኤ ፡ ዒ ፡ የሚባሉ ፡ ስለ ፡ ኾነ ፤ በሔርሞን ፡ ፈንታ ፡ ኤርሞን ፡ አርሞን ፡ ይባላል ፡ (ዘዳ፫ ፡ ፰ ። ማሕ፬ ፡ ፰ ። ሔኖ ፡ ፯ ። ፲፫) ።

**አርማስ ፤—ታንከች ፤—ረሚስ ፡ ረምሰ ፤ ረምስ ።**

**አርማስቆስ ፤ (ጽር ፡ አርሚስኮስ) ፤** ድሪ ፤ ሰደፍ ፤ ቀሀረማን ፤ እንደ ፡ ጨሌ ፡ እንደ ፡ መቍጠሪያ ፡ ያለ ፡ ያንገት ፡ ጌጥ ። ባለብሉዮች ፡ ግን ፡ ግንብ ፡ መንቀል ፡ የብር ፡ ዘንግ ፡ ዘሪት ፡ ይሉታል ። ኤፎትን ፡ ተመልከት ፡ (ማሕ፩ ፡ ፲) ። ቀሀረማን ፡ ብጫ ፡ የንቍላል ፡ አስኳል ፡ የሚመስል ፤ ዕጣን ፡ ዕጣን ፡ የሚሸት ፡ ነው ፤ ፱ኛ ፡ ስሙ ፡ ቈርበት ፡ ካሪም ።

**አርዐት ፤—ቀንበር ፤—ርዒው ፡ ረዐወ ።**

**አረፈ ፤ (ዐረብ) ፤** ጨረሰ ፡ አበቃ ፤ ፈጸመ ፤ ደመደመ ።

**አረፍት ፤ (ፉት) ፤** ግድግዳ ፤ ዐጥር ፡ ቅጥር ፤ ካብ ፡ ግንብ ፤ ሥራው ፡ ያለቀለት ። አረፍት ፡ ይሴውረኒ ። አረፍት ፡ በይምን ፡ ወአረፍት ፡ በፀግም ። አረፋቲሃ ፡ ለኢየሩሳሌም ፡ (ሚራ፳፫ ፡ ፲፰ ። ዘፀ፲፬ ፡ ፲፱ ። መዝ ፡ ፶) ።

**እረፍት ፤—በቈሙ ፤—ዐሪፍ ፡ ዐረፈ ፤ አዕረፈ ።**

**አርቆሚን ፤ (ጽር ፡ አርኪኒም ። ዕብ ፡ ባርቃኒም) ፤** እሾኾች ፤ እሾኻም ፡ ዕንጨቶች ፤ እሾኻቸውና ፡ ቅጠላቸው ፡ ነጫጭ ፡ የኾነ ፤ በረቅ ፡ የሚመስል ፤ ኵሸሽሎች ፡ (መሳ፰ ፡ ፯ ፡ ፲፮) ። ባለብሉዮች ፡ ግን ፡ ግራር ፡ ይሉታል ።

**ኤረር ፤—ሰማይ ፤—አየር ፡ ኢዮር ።**

**አሪር ፤ ሮት ፤ (አረ ፤ አረረ ፡ የአርር ፡ ይአርር ፡ ይእ ። አረየ) ፤** መማረር ፤ ማጨድ ፡ መቍረጥ ፡ መንቀል ፤ መልቀም ፡ መቃረም ፤ መሰብሰብ ፡ ማስር ፤ መጕቸት ፡ መከመር ፤ ወቅቶ ፡ ማምረት ፤ በጐታ ፡ መከተት ፤ ያዝመራ ። ዘዘርዐ ፡ ሰብእ ፡ የአርር ። ትዘርዑ ፡ ወትአርሩ ። ካልእ ፡ ዘይዘርዕ ፡ ወካልእ ፡ ዘየአርር ። ወአንሰ ፡ ፈነውኩክሙ ፡ ትእርሩ ። አረርኩ ፡ ከርቤ ፡ (ገላ፮ ፡ ፯ ። ኢሳ፴፯ ፡ ፴ ። ዮሐ፬ ፡ ፴፯ ፡ ፴፰ ። ማሕ፭ ፡ ፩) ።

— ፤ መጮኽ ፡ እሪ ፡ ማለት ፤ መጥራት ፡ ማቅራራት ፤ ታላቅ ፡ ድምጥ ፡ መስጠት ፡ የሐዘን ፡ የዘፈን ፡ (ዐረብ) ።

**አራሪ ፤ (ሪት ፡ ርያን ፡ ያት) ፤** የሚማርር ፡ ማራሪ ፤ ዐጫጅ ፡ ሰብሳቢ ፡ ለቃሚ ፤ ቃራሚ ። (ተረት) ፡ አራሪ ፡ ለማራሪ ፤ ማራሪ ፡ ለበራሪ ፡ ይተው ።

**አእረረ ፤** አሳጨደ ፤ አሰበሰበ ፤ አስከተተ ። ያአርሮሙ ፡ ማእረሮ ፡ (፩ነገ ፡ ፰ ፡ ፲፪) ።

**ተአረ ፤** ተማረረ ፤ ታጨደ ፤ ተሰበሰበ ፤ ተለቀመ ፡ ተቈረጠ ፡ (ድጓ) ።

**እሩር ፤ (ራን ፡ ራት ፡ ርርት) ፤** የታጨደ ፤ የተሰበሰበ ፤ ነዶ ፡ ክምር ፡ ቃርሚያ ። ጥንግ ።

**ትእሪር ፤** ማረራ ፤ ዐጨዳ ፡ ቈረጣ ፡ ስብሰባ ፡ ከመራ ፤ ለቀማ ፤ አለቃቀም ። ውጤት ፤ ምርት ።

**ማእረር ፤ (ራት) ፤** መከር ፤ አዝመራ ፤ ፍሬ ፡ ያልታጨደ ፡ ያልተሰበሰበ ። በልዑ ፡ ማእረረከ ። መዋዕለ ፡ ማእረር ። ማእረሩሰ ፡ ብዙኅ ። ወምድር ፡ ትሁብ ፡ ማእረራ ። ማእረረ ፡ ምግባሮሙ ፡ (ኤር፭ ፡ ፲፯ ። ሢራ፳፬ ፡ ፳፯ ። ማቴ፱ ፡ ፴፯ ። ዘካ፰ ፡ ፲፪ ። ኢሳ፫ ፡ ፲) ።

**አራራይ ፤** እሪታ ፤ ቅርርት ፡ ታላቅ ፡ ጩኸት ። የዜማ ፡ ስም ፤ የዜማ ፡ ስልት ። ሦስተኛ ፡ ዜማ ፡ የመንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ አምሳል ። ሠለስቱ ፡ ዜማ ፤ ዘውእቱ ፡ ግእዝ ፡ ወዕዝል ፡ ወአራራይ ፡ (ስንክ ፡ ግን፲፩) ።

**አሩራን ፤ (ጽር ። ዕብ ፡ ኤሼል) ፤** ታላቅ ፡ ዛፍ ፡ ቅጠሉ ፡ ጽፍቅ ፡ ቁመቱ ፡ ምጡቅ ፡ የኾነ ፤ ስሙ ፡ ያልታወቀ ፤ ባለብሉዮች ፡ ግን ፡ ሮማን ፡ ይሉታል ። ወቀበርዎ ፡ ታሕተ ፡ አሩራን ፡ (፩ነገ ፡ ፴፩ ፡ ፲፫) ። ታላቅንቱም ፡ ሊታወቅ ፡ በዜና ፡ መዋዕል ፤ ግእዙ ፡ ዘግባ ፡ ዐማርኛው ፡ ሰሌን ፡ ይለዋል ፡ (፩ዜና ፡ ፲ ፡ ፲፪) ።

**አራራት ፤** የኖኅ ፡ ተራራ ፡ ስም ። አራራት ፡ ነበረት ፡ ታቦት ፡ (ድጓ) ።

**አርሺ ፤ (ቅብጥ) ፤** ሊቅ ፤ አለቃ ። አርሲመርቲዳስን ፡ እይ ፤ ከዚህ ፡ ጋራ ፡ ፩ ፡ ነው ። አርሺ ፤ ዲያቆን ፡ (አቡሻ ፡ ፶) ።

**ኤራስ ፤ (ኀራስ ፤ ለጋ ፡ ጨቅላ) ፤** ጨረቃ ፡ የጨረቃ ፡ ስም ፤ አራተኛ ፡ ስሟ ። እብላንን ፡ ተመልከት ።

**አርስጣላብ ፤ (ጽር ፡ አስትሮላበስ) ፤** የፀሐይና ፡ የጨረቃ ፡ የኮከብ ፡ መነጽር ፡ መልካቸውን ፡ አቅርቦ ፡ የሚያሳይ ፡ የሚያስመረምር ። ወይም ፡ መንገዳቸውን ፡ የሚናገርና ፡ የሚያስተምር ፡ የፍልስፍና ፡ መጽሐፍ ። ወነሥአ ፡ አርስጣላበ ፡ ወነጸረ ፡ ውስቴቱ ፡ ዘይብል ፡ እልመክኑን ። ቃይናን ፡ ወልደ ፡ አርፋክስድ ፡ ወጠነ ፡ ጽሒፈ ፡ አርስጣላብ ፡ እምድኅረ ፡ አይኅ ፤ ወእምድኅሬሁ ፡ ጸሐፉ ፡ ህንዳውያን ፡ (ስንክ ፡ ጥቅ፯ ። ዮሐ ፡ መደ ፡ ክ፱) ።

**አርሳይሮስ ፤ (ጽር ፡ አርኺሄሬፍስ) ፤** የገዳም ፡ አባት ፤ ሹም ፡ (መጽ ፡ ምስ) ።

**አርሲመርቲዳስ፤(ጽር፡ አርኪማንድ ሪታስ)፤** ዝኒ፡ ከማሁ፤ የካህናት፡ አለቃ፤ አበ፡ ምኔት፤ አበ፡ ማኅበር፤ ርእስ፡ ባሕታውያን፡ (ስንክ፡ ሐምሌ፳)።

**አርሶን፤(ጽር፡ አርሲን። ዕብ፡ ማሣእ፤ ሳባል)፤** ጭነት፤ ሸክም፡ የሚከብድ፡ የሚያስጨንቅ። ባለብሉዮች፡ ግን፡ ጠርብ፡ ይሉታል፡ (፪ነገ፡ ፮፡ ነ፩። ፩ነገ፡ ፳፡ ፱)።

**አርሲስ፤(ሳን። ጽር፡ ኤሬሲስ፤ ኑፋቄ፤ ዕልወት)፤** መናፍቅ፤ ዐላዊ፤ ባህሉና፡ ትርጓሜው፡ እንደ፡ ካራና፡ እንደ፡ ቅባት፡ ከሰው፡ ከመጣፍ፡ የማይገጥም፡ ዐልዋን፡ ዘይሰመዩ፡ አርሲስ፡ በነገረ፡ ጽርእ። ኢትጸሊ፡ ምስለ፡ አርሲሳን፡ ዘውእቶሙ፡ ዐላውያን፡ (አብጥ፡ ፵፫። ሃይ፡ አበ። ስንክ፡ ሠኔ፲፰)።

**እርሳስ፤—በቁሙ፤—ርሳስ።**

**አሬት፤—በቁሙ፤—አረየ፤አራይታ።**

**አርቶዶክስ፤(ጽርእ)፤** ስመ፡ ጉባኤ፤ የኒቅያ፡ ማኅበር፤ ኦርቶ፡ ርቱዕ፤ ደክስ፡ ባህል፡ ሐሳብ፡ ኅሊና፤ ስብሐት፡ ምስጋና፡ ይኾናል፤ በተገናኝ፡ ርቱዐ፡ ሃይማኖት፡ ማለት፡ ነው፤ ደኩስበተሪን፡ ተመልከት። መጽሐፍ፡ ግን፡ በኦርቶ፡ ፈንታ፡ አርቶ፡ ይላል፤ የጣፊ፡ ስሕተት፡ ነው።

**አርቶዶክሳዊ፤** ዝኒ፡ ከማሁ፤ የኦርቶደክስ፡ ወገን፤ ኒቅያዊ፤ እውነተኛ፤ ቅን፤ በሃይማኖቱ፡ ሐሰትና፡ ስሕተት፡ ጽንት፡ የሌለበት። ይኩን፡ ምእመን፡ ኦርቶዶክሳዌ። ሃይማኖት፡ ኦርቶዶክሳዊት፡ (ፍ፡ ነ፡ ፵፫፡ ፱። ያዕ፡ ዘእል)። ብዙ፡ ሰዎች፡ ይልቁንም፡ ካራና፡ ቅባት፡ ባህላቸውና፡ ትምርታቸው፡ ከቅዱስ፡ መጽሐፍ፡ የሚጣላ፡ ስሕተት፡ የተመላ፡ ክፉ፡ ጥፉ፡ ሲኾን፡ ኦርቶደክሶች፡ ነን፡ ይላሉ። (ሥላሴ፡ ዘድንቅ፡ ማርቆስ፡ ኦርቶዶክሳዊ)። አርዮስ፡ ወመምህሩ፡ ላዐለ፡ ሐዋርያት፡ አመክንዩ፡ ብሂለ፡ ፍጡር፡ ወልድ፡ በቀዳማዊ፡ ልደቱ፤ ለአጽድቆ፡ ሕልም፡ ነገሮሙ፡ ከንቱ። ዮምኒ፡ ይፈጽም፡ ዐመፃ፡ በመስፈርተ፡ እሉ፡ ክልኤቱ፥ እንዘ፡ ፍናዊሃ፡ በኵልቄ፡ ቤቱ፥ ሰብእ፡ ሖሉ፡ ለሃይማኖቱ፥ ይቀብዓ፡ ስመ፡ ምእት፡ ሠለስቱ። የኦርቶደክስ፡ ባህል፡ እንዴት፡ እንደ፡ ኾነ፡ በተዋሕዶ፡ ፍች፡ ተመልከት፡ (ዋሕደ፡ ዋሐደ)።

**አርቴውቂኖን፤(ጽር፡ አርኬፍቲኖን። ዕብ፡ ሻሜን)፤** ዘይት፤ ወይራ፤ ዕፀ፡ ቅብዕ። ባለብሉዮች፡ ግን፡ ዊንዛ፡ ዘግባ፡ ይሉታል፡ (፪ነገ፡ ፮፡ ፵፮)።

**አርቲክል፤(ሮማይ፡ አርቲኩሉስ)፤** የስም፡ ተውሳክ፤ ለ፡ ላ፡ ወንድና፡ ሴት፡ የሚለይበት። እልንና፡ አሐዱን፡ ተመልከት።

**ኤርትራ፤(ጽር፡ ኤሪትራ)፤** የባሕር፡ ስም፤ ከብርቱ፡ ሰይድ፡ እስከ፡ ባሕረ፡ ህንድ፤ ወይም፡ ከስዮስ፡ ወደብ፡ እስከ፡ ባብ፡ እልመንደብ፡ ያለ፡ ባሕር፤ ቀይሕ፡ ቀይሓዊ፡ ማለት፡ ነው። ባሕረ፡ ኤርትራ፡ (ባሕረ፡ ሐምያር)፤ የቀይ፡ ሕዝብ፡ ባሕር፤ ነሞችና፡ ጥቍሮች፡ ያይደሉ፡ ቀያዮች፡ የመንና፡ ሳባ፡ የሚገዙት፤ ወይም፡ ለራሱ፡ ቅላት፡ ቀይነት፡ ያለው፡ ባሕር። መሬቱ፡ ቀይ፡ ስለ፡ ኾነ፡ ቀይ፡ ስልባቦት፡ ይንሳፈፍበታል፤ ቀያይ፡ ዓሣ፡ ይወለድበታል፤ በዙሪያውም፡ ቀያይ፡ ሣር፡ ቅጠል፡ ያበቅላልና፤ ቀይ፡ ያሰኘው፡ ይህ፡ ነው። ባሕርነቱም፡ ከሜዲተራኒ፡ እስከ፡ ህንድ፡ ውቅያኖስ፡ ገጥሞ፡ ተያይዞ፡ በስተምሥራቅ፡ እስያንና፡ አፍሪቃን፡ ይለያል፡ (ዘፀ፲፡ ፲፱። ፲፫፡ ፲፰። ፲፭፡ ፬)።

**አስ፤(ዐማርኛ)፤** የማስደረግ፡ ልማድ፤ አቅተለ፤ አስገደለ። ተ፡ ሲጨመርበት፡ አስተ፡ እየኾነ፡ ወደ፡ ማደራረግ፡ ይለወጣል፤ አስተቃተለ፡ አጋደለ፤ አገዳደለ። በሰ፡ ግስ፡ ላይ፡ ሲነገር፡ ሰን፡ እየዋጠ፡ ይጠብቃል። አስበረ፡ አስተሳበረ፤ አሰበረ፤ አሳበረ፡ አሰባበረ። አስገደ፡ አሥገረ፤ አስገደ፡ አሠገረ። የአንና፡ የአስተን፡ አፈታት፡ ተመልከት። ፪ኛም፡ ሰ፡ በሌለበት፡ ግስ፡ እየገባ፡ ከአ፡ ተለይቶ፡ የጥሬ፡ መነሻ፡ ይኾናል። ዐዘዘ፡ አስዐዘዘ፡ አስያዘዘ፡ ሰያዝዝ።

**እስ፤** ያገባብ፡ ልማድ፡ እንደ፡ እን፡ ያለ፤ እንን፡ የመሰለ። ሣስተኛ፡ ፊደል፡ ከኵመ፡ ሲጨመር፤ እስከ፡ እስኩ፡ እስመ፡ እያለ፡ ርሱ፡ ራሱ፡ ፫፡ አገባብ፡ ይኾናል፤ ልማድነቱም፡ ከአስተና፡ ከእስት፡ የወጣ፡ ነው።

**አስባብ፤—ዘበኞች፤—ሰቢብ፡ ሰበ፤ ሰበበ።**

**አሰድ፤(ዐረ፡ እልአሰድ)፤** አንበሳ። ኮከብ፤ የኮከብ፡ ስም፤ አንበሳዊ፡ አንበስ፡ አንበሶ፡ ማለት፡ ነው። ኮከብነቱም፡ የሐምሌ፡ ነው። ከፀሓይ፡ ጋራ፡ ፴፩፡ ዕለት፡ ፲፡ ኬክሮስ፡ ይመግባል፡ (አቡሻ፡ ፫)።

**አስሀርት፤—ሠርቀ፡ ወርኖች፤—ሣህር።**

**አሲው፤ዎት፤(አሰወ፡ የአሱ፡ ይእሱ። ዕብ፡ ሱር፡ ዐረ፡ አሳ)፤** መፈወስ፡ ማዳን፤ መሾም፡ ማሠልጠን። (ጥፈ)፡ መፈወስ፡ መዳን፤ ጤና፡ ማግኘት፡ ባለጤና፡ መኾን፡ በመዳኒት፡ ወይም፡ በታምራት።

—፤ አስት፡ ማውጣት፤ ቡላድ፡ መምታት፤ ማንደድ፡ ማቃጠል፤ ማሞቅ፡ ማተኰስ፤ ማጋል፡ ማጋም፡ እሳት፡ ማድረግ።

**አሳዊ፤(ዊት፡ ውያን፡ ያት)፤** የሚፈውስ፤ የሚፈወስ፤ ፈዋሽ፡ ተፈዋሽ።

**አሶ፤** ወባ፡ ንዳድ፡ ትኵሳት፤ ሐኪምና፡ ፈውስ፡ የሚያስፈልግ፡ (ትግሬ)።

**አሶት፤** ፈውስ፤ ሀብተ፡ ፈውስ፤ መንፈሳዊ፡ ሥልጣን፡ (፩ቆሮ፡ ፲፪፡ ፱፡ ፳፰፡ ፴)። ንሰይኩ፡ ቅድስና፡ ዘነቢያት፡ ወአሶተ፡ ዘሐዋርያት። እመንፈስ፡ ቅዱስ፡ ነሚእ፡ አሶተ፡ (አርጋ፡ ፯። ድጓ)።

**እሳት** ፤ (ብ፡ እሳውት ። ሱር፡ ኤሽታ ። ዕብ፡ ኤሽ) ፤ በቁሙ ፤ የሚነድ፡ የሚበራ ፤ የሚያቃጥል፡ የሚበላ ፤ የሚፋጅ፡ የሚልጥ ፤ የሚለመጥጥ ። ይቡስ፡ ውዑይ፡ ብሩህ ፤ ከራቱ፡ ባሕርያት፡ አንዱ፡ በኹሉ፡ የሚገኝ ፤ በይብሰቱ፡ ከነፋስ ፤ በውዕየቱ፡ ከመሬት ፤ በብርሃኑ፡ ከውሃ፡ የሚስማማ ። በአምጣነ፡ ዕፀ፡ ለእሳት፡ የዐቢ፡ ነዱ ። እሳት፡ በባዒ ። ደብረ፡ ሚካኤል፡ ወለደት፡ ሊቃውንተ፡ እለ፡ ኮኑ፡ እሳተ፡ እሳተ፡ (ሚራ ፳፰፡ ፲ ። ፴፡ ፴ ። ቅኔ) ።

**እሳተ፡ እሳት** ፤ የሰማይ፡ እሳት ፤ እሳተ፡ ገሞራ ፤ ከዚህ፡ ዓለም፡ እሳት፡ ፯፡ እጅ፡ የሚበልጥ፡ (ሔኖ ፲፬፡ ፳፪) ።

**እሳተ፡ ገሃነም** ፤ ብርቱ፡ ቅጣት ፤ እስራኤል፡ ልጆቻቸውን፡ ለሞሎኽ፡ ሠውተው፡ ያቃጥሉበት፡ የነበረ፡ የሰማያዊ፡ እሳት፡ ምሳሌ፡ (ማቴ፭፡ ፳፪) ።

**እሳት፡ ዘለዓለም** ፤ የማይጠልስ፡ የማይጠፋ፡ የማያልፍ፡ ሥቃይ፡ (ማቴ፲፰፡ ፰) ።

**እሳተ፡ ሕይወት** ፤ መንፈስ፡ ቅዱስ፡ (ማቴ፫፡ ፲፩) ።

**እሳተ፡ መለኮት** ፤ ባሕርይ ፤ አካል ፤ ወይም፡ እሳትነት፡ (ቅዳ) ።

**እሳታዊ** ፤ የእሳት ፤ እሳታም ፤ እሳትማ፡ ቀይ ፤ ውዑይ ፤ ተፈጥሮው፡ ከእሳት፡ የኾነ ፤ እሳትነት፡ ያለው ። ሳውዳ፡ ዘውእቱ፡ ጠባይዕ፡ እሳታዊ ። እሳታውያን፡ እለ፡ ነደ፡ እሳት፡ እሙንቱ፡ ኪሩቤል፡ (ፈላስ ። ቅዳ፡ ሕር) ።

**አስት** ፤ በቁሙ ፤ አስቴ ፤ አስታ ፤ እሳታም፡ ዕንጨት ።

**አስሐወ** ፤—አወለቀ ፤—ስሒው፡ ስሐወ ።

**አስሐትያ** ፤—ውርጭ ፤—ስሒት፡ ስሕተ ፤ አስሐተ ።

**አስጣሮት** ፤ (ዕብ፡ ዐሽታሮት ። ጽር፡ አስታርቲ) ፤ ጣዖታት ፤ የበግ፡ መንጋ፡ የሚመስሉ ፤ በበጎች፡ አምሳል፡ የተቀረጡና፡ የተሣሉ፡ የበግ፡ ምስሎች ። ባለብሉዮች፡ ግን፡ ከዋክብት፡ ሦስቱ፡ ስድስቱ፡ ይሏቸዋል፡ (መሳ፪፡ ፲፫) ። ፪ኛም፡ በአስጣሮት፡ ፈንታ፡ አስጦራጢ ፤ አስጥርጥዮን፡ ይላል ፤ ፍቾው፡ አንድ፡ ነው፡ (፩ነገ፡ ፴፩፡ ፲) ።

**አሰየ** ፤—ሰጠ ፤—ዐስይ፡ ዐሰየ ።

**እስያ** ፤ (ጽር፡ አሲያ) ፤ ስመ፡ ክፍለ፡ ምድር ፤ ስመ፡ ብሔር ፤ ከምስቱ፡ የዓለም፡ ክፍሎች፡ አንዲቱ፡ ታላቂቱ፡ ክፍል ፤ የኤውሮፓ፡ ምሥራቅ ። የቱርክ፡ አገር፡ ደግሞ፡ ለብቻዋ፡ ታናሽ፡ እስያ፡ ትባላለች፡ (ራእ፩፡ ፲፩) ።

**እስከ** ፤ (እስ፡ ከ ። ዐቢይና፡ ደቂቅ፡ አገባብ) ፤ በቁሙ ፤ በቅርብና፡ በሩቅ፡ ሲገባ ፤ እስከ፡ እስኪ ፤ በትርጓሜ፡ ዐማርኛ፡ ድረስ፡ ይኾናል ። እመ፡ ሶበ፡ ጊዜ፡ ኀበ፡ ለ፡ ነ፡ ይዳምቁታል ፤ በር፡ ይከፍቱለታል ፤ ሳይከፍቱለትም፡ እስከ፡ እልህቅ፡ ወእረሥእ ፤ እስከ፡ ይመሲ ፤ እስከ፡ ይጸብሕ፡ እያለ፡ ብቻውን፡ ይገባል ። ሲዘረዝር፡ ግን፡ ነን፡ በር፡ ከፋች፡ አድርጎ፡ እስከኔየ ፤ ኔከ፡ ኔኪ፡ ኔሁ፡ ኔሃ፡ ኔነ፡ እያለ፡ በነ፡ ይዘምታል ። የቦታን፡ የጊዜን፡ የስፍርን፡ የቍጥርን፡ የሥራን፡ ኹሉ፡ ፍጻሜ፡ መድረሻውን፡ መከተቻውን፡ ያሳያል ። እስከ፡ ሶበ፡ እመጽእ ። እስከ፡ ጊዜ፡ ይሠርቅ፡ ፀሓይ ። በጽሐ፡ እስከ፡ ኀበ፡ ልኍመ፡ ፈረስ ። ተከዘት፡ ነፍስየ፡ እስከ፡ ለሞት ። እስከነ፡ ዐረብ ፤ የመዐለው፡ ኹሉ ። አንዳንድ፡ ጊዜም፡ ፍጻሜና፡ ጭራሽ፡ በሌለው ፤ ኢወለደት፡ እስከ፡ አመ፡ ሞተት ። ኢያእመራ፡ እስከ፡ አመ፡ ወለደት፡ እያለ፡ ይገባል፡ (ዕር፲፱፡ ቍ፴፰) ።

**እስኩ** ፤ (እስ፡ ኩ) ፤ የጥያቄና፡ የምክር፡ የልመና፡ ቃል ፤ እስኪ፡ እባክኽ ። ንግርኒ፡ እስኩ ። እስኩ፡ ፍታሕ፡ ለሊከ ። እስኩ፡ ስምዐነ ። እስኩ፡ ሀበነ፡ እያለ፡ በኋላም፡ በፊትም፡ ይገባል ። አንዳንድ፡ ጊዜም ፤ ተምኔት፡ ተግዳሮት፡ ዘቻ፡ ግን፡ ይኾናል ። እስኩ፡ ንርአያ፡ እስኩኬ፡ ንርአያ ። ይዜንዉከ፡ እስኩ፡ ወይንግሩከ ። እስኩ፡ እመ፡ ኢትገንዩ፡ ለምስል፡ ወኢትሰግዱ፡ (ድጓ ። ኢሳ፲፱፡ ፲፪ ። ዳን፫፡ ፲፭) ።

**አሰከ** ፤ (የአስክ፡ ይእስክ ፤ አሲክ፡ ኮት) ፤ ዐሸ፡ አኰላሸ ፤ ሰነጋ ፤ ቀጠቀጠ ፤ ሰለበ፡ ቈረጠ ። ደረሰ፡ ነካ ፤ አዋደደ፡ ሰካ ፤ የተባት፡ ያለሌ፡ ያውራ ።

**እስኪት** ፤ (ብ፡ እስኪታት ፤ አሰከት ። ዕብ፡ ኤሼኽ ። ሱር፡ አሽካ) ፤ ቍላ ፤ የቍላ፡ ፍሬ ፤ ቈለጥ፡ አስካሉ፡ ዕንቍላሉ ። ቍልሕን፡ ተመልከት ። ዘአሐቲ፡ እስኪቱ ። እልዐለት፡ እዴሃ፡ ወአንዘቶ፡ በክልኤሆን፡ አሰከቲሁ፡ (ዘሌ፳፩፡ ፳ ። ዘዳ፳፭፡ ፲፩) ።

**እስኪት** ፤ እባለ፡ ዘርዕ ፤ ላይኛው፡ ዘንጉ ፤ መድረሻ፡ ማለት፡ ነው ። ዘሞተ፡ እስኪቱ፡ በሥራይ ። ሠጠቁ፡ መላእክት፡ እስኪቶ፡ ለማር፡ ኤልያስ፡ ሊቀ፡ ምኔት፡ መነከሳይያት፡ ሶበ፡ ኮነ፡ ምስሌሁ፡ በሀየ፡ ፍትወት ። ለእለ፡ ይዜምዉ፡ በእንስሳ፡ ይትመተር፡ እስኪቶሙ ። ብእሲ፡ ዘይፈኑ፡ እስኪቶ፡ ውስተ፡ መንደቅ ፤ አው፡ ውስተ፡ ስቍረት ፤ አው፡ ውስተ፡ እዴሁ፡ ወይወፅእ፡ እምኔሁ፡ ፍትወት፡ (መጽ፡ ፈ ። ፊልክ፡ ፳፭ ። ፈ፡ መ፡ ፯፡ ፩ ። ፍ፡ ነ፡ ፵፰ ። ሲኖ ደ) ። አንዳንድ፡ መምህራን፡ ሰከየ፡ አስከየ፡ ብለው፡ ይገቡና፡ እስኪትን፡ ከዚህ፡ ያወጣሉ ፤ ፍቹውንም፡ አሶቃሽ፡ አስከሳሽ፡ እስከ፡ ሞት፡ አድራሽ፡ ይሉታል ። ዘየዐቅብ፡ እስኪቶ፡ የዐቅብ፡ ሕይወቶ፡ (ፈላስ) ።

**አሰከት** ፤ ጭጕኝ፡ የጕያ፡ ጠጕር፡ ሸከፉ፡ ቍርንድድ ። አሸከት፡ ወይም፡ አሸክት፡ የገብስና፡ የባቄላ፡

ዐረም ፡ ሽካራ ፡ ቅጠል ፡ በወይና ፡ ደጋ ፡ የሚበቅል ። (ተረት) ፤ ያይጥ ፡ ዱለት ፡ ማስሬያው ፡ አሽክት ።

**ኤስኬዴሬ፤(ጽር፡ኤክሴድሬ)፤** የዕቃ ፡ ቤት ፤ ዕልፍኝ ፡ (ሕዝ፵ ፡ ፵፬) ።

**አስካል ፤—ዘለላ ፡ ፍሬ ፤—ሰኪል ፡ ሰከለ ፤ ሰክል ።**

**አስኬማ ፤ (ጽር ፡ ስኺማ) ፤** ልብስ ፤ መልክ ፤ ቅርጽ ፡ ገጽ ። ነሥአ ፡ አርኣያ ፡ ገብር ፡ ወኮነ ፡ በአምሳለ ፡ ሰብእ ፡ ፀአስኬማሁ ። ወበአስኬማሁ ፡ አስተርአየ ፡ ከመ ፡ ሰብእ ፡ (ቄር ፡ ጸላ) ።

**አስኬማ፤(ሱር፡ኤስኪማ)፤** በቁሙ ፤ ልብስ ፡ ምንኵስና ፤ ከቀሚስ ፡ ከቅናት ፡ ከቆብ ፡ በኋላ ፡ በመጨረሻ ፡ የሚለበስ ፤ የፍጻሜ ፡ ምንኵስና ፡ ምልክት ። ይኸውም ፡ ከነት ፡ ከንቀልባ ፡ እንደ ፡ እንቢያጕሥ ፡ ኹኖ ፡ የሚሠራ ፡ ፲፪ ፡ ትእምርተ ፡ መስቀል ፡ ያለበት ፡ ነው ። ካስኬማ ፡ በኋላ ፡ ባሕታዊ ፡ መኾን ፡ መዝጋት ፡ አጽንዖ ፡ በኣት ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ ከገዳም ፡ መውጣት ፡ ወደ ፡ ዓለም ፡ መግባት ፡ ክልክል ፡ ነው ። መልአኩ ፡ ለእንጦንዮስ ፡ ስለ ፡ ሰጠውና ፡ ምንኵስና ፡ ሕገ ፡ መላእክት ፡ ስለ ፡ ኾነ ፤ ልብሱም ፡ አስኬማ ፡ መላእክት ፡ ይባላል ። አልበስዎ ፡ አስኬማ ፡ ዘመላእክት ። ዳንኤል ፡ አስኬማ ፡ መላእክት ፡ ዘለብሰ ። አስኬማክሙ ፡ አልባቲ ፡ ሙስና ፤ (ስንክ ፡ መስ፲፰ ። ኅዳ፲፯ ። ድጓ) ።

**አስከሬን ፤ (ናት ። ሮማይ ፡ ስክሪኒዉም) ፤** የገንዘብ ፡ መያዥ ፤ ታናሽ ፡ ማኅዳ ፡ ኩረጆ ፤ ቍናማት ፡ ከረጢት ፤ ኪስ ፡ ሙዳይ ፤ ተረንተራ ። የወርቅ ፡ የብር ፡ የገንዘብ ፡ ማጥን ፤ የልብስ ፡ የጌጥ ፡ የሽልማት ፡ መዝገብ ፤ ግምጃ ፡ ቤት ፡ ቤተ ፡ መዛግብት ፡ (ዮሐ፲፪ ፡ ፮ ። ፲፫ ፡ ፳፱) ። መበአ ፡ አስከሬን ፡ ይሁዳ ፡ የዐቅብ ። መጋቤ ፡ አስከሬን ። ይላሕዉ ፡ አስከሬናተ ፡ ስርጐኪ ፡ (ዲድ ፡ ፳፱ ። ሲኖዶ ። ኢሳ፫ ፡ ፳፯) ።

—፤ መቃብር ፤ የሬሳ ፡ ማጥን ፤ ርጥብ ፡ ሬሳ ፡ ወይም ፡ ደረቁ ፡ የፈረሰው ፡ የበሰበሰው ። ይህ ፡ ደግሞ ፡ የንፍስ ፡ ሣጥን ፡ ማለት ፡ ነው ። ምስጢሩ ፡ ከዚያው ፡ አይወጣም ።

**እስኪት ፤—እስከ ፤—አሰከ ።**

**አስል ፤(ትግሬ ፤ ዐረ) ፤** ዘር ፤ ሥር ፤ ጕንድ ፡ የትውልድ ፡ ምንጭ ።

**እስላም ፤—በቁሙ ፤—ሰሊም ፡ ሰለመ ፤ አስለመ ።**

**እስመ ፤ (እስ ፡ መ) ፤** ዐቢይና ፡ ንኡስ ፡ አገባብ ። ና ፡ ስለ ፡ እንደ ፡ ብሎ ፡ ቢል ፡ እኮ ፡ ቢያ ፡ ይኾናል ። አንተ ፡ ይሔስን ፤ እስመ ፡ ኢነስሓ ። ምንትኑ ፡ ዝ ፡ ነገር ፤ እስመ ፡ ይኤዝዘሙ ። ንእዶ ፤ እስመ ፡ ከመ ፡ ጠቢብ ፡ ገብረ ፤ ና ፡ (ማቴ፲፩ ፡ ፳ ። ሉቃ፬ ፡ ፴፮ ። ፲፮ ፡ ፰) ። ሞተ ፡ እስመ ፡ ሐመ ፤ ተርፈ ፡ እስመ ፡ ደክመ ፤ መጽሰወ ፡ እስመ ፡ ጾመ ፤ ስለ ። ናና ፡ ስለ ፡ አንድ ፡ ወገን ፡ ናቸው ፤ ና ፡ በገባበት ፡ ስለ ፤ ስለ ፡ በገባበት ፡ ና ፡ ይገባል ። ዘይክሕድ ፡ ወይብል ፡ እስመ ፡ ኢየሱስ ፡ ኢኮነ ፡ መሲሐ ። እሙን ፡ ነገር ፡ እስመ ፡ ክርስቶስ ፡ መጽአ ፡ ውስተ ፡ ዓለም ። ጽሑፍ ፡ እስመ ፡ አሐዱ ፡ እምአኀው ፡ መጽአ ፤ እንደ ፡ (፩ዮሐ ፡ ፪ ፡ ፳፪ ። ፩ጢሞ ፡ ፩ ፡ ፲፭ ። ሬልክ ፡ ፶፱) ። አምጽኡ ፡ ወርቀ ፡ እስመ ፡ ንጉሥ ፡ ውእቱ ። ንጉሥ ፡ ነውና ፤ ንጉሥ ፡ ስለ ፡ ኾነ ፤ ንጉሥ ፡ እንደ ፡ መኾኑ ፤ ንጉሥ ፡ ነው ፡ ብለው ፤ ንጉሥ ፡ ነኽ ፡ ሲሉ ፡ ያሰኛል ። ብለውና ፡ ሲሉ ፡ የውእቱ ፡ ማቅኛ ፡ ትርፍ ፡ ዐማርኛ ፡ ነው ፡ እንጂ ፤ የእስመ ፡ ዘይቤ ፡ አይደለም ። ጸዐሎ ፡ እስመ ፡ ገብር ፤ አልዐሎ ፡ እስመ ፡ ኄር ፤ ባሪያ ፡ ብሎ ፤ ለጋስ ፡ ብሎ ፡ እያሰኘ ፡ በሚስማማው ፡ ቃል ፡ ይፈታል ። አንዳንድ ፡ ጊዜም ፡ ናሁ ፡ ይኾናል ፤ ናሁ ፡ ደግሞ ፡ እስመ ፡ ይኾናል ። እኮና ፡ ቢያ ፡ ሲኾን ፡ ንኡስ ፡ አገባብ ፡ ነው ። እስመ ፡ ብዙኃን ፡ እሉ ፡ አንትሙ ፤ ብዙ ፡ ናቸው ፡ እኮ ፡ እኮን ። እስመ ፡ ርኢክኒሁ ፡ አመንክኒ ፤ አይተኸ ፡ ቢያ ፤ ስለ ፡ ተብሎም ፡ ይፈታል ። እስመ ፡ እንዘ ፡ ትሰምዕ ፡ ተጸመምከኒ ፤ ሰምተኸ ፡ ቢያ ፤ እየሰማኸ ፡ ቢያ ፡ ያሰኛል ። የቀረውን ፡ ባገባብ ፡ ተመልከት ፡ (ዕር፲፱ ፡ ቍ፳፯) ።

**አስማድዮስ ፤ (ጽር ፡ አስሞዴዎስ) ፤** የጋኔን ፡ ስም ፤ ሾተላይ ፡ ጋኔን ፤ በሴት ፡ ዐድሮ ፡ ወንዶች ፡ በወንዶች ፡ ዐድሮ ፡ ሴቶች ፡ የሚፈጅ ፡ (ጦቢ፫ ፡ ፰ ፡ ፲፯ ። ዮሐ፪ ፡ ፲፰ ። ማቴ፳፪ ፡ ፳፩—፳፯) ።

**አሶንያ ፤** ጨረቃ ፤ የጨረቃ ፡ ስም ። እብላንና ፡ ኤራስን ፡ ተመልከት ፡ (ሔኖ፸፰ ፡ ፪) ።

**አስፈሊጦስ ፤ (ጽር ፡ አስፋሊቶስ) ፤** የጡብ ፡ የሸክላ ፡ ጭቃ ፤ የሙጫ ፡ ቅጥራን ፡ ለጡብ ፡ ለሸክላ ፡ የሚቀባ ፤ የሚለቀለቅ ። ባለብሉዮች ፡ ግን ፡ ሰሊጥ ፡ የባሕር ፡ ዐረፋ ፡ ይሉታል ፡ (ዘፀ፪ ፡ ፫ ። ኩፋ ፡ ፲ ። ፵፯ ። መቃ ፡ ፲፪ ። ስንክ ፡ ታኅ፪) ።

**አስፌም ፤(ጽር ፡ ሄሴፌም ። ዕብ ፡ አሱፊም) ፤** የቦታ ፡ ስም ፤ መከነ ፡ ጉባኤ ፤ መሰብሰቢያ ፡ መከማቻ ፤ ወይም ፡ ከምቹዎች ፡ ማለት ፡ ነው ። ባለብሉዮች ፡ ግን ፡ ዐጥረ ፡ ገጥ ፡ ይሉታል ፤ ለቤተ ፡ መቅደስ ፡ መቅረቡን ፡ ያሳያል ፡ (፩ዜና ፡ ፳፮ ፡ ፲፯) ።

**እስፍንቱ ፤-ስንት ፤ምን ፡ ያኽል ፤—ሰፈን ፡ ሰፈነ ፡ ስፍን ፤ እስፍንት ።**

**እስፍንቶፎኔሕ ፤(ጽር ፤ ቅብጥ ፡ አብሶንቶምፋኔኽ) ፤** የፍልስፍና ፡ ስም ፡ ፈርዖን ፡ ለዮሴፍ ፡ ያወጣለት ፤ ከሣቴ ፡ ኅቡእ ፤ ማእምረ ፡ ኅቡኣት ። ጸፈንን ፡ ተመልከት ። (ዘፍ፵፩ ፡ ፵፭) ።

**አስፋር ፤(ዐረ ፡ አጽፈር) ፤** ያይነት ፡ ስም ፤ ብጫ ፤ ወርቅ ፡ የሚመስል ። አክደር ፡ ወአስፋር ፡ (መቃ ፡ ገ፫) ።

**አስፋርስ ፤(አው ፡ መስፈርስ) ፤** የወፍ ፡ በሽታ ፤ ሰውነት ፡ ወይባ ፡ የሚያስመስል ፡ ብጫ ፡ የሚያ

ደርግ ። ወየሐምም ፡ ሕማመ ፡ መስፈርስ ፡ (ስንክ ፡ ሐምሌ) ።

**አስፈር ፤ (ጽር ፡ ሬጎስ ። ዕብ ፡ ዳሌቄት) ፤** ብርቱ ፡ ትኵሳት ፡ ከልክ ፡ ከመጠን ፡ ያለፈ ። የሆድ ፡ በሽታ ፤ ብጫ ፡ የሚያደርግ ፤ የሚያጠወልግ ። ይቀሥፊከ ፡ እግዚ ፤ በደዌ ፡ ሲሕ ፡ ወበፈፀንት ፡ ወበአስፈር ፡ (ዘዳ ፳፰ ፡ ፳፪) ።

**አስፌር ፤—ዓምና ፤— ሰፌር ፡ ሰፈረ ።**

**ኤስፋር ፤ (ዕብ ፡ ኤሽፋር) ፤** ክፍል ፡ ዕድል ፤ የሥጋ ፡ መቍነን ፤ አንድ ፡ ሙዳ ፤ ጉማ ፤ የልጃገረድ ፡ ጡት ፡ የሚያኽል ። ፋር ፡ የሚዘኑ ፡ ስም ፤ ልኩ ፡ ፯ ፡ ጉማ ፡ የሚያነሣ ፤ ኤስፋር ፡ የፋር ፡ ፯ኛ ፡ እጅ ፤ ከ፯ ፡ አንድ ፡ (፩ዜና ፡ ፲፮ ፡ ፫) ።

**አስፈሬድ ፤ (ዳት ። ጽር ፡ ስፒሪዶስ) ።** ቅርጫት ፤ እንቅብ ፤ ወራንታ ፤ የእንቅብ ፡ የቀፎ ፡ የጉታ ፡ ዐይነት ፤ ከቀጫጭን ፡ ሐረግ ፡ ከለበቅ ፡ ከሸንበቆና ፡ ከቀርካሓ ፡ የሚሠራ ፡ (ማቴ፲፭ ፡ ፴፯ ። ማር፰ ፡ ፰ ። ግብ፱ ፡ ፳፭ ። ገድ ፡ ተክ ። ዳን፲፫ ፡ ፴፫) ።

**አስቀጢን ፤ (ጽር ፡ ስታክት) ፤** ጥሩ ፡ ሽቱ ፤ ከዕጣን ፡ ከከርቤ ፡ የሚወጣ ፤ ለትኵስ ፡ ሬሳ ፡ የሚቀባ ፤ ሬሳን ፡ እንዳይገማና ፡ እንዳይፈርስ ፡ እንዳይበሰብስ ፡ የሚያደርግ ። ሐነጠንና ፡ ስጡቃጤን ፡ እይ ፤ ከዚህ ፡ ጋራ ፡ አንድ ፡ ነው ፡ (አቡሻ ፡ ፵፰) ።

**አስቄጥስ ፤ (ሮማይ ፡ አስኬታ) ፤** በረሓ ፤ የበረሓ ፡ ስም ፡ በምድረ ፡ ግብጽ ፡ ውስጥ ፡ ያለ ፤ የመቃርዮስ ፡ ክፍል ፡ ገዳመ ፡ ሲሃት ። አ ፡ አልበ ፤ ስኬታ ፡ ጽላሎት ፤ በተገናኝ ፡ አልበ ፡ ጽላሎት ፡ ማለት ፡ ነው ። ቀድሞ ፡ ብዙ ፡ ገዳማት ፡ ነበሩበት ፤ ዛሬ ፡ ያሉት ፡ ግን ፡ ፬ ፡ ብቻ ፡ ናቸው ፤ የታላቁ ፡ መቃርዮስና ፡ የመክሲሞስ ፡ የዱማቴዎስ ፡ ያባ ፡ ብሶይና ፡ የዮሐንስ ፡ ከማ ፡ (ስንክ ፡ መጋ፳፯ ፡ ፈልክ) ። በቅብጥ ፡ ቋንቋ ፡ ግን ፡ ሚዛን ፤ የሚዛን ፡ ሳሕን ፡ ማለት ፡ ነው ፡ ይላሉ ። ገዳመ ፡ አስቄጥስ ፡ ዘበትርጓሜሁ ፡ መዳልው ፡ አልባብ ፡ (ስንክ ፡ ጥቅ፳) ።

**አስቀሎብ ፤** አርስጣባብ ፤ የፍልስፍና ፡ ከታብ ፤ መጽሐፈ ፡ ኮከብ ። አስቀሎባና ፡ አርስጣባብ ፡ አንድ ፡ ስም ፡ ናቸው ። ወገብረ ፡ በጥበብ ፡ መጽሐፈ ፡ አስቀሎባ ፡ ወራእየ ፡ ከዋክብት ፡ ወመዳልወ ፡ ፀሓይ ፡ (ክብ ፡ ነገ) ።

**እስቁፍ ፤ (ዐረ ፡ ኡስቁፍ) ፤** ኤጲስቆጶስ ፤ ሲያበዛ ፡ አስቃፍ ፡ ይላል ፡ (ስንክ ፡ ጥቅ፳፫ ። ነሐ፳፱) ።

**አሰር ፤—ፍለጋ ፤—አሢር ፡ አሠረ ።**

(ጥ) **አሰረ ፤—ቀጠረ ፤ ዐሥር ፡ አደረገ ፤—ዐሥሮ ፤ ዐሠረ ።**

**አሶር ፤ (ዕብ ፡ አሹር) ፤** ስመ ፡ ነገድ ፤ ስመ ፡ ሀገር ፤ ታችኛው ፡ ሶርያ ፡ ነነዌ ፡ (ዘፍ፲ ፡ ፲፩ ፡ ፳፪) ።

**አሲር ፤ ሮት ፤ (አሰረ ፡ የአስር ፡ ይእስር ፡ ይእ ። ዕብ ፡ አሳር ። ሱር ፡ ኤሳር ። ዐረ ፡ አሰረ) ፤** ማሰር ፤ ማቈራኘት ፤ ማጣመር ፡ ማዛወግ ፤ ኹለቱን ፡ ሦስቱን ፡ ወይም ፡ ብዙውን ፡ አንድ ፡ ማድረግ ፤ ማከት ፡ መተብተብ ፤ ማጋዝ ፡ ማውገዝ ፤ መገዘት ፡ መለየት ። እስሮ ፡ በእዴሁ ፡ ወእገሪሁ ። ወአሰረ ፡ ኃሊናሁ ፡ ምስለ ፡ እግዚ ። የአስር ፡ በአሥራው ። እስርዎሙ ፡ ክላስስተ ። የአስሩ ፡ ጾረ ፡ ዐቢየ ። አሰሮ ፡ ለሰይጣን ። አውገዝነ ፡ ወአሰርነ ፡ (ሒዝ፲ ፡ ፱ ። ፊልክ ፡ ፳፱ ። ቅዳ ፡ ግሩ ። ማቴ፲፫ ፡ ፴ ። ፳፫ ፡ ፬ ። ድጓ ። መቅ ፡ ታም) ።

**አሳሪ ፤ (ሪት ፡ ርያን ፡ ያት ፤ አሰርት) ፤** በቊሙ ፤ የሚያስር ፡ አንድ ፡ የሚያደርግ ። አግዐዝነ ፡ ለዘልነ ፡ እማእሰረ ፡ ኀጢአት ፡ ዘአሰረነ ፡ አሳሪ ። ወአሳሪሁ ፡ (ግንዘ ። መቅ ፡ ወን) ።

**አእሰረ ፤** አሳሰረ ፤ አስጋዘ ።

**ተአስረ ፤** ታሰረ ፤ ተቈራኘ ፤ አንድ ፡ ኾነ ። ከመ ፡ ከልብ ፡ ዘየሐውር ፡ ለተአስሮ ። ተአስረ ፡ በሊሁ ፡ እደዊሁ ፡ ወእገሪሁ ። ተአስረት ፡ ነፍስ ፡ በሥጋ ። ነፍሰ ፡ ዮናታን ፡ ተአስረት ፡ በነፍሰ ፡ ዳዊት ፡ (ምሳ፯ ፡ ፳፪ ። ግብ፳፩ ፡ ፲፩ ። ዮሴፍ ። ፩ነገ ፡ ፲፰ ፡ ፩) ።

**ተኣሰረ ፤** ተሳሰረ ፤ ተቈራኘ ፤ ተቈላለፈ ።

**እሱር ፤ (ራን ፡ ራት ፡ ስርት) ፤** የታሰረ ፤ የተሳሰረ ፤ የተቈራኘ ፤ አንድ ፡ የኾነ ፤ እስር ፤ እስርስር ። ንዋይ ፡ ዘኢኮነ ፡ እሱረ ፡ ማእሰር ፡ ላዕሌሁ ። እሱራን ፡ ውስተ ፡ ፈለገ ፡ ኤፍራጥስ ። እመ ፡ ኮንከ ፡ እሱረ ፡ ምስለ ፡ ብእሲትከ ። ብእሲት ፡ ዘእስርት ፡ በሕግ ። ዘአሰርከ ፡ በምድር ፡ ይኩን ፡ እሱረ ፡ በሰማያት ፡ (ዘኍ፲፱ ፡ ፲፭ ። ራእ፱ ፡ ፲፬ ። ፍ ፡ ነ ፡ ፳፱ ፡ ፭ ። ፳፭ ። ማቴ ፡ ፲፯ ፡ ፲፱) ።

**እስረት ፤** ማሰር ፤ መታሰር ፤ አስተሳሰር ፤ እስራት ፤ እስርነት ። ውሂብ ፡ እምድኅረ ፡ ስኢል ፡ እስርት ፡ እድ ፡ ውእቱ ፤ ወውሂብስ ፡ ዘእንበለ ፡ ይስአል ፡ ፈቲሐ ፡ እድ ፡ ውእቱ ። በእንተ ፡ እስረቱ ፡ በሐብል ። ለዘ ይደልዎ ፡ እስረት ። አሰርዎሙ ፡ ክቡደ ፡ እስረተ ፡ (ፈላስ ። አዋል ። ፈ ፡ መ ፡ ፪ ፡ ፲፭ ። መቃ ፡ ገ፪) ።

**ማእሰር ፤ (ራት ፤ መአስር ። ማእሰርት ፤ መአስርት ፤ ታት) ፤** ማሰሪያ ፤ መታሰሪያ ፤ የእስራት ፡ ቦታ ፤ መሣሪያ ። ታወፅአሙ ፡ ለሙቁሓን ፡ እማእሰር ። ማእሰርተ ፡ ኀጺን ። መኣስርቲሃኒ ፡ ሰርጉ ፡ ያክንት ፡ (ኢሳ፵፪ ፡ ፯ ። ሔኖ፷፩ ፡ ፫ ። ሢራ፯ ፡ ፴) ።

— ፤ ልባጥ ፡ ልብጣት ፤ የናስና ፡ የግንብ ። ወማእሰሩ ፡ በዕፀ ፡ ብሔር ፡ (፩ዕዝ ፡ ፯ ፡ ፳፱) ።

**ማእሰረ ፡ ግዘት ፤** የግዝት ፡ ቃል ፤ ውጉዝ ፡ ማለት ፡ (አፈ ፡ ተ፱) ።

**ማእሰረ ፡ ልሳን ፤** ድዳነት ፤ ዝምታ ፡ (ማር ፡ ፯ ፡ ፴፭) ።

**ማእሰረ ፡ ዐመፃ ፤** ኀጢአት ፤ ክሕደት ፡ (ቅዳ) ።

**ማእሰረ ፡ ሰላም** ፤ ፍቅር ፤ አንድነት ፡ (ኤፌ ፬ ፡ ፫) ።

**ማእሰረ ፡ ተዋስቦ** ፤ የጋቢ ፡ ሥርዐት ፤ ተክሊል ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ (ፍ ፡ ን ፡ ፳፱ ፡ ፬) ። በነገር ፡ ኹሉ ፡ እየተናበበ ፡ እንደ ፡ ስልቱና ፡ እንዳወራረዱ ፡ ይፈታል ።

**አስተአሰረ** ፤ አስተሳሰረ ፤ አያያዘ ፤ አዋሰበ ፤ አቈራኘ ።

**አስራብ** ፤—ፈሳሾች ፤—ሰሬብ ፡ ሰረበ ፤ ሰርብ ።

**አሶርዮን** ፤ (ጽር ፡ አሳሪዎን ። ዕብ ፡ ኢሳር) ፤ ታናሽ ፡ ገንዘብ ፤ የገንዘብ ፡ ክፍል ፤ እንደ ፡ ሶልድና ፡ እንደ ፡ ቤሳ ፡ ያለች ፡ መዳብ ፤ ንሐስ ፡ (ማቴ፲ ፡ ፲፱ ። ሉቃ፲፪ ፡ ፮) ።

**ኤሲሳህ** ፤ (ዕብ ፡ አሺሻህ) ፤ የወይን ፡ የበለስ ፡ ቋንጣ ፤ የመጠጥ ፡ ዕቃ ፤ ብርጭቆ ፡ ጠርሙዝ ፡ የመሰለው ፡ ኹሉ ፤ በመሣሪያው ፡ ጠጁን ፡ መናገር ፡ ነው ፤ ባለብሉዮችም ፡ የወይን ፡ ጠጅ ፡ የዘቢብ ፡ ጕድጓድ ፡ ይሉታል ። ምስጢሩ ፡ ግን ፡ ስሱንና ፡ ስድስን ፡ ያሳያል ፤ የኢን ፡ ፮ኛ ፡ እጅ ፡ ፮ኛ ፡ ክፍል ፡ ወይም ፡ ከ፮ ፡ ፩ ፡ ማለት ፡ ነው ። የኢንንና ፡ የኤስፋርን ፡ ፍች ፡ እይ ፡ (፩ዜና ፡ ፲፮ ፡ ፫) ።

**እሳት** ፤—በቁሙ ፤—አሲው ፡ አሰወ ።

**አስተ** ፤ (አስ ፡ ተ) ፤ አስ ፡ የማስደረግ ፤ ተ ፡ የመደረግና ፡ የመደራረግ ፡ ልማድ ። በተገናኙ ፡ ኹለቱ ፡ አንድ ፡ ሲኾን ፤ አስተ ፡ የማድረግና ፡ የማስደረግ ፡ የማደራረግ ፡ ይኾናል ፤ መደቡ ፡ ግን ፡ የማደራረግ ፡ ነው ። የማድረግና ፡ የማስደረግ ፡ ሲኾን ፡ ሥርወ ፡ ቀለሙን ፡ ግእዝና ፡ ሳድስ ፡ ያደርጋል ፤ ይኸውም ፡ በአ ፡ ፈንታ ፡ ስለ ፡ ገባ ፡ ነው ። ግእዝ ፡ ሲያደርግ ፤ ገበረ ፡ አስተገበረ ፤ ሐመመ ፡ አስተሐመመ ፤ ሐመቀ ፡ አስተሐመቀ ፤ ሐቀረ ፡ አስተሐቀረ ፤ ዐጸበ ፡ አስተዐጸበ ፤ ቀጸለ ፡ አስተቀጸለ ፤ ረሰየ ፡ አስተረሰየ ፡ ይላል ። ሳድስ ፡ ሲያደርግ ፤ በፅዐ ፡ አስተብፅዐ ፤ በቍዐ ፡ አስተብቍዐ ፤ ነፍሰ ፡ አስተንፈሰ ፤ ነተነ ፡ አስተንተነ ፤ ፈሥሐ ፡ አስተፍሥሐ ፤ ርእየ ፡ አስተርአየ ፤ ሰረየ ፡ አስተስረየ ፡ ይላል ። የማደራረግ ፡ ሲኾን ፡ ግን ፡ ሥርወ ፡ ቀለሙን ፡ ራብዕ ፡ ያደርጋል ፤ መለዮው ፡ ይህ ፡ ነው ። ይህም ፡ በደረ ፡ አስተባደረ ፤ ገብአ ፡ አስተጋብአ ፤ ደለወ ፡ አስተዳለወ ፤ ወደየ ፡ አስተዋደየ ፤ ነበረ ፡ አስተናበረ ፤ ሠነየ ፡ አስተማነየ ፤ ቀተለ ፡ አስተቃተለ ፡ እያለ ፡ መኼዱን ፡ ያሳያል ። ልማድን ፡ ተመልከት ።

**ኤስቴኤኪራን** ፤ (ጽር ፡ ኢኽሲኢራን) ፤ ዓሣት ፤ ዓሦች ፤ ዓሣዎች ። ባለብሉዮች ፡ ግን ፡ ዓሣ ፡ ወጋሮች ፡ ይሉታል ፡ (ንሐ፲፪ ፡ ፴፱) ።

**እስትጉቡእ** ፤—ክምችቱ ፤—ገብአ ፡ አስተጋብአ ።

**ኤስታዎስ** ፤ (ጽር ፡ ኤስ ፡ ቴዎስ) ፤ አሐዱ ፡ አምላክ ፡ (ስንክ ፡ ኅዳ፲፱ ። ሚያ፴) ።

**አስትዓ** ፤—ግብር ፤—ሰቲዕ ፡ ሰትዐ ።

**አስቲር** ፤ (ትግሬ) ፤ ሰማይ ፤ ጠፈር ፤ አየር ፡ ፈለክ ።

**አስታር** ፤ (ዕብራ) ፤ ሰማያዊ ፡ ጠፈራዊ ፡ ኮከብ ፤ ኮከበ ፡ ሠርክ ፡ ፀሓይ ፡ ስትገባ ፡ ወዲያው ፡ ታይቶ ፡ ወዲያው ፡ የሚጠፋ ፤ ከዚህ ፡ የተነሣ ፡ አስታር ፡ ቦሸሽ ፤ ወይም ፡ አስታርቦ ፡ ሸሽ ፡ የሚባል ። ኮከባዊ ፡ ዕንቍ ፤ አበባ ፤ የባሕር ፡ እንስሳ ፤ መልኩና ፡ ቅርጹ ፡ ኮከብ ፡ የሚመስል ፡ የኮከብ ፡ ዐይነት ። እስመ ፡ ኢይሁቦ ፡ እግዚ ፡ አስታረ ፡ ሞገስ ፡ (ሚራ፴፯ ፡ ፳፩) ። ጽርኡ ፡ ግን ፡ ኢተውህቦ ፡ ጸጋ ፡ እግዚ ፡ ይላል ።

**አስትሮን** ፤ (ጽርእ) ፤ ግዘፈ ፡ ብርሃን ፤ ስሌዳ ፤ ክበብ ፤ ወይም ፡ ግዙፋን ፡ ብርሃናት ፤ ፀሓይ ፡ ጨረቃ ፡ ኮከብ ።

**አስታር** ፤ (ዐረ ፡ ኢስታር) ፤ ስጢጥራ ። የስጢጥራን ፡ ፍች ፡ ተመልከት ፤ ከዚህ ፡ ጋራ ፡ አንድ ፡ ነው ። አስታር ፡ ዘይቤ ፡ ፲፪ ፡ ወቄት ፡ ይላል ፤ የግምት ፡ አፈታት ፡ (ጥሬ ፡ ሰዋ) ።

**አስቴር** ፤ (ዕብ ፡ ኤስቴር) ፤ ኅብእት ፤ ስውርት ። ወለት ፡ ዘስማ ፡ አስቴር ፡ (አስቴ፪ ፡ ፯) ።

**አስጳዳቶስ** ፤ (ጽር ፡ አስፓላቶስ) ፤ የሽቱ ፡ ዕንጨት ፤ እሾኻም ፤ ሥሩ ፡ ከሽቱ ፡ ጋራ ፡ የሚቀመም ፡ የሚነጠር ። ባለብሉዮች ፡ ደርሶኒ ፡ ይሉታል ፡ (ሚራ፳፱ ፡ ፲፭ ። አርጋ ፡ ፮) ።

**ኤቲ** ፤ (ጽርእ) ፤ ንጥፍ ፡ ደንጊያ ፤ ሰፊ ፡ ታላቅ ፡ ልሙጽ ፡ (፫ነገ ፡ ፩ ፡ ፱) ።

**አቲው** ፤ **ዎት** ፤ (**አተወ ፤ አቶ ፡ የአቱ ፡ ይእቱ ። ዕብ ፡ አታሀ ። ሱር ፡ አታእ ። ዐረ ፡ አታ**) ፤ መግባት ፤ መመለስ ፤ መምጣት ፤ አቶ ፡ መባል ፡ ከሰው ፡ ቍጥር ፡ መግባት ፤ አቻ ፡ መኾን ፡ መተካከል ፤ ከሚስት ፡ ከባልንጀራ ። ተአቱ ፡ መቃብሪከ ፡፡ እቱ ፡ ኀበ ፡ ሕዝብከ ፡፡ ወአተወ ፡ እምኀበ ፡ መዝበር ፡፡ ለእመ ፡ ዳኅነ ፡ አቶክሙ ፡፡ ይጕነዲ ፡ አቲወ ፡ (ኢዮ፩ ፡ ፳፯ ። ዘዳ ፴፪ ፡ ፶ ። ኤር፲፱ ፡ ፲፱ ። ጦቢ፩ ፡ ፲፯ ። ማቴ፳፱ ፡ ፵፭) ።

**አታዊ** ፤ (**ዊት ፡ ውያን ፡ ያት ፤ አተውት**) ፤ የሚገባ ፡ ገቢ ፤ ተመላሽ ፤ መጪ ፤ አቻ ፡ እኩያ ።

**እትወት** ፤ መግባት ፤ መመለስ ፤ ምለሳ ፤ አመጣጥ ። በንግደትከ ፡ ወበእትወትከ ፡፡ ቡሩክ ፡ ይኩን ፡፡ ውፍረትክሙ ፡ ወእትወትክሙ ፡ (መዝ ፡ ፶፭ ። ግንዘ) ። እንዘ ፡ የአቱ ፡ በማለት ፡ ፈንታ ፡ እትወቶ ፡ ይላል ፤ የመላሽ ፡ ስሕተት ፡ ነው ፡ (ማር፲፩ ፡ ፳፩ ። ሉቃ፳፫ ፡ ፳፮) ።

— ፤ ምርት ፤ ውጤት ፤ የምድር ፡ ዐላባ ፤ ፍሬ ። በአምጣነ ፡ እትወተ ፡ እክለ ፡ ገራህቱ ፡፡ ወይከውን ፡ እትወቱ ፡ ለእለ ፡ ይነድቁ ፡ ሀገረ ፡፡ በእትወተ ፡ አክማሪሁ ፡፡ እንበለ ፡ ዘርዐ ፡ እምድር ፡ እትወተ ፡ (ዘሌ፳፯ ፡ ፲፯ ። ሕዝ፵፭ ፡ ፲፭ ። መቃ ፡ ገ፱ ። ድጓ) ።

**አእተወ** ፤ አገባ ፤ አስገባ ፤ መለሰ ፤ አመጣ ። ዘሎ ፡ ጾረ ፡ ያእትዉ ፡ ኢየሩሳሌም ። ያእትዎሙ ፡ ብሔሮሙ ። ያእትዉ ፡ ጸባሕተ ፡ ለንጉሥ ፡ (ነሐ፲፫ ፡ ፲፭ ። ኢሳ፲፱ ፡ ፱ ። ፩ዕዝ ፡ ፱ ፡ ፯) ።

**ምእታው** ፤ (ዋት) ፤ መግቢያ ፤ ማግቢያ ፤ መመለሻ ፤ መምጫ ፤ ቤት ፡ አገር ። ከሙ ፡ ይኩን ፡ ምእታዊክሙ ፡ ኀበ ፡ መላእክት ። ምእታዊሆሙ ፡ ውስተ ፡ ፈለገ ፡ ሲኦል ። ወምእታዉስ ፡ አርማቴም ። ምእታወ ፡ አፍራሲሁ ፡ እምነ ፡ ግብጽ ፡ (ሄርማ ። ቀሌ ። ፩ነገ ፡ ፯ ፡ ፲፯ ። ፫ነገ ፡ ፲ ፡ ፳፰) ።

**እቶን** ፤ (ናት ። ሱር ፡ አቱና ። ዐረ ፡ አቱን) ፤ የማድ ፡ ቤት ፤ ፋርን ፤ ማብሰያ ፡ መጋገሪያ ፤ ምድጃ ፤ የእሳት ፡ ጕድጓድ ፤ አጐደ ፡ ኖራ ፡ ክሰል ፡ የሚያወጡበት ፤ ጡብ ፡ ሸክላ ፡ የሚተኰሱበት ። ብሱል ፡ በእቶን ። ከመ ፡ እቶን ፡ ዘአንደዱ ፡ ለኀቢዝ ፡ ኅብዝት ። ለእመ ፡ ገብረ ፡ አሐዱ ፡ እቶነ ፡ ዘየዐርግ ፡ እምኔሁ ፡ ጢስ ። በዓለ ፡ እቶን ። እቶነ ፡ ገሃነም ። እቶነ ፡ ኀጺን ፡ (ዘሌ፪ ፡ ፬ ። ሆሴ፯ ፡ ፬ ። ፍ ፡ ነ ፡ ፴፯ ። ፳፫ ። ሱቱ ፡ ዕዝ፯ ፡ ፩ ። ዘዳ፬ ፡ ፳) ።

**እትዌቄህ** ፤ (ዕብ ፡ አቴቄይሃእ) ፤ የግንብ ፡ ዐምድ ፤ ሕንጻውን ፡ ለማጽናት ፡ ዐብሮ ፡ የተሠራ ፤ ዐልፎ ፡ ዐልፎ ፡ የቆመ ፤ ከላይ ፡ በቀስተ ፡ ደመና ፡ የተያያዘ ፡ (ሕዝ ፵፩ ፡ ፲፭) ።

**ኢትዮጵያ** ፤ (ጽር ፡ ኢቲዮፒአ ። ዐረ ፡ ሱዳን ። ዕብ ፡ ኰሽ ፤ ስመ ፡ ነገድ) ፤ የመልክና ፡ የሕብር ፡ የሀገር ፡ ስም ፤ የሱዳኖች ፡ አገር ፡ መላው ፡ ጠቅላላው ፤ ከግብጽ ፡ ቀጥሎ ፡ ያለው ። ጥቍር ፡ ጠቋራ ፡ ከሰልማ ፤ የጥቍሮች ፡ አገር ፡ ማለት ፡ ነው ። ኢትዮጵያ ፡ ታበጽሕ ፡ እደዊሃ ፡ ኀበ ፡ እግዚ ። ዘሎሙ ፡ ኢትዮጵያ ፡ ዘጸሊም ፡ ሥጋሆሙ ። ወቦ ፡ ዘትከውን ፡ ኀሳረ ፡ በኀበ ፡ ካልአኒሃ ፡ ከመ ፡ ቀሪጸ ፡ ገጽ ፡ በኀ ፡ ኢትዮጵያ ፡ ወኖባ ። ኖባ ፡ የነገድ ፡ የሀገር ፤ ኢትዮጵያ ፡ የመልክ ፡ የሕብር ፡ ስም ፡ (መዝ ፡ ፷፯ ። ቀሌ ። ፍ ፡ ነ ፡ ፶፩) ። ዕብራይስጡ ፡ ኰሽ ፡ የሚለውን ፡ የኰሽን ፡ ስም ፡ ኹሉ ፤ ጽርኡ ፡ ኢትዮጵስ ፡ ይለዋል ፤ ከዚህ ፡ የተነሣ ፡ ታሪክ ፡ ጣፎች ፡ ኹሉ ፡ ኰሽን ፡ የኢትዮጵስ ፡ አባት ፤ ወይም ፡ የአክሱማስ ፡ ልጅ ፡ አንደኛ ፡ ኢቶጲስ ፡ ይሉታል ፤ አክሱማስ ፡ ያሉትም ፡ ኰሽን ፡ ነው ። ኹለተኛም ፡ የኰሽ ፡ አገር ፡ ኹሉ ፡ በልጁ ፡ በኢትዮጲስ ፡ ስም ፡ ኢትዮጵያ ፡ ተባለች ፡ ይላሉ ፤ የመላ ፡ የግምት ፡ አነጋገር ፡ ነው ፤ ዕብራይስጥና ፡ ጽርእ ፡ ላላየ ፡ ግን ፡ እውነት ፡ ይመስለዋል ። በጽርእ ፡ ቋንቋ ፡ ኢትዮጲስ ፡ የተባለው ፡ ያው ፡ በዕብራይስጥ ፡ ኰሽ ፡ የተባለው ፡ ዋነኛውና ፡ መደበኛው ፡ ርሱው ፡ ራሱ ፡ በኰሩ ፡ ግንባር ፡ ቀደሙ ፡ የካም ፡ ልጅ ፡ ነው ፡ እንጂ ፤ ሌላ ፡ ፪ኛ ፡ አካል ፡ የኰሽ ፡ ልጅ ፡ አይደለም ። ለኰሽ ፡ በኦሪትና ፡ በዜና ፡ መዋዕል ፡ ከተጻፉት ፡ ሳባ ፡ ሐዊላ ፡ ሰብታ ፡ ረዕማ ፡ ሰብተቃ ፡ ናምሩድ ፡ ከሚባሉት ፡ ከ፮ቱ ፡ ሌላ ፡ ፳፪ ፡ ልጆች ፡ እንዳሉት ፡ የዮናናዊ ፡ ታሪክ ፡ ይናገራል ። ከዚሁ ፡ ከዮናን ፡ የተቀዳው ፡ የሞሪዬም ፡ ታሪክ ፤ የካም ፡ ልጅ ፡ ኰሽ ፡ አርባ ፡ አልቤዎን ፡ ኪሬኔ ፡ ከሚባሉ ፡ ከ፫ቱ ፡ እኅቶቹ ፡ ፳፰ ፡ ወልዷል ፤ ዕድሜውም ፡ ፲፻፹፰ ፡ ነው ፤ መዲናውና ፡ መቃብሩ ፡ አኵስም ፡ ናት ፡ ይላል ። ፳፰ ፡ ያላቸውንም ፡ በየስማቸው ፡ ጥፉቸዋል ፤ የ፮ቱ ፡ ስም ፡ በኦሪት ፡ እንደ ፡ ተጣፈው ፡ ነው ፡ (ዘፍ፲ ፡ ፯ ፡ ፰) ። ከቀሩትም ፡ ከ፳፪ቱ ፡ ነገድ ፡ አቢስ ፡ እንጂ ፡ ኢትዮጲስ ፡ የተባለ ፡ የለም ፤ አቢስን ፡ ግን ፡ የሳባ ፡ ሳብዓይ ፡ የናምሩድ ፡ ተከታይ ፡ ከአልቤዎን ፡ የተወለደ ፡ የኰሽ ፡ ፯ኛ ፡ ልጁ ፡ ብሎ ፡ እናቱ ፡ ሳትቀር ፡ ስሙንም ፡ ቍጥሩንም ፡ ጥፎለታል ፤ አቢስን ፡ ተመልከት ። ኢትዮጵስ ፡ ማለት ፡ በጽርእ ፡ ኹለት ፡ ያሳያል ፤ የሰው ፡ ስም ፡ ሲኾን ፡ ጥቍር ፡ ጠቋራ ፡ ከሰልማ ፤ የሀገር ፡ ስም ፡ ሲኾን ፡ ቈላ ፡ በረሓ ፡ ምድረ ፡ በዳ ። ስምንቱም ፡ ከኰሽ ፡ ሞት ፡ በኋላ ፡ በ፪ ፡ ሺሕ ፡ ከ፬፻፶፱ ፡ ዓመት ፡ ፸ ፡ ሊቃናት ፡ ያወጡት ፡ ከ፸ ፡ ሊቃናት ፡ የተገኘ ፡ ሐዲስ ፡ እንግዳ ፡ ደኃራዊ ፡ ስም ፡ ነው ። በሱዳን ፡ ዙሪያ ፡ ያለችውም ፡ መላይቱ ፡ አፍሪቃ ፤ ይልቁንም ፡ ከነጭ ፡ አባይ ፡ ወዲህ ፡ ያለችው ፡ ክፍል ፤ የጥቍሮች ፡ የኰሽ ፡ ልጆች ፡ አገር ፡ ስለ ፡ ኾነች ፡ በዚህ ፡ ባዲሱ ፡ ስም ፡ ኢትዮጵያ ፡ ትባላለች ፡ (ዘፍ፪ ፡ ፲፫) ። በብሉይ ፡ በሐዲስ ፡ የተጣፈው ፡ ዋነኛውና ፡ መደበኛው ፡ ኢትዮጵያ ፡ ግን ፡ ታላቁን ፡ በረሓ ፡ ሰሐራን ፡ ጨምሮ ፡ የኖባ ፡ ክፍል ፡ ነው ፡ (፪ዜና ፡ ፲፬ ፡ ፱ ፡ ፲፪ ፡ ፲፫ ። ፲፮ ፡ ፰ ። ፬ነገ ፡ ፲፱ ፡ ፱ ። ኢሳ፴፯ ፡ ፱ ። ሕዝ፴ ፡ ፬ ፡ ፭ ፡ ፱ ። ግብ፰ ፡ ፳፯) ። ወዲያ ፡ ማዶም ፡ በእስያ ፡ ክፍል ፡ ያለው ፡ ያረቦች ፡ አገር ፡ ቃዲስ ፡ በርኔና ፡ ሐቅለ ፡ ሲና ፡ ሌላውም ፡ ኹሉ ፤ ቈላ ፡ በረሓ ፡ ፍጹም ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ ስለ ፡ ኾነ ፤ በዕብራይስጥ ፡ (ጺያ) ፡ ጺይም ፡ ይባላል ፡ እንጂ ፤ ኰሽ ፡ አይባልም ፤ በጽርእ ፡ ግን ፡ እንዳፍሪቃ ፡ ክፍል ፡ እንደ ፡ ኖባ ፡ ኢትዮጵያ ፡ ይባላል ። ይገንዩ ፡ ቅድሜሁ ፡ ኢትዮጵያ ። ወወሀብኮሙ ፡ ሲሳዮሙ ፡ ለሕዝበ ፡ ኢትዮጵያ ፡ (መዝ ፡ ፸፩ ። ፸፫) ። የቀረውን ፡ በሰፊው ፡ ታሪክ ፡ ተመልከት ፤ (ክፍል ፡ ፩) ።

**ኢትዮጳዊ** ፤ **ኢትዮጵያዊ** ፤ የኢትዮጵያ ፤ አፍሪቃዊ ፤ ኖባዊ ፡ ሱዳናዊ ፤ ወይም ፡ አፍሪቂ ፡ ኖቤ ፡ ሱዳኔ ። ምስጢሩ ፡ ጥቍረትና ፡ ቈለኛነት ፡ ነው ። ይዌልጥኑ ፡ ኢትዮጵያዊ ፡ ማእሶ ፡ ወነምር ፡ ሕንብርብሬሁ ። ወረከበ ፡ ኢትዮጵያዌ ፡ ንኡሰ ፤ ደቦል ፡ ሸንቅላ ፡ (ኤር፲፫ ፡ ፳፫ ። ፊልክ ፡ ፴፱) ።

**አታሚን** ፤ **አታኒም** ፤ (ጽር ፡ አታኒን ። ዕብ ፡ ኤታኒም) ፤ ስመ ፡ ወርኅ ፤ የዕብራውያን ፡ ፯ኛ ፡ ወር ፡ ጥቅምት ፤ ፯ኛነቱ ፡ ለሚያዝያ ፡ (፫ነገ ፡ ፰ ፡ ፪) ። ኤታን ፤ ጥንት ፡ መሠረት ፤ ጥንተ ፡ ወርኅ ፡ ጥንተ ፡ ዓመት ፤ ጥንተ ፡ ዓለም ፡ ጥንተ ፡ ፍጥረት ። ኤታኒም ፡ ውስጠ ፡ ብዙ ፡ ነው ፡ ፍጥረትን ፡ ያሳያል ፤ ዓለም ፡ የተፈጠረ ፡ በጥቅምት ፡ ነውና ፤ በፀሐይ ፡ ቍጥር ፡ ግን ፡ የመስከረም ፡ ማፍ ፡ ይኾናል ። ይኸውም ፡ አመ ፡ ርእሰ ፡ ሳብዕ ፡ ሠርቀ ፡ ወርኅ ፡ ግበሩ ፡ መጥቅዐ ፡ ባለው ፡ ይታወቃል ፡ (ዘሌ፳፫ ፡ ፳፬) ። የግእዝና ፡ የቅብጥም ፡ ዐውደ ፡

ዓመት ፡ በመስከረም ፡ ራስ ፡ መኾኑ ፡ መጥቅዕን ፡ መሠረት ፡ ይዞ ፡ ነው ። ከአዳም ፡ ዠምሮ ፡ እስከ ፡ ሙሴ ፡ ቀዳማይ ፡ ወርኅ ፡ ኤታኒም ፡ ነበረ ፤ ኋላ ፡ ግን ፡ ከግብጽ ፡ የወጡበት ፡ ኒሳን ፡ ስለ ፡ ኾነ ፤ የፋሲካው ፡ በግ ፡ የክርስቶስ ፡ አምሳል ፡ ነውና ፤ ምሳሌውን ፡ ከአማናዊው ፤ ሥጋዊውን ፡ ከመንፈሳዊው ፡ አያይዞ ፡ ዛሬ ፡ በዚህ ፡ ወር ፡ ከግብጽ ፡ እንደ ፡ ወጣችኹ ፡ ኋላም ፡ በዚሁ ፡ ወር ፡ ከገሃነም ፡ ትወጣላችኹ ፡ ሲል ፤ ዓመ ፡ ከመ ፡ ዮም ፡ እንደ ፡ ማለት ፡ ዝንቱ ፡ ወርኅ ፡ ይኩንክሙ ፡ ቀዳማየ ፡ አውራኅ ፡ ብሎ ፡ የጥቅምትን ፡ ቅድምና ፡ ለሚያዝያ ፡ የሚያዝያን ፡ ፪ኛነት ፡ ለጥቅምት ፡ አዋርሶታል ፡ (ዘፀ፲፪ ፡ ፪) ። ዐውደ ፡ ዓመት ፡ ግን ፡ ምንም ፡ የወር ፡ ቍጥር ፡ ቢፋለስ ፡ ከዚያው ፡ ከጥንቱ ፡ ከጥቅምት ፡ አልወጣም ። ፍጥረተ ፡ ዓለም ፡ በሚያዝያ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ በጥቅምት ፡ አይደለም ፡ ብሎ ፡ የሚያፈችል ፡ ቢኖር ፤ ባህሉ ፤ ይኩንክሙ ፡ ቀዳማየ ፡ አውራኅ ፡ ባለው ፡ ቶሎ ፡ ይፈርሳል ፤ ቀዳማዩ ፡ ቀዳማይ ፡ ይኹን ፡ አይባልምና ። አቡ ፡ ሻህርም ፡ ጥንተ ፡ ፍጥረት ፡ መስከረም ፡ መኾኑን ፡ ለማስታወቅ ፡ የጨረቃን ፡ ቍጥር ፡ ለመጠንቀቅ ፡ ከሚያዝያ ፡ በታች ፡ ፯ ፡ ወሮች ፡ ተውሳክ ፡ ይጨምራል ፡ (አቡሻ ፡ ፴፯) ።

**አቲቅ ፤ (ዕብራ) ፤** የግንብ ፡ ዐምድ ፡ ፬ ፡ ማእዝን ፡ ያለው ። ኹለተኛም ፡ የዕቃ ፡ ቤት ፡ ዐምድ ፡ ስለ ፡ ኾነ ፡ ዕቃ ፡ ቤት ፡ ብለው ፡ ይፈቱታል ፤ እትዌቁሆን ፡ እይ ፡ (ሕዝ፵፪ ፡ ፫) ።

**አቱር ፤ (ቅብጥ ፡ አቶር) ፤** ስመ ፡ ወርኅ ፤ ኅዳር ፡ (አቡሻ ፡ ፰) ።

**አተርጋዎን ፤ (ጽርእ) ፤** ቃል ፡ ድምፅ ፤ ቃለ ፡ መላእክት ፤ ፍሬ ፡ ነገር ፡ የሚሰማበት ፤ አእትፊኮንን ፡ የመሰለ ፡ (ሃይ ፡ አበ) ።

**አትራክስ ፤ (ጽር ፡ አንትራክስ) ፤** የዕንቍ ፡ ስም ፤ ዕንቍ ፡ ፈርጥ ፡ ከደንጊያ ፡ ከሰል ፡ የሚገኝ ፡ (ጦቢ፲፫ ፡ ፲፯ ። ስንክ ፡ መስ፲፯) ።

**አትሮንስ ፤ (ጽር ፡ ትሮኖስ) ፤** የንጉሥ ፡ ዙፋን ፤ የጳጳስ ፡ ወንበር ፡ ታላቅ ፡ ምጡቅ ፤ የሰባኪ ፡ የአንባቢ ፡ ስፍራ ፡ በቤተ ፡ ክሲያን ፡ ውስጥ ፡ የሚሠራ ፤ የመጽሐፍ ፡ ወንበር ፡ ታጥፎ ፡ የሚቀመጥበት ፡ ተዘርግቶ ፡ የሚነበብበት ፡ (፫ነገ ፡ ፲ ፡ ፲፱ ፡ ፲፰ ። ስንክ ፡ ኅዳ፰ ፡ ፴ ። መጋ፲፫ ። ፍ ፡ ነ ፡ ፰ ፡ ፱) ።

(ጥ) **አቲት ፤ ቶት ፤ (አተተ ፡ የአትት ፡ ይእትት ። ዕብ ፡ አቴት ፤ አመለከተ) ፤** መራቅ ፡ ማግለል ፤ መለየት ፡ መነጠል ፤ ገለል ፡ ፈቀቅ ፡ ማለት ። ከመ ፡ ይእትት ፡ እምኔክሙ ። የአትት ፡ ኵሉ ፡ ግላ ። የአትቱ ፡ ኵሎሙ ፡ በሞት ፡ (፩ቆሮ ፡ ፭ ፡ ፪ ። ፪ቆሮ ፡ ፫ ፡ ፲፮ ። ኩፋ ፡ ፯) ።

— ፤ መሻር ፡ መቅረት ፤ መጥፋት ፡ መበላሸት ፤ ምስጢሩ ፡ ከዚያው ፡ ይገባል ። ወይእትት ፡ ሥልጣኖሙ ፡ እምኵሉ ፡ መኳንት ። ለእምሮ ፡ ዘኢየአትት ። ተአትት ፡ ኵላ ፡ አእምሮቶሙ ፡ (ቁድር ። ቅዳ ። ኩፋ ፡ ፳፫) ። ኹለተኛም ፡ በቀደሰ ፡ ቤት ፡ በአተተ ፡ ፈንታ ፡ ተአተተ ፡ ይባል ፤ አያሰኝም ። ኢትትኤተቱ ፡ ወርሐቀ ፡ ኢተሐውሩ ። ተአተተ ፡ ሐቀ ፡ እምሀየ ። ኢይትአተቱ ፡ እምኔሁ ። ይትአተት ፡ በትረ ፡ ግብጽ ፡ (ዘፀ፰ ፡ ፳፱ ። ማቴ ፳፮ ፡ ፴፱ ። ሔኖ፲፱ ፡ ፳፫ ። ዘካ፲ ፡ ፲፩) ።

**አታቲ ፤ (ቲት ፡ ትያን ፡ ያት) ፤** የሚርቅ ፡ የሚያገል ፤ አግላይ ፡ ፈቀቅ ፡ ባይ ።

(ላጥ) **እቱት ፤ (ታን ፡ ታት ፡ ትት) ፤** የራቀ ፡ ያገለለ ፤ የተነቀለ ፡ የተፈነቀለ ፤ ፈቅ ፡ ፈቀቅ ፡ ያለ ፤ ገለልተኛ ። ወእቱት ፡ አረፍተ ፡ ቤቱ ። ረከበት ፡ እብነ ፡ እቱተ ፡ እምአፈ ፡ መቃብር ። ምንባበ ፡ መጻሕፍት ፡ ይኩን ፡ እቱተ ፡ ሐቀ ፡ እምነ ፡ ምሥዋዕ ፡ (ሕዝ፵፩ ፡ ፯ ። ዮሐ፳ ፡ ፩ ። ኪዳ) ።

**እቱተ ፤** የራቀ ፡ ኹኖ ፤ ርቆ ፡ ፈቀቅ ፡ ብሎ ፤ ተለይቶ ፡ ብቻውን ። ትነብር ፡ ምስሌየ ፡ እቱተ ። እለ ፡ ይነብሩ ፡ እቱተ ፡ ምስለ ፡ ንጉሥ ። ይኑም ፡ እቱተ ፡ እምነ ፡ ብእሲቱ ፡ (፩ዕዝ ፡ ፱ ፡ ፲፪ ። አስቴ፩ ፡ ፲፬ ። ፈ ፡ መ ፡ ፲፬ ፡ ፱) ።

**እታቴ ፤** መራቅ ፤ አራራቅ ፤ ርቀት ፤ ሩቅነት ።

**አእተተ ፤** አራቀ ፤ አስራቀ ፤ አስወገደ ፤ አሰደደ ፤ አስጣለ ፡ አሶለቀ ። ናእትቶ ፡ ለልጹቅ ፡ ወናቄርቦ ፡ ለርሑቅ ። አእትቱ ፡ እምፍኖት ፡ እብነ ። ታእትቶ ፡ ለዝሉፉ ። አእትት ፡ አልባሰ ፡ ርሱሐ ፡ እምላዕሌሁ ፡ (ቅዳ ፡ ግሩ ። ኢሳ፷፪ ፡ ፲ ። ኢዮ፲፬ ፡ ፳ ። ዘካ፫ ፡ ፬) ።

— ፤ ገደለ ፤ አጠፋ ፤ በቁሙ ፤ አተተ ፡ ከቍጥር ፡ አወጣ ። ከመ ፡ ያእትቶሙ ። ኢያእተተ ፡ ዘርዖሙ ። ወእምዘተርፈከ ፡ አሐደ ፡ አእትት ፡ (ኩፋ ፡ ፲፯ ። ሚራ፵፯ ፡ ፳፪ ። መር ፡ ዕጢ) ።

**ተአተተ ፤** ተራራቀ ፤ ተለያየ ፤ እየብቻው ፡ ኾነ ። አተታ ፤ የጠፈረና ፡ የዐስየ ፡ ቤትኛ ፡ እንደ ፡ ኾነ ፡ የቀደሰ ፡ ቤት ፡ እንዳይደለ ፡ አስተውል ።

**ኤጳውሎስ ፤ (ጽር ፡ ሄፓፍሌዎስ ። ዕብ ፡ ፊሀሒሮት) ፤** ስመ ፡ ሀገር ፤ እስራኤል ፡ ለፈርዖን ፡ የሠሩለት ፤ ይኸውም ፡ ፊቶም ፡ ነው ፤ መንቶች ፡ ረዣዥሞች ፡ ኹለት ፡ ጣዖታት ፡ የቆሙበት ፡ (ዘፀ፲፬ ፡ ፪ ። ፱ ፡ ፲፩) ።

**አጳይዶን ፤ (ጽር ፡ ሄፓይዶን ። ዕብ ፡ ሐርጡሚም) ፤** መሰግላን ፤ ሟርተኞች ፡ ኮከብ ፡ ቈጣሮች ፤ በፊደል ፡ በሥዕል ፡ በግብጻዊ ፡ ስገል ፡ በሐረግ ፡ በጠልሰም ፡ የሚጠነቍሉ ፡ (ዳን፬ ፡ ፯) ።

**አጴልዮጤን ፤ (ጽር ፡ አፒልዮቲስ) ፤** የበታ ፡ የማእዝን ፡ ስም ፤ ወደ ፡ ምሥራቅ ፡ ያለ ፤ ወይም ፡ መቅሠፍትነት ፡ ያለው ፡ የምሥራቅ ፡ ነፋስ ፡ (ዮዲ፯ ፡ ፲፰) ።

**አጵልዮን ፤ (ጽር ፡ አፖልዮን) ፤** አጥፊ ፤ ጥፋት ፤ ምዝባሬ ፡ ፍርሰት ። አብዶንን ፡ እይ ፤ ከዚህ ፡ ጋራ ፡ አንድ ፡ ነው ፡ (ራእ፱ ፡ ፲፩) ።

**አጵሎን** ፤ (ጽር ፡ አፖሎ) ፤ ጣዖት ፤ የጣዖት ፡ ስም ፡ (ስንክ ፡ ኅዳ፲፰ ፡ የከ፷፫ ፡ ነሐ፲) ።

**አጳሊጴ** ፤ (ጽር ፡ አፖሊፑ) ፤ በቤት ፡ ዙሪያ ፡ ያለ ፡ የውስጥ ፡ ወልወል ፤ የተለየ ፡ ክፍል ፡ (ሕዝ ፵፩ ፡ ፲፪) ።

**ኤጴሚዳስ** ፤ (ጽር ፡ ኤፖሚዴስ) ፤ መትከፈ ፡ አንቀጽ ፤ ደጃፉን ፡ ገብቶ ፡ ግራና ፡ ቀኝ ፡ ያለው ፡ የመዝጊያው ፡ ኋላ ። ባለቅኔዎች ፡ ግን ፡ እብን ፡ በረድ ፡ ይሉታል ፡ (ሕዝ፵ ፡ ፵፰ ፡ ፵፩ ፡ ፪) ።

**ኤጴሞስ** ፤ (ጽር ፡ ኤፖሚዴስ) ፤ ዝኒ ፡ ከማሁ ፤ መትከፍ ፤ ልብስ ፡ መትከፍ ። ባለብሉዮች ፡ ግን ፡ ቀሚስ ፡ ዘይበጽሕ ፡ እስከ ፡ እግር ፡ እምርእስ ፡ ይሉታል ፡ (ዘፀ፳፰ ፡ ፯) ።

**ኤጲፋንያ** ፤ (ጽር ፡ ሄፒፋኒያ) ፤ አስተርእዮ ፤ መታየት ፡ መገለጽ ፤ ዕለተ ፡ ጥምቀት ። በዓለ ፡ ኤጲፋንያ ፡ በዘቦቱ ፡ አርአየ ፡ እግዚ ፡ ስብሐተ ፡ መለኮቱ ፡ በውስተ ፡ ጥምቀት ፡ በቅድመ ፡ ዮሐንስ ፡ በፈለገ ፡ ዮርዳኖስ ። ኤጲፋንያ ፡ ማልሲት ፡ ዘተጠምቀ ፡ ባቲ ፡ ዘኢተጠምቀ ፡ ትካት ፡ (ዲድ ፡ ፳፱ ። ስንክ ፡ ጥር ፲፩ ፡ ፲፫) ።

**ኤጲፋንዮስ** ፤ (ጽር ፡ ሄፒፋኒዉስ) ፤ ዝኒ ፡ ከማሁ ፤ የሰው ፡ ስም ። ይኸውም ፡ ብዙ ፡ ድርሳናት ፡ የጣፈ ፡ የቆጵሮስ ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ ነው ፤ እንደ ፡ ጳውሎስ ፡ ምሁረ ፡ ኦሪት ፡ አይሁዳዊ ፡ ነበር ፤ ጌታ ፡ በታምራት ፡ ማርኮ ፡ መምህረ ፡ ወንጌል ፡ አድርጎታል ፡ (ስንክ ፡ ግንቦ፲፯ ። ሃይ ፡ አበ ። ቅዳ) ።

**አጶርጊ** ፤ (ጽር ፡ አፓርኺ) ፤ የእሸት ፡ በኵራት ፤ በኵረ ፡ ወይን ፤ በኵረ ፡ በለስ ፤ በኵረ ፡ ኅብስት ፤ የመሰለው ፡ ኹሉ ። ናቄርብ ፡ ለከ ፡ አጶርጊ ፡ ቀዳምያተ ፡ ፍሬ ፡ ዘአከ ። አጶርጊ ፡ ባሕቲቱ ፡ ይበልዕ ፡ (መጽ ፡ ኪዳ ። ራእ ፡ ማር ። ሕዝ፵፬ ፡ ፴) ። ተረፈ ፡ መሥዋዕትም ፡ አጶርጊ ፡ ይባላል ።

**አጶሮግዮን** ፤ በኵርነት ፤ ቀዳማዊነት ፤ መዋዕለ ፡ ሠዊት ። እምድኅረ ፡ ዕርገቱ ፡ ለእግዚእነ ፡ ዘበአጶሮግዮን ፡ ለኀበ ፡ ሰማይ ፡ (ማቴ፳፰ ፡ ፳፩) ። ባለሐዲሶች ፡ ግን ፡ ሥጋ ፡ ይሉታል ።

—፤ ዕንቍ ፡ የዕንቍ ፡ ፈርጥ ፤ ፍሬው ፡ ቅንጣቱ ፡ (ድጓ ፡ መስ፲፩ ። አርጋ ፡ ፯) ።

**ኤጲስቆጶስ** ፤ (ሳት ። ጽር ፡ ሄፒስኮፖስ) ፤ ጠባቂ ፤ መምህር ፤ የጳጳስ ፡ ኹለተኛ ፤ የሊቀ ፡ ጳጳስ ፡ ሦስተኛ ። በእንተ ፡ ኤጲስቆጶሳት ። ወይሚም ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ ባሕቲቱ ፤ እስመ ፡ ማልሳይ ፡ ማዕርጊሁ ፡ (ፍ ፡ ነ ፡ ፭ ። ፯) ። ሲኖዶስ ፡ ትእዛዝ ፡ ጴጥሮስ ፤ ሊቃናት ፡ ሠለስቱ ፡ ጾታ ፤ ወሠለስቲሆሙ ፡ አሐቲ ፡ ፍና ፡ ይላቸዋልና ፤ እሊህ ፡ ሦስቱ ፡ በመኾም ፡ በመሻር ፡ አንድ ፡ ስለ ፡ ኾኑ ፤ ኹሉም ፡ በኤጲስቆጶስ ፡ ስም ፡ ይጠራሉ ። ኤጲስቆጶስ ፡ ዅሉ ፡ ፍጥረት ፡ ወልደ ፡ እግዚ ፡ ዐቢይ ፡ ሊቀ ፡ ካህናት ። አትናቴዎስ ፡ ዘኮነ ፡ ቅድመ ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ ላዕለ ፡ ሀገረ ፡ እስክንድርያ ። በከመ ፡ ይቤ ፡ ፊልክስ ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ ዘሮሜ ። (ፍ ፡ ነ ፡ ፬ ። ቄር ። ሃይ ፡ አበ) ። ጳጳስና ፡ ተመልከት ።

**ኤጲስቆጶስና** ፤ ኤጲስቆጶስነት ፤ ኤጲስቆጶስ ፡ መኾን ፤ የኤጲስቆጶስ ፡ ሹመት ፡ ማዕርግ ። እምድኅረ ፡ ኤጲስቆጶስናሁ ፡ (ፍ ፡ ነ ፡ ፵፪ ፡ ፲፩ ። ፳ ። ፊልክ ፡ ፲፩) ።



**በ** ፤ ኹለተኛ ፡ ፊደል ፤ በግእዝ ፡ አልፍ ፡ ቤት ፡ በአበገደ ። ስሙ ፡ ቤት ፤ ቍጥሩ ፡ ኹለት ፤ አኃዝ ፡ ሲኾን ፡ በ ፡ ክልኤት ፡ ቱ ፡ ይባላል ። ዕብራውያን ፡ ግን ፤ ኹለትን ፡ መደብ ፡ አድርገው ፡ ከራሱ ፡ ላይ ፡ ነቍጣ ፡ እየጨመሩ ፡ ኹለት ፡ እልፍ ፡ ይሉታል ። ኹለተኛ ፡ ማለት ፤ ምስጢሩ ፡ ሰኞንና ፡ የሰኞን ፡ ፍጥረት ፡ መደብ ፡ አድርጎ ፡ ኹለተኛውን ፡ አካል ፡ ወልድን ፡ ያሳያል ፡ (ዘፍ፩ ፡ ፯—፰) ።

**በ** ፤ (ደቂቅ ፡ አገባብ) ፤ በቁም ፡ ቀሪ ፡ ማድረጊያ ፡ ን ፡ ጋራ ፡ ቸልታ ፡ ጊዜ ፡ ለ ፡ ወደ ፡ እንደ ፡ ስለ ፡ ይኾናል ። ማድረጊያ ፡ ሲኾን ፡ በኹሉ ፡ ይገባል ፤ የቀረውን ፡ ባገባብ ፡ ተመልከት ፡ (ዕር፳፩ ። ቍ፲፱) ።

**በ** ፤ ነባር ፡ አንቀጽ ። አለ ፤ ኖረ ፤ ነበረ ፤ ኾነ ። ላንድም ፡ ለብዙም ፡ ለወንድም ፡ ለሴትም ፡ ይከታል ። ቦ ፡ ዐርክ ፡ ኀላፊ ። ቦ ፡ ጻድቃን ፡ ውሉደ ፡ ቤትከ ። ቦ ፡ ብእሲት ፡ እንተ ፡ ትሜኒ ፡ እምብእሲት ። ወቦ ፡ አንስትኒ ፡ እለ ፡ ጌሣ ፡ ኀበ ፡ መቃብር ። ቦ ፡ ቦቱ ፡ ባለው ፡ በዝርዝርነት ፡ ሲፈታ ፡ ግን ፡ ላንድ ፡ ብቻ ፡ እንጂ ፡ ለብዙ ፡ አይኾንም ። ይህም ፡ አለው ፡ አለለት ፡ አለበት ፡ እያለ ፡ መኼዱን ፡ ያሳያል ። ቦቱ ፡ ከቦ ፡ ተለይቶ ፡ በርሱ ፡ በት ፡ ይኾናል ። ዘቦቱ ፡ ዅሉ ፡ ከነ ፤ ኹሉ ፡ በርሱ ፡ የተፈጠረ ፤ ወይም ፡ የተፈጠረበት ። ዅሉ ፡ ዘየአምን ፡ ቦቱ ፤ የሚያምንበት ፡ ኹሉ ። በርሱ ፡ ቢል ፡ በት ፡ ቢል ፡ ስልቱ ፡ አንድ ፡ ነው ። ለከፋም ፡ ለበጎም ፡ ይኾናል ።

**በእ** ፤—ገባ ፤—በዊእ ፡ በእ ።

**በኡናህ** ፤ **በውኒ** ፤ (ቅብጥ ፡ ፓዎኒ) ፤ የግብጦች ፡ ፲ኛ ፡ ወር ፡ ሠኔ ፡ (አቡሻ ፡ ፰) ።

**በአኔርጌስ፤** (ጽርእ። ዕብ፡ ብኔይ፡ ር ጎሽ)፤ ደቂቀ፡ ነጐድጓድ፡ (ማር፫፡ ፲፯)።

**በእንተ፤—ስለ፤—እንተ፡ በ።** አገባብ፡ እይ፡ (ዕር፲፱፡ ቊ፷፰)።

**ብኢስ፤ ሶት፤ (ብእሰ፡ ይብእስ፡ ይብ አስ። ዕብ፡ ባአሽ፤ ገማ። ዐረ፡ በኢሰ)፤** መባስ፡ መጽናት፤ መክፋት፤ ማገርሸት፤ መቈጣት፤ እየ ባሰ፡ መኼድ፤ መጕዳት። መጠላት፡ ማስጠየፍ፤ ማስቀ የም፤ የደዌ፡ የቍስል፡ የጠባይ፡ የግብር፡ የክፉ፡ ነገር። በሽታ፡ ቢስ፡ ማለት፡ ከዚህ፡ የወጣ፡ ነው። ወእመሂ፡ አርመምኩ፡ ይብእሰኒ፡ ሕማምየ። ዘባዕለ፡ ኃጥ ኣን፡ ይብእስ፡ ምስብዒተ፡ ዝንቱ፡ ዙሉ። ይብእ ሰከ፡ረኃፀ፡ውስተ፡ቀኖት፡በሊኅ። ብእሶ፡ ለንጉሠ፡ ፋርስ። እበድ፡ ዘይብእሶሙ፡ (ኢዮ፲፯፡ ፯። ሚራ፴፡ ፰። ግብ፱፡ ፭። ፱ነገ፡ ፲፯፡ ፬። ፩ጢሞ፡ ፮፡ ፱)።

—፤ ማደግ፤ መጕልመስ፤ አካለ፡ መጠን፡ ማድረስ፤ መ ግነን፤ ፍጹም፡ ጕበዝ፡ መኾን። መድፈር፡ መጨከን፤ መቀልጠፍ፡ መፍጠን፤ ያርበኛ። ተብዐን፡ እይ፤ የዚህ፡ ጎረ፡ ነው።

**በኣሲ፤ (ሲት፡ ስያን፡ ያት)፤** የሚብስ፤ የ ሚከፋ፤ ጕጂ፡ አስቀያሚ።

**ብኡስ፤ (ሳን፡ ሳት፡ እስት)፤** የባሰ፡ የከፋ፤ የተጠላ፤ ክፉ፡ መጥፎ። ብዑድ፡ ርሑቅ፡ ግዱፍ፡ በማ ለት፡ ፈንታ፡ ብኡስ፡ ይላል፤ አያሰኝም፡ (፪ነገ፡ ፲፱፡ ፲፱)።

**ብእሰት፤** መባስ፤ መክፋት፤ አባባስ፡ አከፋፍ፤ ብሶት፡ ችግር።

**ብእሲ፤ (ዕብ፡ ኢ፡ሽ)፤** ጕልማሳ፤ ኀይለኛ፡ ወጣት፤ የ፳፡ የ፴፡ ዓመት፡ ጕበዝ፤ ምሉ፡ ሰው፤ ባል፤ ተባት፡ ወንድ፤ ሰውነት። ተፈሣሕ፡ ኦ፡ ብእሲ፡ በውር ዙትከ። ወእመ፡ ኮንኩ፡ ብእሴ፡ ነሣእኩ፡ ብእሲተ። ኮነ፡ ብእሴ፡ ወተሰቅለ። ብእሲ፡ ምስለ፡ ብእሲቱ። ትወልድ፡ ወልደ፡ ብእሴ። እስመ፡ ወለደት፡ ብ እሴ። እብል፡ በእንተ፡ ብሉይ፡ ብእሲ፡ (መክ፲፩፡ ፱። ጦቢ፩፡ ፱። ጸሎ፡ ሃይ። ኤር፯፡ ፲፩። ፍ፡ ነ፡ ፳፱፡ ፮። ዮሐ፲፮፡ ፳፩። ኤፌ፬፡ ፳፬)።

**ብእሲሁ፤** ሰውዮው፤ ሰውነቱ፤ ይህ፡ ሰው፤ ያ፡ ሰው። ወሳምራዊ፡ ብእሲሁ። ብእሲ፡ ቅሡፍ። ብሉይ፡ ብእሲነ፡ (ኢሳ፶፫፡ ፫። ሮሜ፮፡ ፮)።

**ብእሲ፡ ብእሲ፤** ሰው፡ ኹሉ፤ አንዱም፡ አን ዱም፤ በየራሱ፡ (ዘፀ፲፮፡ ፳፱። ሕዝ፲፬፡ ፬። ዘሌ፲፫፡ ፪)።

**ብእሴ፡ እግዚ፤** ነቢይ፤ ሐዋርያ፤ ጻድቅ፤ ሰ ማዕት፤ ቅዱስ፡ (፩ነገ፡ ፱፡ ፮፡ ፲። ፩ጢሞ፡ ፮፡ ፲፩)።

**ብእሴ፡ ደም፤** ደም፡ አፍሳሽ፤ ነፍሰ፡ ገዳይ፤ ዐርበኛ፡ የጦር፡ ሰው፡ (መዝ፡ ፭)።

**ብእሴ፡ ሐቅል፤** በረኸኛ፤ ዐዳኝ፤ ወንበዴ፤ ሽፍታ፡ ወያኔ፡ (ዘፍ፳፭፡ ፳፯)።

**ብእሴ፡ ኀይል፤** ኀይለኛ፡ ጕልበታም፡ ባለአ እምሮ፡ (፫ነገ፡ ፩፡ ፵፪)።

**ብእሴ፡ ምድር፤** ዐራሽ፡ ገበሬ፤ ጃን፡ ገበር፤ የርሻ፡ ባለቤት፡ (ዘፍ፵፱፡ ፲፭)።

**ብእሴ፡ ዐመፃ፤** ዐመጠኛ፤ ዋሾ፤ ግፈኛ፤ ሐ ሳዊ፡ መሲሕ፡ (፪ተሰ፡ ፪፡ ፫)።

**ብእሴ፡ ፍትወት፤** መውደድ፡ መወደድ፡ ያ ለው፤ ሥልጡን፡ ስብቅል፡ (ዳን፲፡ ፲፩)።

**ብእሴ፡ ሰላም፤** ፍቅረኛ፤ ፍቅር፡ ወዳድ፤ አስ ታራቂ፡ (መዝ፡ ፴፯)። ብእሲ፤ በስም፡ በግብር፡ በዘር፡ በነባር፡ እየተናበበ፡ በዚህ፡ አምሳል፡ እንደ፡ ስልቱ፡ እንዳመጣጡ፡ ይፈታል።

**ብእሲት፤ (ዕብ፡ ኢ፡ሻ፤ ኢ፡ሽት)፤** ቈንጆ፤ ምሉ፡ ሴት፤ ሚስት። ብእሲት፡ ድንግል። ብእሲ፡ ወ ብእሲት። ብእሲተ፡ ብእሲ፡ (ዘሌ፳፩፡ ፲፫። ዘፀ፳፩፡ ፳፰። ዘዳ፳፭፡ ፲፯)።

**ብእሲታ፤** ይቺ፡ ሴት፤ ያቺ፡ ሴት፤ ሴቲቱ፤ ሴትዮይቱ፤ ሴቷ፡ ሴትነቷ። ምንት፡ ብእሲታ፡ (ሉቃ፯፡ ፴፱)።

**ብእሲቶ፤** የቅርብ፡ ሰሚ፡ ተጠሪ፤ አንቺ፡ ሴት፤ ሴቶ፤ እሜቶ፤ ወይዘሮ፡ (ዮሐ፪፡ ፬። ፬፡ ፳፩። ፳፡ ፲፫፡ ፲፭)። ብእሲና፡ ብእሲት፡ እንደ፡ ወርቅና፡ እንደ፡ ሐራ፡ ውስጠ፡ ብዙዎች፡ ስለ፡ ኾኑ፤ ግልጠ፡ ብዙነት፡ የላቸ ውም፤ ብእሲ፡ ከዕደው፤ ብእሲት፡ ከአንስት፡ ይገባሉ።

**አብአሰ፤** አባሰ፡ አከፋ፤ አስከፋ፤ አስጠላ።

**መብእስ፤ (ስት፡ ሳን፡ ሳት)፤** የሚያብስ፤ የ ሚያከፋ። ክፉ፡ መንገድ፤ ወጥ፡ ገብ፤ ሸካራ፡ ስንከል ካላ፤ ድንጉር። ይኩን፡ ዙሉ፡ መብእስ፡ መጽያሕተ፡ ርቱዐ። ኮነ፡ ፍናዊሁ፡ መብእሰ። የሐውሩ፡ መብ እሰ። መብእስ፡ እበኒሃ፡ ለፍኖተ፡ ኃጥኣን። ሀበኒ፡ ርእሶ፡ ለዮሐንስ፡ ጸያሔ፡ መብእስ፡ (ኢሳ፵፡ ፬። ሱቱ፡ ዕዝ፰፡ ፲፩። ኤር፯፡ ፳፰። ሚራ፳፩፡ ፲። ድጓ)።

**ተባአሰ፤** ተጣላ፤ ተጠላላ፤ ታገለ፡ ተጋደለ፤ ተ ሟገተ፡ ተከራከረ። ደቂቀ፡ እምየ፡ ተባአሱ፡ በእንቲ አየ። ተባአስ፡ በእንተ፡ ጽድቅ። ወተባአሱ፡ ይትመ የጡ፡ መንገለ፡ ምድር። ተባአሰ፡ ያድኅኖ፡ (ማ ሕ፩፡ ፮። ሚራ፬፡ ፳፰። ዮና፩፡ ፲፫። ዳን፮፡ ፲፱)። አ ገበረ፡ በማለት፡ ፈንታ፡ ተባአሰ፡ ይላል። ተባአሳ፡ ወአ ድከማ፡ (፪ነገ፡ ፲፫፡ ፲፱)።

**ባእስ፡ (ሳት)፤** ብርቱ፡ ጥል፤ ጠብ፤ ሙግት፤ ክርክር፤ ስድብ። ቦኑ፡ ባእሰ፡ ተባአሰ፡ ምስለ፡ እስራ ኤል። በባእስ፡ ወበዝንጓጌ፡ ይፌንዎሙ። ጋእዝ፡ ወባእስ፡ (መሳ፲፩፡ ፳፭። ኢሳ፳፯፡ ፰። ምሳ፲፯፡ ፲፱)።

**አስተባአሰ፤** አባባለ፤ አጣላ፡ አጠላላ፤ አሟ ገተ፡ አከራከረ። አባባስ፡ ማለት፡ ዐማርኛው፡ መነሾሉ፡ ይነካል። አስተባአሶሙ፡ በጽልእ። ዘያስተባእስ፡ ወዘያስተሳልም፡ በምንትኒ፡ ግብር፡ ኢይደልዎ፡

ከመ ፡ ይኩን ፡ ስምዐ ፡ በውእቱ ፡ ግብር ፡ (ዮሴፍ ። ፍ ፡ ን ፡ ፵፫ ፡ ፲፪) ።

**መስተባእስ** ፤ (ሳን) ፤ የሚያጣላ ፤ የሚጣላ ፤ ተጣይ ፤ ደመኛ ፤ ተዋጊ ፡ ዐርበኛ ። ኢ.ይኩኑ ፡ መስተባእሳነ ፡ በእኪይ ። መስተባእሳነ ፡ ሃይማኖት ። የዋሃን ፡ ይኩኑ ፡ መስተባእሳነ ፡ (ቀኖ ፡ ኒቅያ ። ቁር ፡ ገ፲፱ ። ዮሴፎ ፡ ፲፭ ። ኩፋ ፡ ፴፯) ።

**ቢስ** ፤ (ዐማርኛ ። ሱር ፡ ቢሳእ) ፤ በቁሙ ፤ ክፉ ፤ ንፉግ ፡ ጩቅ ፤ ቡዳ ፡ ባላይን ፡ ወርቅ ። ቢስ ፡ አይይኽ ፤ ቢስኛኽን ፡ ያርቅ ፤ ልበ ፡ ቢስ ፡ ቀልበ ፡ ቢስ ፡ እንዲሉ ።

## በአት ፤—መግባት ፤—በዊእ ፡ ቦአ ።

(ጥ) **በአት** ፤ –ዋሻ ፤ በዊእ ፡ ቦአ ፤ በአት ።

(ጥ) **በበ** ፤ (ደቂቅ ፡ አገባብ) ፤ በየ ፡ እየ ፤ ደጊመ ፡ ቃል ። ከተጸውዖ ፡ ስም ፡ በቀር ፡ በብትን ፡ ኹሉ ፡ እየገባ ፡ ይዘረዝራል ፤ ሲዘረዝር ፡ እንዳለ ፡ በቁሙ ፡ ይፈታል ፤ ባይዘረዝርም ፡ ተዘርዝሮ ፡ ወይም ፡ በደጊመ ፡ ቃል ፡ ይፈታል ። በበ ፡ ነገዱ ፡ ወበበ ፡ ዘመዱ ፤ በበ ፡ አሕዱ ፤ በየ ፡ እየ ። በበ ፡ ነግህ ፡ በበ ፡ ሠርክ ፡ ጧት ፡ ጧት ፡ ማታ ፡ ማታ ። በበ ፡ ዕለት ፤ በየለቱ ፡ ዕለት ፡ ዕለት ፤ ዘወትር ። በበ ፡ ወርኅ ፡ በበ ፡ ዓመት ፤ በበ ፡ በዓል ፤ በበ ፡ ሕቅ ፡ በበ ፡ ንስቲት ፡ እያለ ፡ እንደዚህ ፡ ይፈታል ። ነሥኡ ፡ በበ ፡ ዲናር ፤ ድሪም ፡ ድሪም ፤ አንዳንድ ፡ ድሪም ። ፈነዎሙ ፡ በበ ፡ ክልኤቱ ፤ ኹለት ፡ ኹለቱን ፡ ወይም ፡ ኹለት ፡ ኹለት ፡ አርጎ ። ወረፈቁ ፡ በበ ፡ ምእት ፡ ወበበ ፡ ኀምሳ ፤ ፻፻ው ፤ ፶፶ው ፤ ወይም ፡ ፻፻ና ፡ ፶፶ ፡ እየኾኑ ፡ ያሰኛል ። ለለንና ፡ ዘዘን ፡ ተመልከት ፤ የዚህ ፡ ጎር ፡ ናቸው ።

(ጥ) **ቡባ** ፤ (ዕብራ) ፤ አሻንጉሊት ፡ በወንድ ፡ ወይም ፡ በሴት ፡ ልጅ ፡ አምሳል ፡ የሚሠራ ፤ የልጅ ፡ የሕፃን ፡ መጫዎቻ ። ልጅን ፡ ና ፡ ልዘልኽ ፡ ሲሉ ፡ እንቡ ፡ እንቡቡ ፡ ማለት ፡ ከዚህ ፡ የወጣ ፡ ነው ።

(ላ) **ባባ** ፤ አያት ፤ ቅድም ፡ አያት ፤ አበ ፡ አበው ፤ የሮም ፡ ጳጳስ ፡ ፓፓ ፡ (ሐረርና ፡ ዐረብ) ። እንዳማርኛ ፡ ግን ፡ ጠብቆ ፡ ሲነገር ፤ አንቀጽ ፡ ኹኖ ፡ ባባ ፡ አባባ ፡ እያስኘ ፡ ፈሪንትንና ፡ ብቡንትን ፡ ያሳያል ።

**ባብ** ፤ (ዐረብ) ፤ በር ፤ ደጅ ፡ አፍ ፤ መዝጊያ ። ነደበን ፡ እይ ።

**ባባህ** ፤ (ዐረ ። ቅብጥ ፡ ፓዎፒ ፤ ፖፔ ፤ ፋዎፊ) ፤ ስመ ፡ ወርኅ ፤ የግብጦች ፡ ኹለተኛ ፡ ወር ፡ ጥቅምት ። ቃሉ ፡ የቅብጥ ፡ ፊደሉ ፡ የዐረብ ፡ ስለ ፡ ኾነ ፡ ፐ ፡ ለበ ፡ ተለውጧል ። ግበሩ ፡ በዓለ ፡ በመንፈቀ ፡ ባባህ ፡ (አቡሻ ፡ ፰) ። በዕብራይስጥ ፡ ግን ፡ ብንተ ፡ ዐይን ፡ ያይን ፡ ማሚቶ ፡ ብሌን ፡ ማለት ፡ ነው ።

**ባበየ** ፤ **ቤበየ** ፤ (ይቤቢ) ፤ ሠየ ፤ ጐመዠ ፤ ሮጠ ፡ ናወዘ ፤ ተቅበዘበዘ ፤ የዝሙት ። በበ ፡ ሠርክ ፡ ትቤቢ ፡ በውስተ ፡ ፍናዊሃ ፡ (ኤር፪ ፡ ፳፫) ። ዕብራይስጡ ፡ ግን ፡ ፈጣን ፡ ቀላል ፤ መንገዷ ፡ ቶታን ፡ የሚመስል ፡ ይላል ።

**ባቢክ** ፤ ፍሬ ፡ ዕፀ ፡ ገነት ፤ አዳም ፡ ይበላው ፡ የነበረ ፡ ወይም ፡ እንዳይበላው ፡ በትእዛዝ ፡ እሾክ ፡ የታጠረ ፤ ቢበሉት ፡ ቢያክ ፡ ቢያክ ፡ የሚያስኝ ፡ (ገድ ፡ አዳ) ።

**ባቢል** ፤ (ዐረ ፡ አባቢል) ፤ ስመ ፡ ያፍ ፤ የተረት ፡ ወፍ ፡ እንደ ፡ ፊንክስ ፡ ያለ ፤ በፍጥረታት ፡ ውስጥ ፡ የሌለ ፤ ያልነበረ ፡ ያልተፈጠረ ፤ ሙሐመዳውያን ፡ ሱር ፡ በሚባለው ፡ መጣፋቸው ፡ የሚያወሩት ፡ የሚናገሩት ፤ ወይም ፡ ባቢሎን ፡ ታመልከው ፡ የነበር ። አዕዋፈ ፡ ባቢል ፡ ዘውእቱ ፡ አጎርጋናት ፡ ሠለስቱ ፡ ምእት ፡ (አዋል) ።

**ባቤል** ፤ (ዕብራ ። ጽር ፡ ባቢሎን) ፤ ስመ ፡ ሀገር ፤ ቱሳሔ ፡ ኑሠት ፡ ሠጠት ፤ ድብልቅልቅ ፡ ዝብርቅርቅ ፤ ቅይጥ ፡ ውጥንቅጥ ፤ ቅልቅል ፡ ምስቅልቅል ፡ ማለት ፡ ነው ። ባለብሉዮች ፡ ግን ፡ ዝሩት ፡ መካነ ፡ ዝርወት ፡ እንተ ፡ ባቲ ፡ ተዘርዉ ፡ አበው ፡ ቀደምት ፡ ወተሌለዩ ፡ ልሳናት ፡ ይሉታል ፡ (ዘፍ፲ ፡ ፲ ። ፲፩ ፡ ፱) ። በእንተ ፡ ዝ ፡ ተሰምየት ፡ ዅላ ፡ ምድረ ፡ ሰናዖር ፡ ባቤል ፤ እስመ ፡ በህየ ፡ ሦጠ ፡ ዅሎ ፡ ልሳናቲሆሙ ፡ ለውሉደ ፡ ሰብእ ፡ (ኩፋ ፡ ፲) ። ኹለተኛም ፡ ናቡከደነጾር ፡ የቀድሞ ፡ ስሟን ፡ ለማደስና ፡ ለማወፈር ፡ በቀድሞው ፡ ግንብ ፡ አምሳል ፡ ኹለተኛ ፡ ግንብ ፡ እንደ ፡ መሥራት ፤ ወርዱ ፡ ደረቱ ፡ ፯ ፡ ክንድ ፤ ቁመቱ ፤ ፰ ፡ ክንድ ፡ የኾነ ፡ ወፍራም ፡ ረዥም ፡ ሰማይ ፡ ጠቀስ ፤ ስሙ ፡ ከስሟ ፡ የተስማማ ፡ ቤል ፡ የሚባል ፡ ጣዖት ፡ ስላቆመበት ፤ ባቤልን ፡ ባ ፡ ቤል ፤ ባቲ ፡ ቤል ፤ ቤተ ፡ ቤል ፡ መካነ ፡ ቤል ። (ባብ ፡ ቤል) ፡ አንቀጸ ፡ ቤል ፡ ማዕጸ ፡ ቤል ፡ ብለው ፡ ፪ ፡ ቃል ፡ አድርገው ፡ ይፈቱታል ፡ (ዳን፫ ፡ ፩ ። ኢሳ፵፯ ፡ ፩) ።

**ባበለ** ፤ ተቀላቀለ ፤ ተዘባረቀ ። ተዘራ ፡ ተበተነ ። በባበለም ፡ ፈንታ ፡ በልበለ ፡ ይላል ፤ ፍችው ፡ ፩ ፡ ነው ። ወተሰምየ ፡ ውእቱ ፡ መካን ፡ ባቢሎን ፡ እስመ ፡ ባቲ ፡ ተበልበሉ ፡ ልሳናት ፡ (ጊ ፡ ወ ፡ ሐ ፡ ገ፲፫) ።

**ባቢሎሳን** ፤ ቱሱሓን ፤ ኅዉማን ፡ ዝርዋን ። አባቢሎሳን ፡ (ዲድ) ።

**አባበለ** ፤ ቀላቀለ ፤ ደባለቀ ፤ ዘባረቀ ። በቁሙ ፡ አባበለ ፡ አሸበለበለ ፤ አቄላመጠ ። መጽሐፍ ፡ ግን ፡ በአ ፡ ፈንታ ፡ ሀ ፡ ይላል ። ሀባባሊ ፡ ለዝሙት ፡ (ፈ ፡ መ ፡ ፳፱ ፡ ፩) ።

**ባቡት** ፤ ዔሊ ፡ ደንጊያ ፡ ልብሱ ፤ ሽልምልም ።

**ባቡቴ** ፤ ክብ ፡ እንክብል ፡ ኅብስት ፡ ሴቶች ፡ በዔሊ ፡ አምሳል ፡ የሚጋግሩት ፤ ይልቁንም ፡ የቡልጋ ፡ ሰዎች ፡ ለሙታን ፡ መክፈልት ፡ የሚያደርጉት ። ዳቦ ፡ ድፎ ፡ ንብሩቴ ፤ ፵ ፡ ባቡቴ ፡ እንዲሉ ።

**በገነ** ፤ (ዕብ ፡ ናጌን) ፤ ቃኘ ፡ ነዘረ ፤ መታ ፡ ደረደረ ፤ የንዋየ ፡ ማሕሌት ። ሲጠብቅ ፡ ግን ፡ ነደደ ፡ ተቈጣ ፡ ያሰኛል ።

**በገና** ፤ በቁሙ ፤ መዝሙር ፡ (ዐማርኛ) ።

**በገን** ፤ (ትግሬ) ፤ ጩብጥ ፤ የሽንት ፡ ምጥ ። ፀበጠን ፡ ተመልከት ።

**በግዖ፤ዖት፤(በግዐ፡ይቤግዕ፡ይበግዕ)፤** በጋ፡ መንጋ፡ መኾን፡ መንጋጋት፡ ወደ፡ ወስዱት፡ መኼድ፡ መነዳት። በጋ፡ የጊዜ፡ የወራት፤ መንጋ፡ የሰው፡ የከብት። ምስጢሩ፡ ግን፡ በጎነትና፡ ቅንነት፡ መሥዋዕትነት፤ እንደ፡ ይሥሐቅ፡ እንደ፡ ዮፍታሔ፡ ልጅ።

**በግዕ፤(ዕት። ዕብ፡ ባግ)፤** የምግብ፡ ክፍል፤ ዕድል፡ ፈንታ፡ ድርሻ፡ መቀነን፡ ድርጎ። በቁሙ፡ ተባት፡ በግ፤ የክርስቶስና፡ የውነተኛ፡ ክርስቲያን፡ ምሳሌ፤ በጎ፡ ማለት፡ ከዚህ፡ ወጥቷል። በግዐ፡ ዘተኀጥአ። ወመጽአ፡ ይጠባሕ፡ ከመ፡ በግዕ። አሕቲ፡ በግዕት፡ (ኢሳ፶፫፡ ፲፩። ፶፫፤ ፯። ሕዝ፵፭፡ ፲፭። ፍ፡ ነ፡ ፴)።

**አባግዕ፤(ዕት፡ ዓት)፤** በቁሙ፤ በጎች፤ የበግ፡ መንጎች፡ ተባቱም፡ እንስቱም፤ ወይም፡ ተባቶች፡ ብቻ። አባግዐ፡ ወአጣሊ። አባግዕ፡ ወአባግዕት፡ (አዋል)። አባግዓት፡ የብዙ፡ ብዙ። አባግዐ፡ አትቡዕ። አባግዕ፡ አንስት። በግዕት፡ አንስት፡ እያለ፡ ይጥፋል፡ የተሳሳተ፡ ነው፡ (፪ዜና፡ ፲፯፡ ፲፩። ዘኍ፯፡ ፲፯። ዘሌ፭፡ ፮)።



አባግዕ፡

ምእመናንም፡ በሥራቸውና፡ ኖላዊያቸው፡ ሳይቀር፡ በምሳሌ፡ በጎች፡ ይባላሉ፡ (ዮሐ፲፡ ፳፱፡ ፴፯። ፲፡ ፯፡ ፰። ፳፩፡ ፲፯። ማቴ፲፡ ፮። ፲፭፡ ፳፬)። መላእክትም፡ በሥራቸው፡ ዳግማይ፡ አዳም፡ ስለ፡ ኾነ፡ እንደ፡ ምእመናን፡ በጎች፡ ይባላሉ፡ (ማቴ፲፰፡ ፲፪። ሉቃ፲፭፡ ፬)።

**በጊር፤ሮት፤(በገረ፡ ይበግር፡ ይብግር። ዕብ፡ ባጋር)፤** ማደግ፡ መጐልመስ፤ ከልጅነት፡ ወዳዋቂነት፡ መውጣት፤ ከታላላቆች፡ መጨመር፤ ዐብሮ፡ መቈጠር፤ አቶ፡ እንጌ፡ መባል። በቁሙ፡ መበገር፤ መሞከር፤ መንደፍ፤ የሥዕል። ብግር፡ ማውጣት፤ ብግራም፡ መኾን። ብግር፡ ፪፡ ወገን፡ ነው፤ የውርዛዌና፡ የደዌ።

**ባጎር፤** ጕበዝ፡ ጕልማሳ፤ ብግራም፤ ሕፃንነቱን፡ የጨረሰ፡ አካለ፡ መጠን፡ ያደረሰ፤ ባለአእምሮ፤ የ፲፭፤ ዓመት፡ ልጅ፡ ወይም፡ የሚበልጥ። ጥበበ፡ ባጎር፡ ወልደ፡ ብዙ፡ (ጥበ፡ ፭)። ባጎር፡ ሰሎሞን፤ ብዙ፡ ዳዊት።

**ብዱ፤(ዐረ፡ ቤዳ)፤** ነጭ፤ ንጣቱ፡ ዕንቍላል፡ ዐመድ፡ ወይም፡ ያህያ፡ ሆድ፡ የሚመስል። ሕብረ፡ ከብድ፡ ባለው፡ ብዱ፡ ይላል። ባለብሎዮች፡ ግን፡ ብጫ፡ ይሉታል፡ (ዘፀ፴፯፡ ፱)።

**በድበደ፤(በድወ። ዐረ፡ ባደ)፤** ታመመ፤ ሞተ፤ ጠፋ፡ ተበላሸ፤ ዛገ፡ መረተ። ወርቀሙኒ፡ በድበደ፡ (ሆሴ፱፡ ፮)፡ አብደን፡ ተመልከት፤ የዚህ፡ ጎር፡ ነው። ትግሬ፡ ግን፡ በድበደ፡ ብሎ፡ ሰደበ፡ አዋረደ፡ ይላል።

**ብድብድ፤** ዛሕል፡ ዝገት። ሞተ፡ ግብት፤ ቸነፈር፤ መቅሠፍት፤ ሰውነትን፡ ቶሎ፡ የሚያዝግ፡ የሚያጠወልግ፤ ፈጥኖ፡ የሚገድል፤ እንደ፡ ነፍጥ፡ ያለ፡ በሽታ። ባለወግ፡ መልአክ፡ ለመፀት፡ ለመቅሠፍት፡ የሚላክ፤ አጥፊ፡ ቀሣፊ። ክፉ፡ ጨካኝ፡ ንጉሥ፤ እንደ፡ ሄሮድስ፡ እንደ፡ ቴዎድሮስ፡ ያለ፡ (ዘኍ፲፯፡ ፲፪—፲፭። ፪ነገ፡ ፳፬፡ ፲፭—፲፯። ዕብ፲፩፡ ፳፰)። ወአውሥእዎ፡ ለውእቱ፡ ብድብድ፡ ንጉሥ። ጕጉእ፡ ወመግእዝ፡ ወነባቢ፡ ብድብድ፡ ስሙ፡ (መቃ፡ ገ፭። ምሳ፳፭፡ ፳፱)።

**አበድበደ፤** አዛገ፡ አሳደፈ፤ ገደለ፡ ቀሠፈ።

**አንበድበደ፤** በቁሙ፡ አስፈራ፤ አንቀጠቀጠ። ፈራ፡ ተንበደበደ።

**እንብድቡድ፤** ፈሪ፡ በድባዳ።

**አበድቢድ፤—ሞኝ፡ ሰነፍ፤—አቢድ፡ አብደ።**

**በዲድ፤ዶት፤(በደ፤በደደ፡ይበድድ፡ ይብድድ። ዕብ፡ ባዳድ)፤** ለየ፡ ነጠለ፤ ብቻ፡ አስቀረ፤ ብቸኛ፡ አደረገ። በድበደ፡ በዲድ፡ በደ፡ ከለው፡ የወጣ፡ ነው። (ዲቃላ፡ ግስ)።

**በደዶ፤** ፈንጣጣ፤ ኵፍኝ፤ ልዩ፡ ብቸኛ፡ በሽታ፤ የሚገድል፡ የሚያቈስል፤ ፊት፡ የሚነቍር፡ ዐይን፡ የሚያሳውር፡ የዕከክ፡ ዐይነት። ሕማመ፡ በደዶ፡ (አዋል)።

**በዲው፤ ዎት፤(በድወ፡ ይበዱ፡ ይብዱ። ትግ፡ በድዐ፤ በዳ)።** መውደም፤ መጥፋት፡ መፈታት፤ መፍረስ፡ መደምሰስ፤ ውድማ፡ በረሓ፡ ባድ፡ ባድማ፡ ምድረ፡ በዳ፡ መኾን፤ ያገር፡ የመዲና፡ የድንግልና። ምድርክሙኒ፡ በድወ። በድወት፡ ኢየሩሳሌም። ንኅለት፡ ወበድወት። አብያቲሆሙ፡ በድዋ፡ ወተመዝበሩ፡ (ኢሳ፩፡ ፯። ፳፬፡ ፲። ስንክ፡ የካ፩። አቡሻ፡ ፶)።

**ብድው፤(ዋን፡ ዋት፡ ዱት)፤** የጠፋ፡ የወደመ፤ ባድ፡ ባድማ፡ የኾነ፤ የተፈታ። ምድር፡ ብዱት። ገዳም፡ ብዱት፡ (ዮሴፍ። ስንክ፡ መስ፫)።

**ብድወት፤** መጥፋት፡ መፈታት፤ ውድማነት፡ ባድነት። ኢይርአይ፡ ብድወታ፡ ለኢየሩሳሌም፡ (ስንክ፡ ሚያ፫)።

**በድው፤** ምድረ፡ በዳ፤ ውድማ፡ ባድማ፤ ደረቅ፡ በረሓ፤ ባድ። በድወ፡ ፋራን። በምድረ፡ በድው፡ ኀበ፡ አልቦ፡ ዕፀ፡ ወማይ። ባሕር፡ በድወ፡ ይመስሎ። በድወ፡ ትከውን፡ ሖላ፡ ምድር። በድው፡ ውእቱ፡ እምሰብእ፡ ወእንስሳ፡ (ኍል፡ ፲፯። መዝ፡ ፳፱። ኢዮ፴፩፡ ፳፰። ኤር፱፡ ፳፯። ፵፡ ፲)።

**በዳ፤** ዝኒ፡ ከማሁ። ኢትሑር፡ ፍኖተ፡ በዳ። ትከውን፡ ምድረ፡ ግብጽ፡ በዳ፡ ወበድወ፡ (ሚራ፴፭፡ ፳። ሕዝ፳፱፡ ፱)።

(ጥ) » **ዳዋ ፤ (ዐማርኛ) ፤** ዝኒ ፡ ዓዲ ፡ ከማሁ ፤ በቁሙ ፡ ዱር ፡ ጥሻ ፡ ጣሻ ። (ተረት) ፤ ዐይጥ ፡ በበላ ፡ ዳዋ ፡ ተመታ ።

**አብደወ ፤** አጠፋ ፤ አስጠፋ ፤ አወደመ ፡ ባይ ፡ አደረገ ። አብደወ ፡ ሀገሮሙ ። ኣበዱ ፡ ፍኖቶሙ ። እሁቦን ፡ ለአብድዎ ፡ ከመ ፡ አልቦ ፡ ዘይነብሮን ፡ (ዮሴፍ ። ሶፎ፫ ፡ ፮ ። ኤር፵፩ ፡ ፳፱) ።

**ተባደወ ፤** ተለያየ ፤ ተበታተነ ፤ ተዘሬ ፡ ተረጨ ፤ በየበረሓው ፡ ተሠራጨ ። እምኍየሰኒ ፡ ተባድዎ ፡ እምኒ ፡ ተጋብኦ ፡ በእንግልጋ ፤ እስመ ፡ ተዘርዎ ፡ ቀጥቀጠ ፡ አልባቢነ ፤ ወሶበ ፡ አድኅነነ ፡ እግዚ ፡ እምተባድዎ ፡ ወአግብአነ ፡ ውስተ ፡ ምድርነ ፡ ዐመፀናሁ ። ይበኪ ፡ ባዕለ ፡ ሙስናሆሙ ፡ ወተባድዎቶሙ ፡ (ዮሴፍ) ።

**በደለ ፤ (ትግሬ ፡ ወዐረ) ፤** ለወጠ ፤ ቀየረ ። (ዐማርኛ) ፡ በቁሙ ፤ በደለኛ ፡ ኾነ ፤ በመልካም ፡ ፈንታ ፡ ክፉ ፡ ሠራ ። ምስጢሩ ፡ ከዚያው ፡ ይገባል ።

**በዲን ፤ ኖት ፤ (በድነ ፤ በደነ ፡ ይበድን ፡ ይብድን) ፤** መብደን ፡ መፍዘዝ ፤ መሞት ፡ መገንዝ ፤ ሬሳ ፡ መኾን ፤ መግማት ፡ መበስበስ ፤ መፍረስ ። ሥጋ ፡ ትበድን ፡ በንዋም ፡ ከመ ፡ ዘምዉት ። ነፍስት ፡ አመ ፡ ፀአተ ፡ ነፍስ ፡ ይበድን ፡ (መጽ ፡ ምስ) ።

**በድን ፤ (ብ ፡ አብድንት) ፤** በቁሙ ፤ ሙት ፡ ሬሳ ፤ ነፍስ ፡ የተለየችው ፡ የማይላወስ ፡ የማይንቀሳቀስ ፤ የፈዘዘ ፡ የተገነዘ ፡ ባይ ፡ ሥጋ ፤ አስከሬን ። ዘአንሥአ ፡ በድነ ፡ እምነ ፡ ሙታን ። መዊቶሂ ፡ ተነበየ ፡ በድኑ ። አልቦ ፡ ቤት ፡ ዘአልቦ ፡ በድን ፡ ውስቴታ ። በዝኃ ፡ አብድንቲሆሙ ። ወተንሥኡ ፡ ብዙኃን ፡ አብድንቲሆሙ ፡ ለጻድቃን ፡ (ሚራ፴፰ ፡ ፩ ፡ ፲፫ ። ኩፋ ፡ ፵፱ ። ኢሳ፩ ፡ ፲፫ ። ማቴ፳፯ ፡ ፶፪) ።

**አብደነ ፤** አበደነ ፡ አፈዘዘ ፤ ሬሳ ፡ አደረገ ።

**አበደን ፤ (ዐረብ) ፤** ግሙራ ፤ መቼም ፡ መች ፤ ፈጽሞ ፡ ጭራሽ ።

**ቢዶን ፤ (ዕብ ፡ ኪዶን ። ጽር ፡ ጋይሶ) ፤** ጦር ፡ ዘገር ፤ ረምሕ ፤ የሚወረወር ፡ ዐጭር ፡ መጠነኛ ። ባለብሉዮች ፡ ግን ፡ ፩ ፡ ገጽ ፡ ያለው ፡ የብረት ፡ በሎታ ፤ መድፍ ፡ ነፍጥ ፡ በድል ፡ ነጐድ ፡ ይሉታል ፡ (ኤር፶ ፡ ፵፪) ። በዕብራይስጥ ፡ ቤትና ፡ ካፍ ፡ ተመሳሳዮች ፡ ስለ ፡ ኾኑ ፡ በኪ ፡ ፈንታ ፡ ቢ ፡ ተጽፏል ።

**በዲቅ ፤ (በደቀ ። ዕብ ፡ ባዳቅ) ፤** ማደስ ፡ መጠገን ። እስከ ፡ ማእዜኑ ፡ ኢትቤድቁ ፡ ቤተ ፡ ለእግዚ ፡ (ጊ ፡ ወ ፡ ሐ ፡ ገ፺) ።

**ቤዴቅ ፤ (ዕብራ) ፤** የማንብ ፡ ንቃቃት ፤ ነቁ ፡ ሥንጥቁ ፤ ወይም ፡ ሊናድ ፡ የቀረበ ፤ ያረገዘ ፡ ያዘበዘበ ፡ የቤት ፡ ግንብ ። ያጥር ፡ የቅጥር ፡ ካብ ። ማናቸውም ፡ የሚታደስና ፡ የሚጠገን ፡ ኹሉ ። ወያጸንዑ ፡ ቤዴቀኪ ፡ (ሕዝ፳፯ ፡ ፱ ። ፬ነገ ፡ ፲፪ ፡ ፭) ።

**በዲር ፤ ሮት ፤ (በደረ ፡ ይበድር ፡ ይብድር ። ዐረ ፡ በደረ ፤ ቄረጠ ። ዕብ ፡ ባዴር ፤ በተነ) ፤** መሮጥ ፤ መፍጠን ፤ መንገድን ፡ በሩጫ ፡ መቀረጥ ። ከዚህ ፡ የተነሣ ፡ መቅደም ፤ ዐልፎ ፡ መኼድ ፤ ፊተኛ ፡ መኾን ። ይበድሩ ፡ እምተሐላተ ፡ ዐረብ ። ይበድሩ ፡ እምአንስርት ፡ አፍራሲሆሙ ። ከመ ፡ ይብድር ፡ እምረዋጺ ፤ ሮጠ ፡ ፈጠነ ፡ (ዕንባ፩ ፡ ፰ ። ኤር፬ ፡ ፲፫ ። ቅዳ ፡ ዮሐ) ። ሕቀ ፡ በደሩክሙ ። ትበድር ፡ ይእቲ ፡ ወትመውእ ፡ ለከ ፡ ጸላኢከ ። ብድሮሙ ፡ ተንሥእ ። ይበድረኒ ፡ ኀበ ፡ ገነት ። በደሮ ፡ ለጴጥሮስ ፡ በጺሐ ፡ ኀበ ፡ መቃብር ፤ ቀደመ ፡ (፪ነገ ፡ ፲፯ ፡ ፰ ። ሢራ፳፱ ፡ ፲፫ ። ፴፬ ፡ ፳፩ ። ፊልክ ፡ ፫ ። ዮሐ፳ ፡ ፬) ።

—፤ ማበደር ፡ ማለቃት ፤ አስቀድሞ ፡ መስጠት ፡ ኋላ ፡ ለመቀበል ፡ (ዐማርኛ) ።

—፤ መውደድ ፤ መምረጥ ፤ ማክበር ፡ ማብለጥ ። ኢኮነ ፡ ለዘበደረ ፡ ወለዘሮጸ ፡ (ሮሜ፱ ፡ ፲፮) ። መጽሐፍ ፡ ግን ፡ በበደረ ፡ ፈንታ ፡ አብደረ ፡ ይላል ፤ አያስኼም ። እመ ፡ አብደሩ ፡ ዘአነ ፡ እፈቅድ ። ምጽዋተ ፡ ኣበድር ፡ እመሥዋዕት ። አብደሩ ፡ ሞተ ፡ እምሕይወት ። አብደረ ፡ ይሕምም ፡ ምስለ ፡ ሕዝቡ ። ዘያበድር ፡ ርእሶ ፡ እምነ ፡ እግዚኡ ። እስመ ፡ ኅረየ ፡ እግዚ ፡ ወአብደራ ፡ (ኢሳ፶፮ ፡ ፬ ። ሆሴ፮ ፡ ፮ ። ኤር ፡ ፰ ፡ ፫ ። ዕብ፲፩ ፡ ፳፭ ። ዲድ ፡ ፳፭ ። መዝ ፡ ፻፴፩) ።

**በዳሪ ፤ (ሪት ፤ ርያን ፡ ያት ፤ በደርት) ፤** የሚሮጥ ፤ የሚቀድም ፤ ሯጭ ፤ መንገድ ፡ ቈራጭ ።

**በድር ፤** ቅድድም ፤ ፍክክር ፤ ሩጫ ፡ ፍጥነት ፤ መልካም ፡ ሥራ ፤ ገድል ፡ ትሩፋት ። በድርየኒ ፡ ፈጸምኩ ። ፈጸመ ፡ በድሮ ፡ ሠናየ ። (፪ጢሞ ፡ ፬ ፡ ፯ ። ስንክ ፡ ታኅ፲፱ ። ጥር፲፬ ፡ ፳ ። የካ፱ ። ግን፱) ።

—፤ የጾመ ፡ አይሁድ ፡ ድሮ ፡ ቅበላ ፤ ጹመው ፡ ከሚውሉበት ፡ ከጾማቸው ፡ ቀን ፡ የሚቀድም ፤ ዋዜማ ፡ ድራር ፡ ማታ ፡ የሚዠመር ። ይኸውም ፡ የጥቅምት ፡ ጨረቃ ፡ በበቀለች ፡ በ፱ ፡ ቀን ፡ ነው ፡ (ዘሌ፳፫ ፡ ፳፯—፴፪) ። ወጾመ ፡ በድሮሙ ፡ በእንተ ፡ ባሐ ፡ ያዕቆብ ፡ (መጽ ፡ ምስ) ።

**በድራ ፤ (ዐረ ፡ በድረት) ፤** ሚዛን ፤ የሚዛን ፡ ስም ። ቍጥሩና ፡ ልኩ ፡ በየሀገሩ ፡ ይለያያል ፤ እልፍ ፡ ድሪም ፤ ሺሕ ፡ ድሪም ፤ ፯ ፡ ሺሕ ፡ ይሉታል ፤ ርግጡ ፡ አልተገኘም ። ፯ ፡ ሺሕ ፡ ማለት ፡ ይለያል ፡ እንጂ ፡ ሺሕ ፡ ማለትና ፡ እልፍ ፡ ማለት ፡ ሊታረቅ ፡ ይችላል ፤ እልፍን ፡ ተመልከት ። ኹለተኛም ፤ በድራ ፡ ማለት ፤ ብድር ፡ ከማለት ፡ ይስማማል ። ወወሀቦሙ ፡ ሠለስተ ፡ ምእተ ፡ በድራ ፡ ወርቀ ፡ (ዮሴፍ) ።

**ቡዲር ፤ (ትግሬ) ፤** ዱሮ ፡ ቀድሞ ፤ ጥንት ፤ ከኹሉ ፡ በፊት ።

**አብደረ ፤ (አስደራጊ) ፤** አስሮጠ ፡ አስቀደመ ። አስተጋይድ ፡ ፈረስከ ፡ ወአብድር ፡ እምዐውሎ ፡ (ደፉሲ) ። አሶደደ ፡ አስመረጠ አስከበረ ፡ አስበ

ለጠ ። ልማዱ ፡ ግን ፡ አድራጊነት ፡ ነው ፤ መንገዱ ፡ እንደ ፡ አእመረ ፡ ተሳስቷል ።

**ተበድረ** ፤ ተቀደመ ። ተወደደ ፤ ተመረጠ ፤ ከበረ ፡ በለጠ ። ይትበደር ፡ ቃል ፡ ሠናይ ፡ እምውሂብ ። ኢይትበደር ፡ ብዕል ፡ እምነቢረ ፡ ጥዑይ ። ይትበደር ፡ ሰብእ ፡ እምዕንቊ ፡ ሰንፔር ፡ ክቡር ፤ እምወርቅ ፡ ወእምብሩር ፡ ይትበደሩ ፡ ጻድቃን ። ጥበብ ፡ ትትበደር ፡ እምወርቅ ፡ (ሢራ ፲፰ ፡ ፲፯ ። ፴ ፡ ፲፮ ። ድጓ ። ፈላስ) ።

—፤ በቁሙ ፤ ተበደረ ፡ ተለቃ ። ተበድሬ ፡ ተቀድሜ ፡ እንዲሉ ።

**ብዱር** ፤ (ራን ፡ ራት ፡ ድርት) ፤ የተበደረ ፤ የተቀደመ ፤ የተወደደ ፤ ምርጥ ።

**ተባደረ** ፤ ተሯሯጠ ፤ ተሽቀዳደመ ፤ ተፈካከረ ። እስመ ፡ ይትባደሩ ፡ ውስተ ፡ ርእሰ ፡ ምርፋቅ ። ተባደሩ ፡ ለሠናይ ። ዘንተ ፡ ስምዑ ፡ ወተባደሩ ፡ ከመ ፡ ትግበሩ ። እለ ፡ ፈጸሙ ፡ ረዊጸ ፡ ወተባድሮ ፡ (ሉቃ ፲፱ ፡ ፯ ። ፩ተሰ ፡ ፩ ፡ ፲፩ ። ቀሌ ። ስንክ ፡ ታኅ፲፪) ።

**አስተባደረ** ፤ አቀዳደመ ፤ አሽቀዳደመ ፤ አፈራረቀ ፤ የፈረስ ፡ የእግር ። አምጣነ ፡ ጊዜ ፡ ሠርከ ፡ ንረውጽ ፡ እንዘ ፡ ናስተባድር ፡ እግረ ፤ እክል ፡ ኀበ ፡ ሀሎ ፡ ወላሕም ፡ ኀበ ፡ ሖረ ፡ (ቅኔ) ።

**ባዶስ** ፤ (ጽር ፡ ባቶስ ። ዕብ ፡ ባት) ፤ የልክ ፡ የመስፈሪያ ፡ ስም ፤ የርጥብ ፡ መስፈሪያ ፤ የዘይት ፡ ገንቦ ። ምእተ ፡ በመስፈርተ ፡ ባዶስ ፡ ቅብዐ ፡ (ሉቃ ፲፮ ፡ ፮) ። መስፈሪያነቱም ፡ የሖሜርን ፡ ፲ኛ ፡ ክፍል ፡ ያኸማል ፤ የባትና ፡ የኢፍ ፡ ልካቸው ፡ አንድ ፡ ነውና ፤ ኢፍን ፡ ተመልከት ፡ (ሕዝ፵፭ ፡ ፲፩) ። ከዚህ ፡ የተነሣ ፡ ባዶስን ፡ ቤድ ፡ ላዳን ፡ የቤት ፡ ቊና ፡ ይሉታል ፤ ቤድ ፡ የወሎ ፡ የተንታ ፡ የደላንታ ፡ ነው ። ወአሐቲ ፡ አስፈሬዳ ፡ ታገምር ፡ አርባዕተ ፡ ባዶስ ፡ (ገድ ፡ ተክ) ።

**ብዱት** ፤—የተፈታች ፡ ባዶ ፤—በድወ ።

**ቦሁ ፤ ቦኑ** ፤ (ቦ ፡ ሁ ፤ ቦ ፡ ኑ) ፤ ቦ ፡ ነባር ፡ አንቀጽ ፤ ሁ ፡ ኑ ፡ የጥያቄ ፡ ቃል ፤ በተገናኝ ፡ አለን ፤ አለ ፡ ይኾን ፡ ያሰኛል ። ቦሁ ፡ ኀበ ፡ ይቤወሩ ፡ እምኔየ ። ቦሁ ፡ ዘተርፈ ፡ ኀቤከ ። ቦኑ ፡ ረአይ ፡ ዝየ ፤ እወ ፡ ቦ ፡ (ኤር፳፫ ፡ ፳፱ ። ዓሞ፮ ፡ ፲ ። ፩ነገ ፡ ፱ ፡ ፲፩) ። ኹለተኛም ፡ በትርፍ ፡ ዐማርኛ ፡ በውኑ ፤ እውን ፡ እያሰኘ ፡ ጥያቄን ፡ መደብ ፡ አድርጎ ፡ ምርመራን ፡ ወቀሣን ፡ ተግሣጽን ፡ ያሳያል ። ትርፍ ፡ ዐማርኛ ፡ ማለት ፤ ቦ ፡ አንቀጽነቱን ፡ ሳይለቅ ፤ ቦሁ ፡ ዘበአልኩክሙ ፤ ቦኑ ፡ ዘዐመፅኩክሙ ፡ እያለ ፡ ይህን ፡ በመሰለ ፡ ሲገባ ፤ በውኑ ፡ የለመንኋችኹ ፡ የበደልኋችኹ ፡ አለን ፡ ያሰኛልና ፤ ስለዚህ ፡ ነው ። አንቀጹ ፡ ሌላ ፡ ሲኾን ፡ ግን ፡ ፍችው ፡ በውኑ ፡ ብቻ ፡ ነው ፤ ስለዚህ ፡ በጥያቄ ፡ ኹሉ ፡ ይገባል ፤ በውኑ ፡ ማለት ፡ ርሱው ፡ ራሱ ፡ ጥያቄ ፡ ነውና ። ቦኑ ፡ በአትፈይት ፡ ውእቱ ፡ ቤትየ ። ቦኑ ፡ ለባሕቲትሙ ፡ ለአይሁድ ፡ እግዚ ። ቦኑ ፡ አባእክሙ ፡ ሊተ ፡ መሥዋዕተ ፡ ወቍርባነ ። ዘአባእክሙ ፡ ቢል ፡ ግን ፡ አለን ፡ ያሰኛል ፤ በውኑ ፡ ሲጨመር ፡ ያምርለታል ፡ (ኤር፯ ፡ ፲፩ ። ሮሜ፫ ፡ ፳፱ ። ግብ፯ ፡ ፵፪) ።

**ብሂል** ፤ ሎት ፤ (ብህለ ፡ ይብል ፡ ይብሀል ። ዐረ ፡ በሀለ ፤ ተረገመ ። ዕብ ፡ ባሄል ፤ ደነገጠ) ፤ አው ፡

**በዪል** ፤ ሎት ፤ (ቤለ ፡ ይበይል ፡ ይቢል ፤ ወይም ፡ ቤለ ፡ ይቤ ፡ ይበል ። ዐረ ፡ ቃል ። ዕብ ፡ ንኡም ፤ አማር) ፤ ማለት ፤ መንገር ፡ መናገር ፤ ፍሬ ፡ ቃል ፡ መስጠት ፡ ማስማት ፤ በአፍ ፡ በመጽሐፍ ፡ መንበብ ፤ ማንበብ ። ብሂል ፡ ፪ ፡ ነገር ፡ ይኾናል ፤ አንቀጽና ፡ አገባብ ። በአንቀጽነቱ ፡ አንቀጽ ፡ ይሰባል ፤ ስም ፡ ይተረጐማል ። ባገባብነቱ ፡ ማሰሪያ ፡ ያስቀራል ፤ አገባቡን ፡ ባገባብ ፡ ተመልከት ። ብሂለ ፡ ይብሉ ። እስመ ፡ ጼዴቅ ፡ ብሂል ፡ ጽድቅ ፡ ብሂል ። ብህለ ፡ ካልእ ፤ በከመ ፡ ብህልከ ። ዘብህልዎ ፡ አበዊነ ። ከዊነ ፡ ውሳጤ ፡ ዘብህሎ ፡ ቅዱስ ፡ አባ ፡ ወግሪስ ። እሳት ፡ እንተ ፡ ብህላ ፡ እግዚእነ ፡ (ኤር፴፰ ፡ ፳፪ ። አፈ ፡ ድ፲፱ ። አዋል ። አረጋ) ። መሐለን ፡ እይ ፡ የዚህ ፡ መንቲያ ፡ ነው ። የብህለና ፡ የክህለ ፡ አካኼድ ፡ አንድ ፡ ስለ ፡ ኾነ ፡ ሀ ፡ በካልኣያቸው ፡ እየታጣ ፡ በሣልሳያቸው ፡ ይገኛል ፤ ባላገባቦች ፡ ግን ፡ ብህለን ፡ ከክህለ ፡ ለይተው ፡ ይብህል ፡ ይሉታል ፤ አያሰኝም ። ፪ኛም ፡ በበዪል ፡ አካኼድ ፡ እንደ ፡ ሐባብና ፡ እንዳርጌው ፡ ግእዝ ፤ ቤለ ፡ ይበይል ፡ ይቢል ፤ ወይም ፡ ቤለ ፡ ይቤ ፡ ይበል ፡ በማለት ፡ ፈንታ ፡ ብህለንና ፡ ቤለን ፡ አዛንቀው ፤ ቤለን ፡ አውጥተው ፡ በርሱ ፡ ፈንታ ፡ ይቤን ፡ አግብተው ፤ የብህለን ፡ ካልኣይ ፡ ይብልን ፡ ለይቤ ፡ ሰጥተው ፤ ይቤ ፡ ይብል ፡ ይበል ፡ እያሉ ፡ አለመንገዱ ፡ ያረቡታል ። መጻሕፍትም ፡ ከዚህ ፡ የተነሣ ፡ በቤለ ፡ ፈንታ ፡ ይቤ ፡ ይብል ፡ ይበል ፡ ሲሉ ፡ እንጂ ፤ በብሂል ፡ አካኼድ ፡ ብህለ ፡ ብለው ፤ ይብህል ፡ ሲሉ ፡ አይገኙም ። ሀሎ ፡ የሀለወ ፡ ክፋይ ፡ መንቲያው ፡ ወንድሙ ፡ እንደ ፡ ኾነ ፤ ይቤም ፡ ከበዪል ፡ የወጣ ፤ የቤለ ፡ ካልኣይ ፡ የይበይል ፡ ድርብ ፡ ወይም ፡ መንቲያ ፡ ትንቢት ፡ አንቀጽ ፡ ሲኾን ፤ መምህራን ፡ አርእስትና ፡ ዘር ፡ ቦዝና ፡ ቅጽል ፡ የለውም ፡ ነባር ፡ አንቀጽ ፡ ነው ፡ ብለው ፤ እኩሌቶቹም ፡ የብህለ ፡ ድርብ ፡ ነው ፡ ብለው ፡ ቀዳማይ ፡ አንቀጽ ፡ ማድረጋቸው ፤ ትንቢትነቱ ፡ ስላልታወቀ ፡ ነው ። በኋምስ ፡ መጕረዱም ፡ በመካከሉ ፡ የ ፡ ስላለበት ፡ ነው ። ፪ኛም ፡ ለን ፡ የ ፡ የሚሉ ፡ ሰዎች ፡ የለ ፡ ጸያፎች ፤ ብህለን ፡ ሲያረቡ ፡ ብህየ ፡ ይብይ ፡ ይበይ ፡ ይላሉና ፤ በጸያፍ ፡ እንደበት ፡ የገባ ፡ ነው ፡ ልንል ፡ እንችላለን ። ይብልን ፡ ይብይ ፡ እንደሚሉት ፤ ይብይን ፡ ደግሞ ፡ ይቤ ፡ ብለውት ፡ ይኾናል ፤ አለዚያስ ፡ በኃምስ ፡ ሲጕርድ ፡ ባልተገኘም ። በጸያፍ ፡ አንደበት ፡ መለወጥም ፡ የግስ ፡ ልማድ ፡ ነው ፤ ረን ፡ ለ ፡ የሚሉ ፡ ሰዎች ፡ የረ ፡ ጸያፎች ፤ በሐረረ ፡ ፈንታ ፡ ሐለለ ፡ ብለው ፡ ኹለተኛ ፡ አንቀጽ ፡ እንዳወጡ ። ባማርኛም ፡ ለን ፡ የ ፡ ይወርሰዋል ፤ ይልቁንም ፡ በሣልስ ፡ ቅጽል ። ቀታሊ ፡ ከሃሊ ፡ ሐባሊ ፡ ጠን

ቋሊ ፣ ገዳይ ፣ ቻይ ፣ ፀባይ ፣ ጠንቋይ ፤ የመሰለው ፣ ኹሉ ። ጕራጅነቱም ፣ ለሩቅ ፣ ወንድና ፣ ሴት ፣ ለቅርቡ ፣ ወንድና ፣ ለእኔ ፣ ለንሕነ ፣ ለነዚህ ፣ ላምስቱ ፣ ብቻ ፣ ነው ። ይህም ፤ **ቤለ ፡ ይቤ ፡ ይበል ። ቤለት ፡ ትቤ ፡ ትበል ። ቤልከ ፡ ትቤ ፡ በል ። ቤልኩ ፡ እቤ ፡ እበል ። ቤልነ ፡ ንቤ ፡ ንበል** ፡ እያለ ፣ መኼዱን ፣ ያሳያል ። በቀሩት ፣ ግን ፣ ባምስቱ ፣ ስራዊት ፤ **ቤሉ ፡ ይቤሉ ፡ ይበሉ ። ቤላ ፡ ይቤላ ፡ ይበላ ። ቤልኪ ፡ ትቤሊ ፡ በሊ ። ቤልክሙ ፡ ትቤሉ ፡ በሉ ። ቤልክን ፡ ትቤላ ፡ በላ** ፡ እያለ ፣ ዘሩን ፣ በዱልን ፣ መስሎ ፣ ተካክሎ ፣ ይኼዳል ። የበዱል ፣ ዘርና ፣ የቤለ ፣ ክልኣይ ፣ የይበይል ፣ ወንድም ፣ ፍጹም ፣ ትንቢት ፣ አንቀጽ ፣ መኾኑ ፤ ነባር ፣ ቀዳማይ ፣ አለመኾኑ ፣ በ፫ ፣ ምስክር ፣ ይረዳል ። መዠመሪያ ፤ በማልባዩና ፣ ባምስቱ ፣ ስራዊት ፣ ለን ፣ እየጨመረ ፣ በመኼዱ ፤ ፈጽሞ ፣ ባለመጕረዱ ። ኹለተኛ ፤ የትንቢት ፣ አሥራው ፣ መነሾቹ ፣ ፬ ፣ ፊደሎች ፣ የተአነ ፣ ብቻ ፣ ናቸውና ፤ **ይቤ ፡ ትቤ ፡ እቤ ፡ ንቤ** ፡ እያለ ፣ በነዚህ ፣ ባራቱ ፣ በመኼዱ ። ሦስተኛ ፤ ለነባር ፣ አንቀጽ ፣ ክልኣይ ፣ ማልሳይ ፣ የለውምና ፤ በዘንዱና ፣ በትእዛዙ ፣ ይታወቃል ። አስተውል ፤ ነባር ፣ ቀዳማይ ፤ ወይም ፣ ትእዛዝ ፣ አንቀጽ ፣ ኹኖ ፣ ቢኾን ፣ መንገዱ ፣ እንደ ፣ ሀብና ፣ እንደ ፣ ነዐ ፣ ነበር ፤ ሀብና ፣ ነዐ ፣ ሥርወ ፣ ቀለሙን ፣ ሳይለውጥ ፣ በጫፉ ፣ ሌላ ፣ ባዕድ ፣ ፊደል ፣ ሳይጨምር ፤ **ሀብ ፡ ቡ ፡ ቢ ፡ ባ ፤ ነዐ ፡ ንዑ ፡ ንዒ ፡ ንዓ** ፡ ተብሎ ፣ ባራት ፣ ቅርቦች ፣ ብቻ ፣ እንዲረባ ፤ ይቤም ፣ ሥርወ ፣ ቀለሙን ፣ ሳይለውጥ ፤ ለን ፣ ከቤለ ፣ ከብህለ ፤ ሳይቀላውጥ ፤ ባራት ፣ ስራዊት ፣ በሩቆች ፣ ብቻ ፣ **ይቤ ፡ ይቡ ፡ ይቢ ፡ ይባ** ፡ ተብሎ ፣ በተረባ ፣ ነበር ። የብሂል ፣ አፈታት ፣ ጓዙ ፣ ብዙ ፣ ነውና ፣ የቀረውን ፣ በርባ ፣ ቅምርና ፣ ባገባብ ፣ በሠምና ፣ ወርቅ ፣ ተመልከት ፣ (፪ኛና ፣ ፲፱ኛ ፣ ፳፪ኛ ፣ ዕር ። ፳፬ ፣ ፹፫ ፣ ፻፳፭ቍ) ።

**ብሂል ፤ በዱል ፤** መምታት ፤ በበትር ፣ ማለት ፣ መደብደብ ፤ ወይም ፣ አስቀድሞ ፣ መስደብ ፤ በነገር ፣ መቀንደብ ፣ ጽዕለትን ፣ ተመልከት ። ብሂላና ፣ ብላዕ ፤ ባማርኛ ፣ ይተባበራሉ ፤ ብላ ፣ ብላ ።

**በሃሊ ፤ (ሊት ፡ ልያን ፡ ያት ፤ በሀልት) ፤** ያለ ፣ የሚል ፣ የሚናገር ፤ ባይ ፣ ተናጋሪ ፤ አልኹ ፣ ባይ ፣ እንዲሉ ። **ከመ ፡ ኢይኩን ፡ በሃሌ ፡ አነ ፡ አብዐልኩ ፡ አብራምሀ ። አሆ ፡ በሃሊ ። ወእመሰ ፡ ይቤ ፡ በሃሊ ። በሀልተ ፡ ጽድቅ ፡** (ኩፋ ፣ ፲፫ ። ያዕ፫ ፣ ፲፯ ። አፈ ፣ ተ ፳፯ ። አዋል) ።

**ባህል ፤ (ላት) ፤** በቁሙ ፤ ነገር ፣ ክርክር ፤ አባባል ፤ አነጋገር ፤ የነገር ፣ ስልት ፤ ትርጓሜ ፣ ምስጢር ፤ ድርሳን ፤ ልማድ ፣ ሕግ ፣ ሥርዐት ፤ የሃይማኖት ፣ ትምርት ፤ ቃል ፣ ድምፅ ። **ባህለ ፡ ልሳን ። ከሠትከ ፡ ባህለ ፡ መጻሕፍት ፡ ክዱነ ። ወካዕበ ፡ ይቤ ፡ አባ ፡ ቄርሎስ ፡ በውስተ ፡ አሐዱ ፡ እምባህላት ። ይቤ ፡ በእንተ ፡ ትርጓሜ ፡ ባህላት ። ያስተናክሩ ፡ ሥነ ፡ ባህሎሙ ። ባህለ ፡ ብካይ ፡ ሰሚዖ ፡** (መዝ ፣ ፴ ። ስንክ ፣ ጥር፲፱ ። ፈ ፣ መ ፣ ፳፱ ፣ ፬ ። ማር ፣ ይሥ፭ ። ቄር ፣ ጸላ ። ስንክ ፣ ጥቅ፭) ።

**አብህለ ፤ (ያብህል) ፤ አው ፡ አበለ ፡ (ያብል) ፤** አሰኘ ፤ አናገረ ፣ (ማቴ፳፯ ፣ ፳ ። ግብ፭ ፣ ፵) ። **አሆ ፡ በልኒ ፡ ወአሆ ፡ አብሊዮ ። ስእኑ ፡ አሆ ፡ አብሎቶ ። ንለየ ፡ ከመ ፡ እሙ ፡ አሆ ፡ አበለቶ ፡ ለተወክፎ ፡ ትእዛዝ ። አንጠይዎ ፡ ከመ ፡ አሆ ፡ ያብልዎ ፡** (አርጋ ። ስንክ ፣ ታኅ፭ ። ዮሴፍ) ።

**አብሃሊ ፤ መብሃሊ ፤ መብህል ፤** የሚያሰኝ ፣ የሚያናግር ፤ አሰኝ ፣ አናጋሪ ።

**ምብሃል ፤ (ላት) ፤** መባያ ፣ መናገሪያ ። ማሰኛ ፤ ማናገሪያ ።

**ተብህለ ፤** ተባለ ፣ ተተነባ ፤ ተወራ ፣ ተነገረ ፤ ተጠራ ፣ ተሰየመ ። **ተብህለ ፡ ለቀደምት ። ዘተብህለ ፡ በዳንኤል ፡ ነቢይ ። ብፅዕት ፡ አንተ ፡ ተብህለት ፡ ሊብዙኃን ። መጽሐፍ ፡ ዘይትበሀል ፡ ፈውስ ፡ መንፈሳዊ ። ዘሀሎ ፡ ይትበሀል ፡ ውስተ ፡ ዓለም ፡ ወልድ ። እስመ ፡ ኅሊና ፡ ፅቡስ ፡ ምኑነ ፡ ይትበሀል ፡** (ማቴ፭ ፣ ፳፩ ። ፳፬ ፣ ፲፭ ። ፊልክ ፣ ፸፱ ። ፈ ፣ መ ። ዕር ፣ ኢሳ፳ ፣ ፳፭ ። ጥበ፱ ፣ ፲፭) ።

**ብሁል ፤ (ላን ፡ ላት ፡ ብህልት) ፤** የተባለ ፤ የተነገረ ፤ ንግር ። **አባ ፡ ብሁል ፡ ሊተ ፡** (አፈ ፣ ድ፲) ።

**ተባህለ ፤** ተባባለ ፣ ተማከረ ፤ ተነጋገረ ፤ ተሟገተ ፣ ተከራከረ ። **ተባሀሉ ፡ አሐዱ ፡ ምስለ ፡ ካልኡ ። ተባህሉ ፡ በበይናቲሆሙ ፡ ከመ ፡ የሀቦ ። እሉ ፡ እሙንቱ ፡ እለ ፡ ተባህልዎ ፡ ለፈርያን ። ወእፎ ፡ እክል ፡ ባሕቲትየ ፡ ተባህሎቶሙ ። አመ ፡ ይትባሀሉ ፡ ለሰይጣን ፡** (ዘፍ፲፭ ፣ ፫ ። ኩፋ ፣ ፳፰ ። ዘፀ፮ ፣ ፳፯ ። ዘዳ፭ ፣ ፲፪ ። ይሁ ፣ ፱) ።

**አስተባህለ ፤** አባባለ ፤ አሟገተ ፣ አከራከረ ።

**ብሂም ፤ ሞት ፤ (ብህመ ፡ ይብህም ፡ ይብህም) ፤** ድዳ ፣ መኾን ፤ አለመናገር ፤ ልናገርም ፣ ቢሉ ፣ አለመቻል ፤ እንደ ፣ ከብት ፣ መኾን ። **ይኄይስ ፡ ብሂም ፡ እምነቢብ ፡ በሐሰት ። ይብህም ፡ ልሳን ። ብህመ ፡ ልሳኑ ። ሜጥኩ ፡ ገጽየ ፡ ወብህምኩ ፡** (ፈላስ ። ግንዘ ። ስንክ ፣ የካ፯ ። ዳን፲ ፣ ፲፭) ።

**በሃም ፤ (ምት ፡ ማን ፡ ማት) ፤** ድዳ ፤ መናገር ፣ የማይችል ፤ ከድምጥ ፣ በቀር ፣ ፍሬ ፣ ቃል ፣ የማይሰጥ ። **ከነ ፡ ጽሙመ ፡ ወበሃመ ፡ እምአውሥኦትክሙ ። ኢትከውን ፡ እንከ ፡ በሃመ ። ወከመ ፡ በሃም ፡ ዘኢይከሥት ፡ አፉሁ ። ለበሃማን ፡ ከኖሙ ፡ ቃለ ፡** (ግንዘ ። ሕዝ፳፬ ፣ ፳፯ ። መዝ ፣ ፴፯ ። ኪዳ) ።

**ብሁም ፤ (ህምት) ፤** ድዳ ፣ የኾነ ፤ አፍ ፣ እያለው ፣ የማይናገር ። **ብእሲት ፡ ብህምት ፡** (ስንክ ፣ ሐም፳) ።

**ብህመት ፤** ድዳ ፣ መኾን ፤ ድዳነት ። **ብህመተ ፡ ልሳን ። ተፈትሐ ፡ ልሳኑ ፡ እምብህመት ፡** (መጽ ፣ ምስ ። ስንክ ፣ ሠኔ፴) ።

**ብሄማ ፤ (ዕብራ ። ዐረ ፡ በሀኢ.ም) ፤** ክብት ፤ እንስሳ ፤ ኢንባቢ ።

**ብሄሞት ፤ (ዕብራ) ፤** ጉማሬ ፡ የወንዝ ፡ አ ውሬ ፤ የባሕር ፡ ፈረስ ፤ በአፍሪቃ ፡ ወንዞች ፡ በየሐይቆቿ ፡ የሚገኝ ፤ ከውሃ ፡ እየወጣ ፡ ሣርና ፡ ቅጠል ፡ የሚበላ ፤ ታ ላቅ ፡ ገናና ፤ ቈርበተ ፡ ወፍራም ፡ ዐንገተ ፡ ደንዳና ፤ ቈር በቱ ፡ ኰርባጅ ፡ ዐለንጋ ፡ የሚኾን ፤ መልኩ ፡ ያንድስ ፤ ድ ምጡ ፡ የፈረስ ፤ ሲያሽካካ ፡ ፈረስ ፡ የሚመስል ። ዲኖ ፡ ጅን ፡ የባሕር ፡ የበረሓ ፡ ጕሽ ፤ ጠባዩ ፡ ያውሬ ፤ መልኩ ፡ የበሬ ። ናሁኬ ፡ ብሄሞት ፡ ዘገበርኩዎ ፡ ምስሌከ ፡ ይበ ልዕ ፡ ሣዕረ ፡ ከመ ፡ ላሕም ፡ (ኢዮ፵ ፡ ፲፭) ።

**ብሄሞት ፤** በቁሙ ፤ የየብስ ፡ ዐንበሪ ፡ ከባሕር ፡ ተፈጥሮ ፡ በየብስ ፡ የሚኖር ፤ ግሩማን ፡ አራዊት ፡ የሚፈ ሩትና ፡ የሚገዙት ፡ ከአራዊት ፡ ኹሉ ፡ የሚበልጥ ፡ መጨ ረሻ ፡ ግዙፍ ፡ የእንስሳት ፡ ራስ ፡ የአራዊት ፡ ንጉሥ ፤ በዥ ራቸው ፡ ቀዳማያቸው ፤ በተፈጥሮ ፡ የሌዋታን ፡ ወንድም ፡ ባሏ ፡ መስሏ ። የሌዋታንን ፡ ፍች ፡ ተመልከት ፤ ባለብሉ ዮች ፡ ግን ፡ ዝኆን ፡ ይሉታል ። ወይትከፈሉ ፡ በይ እቲ ፡ ዕለት ፡ ክልኤቱ ፡ ዐናብርት ፤ ዐንበሪ ፡ አንስቲያ ዊት ፡ ዘስማ ፡ ሌዋታን ፡ ከመ ፡ ትኅድር ፡ በልጕተ ፡ ባሕር ፤ ወለተባዕታይ ፡ ስሙ ፡ ብሄሞት ፡ ዘይእኅዝ ፡ በእንግድዓሁ ፡ በድወ ፡ ዘኢያስተርኢ ፤ ወስሙ ፡ ዴ ንዳ ፡ በምሥራቀ ፡ ገነት ፡ (ሔኖ፷ ፡ ፰) ።

**አብሀመ ፤** ድዳ ፡ አደረገ ፤ አፍ ፡ አስያዘ ፤ ዝም ፡ አሰኘ ።

**አብሃሚ ፤ መብሀም ፤** ድዳ ፡ የሚያደርግ ፡ አፍ ፡ የሚዘጋ ፡ የሚለጕም ።

**በሀነ ፤ (ይብሀን ፡ ይብሀን ፡ ብሂን ። ዕብ ፡ ባሐን ፤ ፈተነ) ፤** በነነ ፡ ቡን ፡ አለ ፤ የደቄት ፡ ያመድ ፡ የትቢያ ።

**ባህንዋ ፤ ዎት ፤ (ባሀነነ ፡ ይባሀንን ፡ ይ ባሀንን) ፤** መብነን ፡ መባከን ፤ ብን ፡ ብን ፤ ብንን ፡ ብ ንን ፡ ማለት ፤ ማነስ ፡ መጕደል ፤ መጥፋት ፡ መበላሸት ፤ ከንቱ ፡ መኾን ። መጽሐፍ ፡ ግን ፡ በባሀነነ ፡ ፈንታ ፡ ተባ ሀነነ ፡ ይላል ፤ አያስኘም ። ይኄይሰኒ ፡ መዊት ፡ እምይት ባሀነኒ ፡ ምዝጋናየ ፡ (፩ቆሮ ፡ ፱ ፡ ፲፭ ። ስንክ ፡ መስ፳) ።

—፤ በቁሙ ፤ መባነን ፤ መበርገግ ፤ ደንግጦ ፡ ከንቅልፍ ፡ መነሣት ፡ (ዐማርኛ) ።

**ብሀኑን ፤ (ናን ፡ ናት ፡ ንንት) ፤** የባነነ ፤ የ በነነ ፡ የባከነ ፤ ብኑን ፡ ከንቱ ፤ በናና ፡ በካና ፤ ፍሉጥ ፡ ብዑድ ። ቃላተ ፡ ሕስወ ፡ ወብሀኑነ ፡ ታርኢ ። ይሜ ህሩ ፡ ብሀኑነ ፡ ሥጋዌ ፡ ዘእንበለ ፡ ፅምረተ ፡ መለኮት ። ኢብሀኑን ፡ ትስብእቱ ፡ እምድማሬ ፡ መለኮቱ ፤ ወኢ ብሕትው ፡ መለኮቱ ፡ እምትስብእቱ ፡ (ቄር ፡ ጸላ ። መጽ ፡ ምስ) ።

**ባሀን ፤ ባሀናን ፤** ብናኝ ፤ ትቢያ ፤ ጕድፍ ።

**በዊእ ፤ አት ፤ (በአ ፡ ይበውእ ፡ ይባእ ። ዕብ ፡ ቦእ ። ዐረ ፡ ባእ) ፤** መግባት ፤ መከተት ፤ ጥ ልቅ ፡ ስምጥ ፡ ማለት ፤ ማደር ፤ ወደ ፡ ውስጥ ፡ ማለፍ ፡ መኼድ ፤ ውሳጣዊ ፡ ማእከላዊ ፡ መኾን ። ቦአ ፡ ቤተ ። ባኡ ፡ ሀገረ ። ባእ ፡ ውስተ ፡ ታቦት ። ኢትባኢ ፡ ውስተ ፡ ገራህተ ፡ ባዕድ ፡ (ዳን፪ ፡ ፲፯ ። ኤር፬ ፡ ፭ ። ዘፍ፯ ፡ ፩ ። ሩት፪ ፡ ፰) ። በቦአ ፡ ፈንታ ፡ ተባውአ ፡ ይላል ፤ ስሕተት ፡ ነው ፡ (ሮሜ፩ ፡ ፰ ። ገላ፪ ፡ ፬ ። ፪ጢሞ ፡ ፫ ፡ ፯) ። በዊ እና ፡ በዒት ፡ አንድ ፡ ሥር ፡ ናቸው ።

**በዋኢ ፤ (ኢት ፡ እያን ፡ ያት) ፤** የሚ ገባ ፡ ገቢ ፤ መጪ ። ጽፉቅ ፡ በዋኤ ፡ ቤታ ። ኅበ ፡ ብ ዙኅ ፡ በዋኢት ። በእንተ ፡ ብዝኅ ፡ በዋእያን ፡ ወወፃ እያን ፡ (ምሳ፳፬ ፡ ፵፩ ። ሚራ፵፪ ፡ ፮ ። ፊልክ ፡ ፺ ፡ ፳፪) ።

**ቡአት ፤ በአት ፤** መግባት ፤ አገባብ ፤ መባት ፤ አባባት ። በበአትከ ፡ ወበፀአትከ ። በአተነ ፡ ወፀአተነ ፡ በሰላም ፡ ዕቀብ ። ጥንተ ፡ ወበአት ፡ ውስተ ፡ ትሥ ጉት ። በዛቲ ፡ ዕለት ፡ ኮነ ፡ በአቱ ፡ ውስተ ፡ ቤተ ፡ መ ቅደስ ። በአተ ፡ ክረምት ። በአተ ፡ ሰንበት ። በአተ ፡ ሌሊት ። በአተ ፡ ጾም ፡ (ዘዳ፳፰ ፡ ፯ ። ግንዘ ። ቄር ፡ ጸላ ። ስንክ ፡ የካ፳ ። ሠኔ፳፩ ። ማር፲፭ ፡ ፵፪ ። አቡሻ ፡ ፲፪ ። መር ፡ ዕዉ) ።

**በአት ፤** ዐቢይና ፡ ንኡስ ፡ ደቂቅ ፡ አገባብ ፡ የብ ትን ፡ ሰዋስው ፡ መግለጫ ፡ እኍል ፡ ገብ ፡ ቃልና ፡ ፊደል ። (ጥት) **በአት ፤ (ታት) ፤** የመነኰሴ ፡ ቤት ፤ ጐሬ ፡ ዋሻ ፡ ፍርኵታ ፤ ውስጥ ፡ ያለው ፡ ቦታ ፤ ጋጥ ፡ በረት ። በደብረ ፡ መቃርዮስ ፡ ኅበ ፡ ተሐንጸ ፡ በኣት ። ንበር ፡ በበኣትከ ። ወኮነ ፡ ይትፋለስ ፡ እምበኣት ፡ ውስተ ፡ በኣት ፤ ቤት ፡ (ስንክ ፡ የካ፳ ። ፊልክ ፡ ፳፱ ። ፶፯) ። በኣተ ፡ ፈደት ። በ ኣተ ፡ መዛግብት ። በኣታተ ፡ ኵዙሕ ። በኣታት ፡ ለመ ራዕይሁ ፤ ዋሻ ፡ (ኤር፳ ፡ ፲፭ ። ቀሌ ። ኢዮ፴፱ ፡ ፳፫ ። ፪ዜና ፡ ፴፪ ፡ ፳፰) ። ቦታ ፡ ማለት ፡ ከዚህ ፡ ወጥቷል ። ፈረንሳዊ ፡ ቢት ፡ የሚለውም ፡ ከዚህ ፡ ይስማማል ፤ ዱብ ልንና ፡ ሴክልን ፡ ተመልከት ።

**አብአ ፤** አገባ ፤ አስገባ ፤ መለሰ ። አባእናሁ ፡ ው ስተ ፡ ገነት ። ኢታብእ ፡ ዙሎ ፡ ሰብአ ፡ ዘረከብከ ፡ ው ስተ ፡ ቤትከ ። ዘያወፅእሙ ፡ ወዘያበውእሙ ። እብ እሙ ፡ ውስተ ፡ አእምሮ ፡ እግዚአብሔር ፡ (ኩፋ ፡ ፫ ። ሚራ፲፩ ፡ ፳፱ ። ዘኍ፳፯ ፡ ፲፯ ። ስንክ ፡ ግን፯) ።

**—፤** ሰጠ ፤ አቀረበ ። እምከመ ፡ አባእኩ ፡ ለእግዚ ኣህነ ፡ ዘያበውእ ፡ መሥዋዕተ ። አነ ፡ አባእኩ ፡ ተዝ ካረ ፡ ስእለትክሙ ፡ ቅድሜሁ ፡ (ሚራ፯ ፡ ፬ ። ዘሌ፯ ፡ ፰ ። ጦቢ፲፪ ፡ ፲፪) ።

**አባኢ ፤ መብእ ፤ (እት ፡ ኣን ፡ ኣት) ፤** የሚያገባ ፤ አግቢ ፤ መላሽ ። ሰጭ ፡ አቅራቢ ፡ (ቅዳ ፡ ሕር) ።

**ሙብእ ፤ (ኣት) ፤** መግቢያ ፤ ማግቢያ ፤ ማስ ገቢያ ፤ በር ፤ ደጃፍ ። ኢየአምር ፡ ሙብእየ ፡ ወሙፃ እየ ። እስመ ፡ አንተ ፡ ህየ ፡ ቦቱ ፡ ሙብእ ፡ ላዕለ ፡ ይ ሁዳ ። ሙብአ ፡ ግብጽ ። ሙብአ ፡ ባቢሎን ። ሙብኣ ቲሁ ፡ (፫ነገ ፡ ፫ ፡ ፯ ። ዮዲ፬ ፡ ፯ ። ኩፋ ፡ ፲ ። ፳ ። ሕዝ ፵፫ ፡ ፲፩) ።

**መባእ፤ (ኣት)፤** በቁሙ፤ መባ ፣ እጅ ፣ መንሻ፤ በረከት፤ ቍርባን፤ መሥዋዕት ። ጸሎተ ፡ መባእ ። ወርቀ ፡ መባእ ፡ ዘማጺን ። ኢትበል ፡ በብዝኅ ፡ መባእየ ፡ ይሰሪ ፡ ሊተ ። አብእ ፡ መባአ ፡ ለእግዚ ፡ (ቅዳ ። ፈ ፣ መ ፣ ፲፯ ፣ ፩ ። ሢራ ፣ ፯ ፣ ፱ ። ፲፱ ፣ ፲፩ ። ማቴ፳ ፣ ፳፱) ።

**ተባውአ፤** ተጋባ፤ ተገባባ፤ ባልና ፣ ሚስት ፣ ኾነ ።

**አስተባውአ፤** አጋባ፤ አገባባ፤ አዛወገ ።

**ባእ፤—ስንዝር፤—ባዕ ።**

**በዊዝ፤ዘት፤(ቦዘ፡ይበውዝ፡ይቡዝ)፤** መቦዝ፤ መፍዘዝ፤ መቦዘን ፣ መስነፍ ።

**ቦዝ፤** ቸልታ ፣ አንቀጽ፤ ንባቡ ፣ ስያፍ ፣ ቃሉ ፣ ስንፍ ፣ ነገር ፣ የማያስር፤ ቀቲሎ ፣ ባሪኮ ፣ ቀዲሶ ፣ ይህን ፣ የመሰለ ። ከሥሩ ፣ አውታረ ፣ በገና ፣ ያንዱ ፣ ስም ። ቦዝ ፣ ድንጉል ፣ እንዲሉ ። ነጮችም ፣ ባውዛ ፣ የሚሉት ፣ የታላቅ ፣ መብራት ፣ ስም ፣ ከቦዝና ፣ ከቤዝ ፣ ይስማማል ።

**በዊሕ፤ ሖት፤ (ቦሐ ፡ ይበውሕ ፡ ይባሕ ። ዐረ ፡ ባሐ)፤** መታየት ፣ መገለጥ፤ መጕላት ፣ ብሩህ ፣ ጽዱል ፣ ጸዐዳ ፣ መኾን፤ ኖራ ፣ በረቅ ፣ ብሕክ ፣ መምሰል ። ቡሔ ፣ ቡሓ ፣ ብሓ ፣ ማለት ፣ ከዚህ ፣ የወጣ ፣ ነው ። መሠልጠን፤ ሹመት ፣ መብት ፣ ማግኘት፤ ፈቃድ ፣ ሥልጣን ፣ መቀበል፤ ከበላዩ ። ብሕትን ፣ ተመልከት፤ የዚህ ፣ መንቲያ ፣ ነው ።

**አብሐ፤ (ያበውሕ ፡ ያብሕ)፤** አሠለጠነ፤ ፈቀደ ፣ አስናበተ፤ ሾመ፤ ሥልጣን ፣ ሰጠ ። ኢያብሖ ፡ አቡሁ ። ወዘንተኒ ፡ እምገበርኑ ፡ ሶበ ፡ ያበውሕ ፡ እግዚ ። ንብብ ፡ ለእመ ፡ አብሐኩከ ። ወአብሖሙ ፡ ላዕለ ፡ አጋንንት ፡ (ኩፋ ፣ ፴፩ ። ዕብ ፣ ፯ ፣ ፫ ። ሢራ፴፩ ፣ ፯ ። ማር ፣ ፯ ፣ ፯) ።

**አስተበውሐ፤** አስፈቀደ፤ ዕሺ ፣ አሰኘ፤ አስጨከነ ፣ አስደፈረ ። አስተበዊሖ ፡ በኀበ ፡ ሊቀ ፡ ካህናት ፡ መጽአ ፡ ከመ ፡ ይሞቅሕ ፡ ኵሎ ። አስተበውሓ ፡ ለበሊዐ ፡ ዕፀ ፡ ዕልወት ። አስተበውሖቶሙ ፡ ለበሊዐ ፡ ንዋየ ፡ ውስጥ ፡ (ግብ፱ ፣ ፲፬ ። መጽ ፣ ምስ ። ጥበ፲፱ ፣ ፳) ።

**ተበውሐ፤ (ይትበዋሕ)፤** ሠለጠነ፤ ሥልጣን ፣ አገኘ ፣ ተቀበለ፤ ባለመብት ፣ ኾነ ። ኢይትበውሑ ፡ ላዕለ ፡ ውሉደ ፡ ጻድቃን ። አሜሃ ፡ ተበውሐ ፡ ጢጦስ ፡ በኵሉ ፡ አህጉር ። እስመ ፡ ተበዋሕኩ ፡ እትናገር ። ሥርዐት ፡ ቅድስት ፡ ዘተበዋሕክሙ፤ የተቀበላችኋት ፣ (ኩፋ ፣ ፲ ። ዮሴፍ ። ዘፍ፲፰ ፣ ፴፩ ። ቀሌ) ።

**ብዉሕ፤ (ሓን ፡ ሓት ፡ ውሕት)፤** የሠለጠነ፤ ሥሉጥ፤ የተገባ ። ብእሲት ፡ ኢኮነት ፡ ብውሕተ ፡ ላዕለ ፡ ርእሳ፤ ወከማሁ ፡ ብእሲኒ ፡ ኢኮነ ፡ ብዉሐ ። ወአኮሰ ፡ ዘኢኮነ ፡ ብዉሓነ ። ኢኮነኑ ፡ ብዉሐ ፡ ለብሓዊ ፡ ይግበር ፡ (፩ቆሮ ፣ ፯ ፣ ፬ ። ፪ተሰ ፣ ፫ ፣ ፱ ። ሮሜ ፱ ፣ ፳፩) ።

**ብዉሕ፤ (ይደሉ፤ መፍትው፤ ርቱዕ)፤** ይገባል፤ የተገባ፤ የሚገባ፤ ግቡ፤ አገባብ ። ይደሉ ፣ ሲኾን ፣ በቁሙ፤ ውስጠ ፣ ዘ ፣ ሲኾን ፣ ውእቱ ፣ አለበት ። ኢብዉሕ ፡ ይባእ ፡ ውስተ ፡ ቤተ ፡ መቅደስ ፡ ዘእንበለ ፡ ካህን ። ብዉሕ ፡ ለኤጲስቆጶስ ፡ ከመ ፡ ይፍታሕ ። ብዉሕ ፡ ለከ ፡ ትንብብ ፡ ወትግበር ፡ ዘፈቀድከ ። ኢኮነሁ ፡ ብዉሐ ፡ ለልዑል ፡ ይግበር ፡ ዘፈቀደ ፡ (ዮሴፍ ። ፈ ፣ መ ፣ ፯ ፣ ፱ ። ቀሌ ። ኢዮ፳፱ ፣ ፲፱) ።

**ብውሕና፤** ጌትነት፤ ሥሉጥነት ። ኀልዮተ ፡ ብውሕናሁ ፡ (ማር ፣ ይሥ፪ ፣ ፱) ።

**መባሕት፤** ሥልጣን ፣ መብት፤ ሹመት፤ ትእዛዝ፤ ፈቃድ ። ተውህበ ፡ ሎቱ ፡ መባሕት ። በመባሕተ ፡ መኑ ፡ ትገብር ፡ ዘንተ ። ወሰአለ ፡ መጽሐፈ ፡ መባሕት ። ዲያቆን ፡ ኢይግበር ፡ ምንተኒ ፡ ዘእንበለ ፡ መባሕተ ፡ ኤጲስቆጶስ ፡ አቡሁ ። እስከ ፡ ይረክብ ፡ መባሕተ ፡ ቃልየ ። ይጽሐፍ ፡ መባሕተ ፡ (ዳንኤ ፣ ፯ ። ማቴ፳፩ ፣ ፳፫ ። ግብ፱ ፣ ፪ ። ዲድ ፣ ፳ ። ቀሌ ። ሲኖድ) ።

**ቦክ፤ (ዕብ ፡ ቡኽ)፤** በዊክ፤ መባከን ፣ መቅበዝበዝ፤ እንቡዝ ፣ መኾን፤ ተለል ፣ ተለል ፣ ማለት፤ የመንገደኛ ፣ የድውይ ። ባለብሉዮች ፣ ግን ፣ ቍስለ ፣ ሥጋ ፣ ይሉታል ። መጽአከ ፡ ሕማም ፡ ወገሰሰከ ፡ ቦክ ፡ (ኢዮ ፬ ፣ ፭) ። ክዳን ፣ ገዚፍ ፣ በማለት ፣ ፈንታ ፣ ክዳን ፣ ቦክ ፣ ይላል፤ የተሳሳተ ፣ ነው ። ዕብራይስጡ ፣ ግን ፣ ማክቤር ፣ ይላል፤ ልብድ ፣ ለሐፍ ፣ የሌት ፣ ልብስ ፣ እንደ ፣ ቡልኮ ፣ ያለ ፣ ማለት ፣ ነው ፣ (፩ነገ ፣ ፳ ፣ ፲፭) ።

**ባውላ፤** ስመ ፣ ጭፍራ፤ ከቡልዮስ ፣ ቄሳር ፣ የወጣ ፣ (ዮሴፍ) ።

**ባውኒ፤—የወር ፡ ስም፤—በኡናህ ።**

**ቦዐ፤ (ዐረ ፡ ባዐ)፤** ዘረጋ፤ ጋተ፤ ስንዘረ ።

**ባዕ፤** ስንዝር፤ ውስጥ ፣ እጅ ። ባለብሉዮች ፣ ግን፣ ክንድ ፣ ይሉታል ፣ (ዘፀ፴፯ ፣ ፲፯) ።

**ቦቀ፤ (ይበውቅ ፡ ይቡቅ፤ በዊቅ ። ዐረብ ፡ በወቀ)፤** ነፋ ፣ መታ ፣ አስጮኸ፤ ባፍ ፣ በትን ፋሽ ።

**ቡቅ፤(ብ፡አብዋቅ)፤** ቀንዳ ፣ መለከት፤ ሥሥ ፣ ውስጠ ፣ ክፍት ። ወይትነፋኅ ፡ ቀርን ፡ ወብዐዛት ፡ ወአብዋቅ ፡ ፡ (ሥር ፣ አኵ) ። አንቦቀቦቀ ፣ ተንቦቀቦቀ ፣ ቦቅቧቃ ፣ ማለት ፣ ከዚህ ፣ ወጥቷል ።

**ባቅቡቅ፤ (ዕብ)፤** ታናሽ ፣ የውሃ ፣ ዕቃ፤ ቅል ፣ መንቀል ፣ ጠርሙዝ፤ አፈ ፣ ጠባብ ፣ ዐንገተ ፣ ረዥም ። ጋላም ፣ ቅሉን ፣ ቡቄ ፣ ይለዋል ።

**በዘ፤ (ዐቢይ ፡ አገባብ)፤** ፍችው ፣ ገንዘብ፤ ምስጢሩ ፣ እንደ ፣ ስለ ፣ ዘንድ ። በኀላፊና ፣ በትንቢት ፣ ይገባል፤ በዘወድአ ፡ ሞተ ፡ ኵሎ ። በዘቀነዮሙ ፡ ሞት፤ ሞት ፣ ኹሉን ፣ በጨረሰ ፣ ገንዘብ፤ በገዛቸው ፣ ገንዘብ ። ወትሜህር ፡ በዘታስሕቶሙ፤ በምታስታቸው ፣ ገንዘብ ።

ገብሩ፡ ልዘያምዕዑ፡ በሚያሳዝኑኝ፡ ገንዘብ ። በምስ ጢር፡ እንጂ፡ በንባብ፡ እንደና፡ ስለ፡ ሲኾን፡ ምስክር፡ የለውም ። በርሥኡ፤ እንዘ፡ አልቦ፡ በማለት፡ ፈንታ፡ በዘረሥአ፡ በዘአልቦ፡ እያለ፡ ይገኛል፤ የመላሽ፡ ስሕ ተት፡ ነው፡ (ዘፍጽ፱፡ ፴፯ ። ፵፡ ፲፭) ።

**በዘ፤(በ፡ዘ)፤** በ፡ በቁም፡ ቀሪ፤ ዘ፡ ቅጽልና፡ በቂ፤ ወይም፡ የዘርፍ፡ ደፊ፡ ይኾናል ። ለምንት፡ ትት ናገር፡ በዘይሰምዑ፡ሕዝብ፤በሚሰሙት፡ቋንቋ ። በዘ ርእየ፡ ወበዘሰምዐ፡ ሰማዕተ፡ ይከውን ። ባየው፡ በሰ ማው፡ ነገር፤ እንደ፡ ፊተኛውም፡ ባየ፡ በሰማ፡ ገንዘብ፡ ያሰኛል፤ ምስጢሩ፡ እንዳየ፡ እንደ፡ ሰማ፡ መጠን፤ ስ ላየ፡ ስለ፡ ሰማ፤ ያየውን፡ የሰማውን፤ አይቶ፡ ሰምቶ፡ ማለት፡ ነው፤ ይህ፡ ኹሉ፡ የበን፡ አፈታት፡ ያሳያል ። በ ዘአይኒራም፡ ዕፅ፡ ወበዘአቤሴሎም፡ እብን፤ ባይኒ ራም፡ ዕንጨት፡ ባቤሴሎም፡ ደንጊያ፤ በቁም፡ ቀሪና፡ ደፊ ። አንዳንድ፡ ጊዜም፡ ዘ፡ ቅጽል፡ ሲኾን፡ በ፡ አዳ ማቂ፡ ኹኖ፡ ይቀራል ። ነሥአ፡ ሰይፈ፡ በዘይቀትል ። ልብስ፡ በዘያስተባሪ፤ ምክንያት፡ በዘያስተዋርድ ። በንና፡ ዘን፡ ተመልከት፡ (ዕር፲፱፡ ቍ፸፱) ።

**በዚዝ፤ዘት፤(በዘ፡ይበዝዝ፡ይብዝዝ። ዐረ፡ ዕብ፡ ባዛዝ)፤** መዘት፤ ጕራ፡ መንዛት ።

**በዝበዘ፤(ዕብ፡ ባዝቤዝ)፤** በቁሙ፤ በዘ በዘ፡ ዘረፈ፡ ቀማ፡ በረበረ ። ዘራ፡ በተን፤ መንዘረ፡ አባ ከነ፡ በከንቱ ። ዐማ፡ ነቀፈ፤ ሰደበ፡ አዋረደ፤ ናቀ፡ አቃ ለለ ።

**በዝግና፤—ዝርግፍ፤—ዘጊን፡ ዘገነ ።**

**ቤዘወ፤—ተቤዝ፤—በዪዝ፡ ቤዘ ።**

**በዚኀ፤ ኆት፤ (በዝኀ፡ ይበዝኅ፡ ይብ ዛኅ)፤** መብዛት፤ መርባት፡ መበርከት፤ መውለድ፡ መክ በድ፡ መፈድፈድ፤ ማየል፡ መበርታት፡ (ዘፍ፩፡ ፳፱፡ ፳፰ ። ፰፡ ፲፯ ። ዘፀ፩፡ ፯) ። ጸንዐ፡ ማይ፡ ወበዝኀ ። በዝኀ፡ ድምፀ፡ ሁከት፡ (ዘፍ፯፡ ፲፰፡ ፲፱ ። ፩ነገ፡ ፲፬፡ ፲፱) ።

**ብዙኅ፤(ኃን፡ ኃት፡ ዝኅት)፤** የበዛ፤ ብዙ፡ እጅግ፤ ዐያሌ ። ዕንቍ፡ ዘብዙኅ፡ ሤጡ ። ብዙኃን፡ እምውሉደ፡ ግብጽ ። ብዙኃት፡ አዋልድ ። ሀገር፡ ብዝኅት፡ ሰብእ፡ (ዮዲ፲፡ ፳፭ ። ኩፋ፡ ፴፱ ። አስቴ፱፡ ፰ ። ሕዝ፴፱፡ ፲፮) ።

**ብዙኀ፤** በዝቶ፤ ብዙ፡ ኹኖ፤ ብዙ፡ ጊዜ፤ በ ብዙ ። መጽአ፡ ብዙኀ፡ ወተመይጠ፡ ኀዳጠ ። ኢት ትአመኖ፡ ብዙኀ ። ዘብዙኀ፡ ተመንደበ፡ ብዙኀ፡ ይ ትሜየን፡ (ዘረፋ ። ሚራ፯፡ ፯ ። ፴፩፡ ፲፩) ።

**ብዝኀት፤** መብዛት፤ አበዛዝ፤ ብዛት፤ ብዙ ኀት ። ብዝኀተ፡ ሰብእ፡ (ዮሴፍ) ።

**ብዝኅ፤(ኃት)፤** ብዛት፤ ብዙኅነት፤ ብዥ ። ብ ዝኀ፡ መዋዕል ። ብዝኀ፡ ዓማት ። በብዝኀ፡ ዓመታት፡ ወበብዝኀ፡ ንብረት፡ (ዘካ፰፡ ፲ ። ዮሐ፳፩፡ ፮ ። ኢዮ ፲፱፡ ፲፱) ።

**አብዝኀ፤** አበዛ፡ አረባ፤ አበረከተ ። አስበዛ፡ አስረባ፤ አስበረከተ ። አብዝኖ፡ ኣብዝኖ፡ ለሕማምኪ ። ዘአብዝኀ፡ ብዕለ ። ዘአብዝኀ፡ ጥበበ፡ አብዝኀ፡ ሐ ዘነ፡ (ዘፍ፫፡ ፲፮ ። መክ፩፡ ፲፰ ። ፭፡ ፲፰) ።

**አብዛኂ፤(ኂት፡ ኃያን፡ ያት)፤** የሚያበዛ፤ የሚያስበዛ፤ አብኝ፡ አስበኝ ። ኢይኩን፡ አብዛኄ፡ ነ ገር ። አብዛኃያነ፡ ሠሐቅ፡ (ፍ፡ ነ፡ ፰፡ ፩ ። ፈ፡ መ፡ ፴፱፡ ፪) ።

**መብዝኂ፤** ዝኒ፡ ከማሁ ። መብዝኃያነ፡ ነገር ። መብዝኄ፡ ነቢብ ። ወንሕነ፡ በኀቤክሙ፡ ከመ፡ መ ብዝኄ፡ ነገር፡ (ኪዳ፡ ገ፱ ። ፈ፡ መ፡ ፳፩፡ ፫ ። አፈ፡ ተ፳፫) ።

**መብዝኀት፤** የተከፍሎ፡ ብዛት፤ ላቂያ፤ ብ ልጫ ። ሲነበብና፡ ሲዘረዘር፡ የቅጽል፡ አፈታት፡ ይፈ ታል ። መብዝኀተ፡ መዋዕሊሆሙ ። መብዝኀተ፡ ሕ ዝብ፡ (ኩፋ፡ ፳፫፡ አርጋ) ። የሚበዛው፡ የሚልቀው፡ የሚ በልጠው፤ ብዙው፡ ያሰኛል ። መብዝኀትሙ፡ ተነፅኑ፡ በገዳም ። ወመብዝኀትሙ፡ ሀለዉ፡ እስከ፡ ዮም፡ (፩ቆሮ፡ ፲፡ ፭ ። ፲፭፡ ፮) ።

**መብዝኅቶ፤** ብዙዉን፤ ይልቁን፤ ብዙ፡ ጊዜ ። መብዝኅቶ፡ ይወድቅ፡ ውስተ፡ እሳት ። ወአንተሰ፡ መብዝኅቶ፡ ትትሜሰል፡ ከመ፡ ኆጥእ፡ (ማቴ፲፯፡ ፲፭ ። ሱቱ፡ ዕዝ፰፡ ፶፯ ። ጦቢ፩፡ ፯) ።

**ተበዝኀ፤** ተባዛ፡ ተራባ፤ ተዋለደ ። ወይት ባዝኃ፡ በሙፋሪሆን፡ (መዝ፡ ፻፵፫ ። ዘፍ፩፡ ፳፪) ። በ በዝኀ፡ ፈንታ፡ ተባዝኀ፡ ይላል፤ ፈጽሞ፡ ለማለት ። ከመ፡ ትትባዛኃ፡ በሕይወትከ ። ወትትባዛኃ፡ በረ ከቱ፡ ለጻድቅ ። ተባዝኁ፡ በእግዚእ፡ (ሚራ፪፡ ፫ ። ፲፭፡ ፳፱ ። ፪ጴጥ፡ ፫፡ ፲፰) ።

**አስተባዝኀ፤** አባዛ፡ አራባ፤ አዋለደ፡ አበራ ከተ ። ኣስተባዝኀከ፡ ጥቀ፡ (ዘፍ፲፯፡ ፮፡ ፰) ።

**በዜቃ፤(ዐረ፡ ዘይበቅ)፤** በቁሙ፤ ፈሳሽ፡ የማዕደን፡ ዐይነት፡ የሚዝበቀበቅ ። ጥሩ፡ ብር፡ ቅል ቅል፡ የሌለው ። እንዘ፡ ትሰወጢ፡ ከመ፡ ባዜቃ፡ (ደራሲ) ።

**በዚቃ፤(ዕብ፡ ባዛቅ)፤** መብረቅ፤ ነጸብራቅ፡ (ሕዝ፩፡ ፲፱) ።

**ብዝር፤(ዐረብ)፤** ፍሬ፤ ቅንጣት ።

**ብዝር፡ ክታን፤** የተልባ፡ ፍሬ፤ እንቡጡ፡ ቅንጣቱ ።

**በዝራ፤(ዐማርኛ)፤** በቁሙ፤እንስት፡ ፈረስ፤ ፍሬያማ፡ ፍሬያም፤ መፍርዪት ።

**በዝቶ፤ ቶት፤ (በዘተ፡ ይቤዝት፡ ይበ ዝት)፤** ማባዘት፤ መፈለቀቅ፡ ማፍታታት፤ መንቀስ፡ እጅ፡ ሥራ፡ ማግባት፤ ለመፍተል ። እንዘ፡ ትቤዝት፡ ፀምረ፡ (ምሳ፴፱፡ ፴፩) ።

**በዛቲ፤(ቲት፡ ትያን፡ ያት)፤** የሚያባዝት፡ አባዛች፤ እጅ፡ ሥራ፡ አግቢ ።

**ተበዘተ** ፤ ተባዘተ ፤ ተፍታታ ፤ ተንቀሰ ፡፡

**ብዙት** ፤ የተባዘተ ፤ ብዝት ፤ ባዘቶ ፤ ፍልቅቅ ፡፡ ፀምር ፡ ብዙት ፡ (መሳ፳ ፡ ፲፯ ፡፡ ሰንክ ፡ ታኅ፲፰) ፡፡

**በሓ ፤ ባሕ ፤ (ዐረ ፡ በኅ ፡ አይዞኽ)** ፤ የሰላምታ ፡ የቡራኬ ፡ ቃል ፤ ፍሥሓ ፡ ሰላም ፡፡ እንዴት ፡ ዋልኽ ፡ እንደት ፡ አደርኽ ፤ ጤና ፡ ይስጥኽ ፤ ደስታ ፡ ሰላም ፡ ላንተ ፡ ይኹን ፤ ጠላትኽን ፡ ያውድቅ ፡ ቢሳኛኽን ፡ ያርቅ ፡ ማለት ፡ ነው ፤ በሓክ ፡ ኪ ፤ በሓክሙ ፡ ክን ፡ እያለ ፡ በቅርብ ፡ በቅርቦች ፡ ይዘረዝራል ፡፡ ኢትበሎ ፡ በሓ ፡ ወአመ ፡ ይቤለክ ፡ በሓ ፡፡ በሓ ፡ በልዎ ፡ ተሳለምዎ ፡፡ ወበሓኒ ፡ ኢትበልዎ ፡፡ ባሕ ፡ ሄርማ ፡፡ ኢትበልዎሙ ፡ ባሕ ፡ (፪ነገ ፡ ፱ ፡ ፳፱ ፡፡ ድጓ ፡፡ ፪ዮሐ ፡ ፲ ፡፡ ሄርማ፭ ፡ ፪ ፡፡ ቀሌ) ፡፡ በሓክ ፡ ባሮክ ፡፡ ባሕክ ፡ ሄርማ ፡፡ በሓኪ ፡ ማርያም ፡፡ በሓክሙ ፡ አበው ፡ ቅዱሳን ፡፡ ባሕክን ፤ አው ፡ በሓክን ፡ (ራእ ፡ ባሮ ፡፡ ሄርማ ፡ ገ፳፩ ፡፡ ደራቢ ፡፡ ማቴ፳፰ ፡ ፱) ፡፡

**ቢሕ ፤ ብሔ ፤ (ዕብ ፡ ብሄሞት)** ፤ ጕማሬ ፤ የወንዝ ፡ የባሕር ፡ አውሬ ፡፡ ብህመን ፡ እይ ፡፡ ተጠምቀ ፡ በማይ ፡ ዕራቀ ፡ ከመ ፡ ቈርነናዓት ፡ ወዐንጐጕ ፡ ወብሔ ፡ (መጽ ፡ ምስ) ፡፡

ቢሕ ፡

**ቢሓት ፤ ብሔያት** ፤ ጕማሮች ፤ ጕማሬዎች ፡፡ አክይስት ፡ ወፀናብርት ፡ ወሐርገፃት ፡ ወዐናጕግ ፡ ወቢሓት ፡ ወቈርነናዓት ፡ (መቃ ፡ ፯፲፪) ፡፡

**ብሒእ ፤ አት ፤ (ብሕአ ፡ ይብሕእ ፡ ይብሕእ ፡፡ ዕብ ፤ በሄእ ፤ እጅግ ፡ ፈራ ፤ ተደነቀ)** ፤ መቡካት ፤ መሖምጠጥ ፤ መብሰል ፡፡ ሐሊብ ፡ ዘኢብሑአ ፡፡ ይፈርሆሙ ፡ ኢይብሕኡ ፤ እስመ ፡ ጻሕብ ፡ ዘቅቡል ፡ ፍጡነ ፡ ይብሕእ ፡ (ግንዘ ፡፡ ሄርማ ፡ ገ፵፰) ፡፡ በብሕአ ፡ ፈንታ ፡ ተብሕአ ፡ ይላል ፤ አያስኼም ፡፡ እስከ ፡ ይትበሐእ ፡ (ሆሴ፯ ፡ ፬ ፡፡ ዘፀ፲፪ ፡ ፴፱) ፡፡ በጕበንጕን ፡ ተመልከት ፤ የዚህ ፡ መንቲያ ፡ ነው ፡፡

**ብሑእ ፤ (ኣን ፡ አት ፡ ሕአት)** ፤ የቦካ ፤ የበሰለ ፤ የሖመጠጠ ፡፡ ምስለ ፡ ኅብስት ፡ ዘብሑእ ፡፡ ኢትግበርዎ ፡ ብሑአ ፡፡ ኢትዝባሕ ፡ በብሑእ ፡ ደምየ ፤ ያደረ ፡ (ዘሌ፯ ፡ ፲፫ ፡፡ ፪ ፡ ፲፩ ፡፡ ዘፀ፳፫ ፡ ፲፰) ፡፡ በብሑእ ፡ ፈንታ ፡ ብሒእ ፡ ይላል ፤ አያስኼም ፡፡ ብሒእ ፡ ወይን ፡፡ ብሒእ ፡ ሜስ ፡፡ ሐምለ ፡ ብሒእ ፡ (ዘኍ፮ ፡ ፫ ፡፡ ፱ ፡ ፲፩ ፡፡ ዘፀ፲፪ ፡ ፰) ፡፡

**ብሕአት** ፤ መቡካት ፤ አቦካክ ፤ ቡሖነት ፤ ርሾ ፡ (ማቴ፲፮ ፡ ፲፩ ፡ ፲፪) ፡፡

**ብሕእ ፡ (አት)** ፤ ቡሖ ፤ ርሾ ፡ (ሉቃ፲፪ ፡ ፩) ፡፡ በብሑእ ፡ ፈንታ ፡ ብሒእ ፡ እንደሚል ፤ በብሕእ ፡ ፈንታ ፡ ብሑእ ፡ ይላል ፤ ጥሬን ፡ በቅጽል ፡ ቅጽልን ፡ በጥሬ ፡ መለዋወጥ ፡ የጣፊና ፡ የመላሽ ፡ ስሕተት ፡ ነው ፡፡ ወለአመ ፡ ኮነት ፡ ቀዳሚሃ ፡ ቅድስተ ፡ ወብሑእኒ ፡ ቅዱስ ፡ ከማሁ ፤ ቡሖ ፡ ሊጥ ፡፡ ኅዳጥ ፡ ብሑእ ፡ ብዙኅ ፡ ሐሪጸ ፡ ያብሕእ ፡፡ አንጽሑ ፡ እንከ ፡ ብሑአ ፡ ብሉየ ፡ እምኔክሙ ፡፡ ብሑእ ፡ ዘኑሥአት ፡ ብእሲት ፡ ወኀብአቶ ፡ ውስተ ፡ ሐሪጽ ፤ ርሾ ፡ (ሮሜ፲፩ ፡ ፲፯ ፡፡ ፩ቆሮ ፡ ፭ ፡ ፮ ፡ ፯ ፡፡ ማቴ፲፫ ፡ ፴፫) ፡፡

**ብሒእ** ፤ ርሾ ፤ ሎስን ፡ እይ ፡፡ መጣጣ ፡ ዐይብ ፤ ዐዞ ፡ ክል ፤ የተበላሸ ፡ ጠጅ ፤ ሖምጣጤ ፡፡ ትጸብኒ ፡ ኅብስትኪ ፡ በብሒእ ፡፡ ወአስተዩኒ ፡ ብሒአ ፡ ለጽምእየ ፡፡ ከመ ፡ ብሒእ ፡ ኢይደልዎ ፡ ለቍስል ፡፡ ወቦ ፡ ህየ ፡ ፃምዒ ፡ ብሒእ ፡ ዘምሉእ ፤ ወመልኡ ፡ ሰፍነገ ፡ እምብሒእ ፡ (ሩት፪ ፡ ፲፬ ፡፡ መዝ ፡ ፷፰ ፡፡ ምሳ፳፭ ፡ ፲ ፡፡ ዮሐ፲፱ ፡ ፳፱) ፡፡

**አብሐአ** ፤ አቦካ ፤ አስቦካ ፤ በርሾ ፡ ለወሰ ፤ አስለወሰ ፤ አሖመጠጠ ፤ ሖምጣጣ ፡ አደረገ ፤ አስደረገ ፡፡ አፍጥኒ ፡ ወአብሕኢ ፡ ሠለስተ ፡ መሣልሰ ፡ ወግበሪ ፡ ጻፍንተ ፡ (ዘፍ፲፰ ፡ ፮ ፡፡ ማቴ፲፫ ፡ ፴፫ ፡፡ ሉቃ፲፫ ፡ ፳፩) ፡፡

**ተብሕአ** ፤ ተቦካ ፡ ተለወሰ ፤ ሊጥ ፡ ኾነ ፡፡

**ተባሕአ** ፤ ተቧካ ፤ ተቦካካ ፡ ርስ ፡ በርሱ ፤ የዱቄት ፡ የነገር ፡፡

**በሕብሐ ፤ (ዕብ ፡ ቃራጽ ፤ ቀረጸ)** ፤ ሣለ ፡ መሰለ ፤ ዐነጠ ፡ ቀረጠ ፤ ሠራ ፡ ፈጠረ ፤ የቡሖ ፡ የሸቃ ፤ የዳቦ ፡ የብስኵት ፤ የሠምዕ ፡ የልሕኵት ፡፡

**ተበሕብሐ ፤ (ይትበሐባሕ ፡ ይትባሕባሕ)** ፤ ተሣለ ፡ ተመሰለ ፤ ተፈጠረ ፡፡

**ብሕባሔ** ፤ መፍጠር ፤ መፈጠር ፤ አፈጣጠር ፡ ፈጠራ ፤ ተፈጥሮ ፡፡ ዕብራይስጡ ፡ ሜሖሜር ፡ ቀራጽቲ ፡ ያለውን ፤ ግእዙ ፡ ተቀረጽኩ ፡ ተገበፍኩ ፡ በማለት ፡ ፈንታ ፤ እምጽቡር ፡ ብሕባሔክ ፡ ወእምኔሁ ፡ ቅሳሜነ ፡ ይላል ፤ (ኢዮ፴፫ ፡ ፮) ፡፡ ከዚህ ፡ በቀር ፡ በሕብሐ ፡ ብሎ ፡ ፈጠረ ፡ የሚል ፡ አይገኝም ፡፡

**ብሕውስ ፤ (ዕብ ፡ ባእሻህ)** ፤ አብሾ ፡ አስተናግር ፤ የደሮ ፡ ኵስ ፤ ግማታም ፡ ቅጠል ፤ በባድማና ፡ በድብድባ ፡ የሚበቅል ፡ ቋያ ፤ መጥፎ ፡ ቡቃያ ፡፡ ወከነት ፡ ሀገር ፡ በድወ ፤ ወበቈለ ፡ ላዕሌሃ ፡ ሦክ ፡ ወአሜከላ ፤ ወኰነት ፡ ብሕውስ ፡ ወምጕሕያ ፡ (መቃ ፡ ፯፲፫) ፡፡

**በሐኰ ፤ (ብ ፡ አባሕኰ ፤ አብሓኰ)** ፤ የቦግ ፡ የፍየል ፡ ተባት ፤ አውራ ፤ ኰርማ ፡ የሚታዘል ፡ የሚንጠለጠል ፡፡ በሐኰ ፡ እንዘ ፡ ይሜብል ፡ ላዕለ ፡ መርዔት ፡፡ ቢሐኰ ፡ ወዳቤላ ፡፡ ዳቤላት ፡ ወአባሕኰ ፡፡ አባሕኩ ፡ አባግዐ ፡፡ አባሕኰ ፡ ዘአባግዐ ፡ ወዘአጣሊ ፡ (ምሳ፴፱ ፡ ፳፯ ፡፡ ሕዝ፴፱ ፡ ፲፯ ፡፡ ፴፱ ፡ ፲፰ ፡፡ መዝ ፡ ፷፬ ፡፡ ዘፀ፴፩ ፡ ፲ ፡ ፲፪ ፡፡ ፴ ፡ ፴፩) ፡፡

**ብሔሞት** ፤—በቁሙ ፤—ብሂም ፡ ብህመ ።

**በሕቁ** ፤—በጅጉ ፤ በጥቂቱ ፤—ሐቂቅ ፡ ሐቀ ፤ ሐቀቀ ፤ ሕቅ ።

**ባሕቀወ ፤ አንባሕቀወ** ፤—አፋሸዥ—በቀወ ።

**ባሕቀቀ ፤ ተባሕቀቀ** ፤—አወከ ፡ ታወከ ፤—ሐብቀቀ ።

**ብሒር ፤ ሮት** ፤ (ብሕረ ፡ ይብሕር ፡ ይብሐር ። ፀረ ፡ ባሐረ ። ዕብ ፡ ባሐር ፤ መረጠ) ፤ መስፋት ፡ መንጣለል ፤ መዘርጋት ፤ ሰፊ ፡ ዝርግ ፡ ወርዳም ፡ ረዥም ፡ መኾን ፤ የቦታ ፡ የመሬት ፡ የርስት ፡ የግዛት ።

**ብሔር ፤ (ራት ፤ በሓይርት ፤ በሓውርት ። ፀረ ፡ ቢሓር ፤ ብ ፡ በሕረት)** ፤ ቦታ ፡ ስፍር ፤ ስፍራ ፤ በሀገር ፡ ውስጥ ፡ ያለ ፡ ታናናሽ ፡ ክፍል ። ይጹብበነ ፡ ብሔር ፤ ግበሪ ፡ ለነ ፡ ብሔረ ፡ ኀበ ፡ ንነብር ። ቦ ፡ ብሔር ፡ እምኀበ ፡ ይወፅእ ፡ ብሩር ። አይቴ ፡ ብሔራ ፡ ለጥበብ ። ገዳም ፡ ውእቱ ፡ ብሔር ። ወበጺሖሙ ፡ ብሔረ ፡ ዘስሙ ፡ ጎልጎታ ። ወወፅአ ፡ ስሙዓቱ ፡ በዙሉ ፡ በሓውርተ ፡ ኢ.ድያም ፡ (ኢሳ፴፬ ፡ ፳ ። ኢዮ፳፰ ፡ ፩ ፡ ፲፪ ። ማቴ፲፱ ፡ ፲፭ ። ፳፯ ፡ ፴፫ ። ሉቃ፬ ፡ ፴፯) ። ብሔር ፡ ጥሉል ፤ ወፍራም ፡ ሥብ ፡ ውሃማ ፡ መሬት ፡ ለተክል ፡ የተመቸ ። ብሔር ፡ ሥዑር ፤ ሣራም ፤ የሣር ፡ ቦታ ፡ መስክ ፡ ጨፌ ፡ ክልክል ፡ (ኢሳ፩ ፡ ፩ ። መዝ ፡ ፳፪) ።

—፤ ምድር ፤ ሀገር ፤ ከተማ ፤ ገጠር ፤ አውራጃ ፡ ግዛት ፤ ታላላቅ ፡ ክፍል ፡ በስምና ፡ በሹም ፡ በወሰን ፡ በደንበር ፡ የተለየ ። መላይቱ ፡ ምድር ፤ የብስ ፡ ዓለመ ፡ ሰብእ ። አይቴ ፡ ብሔርከ ። ብሔረ ፡ ሕያዋን ። ብሔረ ፡ ብንያም ። ኢመሀከሙ ፡ ለበሓውርት ፡ ኀበ ፡ ነበረ ፡ ሎጥ ። በሓውርተ ፡ አሕዛብ ። ውእቱ ፡ ተርፈ ፡ ለብሔር ። ነሥእዎ ፡ እምነ ፡ ብሔር ፡ (ዮና፩ ፡ ፰ ። መዝ ፡ ፻፵ ። ኤር፩ ፡ ፩ ። ሚራ፲፯ ፡ ፰ ። ኢሳ፲ ፡ ፲፫ ። ሚራ፵፱ ፡ ፲፯ ። ፵፱ ፡ ፲፱) ።

—፤ ሰው ፤ ወገን ፡ ነገድ ፤ ሕዝብ ፡ አሕዛብ ፡ በቋንቋ ፡ በመንግሥት ፡ በሕግ ፡ በሥርዐት ፡ የተለየ ። ሎሉ ፡ ብሔር ፡ ኢመስሐ ። መፍቅደ ፡ ብሔር ። አንከሩክ ፡ በሓውርት ። መጽኡ ፡ ኵሉ ፡ በሓውርት ፡ ውስተ ፡ ግብጽ ። ኵሉ ፡ በሓውርት ፡ ዘቤተ ፡ እስራኤል ። በበ ፡ በሓውርቲክሙ ፡ ደቂቀ ፡ ዕጓለ ፡ (፩ነገ ፡ ፲፱ ፡ ፳፱ ። ሚራ፴፰ ፡ ፴፱ ። ፵፯ ፡ ፲፯ ። ዘፍ፵፩ ፡ ፶፯ ። ኤር፪ ፡ ፱ ። መዝ ፡ ፵፰) ።

—፤ ሰማይና ፡ ምድር ፤ ሰማይ ፡ ከነግሡ ፡ ምድር ፡ ከነልብሱ ፤ መላው ፡ ዓለም ። ሳዩም ፡ ታቹም ፡ ያንድ ፡ አምላክ ፡ ግዛት ፡ ስለ ፡ ኾነ ፤ በምሳሌ ፡ ብሔር ፡ ተብሏል ። ከመ ፡ ዝ ፡ ይቤ ፡ እግዚአ ፡ ብሔር ፡ (እግዚአብሔር) ፡ ሰማይኒ ፡ መንበርየ ፡ ወምድርኒ ፡ መከየደ ፡ እገርየ ። እስመ ፡ ዚአየ ፡ ውእቱ ፡ ኵሉ ፡ ዓለም ፡ በምልኡ ፡ (ኢሳ፷፮ ፡ ፩ ፡ ፪ ። መዝ ፡ ፵፱) ።

—፤ ጊዜ ፤ ሰዓት ፤ ወራት ፡ ባመትና ፡ በወር ፡ በዕለት ፡ ያለ ፡ ክፍል ። ክረምት ፡ ብሔር ። እስመ ፡ ነግህ ፡ ብሔሩ ። ወጸቢሖ ፡ ብሔር ። እስከ ፡ ጸብሐ ፡ ብሔር ። ጽልመት ፡ ብሔር ። መስየ ፡ ብሔር ፡ (፩ዕዝ ፡ ፲ ፡ ፲፫ ። ግብ፪ ፡ ፲፭ ። ፳፯ ፡ ፴፫ ። ፩ነገ ፡ ፳፭ ፡ ፴፮ ። ሚራ፳፫ ፡ ፲፰ ። ገድ ፡ ተክ) ።

—፤ የመጽሐፍ ፡ ክፍል ፤ ታላቅ ፡ ዐቢይ ፡ አንቀጽ ፤ አንድ ፡ ክፍል ፡ መጽሐፍ ፤ ለብቻው ፡ አንድ ፡ ተብሎ ፡ የሚቈጠር ፤ በውስጡ ፡ ብዙ ፡ ምዕራፍ ፡ ያለበት ፤ እንደ ፡ ኦሪትና ፡ እንደ ፡ ነገሥት ፤ እንደ ፡ ወንጌል ፡ እንደ ፡ ሐዲሳት ፡ ያለ ። ይቤ ፡ በኦሪት ፡ ውስተ ፡ ሣልስ ፡ ብሔር ፡ ዘሌዋውያን ። በውስተ ፡ ዳግም ፡ ብሔረ ፡ ኦሪት ። ለኦሪት ፡ ባቲ ፡ ኀምስቱ ፡ ብሔር ። አርባዕቱ ፡ ብሔረ ፡ ነገሥት ። ክፍል ፡ ኃምስ ፡ እምዳግም ፡ ብሔር ፡ ዘመጽሐፈ ፡ ነገሥት ፡ (ፈ ፡ መ ፡ ፪ ፡ ፮ ። ፬ ፡ ፩ ። አብጥ ፡ ፹፩ ። አቡሻ ፡ ፲፱) ።

**ባሕር ፤ (ብ ፡ አብሕርት ። ፀረ ፡ በሕር ። ሱር ፡ ባሕራ)** ፤ በቁሙ ፤ መካነ ፡ ማይ ፤ ምቋመ ፡ ማይ ፤ ዓለመ ፡ ማይ ፤ ምእላደ ፡ ማይ ፤ ሰፊ ፡ ጥልቅ ፡ ዕሙቅ ፤ ውሃው ፡ የማያልቅ ፡ የማይደርቅ ፤ ስፋቱ ፡ ከየብስ ፡ የሚበልጥ ፡ ፫ ፡ እጅ ፡ የሚልቅ ፡ (ዘፍ፩ ፡ ፱ ፡ ፲) ። ባሕር ፡ ዐቢይ ። ባሕረ ፡ ኤርትራ ። አብሕርት ፡ ወቀላያት ፡ (ዳን ፡ ፯ ፡ ፪ ። ዘፀ፲ ፡ ፲፱ ። ኩፋ ፡ ፪) ። ስፋት ፡ ለሌለውም ፡ ለታናናሹ ፡ ሐይቅ ፤ ለኵሬ ፡ ባይቀር ፡ ለወንዝ ፡ ለፈሳሽ ፡ ይነገራል ። ባሕረ ፡ ጼው ፤ ባሕረ ፡ ገሊላ ፤ ባሕረ ፡ ዟይ ፤ ባሕረ ፡ ጣና ፡ እንዲሉ ። ባሕረ ፡ ኒል ። ተከዜ ፡ ዮርዳኖስ ፡ ባሕር ፡ (አቡሻ ፡ ፳ ። ስንክ ፡ ሠኔ፬ ። መስ፪) ።

**ባሕረ ፡ እሳት** ፤ በቁሙ ፤ ረቂቅ ፡ ሰማያዊ ፡ እሳት ፤ ወይም ፡ ፍል ፡ ውሃ ፡ (መቃ ፡ ገ፱) ።

**ባሕረ ፡ ብርት** ፤ የብርት ፡ ውሃ ፤ በብርት ፡ ምዕቃል ፡ የተመላ ፡ መታጠቢያ ፡ ኵሬ ፡ ሰሎሞን ፡ እንደ ፡ ባሕር ፡ አስፍቶ ፡ የሠራው ፡ (ኤር፶፪ ፡ ፲፯ ። ፬ነገ ፡ ፲፮ ፡ ፲፯) ።

**ባሕረ ፡ ሐሳብ** ፤ ቍጥር ፡ ያለው ፡ ዘመን ፤ ዓመተ ፡ ዓለም ። ሐሳበ ፡ ባሕር ፤ የዘመን ፡ ቍጥር ። ወበመስፈርት ፡ ሰፈሮ ፡ ለባሕር ፡ (ሱቱ ፡ ዕዝ፪ ፡ ፵፯) ።

**ባሕረ ፡ ጥበባት** ፤ ስሙ ፡ ስርጋዌ ፤ ዮሐንስ ፡ ወንጌላዊ ፡ (ድጓ) ።

**ባሕር** ፤ ምዕራብ ፤ ግራ ፡ (ዘፍ፲፪ ፡ ፰ ። ፲፫ ፡ ፲፬ ። ፳፰ ፡ ፲፬ ። ዳን፰ ፡ ፬) ። እመንገለ ፡ ባሕር ፡ ባሕረ ፤ ወእመንገለ ፡ ጽባሕ ፡ ጽባሐ ፡ (ሕዝ፵፭ ፡ ፯) ።

—፤ ንኡስ ፡ ማእዝን ፡ በሰሜንና ፡ በምዕራብ ፡ ማኸል ፡ ያለ ፤ የሰሜን ፡ ምዕራብ ፤ የሊባ ፡ አፋዛኘ ፡ ትይዩና ፡ አንጻር ። ባሕረ ፡ ወሊባ ፡ (ቅዳ) ።

**ባሕራዊ** ፤ የባሕር ፤ የምዕራብ ፤ ምዕራባዊ ።

**ባሕርይ ፤ (ያት ። ፀረ ፡ በሕሪይ)** ፤ ባሕራይ ፡ ባሕራዊ ፤ የባሕር ፡ ዕንቍ ፤ ሉል ፡ ከስደፍ ፡ የሚገኝ ፤ ደረቅ ፡ ክራራ ፡ ጠንካራ ፡ እብናዊ ፤ የወፍ ፡ ዕንቍ

ላል፡ የሚመስል፤ ታናሽ፡ ክብ፡ እንክብል፡ ድብልብል፤ የሚበርቅ፡ የሚያንጸበርቅ። ዕንቍላል፡ ቅሉ፡ ዕንቍ፡ ሉል፡ ማለት፡ ነው፤ ስሙን፡ ከሉል፡ ወስዷል፤ መመሳሰል፡ የጋራ፡ ነውና፡ (ማቴ፯፡ ፮። ፲፫፡ ፵፭፡ ፵፮። ራእ፳፩፡ ፳፩)። **እስመ፡ ሰደፍ፡ ይወልዶ፡ ለዕንቍ። ተናገር፡ ዕንቍ፡ ባሕርይ፡ ወክሥት፡ እፎ፡ ህላዌከ። ባሕርይ፡ ዘያንጸበርቅ። እማንቱ፡ ዕንቍ፡ ባሕርያት፡ ክቡራት። መጽሐፈ፡ ባሕርይ፡** (ማር፡ ይሥ ፳፰። ሃይ፡ አበ፡ ኤፍ። አርጋ፡ ፪። ስንክ፡ ሚያ፳። ቄድር)።

—፤ ክቡር፡ ደንጊያ፤ የየብስ፡ ዕንቍ፤ ሉል፡ የሚመስል፤ ባሕርያዊ። **እብን፡ ባሕርይ፡** (ሔኖ፲፰፡ ፯። ጥበ፯፡ ፱። ፲፰፡ ፳፱። ዮሴፍ)።

**ባሕርይ**፤ **(ዐረ፡ ጀውሀር። ዕብ፡ ጌጼም)**፤ በቁሙ፤ የነገር፡ ኹሉ፡ ሥር፡ መሠረት፡ ምንጭ፤ መውጫ፡ መፍለቂያ፡ መገኛ፤ ጠባይዕ፡ ህላዌ፡ ከዋኔ። ጀውሀር፡ በዐረብ፤ ጌጼም፡ በዕብራይስጥ፤ ባሕርይም፡ አካልም፡ ይኾናል፤ እንደ፡ ህላዌና፡ እንደ፡ ጠባይዕ፡ ነው፤ ባሕርይ፡ ግን፡ በግእዝ፡ ቋንቋ፡ አካላዊ፡ ፍጹመ፡ አካል፡ ቢባል፡ እንጂ፤ አካል፡ አይባልም፤ አካልም፡ ባሕርያዊ፡ ሕያው፡ ባሕርይ፡ ቢባል፡ እንጂ፤ ባሕርይ፡ አይባልም። በምድር፡ ያለ፡ የፍጥረት፡ ኹሉ፡ ሥር፡ ማይ፡ መሬት፡ ነፋስ፡ እሳት፡ ናቸው፤ እሊህ፡ አራቱ፤ ባሕርያትም፡ ጠባይዓትም፡ ይባላሉ፤ ባሕርይ፡ ከብሕረ፡ እንደ፡ ወጣ፤ ጠባይዕም፡ ከጠብዐ፡ ይወጣል። ባሕር፡ ለታውዕእ፡ ተብላ፡ ብዙ፡ ሥን፡ ፍጥረት፡ እንዳስገኘች፤ ባሕርይም፡ መገኛ፡ ማስገኛ፡ ስለ፡ ኾነ፤ የአካል፡ የስም፡ የህላዌ፡ ጥንት፤ የሥራ፡ ምንጭ፡ የግብር፡ መሠረት፡ ይባላል፤ ይኸውም፡ እንቀጽና፡ ቅጽል፡ ብትን፡ ጥሬ፡ ኹሉ፡ ከዘር፡ እንዲገኝ፡ እንደዚያ፡ ማለት፡ ነው። ከባሕርይ፡ ለሚገኝ፡ ባሕርያዊ፡ ሥራ፡ ሠሪው፡ አካል፡ መሣሪያው፡ ባሕርይ፡ ነው፤ አካል፡ ሠሪ፡ እንዲባል፡ ባሕርይ፡ ደግሞ፡ ሠሪ፡ አይባልም፤ ማጭድ፡ ማጨጃ፡ እንጂ፡ ዐጫጅ፡ እንዳይባል፤ አሠሪም፡ ቢሉት፡ ምስጢሩ፡ ከዚያው፡ ከመሣሪያነት፡ ይገባል፤ የሥራ፡ ባለቤት፡ ወትሮ፡ አካል፡ ነው። **ወአካላኒ፡** (ሠሪዋ፡ ፈጻሚዋ)፡ **እግዚአብሔር፡ ውእቱ፡** (አረጋ፡ ድ፲፰)። አካልን፡ ከባሕርይ፡ ገባሪን፡ ከግብር፡ በየስሙና፡ በየስልቱ፡ ለይቶ፡ የማያውቅ፡ መምህር፡ ግን፤ አካል፡ ሲሉት፡ ባሕርይ፤ ባሕርይ፡ ሲሉት፡ አካል፡ እያለ፤ የግእዝን፡ ቋንቋ፡ የመጻሕፍትን፡ ቃል፡ የሊቃውንትን፡ ባህል፤ ትርጓሜና፡ ምስጢር፡ ያበላሻል። **እስመ፡ ብሂሎቱ፡ ኀየሰ፡ እመላእክት፡ አኮ፡ ዘይኤምር፡ ኀበ፡ ባሕርዩሁ፡ ዘእምአብ፤ እስመ፡ ባሕርየ፡ መለኮቱ፡ አኮ፡ ዘኮነ፡ ሥጋ፡ አላ፡ ተወልደ፤ ወባሕቱ፡ ይኤምር፡ ኀበ፡ ባሕርየ፡ ሥጋዌሁ፡** (አፈ፡ ድ፩። ዕብ፡ ፩፡ ፬)። የፈጣሪ፡ ባሕርይ፡ እንደ፡ ፍጡር፡ ባሕርይ፡ ከባት፡ ወደ፡ ልጅ፡ የማይወርድ፡ ሊቀዳ፡ ሊከፈል፡ ወይም፡ ሊበረዝ፡ የማይቻል፡ አንድ፡ ሥር፡ አንድ፡ ነቅ፡ ስለ፡ ኾነ፤ ወልድ፡ በተለየ፡ አካሉ፡ የኛን፡ ባሕርይ፡ ነሥቶ፡ ፍጹም፡ ሰው፡ በኾነ፡ ጊዜ፤ ሰው፡ የኾነው፡ አካሉ፡ ነው፡ እንጂ፡ ባሕርዩ፡ ሰው፡ አልኾነምና፤ **አኮ፡ ዘኮነ፡ ሥጋ፡** አለው። በተዋሕዶ፡ ወልድ፡ ዋሕድ፡ አንድ፡ አካል፡ አንድ፡ ልጅ፡ ብሎ፡ በተዐቅቦ፡ ኹለት፡ ባሕርይ፡ ማለት፡ ስለዚህ፡ ነው። ፫፡ መለኮት፡ የሚሉ፡ ግን፤ ጥንቱን፡ ከተዋሕዶ፡ በፊት፡ ወይም፡ ተለውጦ፡ ሰው፡ የኾነ፡ አይደለም፡ ብለው፡ እንደ፡ ባህላቸው፡ ይፈቱታል፤ ባህላቸውም፡ ባሕርዩ፡ ሰው፡ ኹኖ፡ አንድ፡ ባሕርይ፡ ኹኗል፡ ማለት፡ ነው። ቅዱሳት፡ መጻሕፍት፡ ሊቃውንት፡ አሐዱ፡ ያሉትን፡ የሥላሴን፡ ባሕርይ፡ ከፋፍሎ፡ ሠለስቱ፡ ማለት፤ በተዐቅቦ፡ ክልኤቱ፡ ያሉትን፡ የወልድን፡ ባሕርያት፡ ቀላቅሎ፡ አሐዱ፡ ማለት፤ ያሉታና፡ የሸፍጥ፡ የምፀት፡ ቃል፡ ነው፤ እውነተኛ፡ ትርጓሜና፡ አፈታት፡ አይደለም፤ ምንም፡ ለተርጓሚው፡ ቀኝ፡ ቢኾን፡ ለሰሚው፡ ግራ፡ ነው። ይወልደዋል፡ ብሎ፡ አይቀድመውም፡ አይበልጠውም፡ ማለት፡ ባሕርይ፡ ባይከፈል፡ ነውና፤ ባሕርዩ፡ ሰው፡ ቢኾን፡ አባቱ፡ መንፈሱ፡ ሳይቀሩ፡ በግድ፡ ሥላሴ፡ ሰው፡ ኾኑ፡ ያሰኛል፤ እንደ፡ አካላትም፡ ሠለስቱ፡ ቢሉት፡ በግድ፡ ሦስት፡ አማልክት፡ ያሰኛል፤ ኹሉም፡ የታነቀፈና፡ የተወገዘ፡ ነው። ሰው፡ መኾንና፡ ሥጋ፡ መልበስ፡ አካቶ፡ ፈጽሞ፡ ለአካል፡ ብቻ፡ እንጂ፡ ለባሕርይ፡ ሊነገር፡ አይቻልም። **ናወግዝ፡ እለ፡ ይብሉ፡ አው፡ ይኄልዩ፡ ከመ፡ ሥሉስ፡ ቅዱስ፡ ዘውእቶሙ፡ ሠለስቱ፡ አካላት፡ ተሠገዉ፤ በብሂሎቶሙ፡ ከመ፡ መለኮት፡ ዙለንታሁ፡ ዘንሬኢ፡ ከመ፡ ውእቱ፡ በአብ፡ ወወልድ፡ ወመንፈስ፡ ቅዱስ፡ ተሠገወ። ወናወግዝ፡ ዓዲ፡ እለ፡ ይብሉ፡ ሠለስተ፡ መለኮተ፡ እንተ፡ ዘአብ፡ ወወልድ፡ ወመንፈስ፡ ቅዱስ። ወለእመ፡ ትቤ፡ መለኮት፡ ምት፡ አንተ፡ ትክውን፡ ቀታሊሆሙ፡ ለሥሉስ፡ ቅዱስ፤ እስመ፡ ባሕርየ፡ ሥላሴ፡ አሐዱ፡ ውእቱ፤ ዘውእቱ፡ መለኮት፡** (ሃይ፡ አ፡ ዮሐ፡ ዘእስ፡ ወዘአን። አግና)። ከዚህ፡ የቀረውን፡ የባሕርይን፡ ምስጢርና፡ አፈታት፡ በህላዌና፡ በጠባይዕ፡ በመለኮት፡ ተራ፡ ተመልከት።

**ባሕርያዊ**፤ የባሕርይ። ስምን፡ ግብርን፤ አካልን፡ ያሳያል።

**ባሕረረ**፤ **(ዐረ፡ በሐረ)**፤ ተቀጥላ፡ ግስ፤ ባነነ፡ በረገገ፤ ደነገጠ፡ ደነበረ፤ ከባሕር፡ ልማድ፡ አለ።

**አባሕረረ**፤ አባነነ፡ አስደነበረ፤ ከባሕር፡ አገባ፡ አስጠመ። **እንበለ፡ ያደንግፆ፡ ምት፡ ወኢያባሕርሮ፡** (ስንክ፡ ኅዳ፪። ጥር፳፩። ማቴ፳፡ ፴፪)።

**ባሕሩስ**፤ ቀለም፤ የጕሽ፡ መቃ፤ የሸንበቆ፡ የስንበሌጥ፡ ዐይነት፤ ቀጫጭን፡ ውስጠ፡ ክፍት፡ ዐረቦች፡ ብርዕ፡ አድርገው፡ የሚጥፉበት፤ በወንዝ፡ ዳር፡ በባሕር፡ ጠረፍ፡ የሚበቅል። ቅልጥሙ፡ ቀጥ፡ ያለ፡ የተካከለ፡ ክስ፡ ኾነ፡ ላንገትና፡ ለጣት፡ ምሳሌ፡ ኹኖ፡ ይነገራል፤ ጣተ፡ መቃ፡ ዐንገተ፡ መቃ፡ እንዲሉ። (ሙሾ፤ ጣተ፡ መልካም፡ እቴ፡ ስለ፡ ሞተች፡ ወንድሟ)፤ ትመታኝን፡

ብዬ፡ ሴቲቱ፡ ወንዱን፤ በመቃጣቷ፡ ነው፡ እኔስ፡ የማዝን ። ብርዐ፡ ባሕሩስ ። በትረ፡ ባሕሩስ፡ (ኢሳ፳፡ ፴፭ ። ፪ነገ፡ ፲፰፡ ፳፩) ። ጽሕድ፡ በማለት፡ ፈንታ፡ ብሮሽ፡ እንደማለት፡ ባሕሩስ፡ ይላል፤ የተሳሳተ፡ ነው ። ለየዐይ፡ ባሕሩስ ። ንጹን፡ ኮነ፡ ብዙኀ፡ ከመ፡ ዕፀ፡ ባሕሩስ፡ ወከመ፡ ብርዐ፡ ገዳም፡ (ዘካ፲፩፡ ፪ ። ክብ፡ ነገ) ።

**ብሒት፤ ቶት፤ (ብሕተ፡ ይብሕት፡ ይብሐት፤ ቦሐ)፤** መሠልጠን፤ መሾም፤ መብት፡ ችሎት፡ ምቾት፡ ማግኘት ። እንዘ፡ ትብሕት፡ አንተ፡ በዙሉሂ ። ወሶበ፡ ብሕትኩ፡ እልእክ፡ ዘይጼውዐከ፡ (አርጋ፡ ፪ ። ግብ፳፱፡ ፳፩) ።

**አብሐተ፤** አባተ፤ ሾመ፡ አሠለጠነ ። አሸነፈ፡ በላይ፡ ኾነ፡ (ዐማርኛ) ።

**ተባሐተ፤** ተባባተ፤ ተሳለፈ፡ ተዋጋ፤ ታገለ፤ ተጋደለ ። ይትባሐቱ፡ አጋንንት፡ ምስለ፡ ሰብእ፡ ወይወድዩ፤ ውስተ፡ ልቦሙ፡ ኀሊና፡ እኩየ ። ዕቀበኒ፡ እግዚኦ፡ በዛቲ፡ ሰዓት፡ እምእለ፡ ይትባሐቱ፡ አጋንንት፡ (ቄስጠ፡ ፩ ። ደራሲ) ።

**ብሑት፤ (ታን፡ ታት፡ ሕት)፤** ብዉሕ፤ የሠለጠነ፡ የተሾመ፤ መብት፡ ያለው ። ወደቂቀ፡ አርንሰ፡ ብሑታን፡ በበ፡ አብሬቶሙ ። ሳቁኤል፡ ብሑት፡ ዲበ፡ መናፍስት ። ኦ፡ ዛቲ፡ ዕለት፡ ብሕት፡ ከመ፡ አብ፤ ህሉት፡ ከመ፡ ወልድ፤ ስፍንት፡ ከመ፡ መንፈስ፡ ቅዱስ፡ (፩ሄና፡ ፳፱፡ ፩ ። ስንክ፡ ሐምሌ ። ቅዳ፡ አት) ።

**መባሕት፤—መብት፤—በዊሕ፤ በሐ፡ ተበውሐ ።**

**በሐተ፤ (ዋሐደ ። ዐረ፡ በሑተ፤ ጥሩ፡ ኾነ)፤** ባተ፡ ገባ፡ ተሾመ፤ ተዠመረ፡ ተቈጠረ፤ የወር፡ ያመት ። ብቸኛ፡ ኾነ፤ ከሰው፡ ተለየ፡ ተነጠለ፤ እንደ፡ መባቻ፡ ቀን፡ አንድ፡ ተባለ ። መጽሐፍ፡ ግን፡ በበሐተ፡ ፈንታ፡ ባሕተወ፡ ይላል ።

**ብሑት፤** የባተ፤ ብቸኛ፡ የኾነ፤ ብቸኛ ። ብሑት፡ ልደት ። ብሑት፡ ዘእንበለ፡ አዝማድ ። መነኮስ፡ ብሑት ። ገዳማዊ፡ ብሑት፡ (ኪዳ ። ቅዳ፡ ኤጲ ። ፊልክ፡ ፫ ። ስንክ፡ የካ፲) ።

**ባሕቱ፤ (ባሕት)፤** ብቻ፤ እንጂ፤ ግን፡ ግና፡ ነገር፡ ግን ። እንጂ፡ ሲኾን፡ ዐቢይ፡ አገባብ፡ ነው፤ እንደ፡ አኮኑና፡ እንደ፡ ዳእሙ፡ በፊትም፡ በኋላም፡ ይገባል ። በዝንቱ፡ ባሕቱ፤ ብቻ ። ባሕቱ፡ ዘንተ፡ ረከብኩ ። መበለተ፡ ባሕቱ፡ ኢታውስብ፤ ግን፡ (ዘፍ፴፱፡ ፲፩ ። መክ፯፡ ፴ ። ዘሌ፳፩፡ ፲፱) ። ብቻ፡ የሚኾን፡ አገባብ፡ ባሕቱ፡ ብቻ፡ ነበረ፤ በመጽሐፍ፡ ግን፡ ዳእሙ፡ አብዶት፡ እጅግ፡ አይገኝም ። ያባተበትም፡ ምክንያት፡ መላሽና፡ ጣፊ፡ በባሕቱ፡ ስፍራ፤ ኢትፍራህ፡ ተአመን፡ ዳእሙ ። ወለዘሂ፡ ቈላፍ፡ በአሚን፡ ዳእሙ፡ ያጸድቀ ። እሉኑ፡ ዳእሙ፡ ደቂቅከ፡ እያሉ፡ ስላገቡት፡ ነው ። የዳእሙን፡ ፍች፡ ተመልከት፡ (ዕር፲፱፡ ቍ፹፩) ።

**ባሕቲት፤ (ዕብ፡ ልበድ)፤** ብቻ፤ ብቸታ፤ ብቻንት፤ ጥሬት፤ ጥሩነት ። ቅጽልና፡ ዐጸፋ፡ ይኾናል፤ ባሕቲቱ፡ ታ፡ ቶሙ፡ ቶን፤ ባሕቲትየ፡ እያለ፡ እስከ፡ ሥር፡ ይረባል፤ ሳይዘረዘር፡ ግን፡ በሳድስነት፡ አይገኝም፤ እንደ፡ ለልና፡ እንደ፡ ባሕቱ፡ ነው ። ኖኅ፡ ባሕቲቱ ። ኀጢአት፡ ባሕቲታ ። ለከ፡ ለባሕቲትከ ። እሉ፡ ባሕቲቶሙ ። አነ፡ ባሕቲትየ ። ኪያሁ፡ ባሕቲቶ ። ባሕቲት፡ ዘበልዐ፡ እስመ፡ ይመውት፡ ባሕቲቶ ። (ኩፋ፡ ፭ ። ውዳ፡ ፯ ። መዝ፡ ፶ ። ዮሐ፲፯፡ ፳ ። ኢዮ፩፡ ፲፭ ። ማቴ፱፡ ፲ ። ቅኔ) ። በፈቃደ፡ ባሕቲቱ፤ በራሱ፡ በብቻው፡ ፈቃድ ። በባሕቲቶሙ፡ ተስእልዎ፤ ብቻቸውን፡ በኾኑ፡ ጊዜ፤ ኹነው ። ሠሐቀት፡ በባሕቲታ፤ በራሷ፤ በሰውነቷ ። ዕብራይስጡ፡ ግን፡ ብቂርባ፡ ይላል ። በሆዷ፡ በልቧ፡ በሐሳቧ፡ ብቻ፤ ጥርስ፡ ሳይገጥ፡ ከንፈር፡ ሳይገለጥ፡ ማለት፡ ነው ። አቀምን፡ እንተ፡ ባሕቲቶን፤ ለብቻቸው፤ እየብቻቸው፤ ብቻቸውን፤ ለ፡ እየ፡ ን፡ የእንተ፡ ፍች፡ ነው፡ (ፍ፡ ነ፡ ፯ ። ማር፪፡ ፲ ። ዘፍ፲፰፡ ፲፪ ። ፳፩፡ ፳፰) ።

**መብሕት፤** ፍጹም፡ ጥሩ፤ እድፍ፡ ጕድፍ፡ እንከን፡ የሌለበት፤ ያልተነካ፡ ድፍን ። ምሥዋዕ፡ ዘእብን፡ መብሕት፡ ዘኢተወቅረ፡ (ኢያ፰፡ ፴፫) ።

**ባሕተወ፤ (በሐተ)፤** ብቸኛ፡ ኾነ፤ ተለየ፤ ተነጠለ ። ኢባሕተወ፡ መለኮቱ፡ እምትስብእቱ፡ ወኢትስብእቱ፡ እመለኮቱ፡ (መጽ፡ መስ) ። ዐዘነ፡ አለቀሰ፤ ፈራ፡ ተጨነቀ፤ ብቻ፡ ከመኾን፡ የተነሣ ። ምናሴ፡ ንሥሠ፡ ገጸ፡ እግዚአብሔር፡ ወባሕተወ፡ በሕቁ፡ እምቅድመ፡ ገጹ፡ ለአምላኩ፡ አበዊሁ፡ ወጸለየ፡ (ዲድ፡ ፯ ። ፪ዜና፡ ፴፫፡ ፲፪) ። በባሕተወ፡ ፈንታ፡ ተባሕተወ፡ ይላል፤ በዐገለ፡ ፈንታ፡ ተዐገለ፡ እንዲል ። ፍችው፡ አንድ፡ ነው፤ አይለወጥም ። ወእመ፡ ወለደ፡ ኢተባሕተወ፡ አቡሁ፡ ሎቱ ። አመ፡ ይትባሐት፡ ወይትባአስ፡ ምስለ፡ ጎልያድ ። እለ፡ ይትባሐተዉ፡ ውስተ፡ አድባር፡ ወየዐይሉ፡ ውስተ፡ ገዳማት፡ (ቅዳ፡ ግሩ ። መዝ፡ ፻፶፩ ። አፈ፡ ተ፡ ፲) ።

**ባሕትዎ፤ ተባሕትዎ፤** ብቻ፡ ብቸኛ፡ መኾን፤ ብቻኝነት ። ወፂአ፡ እማኅበር፡ ወተባሕትዎ፡ ውስተ፡ በዳ፡ (ፊልክ፡ ፵፱) ።

**ባሕታዊ፤ (ዊት፡ ውያን፡ ያት)፤** ብቻውን፡ የሚኖር፤ ባታይ፡ ባተሌ፤ ብቸኛ፡ ስደተኛ፤ የዘመድ፡ ድኻ ። እስመ፡ ባሕታዊ፡ ወነዳይ፡ አነ ። ከመ፡ ዖፍ፡ ባሕታዊ ። ርድአኒ፡ ሊተ፡ ለባሕታዊት ። ተማሀልኩሙ፡ ለክልኤ፡ ባሕታውያን፡ (መዝ፡ ፳፬ ። ፻፩ ። አስቴ፬፡ ፲፯ ። ጦቢ፰፡ ፲፯ ። መዝ፡ ፳፯) ።

—፤ በቁሙ፤ መናኝ፡ መነኰሴ፤ ዝጉሕ፤ ከዓለም፡ ከሰው፡ ተለይቶ፡ ከአራዊት፡ ጋራ፡ በዱር፡ በጣሻ፡ በገደል፡ በዋሻ፡ የሚኖር፤ ከቀድሞ፡ ሰዎች፡ እንደ፡ ኤልያስ፡ እንደ፡ ዮሐንስ፤ ከኋላ፡ ሰዎች፡ እንደ፡ ጳውሊና፡ እንደ፡

እንጦንስ ፣ ያለ ። ጳውሊ ፣ ፹ ፣ ዘመን ፣ ሰው ፣ ሳያይ ፣
በበረሐ ፣ ኑሯል ፤ ስለዚህ ፣ ሊቀ ፣ ባሕታውያን ፣ ይባላል ፣
(ስንክ ፣ የካ፪) ። ባሕታዊ ፡ ዘሞቅሐ ፡ ርእሶ ፡ በጾማ
ዕቱ ። መነኮስ ፡ ባሕታዊ ። ወነበረ ፡ ሐቅለ ፡ ምስለ ፡
አራዊት ፡ (ፊ ፣ መ ፣ ፫ ፣ ፯ ። ስንክ ፣ ታኅ፳፫ ። ማርቆ ፣ ፲፫) ።

**ብሕትው ፤ (ዋን ፡ ዋት ፣ ቱት)** ፤ ብቻ
ውን ፣ የኾነ ፤ ብቻውን ፣ የሚኖር ፤ ብቸኛ ፣ ለብቻው ፣
የቆመ ፣ የተለየ ፤ ገላ ፣ አካል ፣ ሰውነት ። ትኩን ፡ ብሕ
ቱተ ፡ በእንተ ፡ ጸሎት ። ብሕቱትየ ፡ (ኪዳ ። መዝ ፣ ፳፩ ።
፴፱) ።

**ብሕታዌ** ፤ ብቻ ፣ መኾን ፤ ብቻ ፣ ብቸታ ፤ ብ
ቻነት ። ትምህርት ፡ መዜንው ፡ በውስተ ፡ ሐዊር ፡ ወ
በብሕታዌ ። ሰላም ፡ ለብሕታዌሁ ። ብሕታዌ ፡ ንብ
ረት ፡ (ፈላስ ። ስንክ ፣ ጥር፳፪ ። ግንቦ፩) ።

**ብሕትውና** ፤ ባሕታዊነት ፤ ብቸኝነት ፤ ፍጹም ፣
ምናኔ ። በእንተ ፡ ዘከመ ፡ ይኄይስ ፡ ሥርዐተ ፡ ብሕት
ውና ፡ እምሥርዐተ ፡ ማኅበር ። ለመደ ፡ ብሕትውና ።
በኣተ ፡ ብሕትውና ፡ (ፊልክ ፣ ፩ ። ስንክ ፣ ሐም፲ ። ፊ ፣
መ ፣ ፫ ፣ ፯) ።

**ብሕትውናዊ** ፤ የብሕትውና ፤ የባሕታዊነት ፤
ግብር ፣ አኗኗር ፣ ሕግ ፣ ሥርዐት ። ምንዙስና ፡ ብሕትው
ናዊት ፡ (ገድ ፣ ተክ) ።

**ተብሕተወ ፤ (ተደራራጊ)** ፤ ተለያየ ፤ ተነጣ
ጠለ ፤ እየብቻው ፣ ኾነ ።

**በኊበኆ ፤ (ብሕአ)** ፤ ቦኸቦኸ ፤ ቦነቻ ፤ በሰ
በሰ ፤ ተበላሸ ፤ ነቀዘ ፣ ጠነጠነ ፤ ተላ ፤ ገማ ፣ ከረፋ ፣ በሸቀጠ ፤
የንጨት ፣ የግንድ ፣ የገላ ፣ የቍስል ። በኊበኈ ፡ ሥጋየ ፡
በዕፄያት ። በቍስለ ፡ ኀጢአት ፡ ሥጋየ ፡ በኊበኈ ፡
ወጼአ ፡ (ኢዮ፯ ፣ ፭ ። ስንክ ፣ ነሐ፳፩) ። ይበልዕ ፡ ይት
ክዐው ፣ በማለት ፣ ፈንታ ፣ ይበኈብኍ ፣ ይላል ፣ ስሕተት ፣
ነው ፣ (ኢዮ፲፰ ፣ ፲፫ ። ሕዝ፯ ፣ ፲፯ ። ፳፩ ፣ ፯) ።

**ብኊብኍ ፤ ብኅቡኅ** ፤ የቦኸቦኸ ፤ የቦነቻ ።
ከመ ፡ ዕፀ ፡ ብኅቡኅ ፡ (ኢዮ፳፱ ፣ ፳ ። ፵፩ ፣ ፲፰) ።

**ብኊባኄ ፤ ብኅባኄ** ፤ ግማት ፣ ክርፋት ፤ ሽ
ታው ፣ የሚያስቀቅ ፣ የሚጐፈንን ። እሬኢ ፡ ንስንተ ፡
ሥጋየ ፡ ከመ ፡ ብኅባኄ ፡ አንበሳ ፡ (ኢዮ፯ ፣ ፯) ። ባለብ
ሉዮች ፣ ግን ፣ ኀይል ፣ ብርታት ፣ ይሉታል ።

**ብኅባኄ፤—መፈጠር፤—በሕብሐ ።**

**ቤጣ— ፤ ስመ ፣ ፊደል፤—በየጣ ።**

**በጢሕ ፤ ሖት ፤ (በጥሐ ፣ ይበጥሕ ፣ ይብ
ጣሕ ። ዕብ ፣ ባጻዕ ። ሱር ፣ ብዛዕ ። ዐረ ፣ ፀፀዐ)** ፤
መብጣት ፤ መፍቃት ፤ መተፍተፍ ፤ መሠንበጥ ፤ ለፈሙስ ፣
ወይም ፣ ለጌጥ ። (ተረት) ፤ ሲያጌጡ ፣ ይመላለጡ ። ጠቢ
ባን ፡ ሶበ ፡ ይበጥሑ ፡ በጽኑዕ ፡ እስከ ፡ ይረክብዎ ፡ ለ
ሕማም ፡ ይጠበቡ ፡ ሶቤሃ ፡ በዘያዐርፍዎ ፡ ለሕ
ሙም ፡ እምተሀውከ ፡ ወእምድንጋፄ ፡ ነፍስ ፤ ወኢ
ይበጥሑ ፡ ዳግመ ፤ አላ ፡ ይወድዩ ፡ ፈውሰ ። ሚ ፡
መጠነ ፡ ይጼዐሉ ፡ እለ ፡ ይበጥሑ ፡ እምእለ ፡ ይበ
ጥሕዎሙ ። ኢትብጥሑ ፡ ሥጋክሙ ፡ (አፈ ፣ ተ፴ ።
ዘሌ፳፩ ፣ ፭) ።

**በጥሐ ፤ (ዕብ ፣ ባጣሕ)** ፤ አመነ ፤ ተወከለ ፤
ተስፋ ፣ አደረገ ፤ ዐረፈ ፣ ተዘለለ ፤ ገላውን ፣ ሰደደ ፤ ምን ፣
አለብኝ ፣ አለ ፤ የድውይ ፣ የባለጤና ።

**በጣሒ ፤ (ሒት ፣ ሕያን ፣ ያት)** ፤ የሚበጣ ፤
በጭ ፤ በጪ ። በጣሕያን ፡ (አፈ ፣ ተ፴) ።

**ተበጥሐ** ፤ ተበጣ ፣ ተፈቃ ፤ ተተፈተፈ ፤ እንደ ፣
ሱዳን ።

**ብጡሕ ፤ (ሓን ፣ ሓት ፣ ጥሕት)** ፤ የተበጣ ፤
ብጥ ፣ ሥንብጥ ፤ ትፍትፍ ።

**ብጥሐት** ፤ መብጣት ፤ መበጣት ፤ አበጣጥ ፤ ብ
ጥንት ፤ ብጥታት ። ብጥሐተ ፡ ገጽ ፡ (መ ፣ ፈ--፲) ።

(ጥ) **በጢሕ ፤ (ሓት ። ዐረ ፣ በጢኅ)** ፤ በቁሙ ፤
የዱባ ፣ ዐይነት ፣ ተክል ፤ ውስጠ ፣ ቀይ ፣ ክብ ፣ እንክብል ፤
ማር ፣ ማር ፣ የሚል ፤ በጥተው ፣ አይተው ፣ የሚገዙት ።
በምጥዋ ፣ ብርጭቅ ፣ ይባላል ።



በጢሕ ፣

**በጢጥ ፤ ጦት ፤ (በጠ ፣ ይበጥጥ ፣ ይብ
ጥጥ)** ፤ መበጠጥ ፤ በጠጥ ፣ ፋንድያ ፣ መጣል ፤ ባጥ ፣ እ
ንጣጥ ፣ ማለት ፣ ለመራገጥ ፣ የእንስሳ ። መዝለል ፣ ጮቤ ፣
መምታት ፣ መራገጥ ፣ የጐበዛዝት ። በጥ ፣ ለጥ ፣ ሰጥ ፣
ብሎ ፣ በልብ ፣ መተኛት ፣ ዝርባን ፣ ለገራፊና ፣ ለረጋጭ ፣
አስመችቶ ፣ መስጠት ። ትግሬ ፣ በጥ ፣ በል ፤ ዐማራ ፣ ው
ደቅ ፣ ወይም ፣ ጣለው ፣ እንዲል ።

**በጣጣ ፤ በጣጥስ ፤ (ዐረብ)** ፤ ድንች ፤ የድ
ንች ፣ ወገን ።

**በጥበጠ** ፤ በቁሙ ፤ በጠበጠ ፤ ጣለ ፤ የኮሶ ፣ የድ
ፍድፍ ፣ የጠጅ ። ጥሕለን ፣ ተመልከት ። ለቤተ ፣ ክሲያ
ንም ፣ ይኾናል ። ደብረ ፣ በጥብጥ ፣ እንዲሉ ።

**በጢል ፤ ሎት ፤ (በጠለ ፣ ይበጥል ፣ ይ
ብጥል ። ዕብ ፣ ባጣል ። ሱር ፣ ቤጤል ። ዐረ ፣
በጠለ)** ፤ መቦዘን ፤ ማረፍ ፤ መሰንፍ ፤ ሥራ ፣ መፍታት ።
መጥፋት ፣ መፍረስ ፤ መሻር ፣ መቅረት ፤ ከንቱ ፣ ብላሽ ፣
መኾን ። ኢበጠለ ፡ ጸልዐ ፡ አላ ፡ ጸንዐ ። በጠለት ፡ ት
ንቢት ፡ በስብከተ ፡ ሐዋርያት ። ትበጥል ፡ እንተ ፡ መ

ክርኩ ። በጠለ ፡ ዕፂበ ፡ ትእዛዝ ፡ እምኔየ ። በጠለ ፡ ተአምኖቱ ፡ ቦቱ ። ዘስሕተታት ፡ በጠላ ፤ በትእዛዝከ ፡ (መጽ ፡ ምስ ። ክብ ፡ ነገ ። አርጋ ፡ ፳ ። ፍ ፡ ነ ፡ ፺፱ ፡ ፫ ። ኪዳ) ። በበጠለ ፡ ፈንታ ፡ ተበጥለ ፡ ይባል ፤ አያስኝም ። እመ ፡ ትትቤጠል ፡ ኦሪት ፡ በሃይማኖት ፡ (ቄር ። ገድ ፡ አዳ) ።

**በጣሊ ፤ (ሊት ፡ ልያን ፡ ያት ፤ በጠልት) ፤** የሚጠፋ ፡ ጠፊ ፤ ፈራሽ ፡ ቀሪ ፡ ኀላፊ ። መንግሥት ፡ ምድር ፡ በጣሊ ። መርዓ ፡ በጣሊ ፡ (ስንክ ፡ ሐምሯ ። መስጃ፯) ።

**ብጡል ፤ (ላን ፡ ላት ፡ ጥልት) ፤** የበጠለ ፤ የጠፋ ፡ ጥፉ ፤ መጥፎ ፤ ብልሹ ፤ ከንቱ ። ስብሐት ፡ ብጡል ። ዝንቱ ፡ ብጡል ። ኦሪተ ፡ አይሁድ ፡ ብጡል ። ዛቲ ፡ ተደምሮ ፡ ብጥልት ፡ እምሕገ ፡ ስብሳብ ፡ ወእሰምያ ፡ ኀጢአተ ፡ (ፊልክ ፡ ፳፱ ። ገድ ፡ ተክ ። ፍ ፡ ነ ፡ ፺፪ ፡ ፩ ። አቡሻ ። ፈ ፡ መ ፡ ፲ ፡ ፫) ። ድልድል ፡ ቅምጥል ፤ ሥራ ፡ ፈት ፡ አውታታ ፤ ወይም ፡ ዘመናይ ፡ ጌታ ። ብጡል ፤ ወሌ ፡ ብጡል ፡ እንዲል ፡ (የጁዬ) ።

**ብጥለት ፤** መጥፋት ፤ አጠፋፍ ፤ ጥፋት ፤ ከንቱነት ። እስመ ፡ አበው ፡ ዘዝንቱ ፡ ዘመን ፡ ረሰይዎ ፡ ብጥለተ ፡ (ፈ ፡ መ ፡ ፲፫) ።

**አብጠለ ፤** አባጠለ ፤ አብጠለጠለ ፤ አበጠለለ ፤ አባጨ ፡ ነቀፈ ፤ አጸየፈ ፡ (ዐማርኛ) ። አጠፋ ፡ አበላሸ ፤ ከንቱ ፡ አደረገ ፤ አስቀረ ፤ ከለከለ ፤ አስተጓጐለ ፤ ዐሎ ፡ አለ ። አብጠለ ፡ ተቃትሎቶሙ ። አብጠልከ ፡ ነገረከ ። አብጠለ ፡ ነሚአ ፡ ሕልያን ፡ በእንተ ፡ ሚመተ ፡ ክህነት ። ሶበ ፡ ኮኑ ፡ ሰይጣናት ፡ የሐውሩ ፡ ኀበ ፡ ብሑታን ፡ ከመ ፡ ያስሕትዎሙ ፡ ወያብጥልዎሙ ፡ እምተግባሮሙ ፡ መንፈሳዊ ። እለ ፡ ያበጥሉ ፡ ልደቶ ፡ እምአብ ፡ እምቅድመ ፡ ኵሉ ፡ ፍጥረት ፡ (ዮሴፍ ። አቡሻ ፡ ፶ ። ፊልክ ፡ ፴ ። ዲድ ፡ ፴፫) ። በአብጠለ ፡ ፈንታ ፡ በጠለ ፡ ይላል ፤ አያስኝም ። ኦሪተ ፡ ንቤጥሎኑ ፡ በሃይማኖት ። ይቤጥሎሙ ፡ ጠቢብ ፡ ጳውሎስ ። በጠለ ፡ እግዚ ፡ እምኔሆሙ ፡ መንግሥተ ፡ (ቄር) ።

**አብጣሊ ፤ መብጠሊ ፤** የሚያጠፋ ፡ አጥፊ ፤ አስጠፊ ። ከመ ፡ ይኩን ፡ ዝንቱ ፡ መብጠሌ ፡ ሀጕሎሙ ፡ ለግብጽ ፡ (አፈ ፡ ድጓ፯) ።

**ብጥም ፤ ቡጥም ፤ (ዐረ ፡ ቡጥም ። ሱር ፡ ቤጥማ) ፤** በቁሙ ፤ የዛፍ ፡ ስም ፤ ጠርቤንቶስን ፡ እይ ፤ ከዚህ ፡ ጋራ ፡ አንድ ፡ ነው ። ይዘብሑ ፡ ታሕተ ፡ ባሉጥ ፡ ወቡጥም ፡ ወገውዝ ፡ ወሰውዝ ፡ (ሆሴ፬ ፡ ፲፫ ። አቡሻ ፡ ፺፯) ።

**በጢር ፤ ሮት ፤ (በጠረ ፡ ይበጥር ፡ ይብጥር) ፤** መበጠር ፡ ማበጠር ፤ ማንጠርጠር ፤ ማንፈስ ፡ መንቀስ ፡ የእኽል ፡ የጠጕር ፡ የነገር ። ከግእዝ ፡ ወዳማርኛ ፡ ስለ ፡ ኼደ ፡ ባለቅኔዎች ፡ አይገሱትም ።

**አብጠረ ፤** አስበጠረ ፤ አስነፈሰ ፡ አስነቀሰ ።

**ተበጥረ ፤** ተበጠረ ፤ ተንጠረጠረ ፤ ተነፈሰ ፤ ተነቀሰ ፡ ጥሩ ፡ ኾነ ።

**ምብጣር ፤ (ራት) ፤** ማበጠሪያ ፡ ማንጠርጠሪያ ፤ ሚደ ፤ ስፌድ ፤ ፍርድ ፡ ዳኛ ፡ ወይም ፡ ነቃሽ ፡ ምስክር ፡ ፍትሐ ፡ ነገሥት ።

**በጥሪቃ ፤ (ሮማ ፡ ፓትሪሺያ ። ዐረ ፡ በጥሪቀት) ፤** ታላቅ ፡ ወይዘሮ ፡ ባላባት ፤ የነገሥታት ፡ ወገን ፤ ልዕልት ፤ እግዝእት ። ዛቲ ፡ ይእቲ ፡ ቀዳሚት ፡ በጥሪቃ ፡ ዘሀገረ ፡ ቍስጥንጥንያ ፡ (አዋል ። ገድ ፡ ዳን) ።

**በጢስ ፤ ሶት ፤ (በጠሰ ፡ ይበጥስ ፡ ይብጥስ) ፤** መበጠስ ፡ መበጣጠስ ፤ መቍረጥ ፡ መቈጥቈጥ ፤ የቅጠል ፡ የዕጽቅ ።

**ባጦስ ፤** እምባ(ቧ)ሜ ፡ የሚቈረጥ ፡ የሚቈጠቈጥ ፤ ለጋውን ፡ ልጆች ፡ እየላጡ ፡ የሚበሉት ። (ዘፈን) ፤ ስለሚያለቅስ ፡ ልጅ ፤ እናትኽ ፡ ውሃ ፡ ወርዳለች ፤ እምባሜውን ፡ ታመጣልኻለች ።

**ባጦስ ፤ (ጽር ፡ ባቶስ ። ዕብ ፡ ስኔ) ፤** ጳጦስ ፤ ሳቤቅ ፤ የሾኽ ፡ ቍጥቋጦ ፤ እሾኽም ፡ ዛፍ ፤ ፍሬው ፡ ቀይ ፤ መዐዛው ፡ ሠናይ ። ዕፀ ፡ ባጦስ ፡ (ዘዳ፴፫ ፡ ፲፮ ። ሉቃ፳ ፡ ፴፯) ። ሳቤቅንና ፡ ጳጦስን ፡ እይ ።

**ቤበየ ፤—ሠየ ፡ ጐመዠ ፤—ባበየ ።**

**ቤዝ ፤ (ብ ፡ ቤዛት ፤ አብያዝ) ፤** ጕልሕ ፡ ኮከብ ፤ ኮከበ ፡ ጽባሕ ፡ ብርሃኑ ፡ የሚቦዝ ፡ የሚበዘብዝ ። አንተ ፡ ቤዝ ፡ ኮከበ ፡ ጽባሕ ። አዕይንቲሃ ፡ ይመስል ፡ ሥርቀተ ፡ ቤዝ ። በሰዓተ ፡ ሞታ ፡ ደመነ ፡ ቤዝ ። ቦ ከመ ፡ ኮከበ ፡ ጽባሕ ። ይፈደፍድ ፡ ብርሃነ ፡ እምዘተርፉ ፡ ቤዛት ። ሰላም ፡ ለአዕይንትኪ ፡ ዘተመሰላ ፡ አብያዘ ፡ (ቄድር ። ገድ ፡ ተክ ። ስንክ ፡ መስ፲፩ ። ፊልክ ፡ ፪፻፸ ። ደራሲ ። አርጋ ፡ ፯ ። ኢዮ፮ ፡ ፱) ።

**ቤዘ ፤ (ይበይዝ ፡ ይቢዝ ፤ በዩዝ ፡ ዘት) ፤** በራ ፡ አበራ ፤ በዘበዘ ።

**ቤዝዎ ፤ ዎት ፤ (ቤዘወ ፡ ይቤዙ ፡ ይቤዙ ። ዐረ ፡ ባዘ ፤ ሸሸ ። ዕብ ፡ ፋዳ) ፤** መቤዠት ፡ ማዳን ፤ መታደግ ፤ ማስጣል ፤ ከጭንቅ ፡ ከባርነት ፡ ማውጣት ፤ ከባለዳ ፡ እጅ ፡ መግዛት ፤ መዋጀት ፤ ለውጥ ፡ መስጠት ፤ ገንዘብን ፡ ወይም ፡ ራስን ፤ እንደ ፡ ክርስቶስ ። አኮ ፡ በወርቅ ፡ ዘእቤዝወክሙ ። በነፍስክሙኑ ፡ ትቤዝውዋ ፡ ለነፍስየ ። መጽአ ፡ ይቤዝወነ ፡ እምኵሉ ፡ አበሳነ ፡ (ኢሳ፶፪ ፡ ፫ ። ኢዮ፲፯ ፡ ፬ ። መዋሥ ። ዘፀ፲፫ ፡ ፲፫ ። ፴፬ ፡ ፳) ። በቤዘወ ፡ ፈንታ ፡ ተቤዘወ ፡ ይላል ፤ አያስኝም ፤ ተ ፡ ያማርኛ ፡ ነው ። ተቤዘውዎሙ ፡ ለፂዉዋን ። አልቦ ፡ ዘይክል ፡ ተቤዝዎትየ ። ኢያድኅን ፡ ወርቅ ፡ ወኢይትቤዘው ፡ ብሩር ፡ (ዲድ ፡ ፳፩ ። አርጋ ። ስንክ ፡ ሐም፬ ። ዘሌ፳፭ ፡ ፴፩ ፡ ፴፫ ። ፩ጴጥ ፡ ፩ ፡ ፲፰) ። ቤዘወ ፡ የቤዘ ፡ ቅጥይ ፡ እንደ ፡ ኾነ ፡ አስተውል ።

**ቤዛዊ** ፤ (ዊት ፡ ውያን ፡ ያት ፤ ዘውት) ፤ የሚቤዥ ፤ የሚታደግ ፤ ታዳጊ ። ማርያም ፡ ቤዛዊተ ፡ ዓለም ። እስመ ፡ ቤዛዊሃ ፡ ለነፍስየ ፡ አንተ ፡ (ደራሲ) ።

**መቤዝዊ** ፤ ው ፤ ዝኒ ፡ ከማሁ ። መድኅኒት ፡ መቤዝዊተ ፡ እሞ ፡ ቅድስተ ። ወልደከ ፡ መድኅኒ ፡ ወመቤዝወ ። መቤዝወ ፡ ዓለም ፡ (ድጓ ። ስንክ ፡ ታኅሣ ። ቅዳ ፡ ሐዋ ፤ ኤጲ ። ደራሲ) ።

**ቤዛ** ፤ (ዛት) ፤ በቁሙ ፤ ዋጋ ፤ ካሳ ፤ ለውጥ ፤ ምትክ ፤ ዐላፊ ፤ ዋቢ ፤ ዋስ ፤ መድኅን ፤ ተያዥ ፤ ጫማ ፡ ጥላ ፡ ጋሻ ፡ የመቀለው ፡ ኹሉ ። ቤዛ ፡ ነፍሱ ፡ ለብእሲ ፡ ጥሪቱ ፡ ብዕሉ ። አኮ ፡ በቤዛ ። ቤዛ ፡ ሖሉ ፡ ኀጢአትከ ። ማእስ ፡ ቤዛ ፡ ማእስ ፡ (ምሳ፲፫ ፡ ፰ ። ኢሳ፵፫ ፡ ፲፫ ። ኤር፲፭ ፡ ፲፫ ። ኢዮ፪ ፡ ፬) ።

**ቤዛ** ፤ (ደቂቅ ፡ አገባብ) ፤ ስለ ፤ ፈንታ ፤ ምክንያት ። እሜጡ ፡ ነፍስየ ፡ ቤዛ ፡ አባግዐየ ፤ ስለ ፡ በጎቼ ። ዐይን ፡ ቤዛ ፡ ዐይን ፤ ወስን ፡ ቤዛ ፡ ስን ፤ በዐይን ፡ ፈንታ ፤ በጥርስ ፡ ፈንታ ። ተሰቅለ ፡ ቤዛነ ፤ ስለኛ ፡ በኛ ፡ ምክንያት ፤ ወይም ፡ ቤዛችን ፡ ተብሎ ፡ በቂ ፡ ይኾናል ። ቤዛሁ ፡ ሃ ፡ እያለ ፡ ይዘረዝራል ፤ በብትን ፡ እንጂ ፡ በአንቀጽ ፡ አይገባም ።

**አቤዘወ** ፤ አስቤዠ ፤ ቤዛ ፡ አሰጠ ፤ አስለወጠ ፤ አስያዘ ። ታቤዝዉ ፡ ምድረ ፡ (ዘሌ፳፭ ፡ ፳፬) ።

**ተቤዝወ** ፤ **ተቤዘወ** ፤ ተዋጀ ፡ ተገዛ ፤ ቤዛ ፡ አገኘ ፤ ዳነ ፡ ነጻ ፡ ወጣ ። በደሙ ፡ ትትቤዘው ፡ ነፍስ ። እለ ፡ ተቤዘዉ ፡ እምነ ፡ ምድረ ፡ ግብጽ ፤ እለ ፡ ቀደሙ ፡ ተቤዝዎ ። እስመ ፡ እምኢተቤዘውነ ፡ እመ ፡ ኢኮነ ፡ ከመ ፡ ዝ ፡ (ዘሌ፲፯ ፡ ፲፩ ። ራእ፲፬ ፡ ፫ ፡ ፲፬ ። ቄር) ።

**ቢዝው** ፤ (ዋን ፡ ዋት ፡ ዙት) ፤ የዳነ ፤ የተዋጀ ፡ ውጁ ፤ ቤዛ ፡ ያገኘ ።

**ቤጣ** ፤ (ጽር ፡ ቤታ) ፤ ፪ኛ ፡ ፊደል ፡ በ ፡ ቤት ፡ በጽርእና ፡ በቅብጥ ። አልፋ ፡ ወቤጣ ። ምንት ፡ ውእቱ ፡ ቤጣ ፡ (ሥር ፡ ጳኵ ። ኪዳ) ።

**ቤጤልዋ** ፤ ስመ ፡ ሀገር ፡ (ዮዲ፬ ፡ ፮) ።

**ቤለ** ፤ **ይቤ** ፤ **ይበል** ፤—**አለ** ፤—**ብህለ** ፡ **ይብል** ፡ **ይብሀል** ።

**ቤል** ፤ (ዕብ) ፤ የባቢሎን ፡ ክፉል ፤ ስመ ፡ ጣዖት ፡ ባቢሎናዊ ፤ ናቡከደነጸር ፡ ያቆመው ፡ ምስል ። ባለ ብሎዮች ፡ ግን ፡ የፈረስ ፡ ምስል ፡ ይሉታል ፡ (ኢሳ፵፮ ፡ ፩ ። ዳን፫ ፡ ፩) ።

(ጥ) **በይኖ** ፤ **ኖት** ፤ (**በየነ** ፡ **ይቤይን** ፡ **ይበይን** ። **ዐረ** ፡ **ባነ** ። **ዕብ** ፡ **ባን**) ፤ መበየን ፤ መለየት ፡ መምረጥ ፤ ማስተዋል ፡ መመልከት ፤ ለይቶ ፡ ማወቅ ፡ መረዳት ፤ አስተውሎ ፡ መፍረድ ። ይቤይንዎሙ ፡ ወያነጽሕዎሙ ። ለምንት ፡ ኢትቤይን ፡ እምውስቴቶን ፡ እለ ፡ የዐብያሆን ። ወሠርዌ ፡ ዘውስተ ፡ ዐይንከ ፡ ኢትቤይን ። ይቤይኖ ፡ ለኃጥእ ፡ እንበለ ፡ ይግበር ፡ ኀጢአተ ፡ (ዳን፲፪ ፡ ፲ ። ሄርማ ። ማቴ፯ ፡ ፫ ። ቅዳ ፡ ኤጲ) ።

በበይኖ ፡ ፈንታ ፡ አበይኖ ፡ ይላል ፤ አያሰኝም ። ሕቱ ፡ በአበይኖ ፡ (ቅዳ ፡ አት ። ፩ቆሮ ፡ ፲፬ ፡ ፲፮) ።

**በያኒ** ፤ (ኒት ፡ ንያን ፡ ያት) ፤ የሚበይን ፡ በያኝ ፤ ዐዋቂ ፡ ፈራጅ ፤ አስተዋይ ፤ ዳኛ ፡ መምር ።

**መበይን** ፤ (ንት ፡ ናን ፡ ናት) ፤ ዝኒ ፡ ከማሁ ። ኢነሣኤ ፡ ገጽ ፡ መበይን ፡ (ዲድ ፡ ፬) ።

**አበየነ** ፤ አስበየነ ፡ አስፈረደ ፤ አስለየ ። አስረዳ ፤ አስታወቀ ። ንፈቅድ ፡ ከመ ፡ ታበይን ፡ ለነ ፡ ስምዓታተ ። ያቤይን ፡ ሎሙ ፡ ክሕደቶ ። ከመ ፡ ታበይን ፡ ዐመፃየ ። አበይኖት ፡ (ፊልክ ፡ ፫ ። ስንክ ፡ ሠኔ፯ ። ዮሴፍ ። ገድ ፡ አዳ) ።

**ተበየነ** ፤ ተለየ ፤ ታወቀ ፡ ተረዳ ፤ ታየ ፡ ተገለጠ ። በከመ ፡ ተበየነ ፤ ወበእንተ ፡ ተበይኖ ። ውእቱኬ ፡ ይትቤየን ፡ እምግባረ ፡ ማርታ ፡ ወማርያም ። ናሁ ፡ ተበየነ ፡ ለከ ፡ ጥያቄ ፡ ነገርየ ። ተበየነ ፡ ንዝህላልከ ፡ (ፊልክ ፡ ፫ ። ፶፬ ። ዮሴፍ) ።

**ብዩን** ፤ (ናን ፡ ናት ፡ ይንት) ፤ የተለየ ፤ የታወቀ ፤ የተረዳ ፤ ግልጥ ፡ ጉልሕ ። ዝንቱ ፡ ብዩን ፡ (ዮሴፍ) ።

**ብያኔ** ፤ (ያት) ፤ መለዮ ፤ ልዩነት ፤ በቁሙ ፤ ብይን ፡ ፍርድ ፤ አፈራረድ ፤ ፈሊጥ ፡ ዕውቀት ፤ ሥርዐት ። ማእምረ ፡ ብያኔ ። ብያኔ ፡ ልባዊ ። ብያኔ ፡ ሮማዊ ፡ (ታሪ ፡ ነገ ። ፍ ፡ ነ ፡ ፱) ።

**በይነ** ፤ (**በይን** ። **ዕብ** ፡ **ቤን** ። **ሱር** ፡ **ባይናይ** ። **ዐረ** ፡ **በይነ** ፤ **ማእከል**) ፤ ዐቢይና ፡ ደቂቅ ፡ አገባብ ። ስለ ፤ ምክንያት ። ዐቢይ ፡ ሲኾን ፡ ዘን ፡ በር ፡ ከፋች ፡ አድርጎ ፤ ተሰብአ ፡ በይነ ፡ ዘአፍቀረ ፡ ሰብአ ፤ ተቀብዐ ፡ በይነ ፡ ዘተሰብአ ፤ ተሰምየ ፡ መሲሐ ፡ በይነ ፡ ዘተቀብዐ ፡ እያለ ፡ ይገባል ። (ዕር፲፱ ፡ ቊ፳፰) ። ደቂቅ ፡ ሲኾን ፡ እንደ ፡ ቤዛ ፡ በብትን ፡ ይገባል ፤ በይነ ፡ ምንት ፤ ስለ ፡ ምን ፡ በምን ፡ ምክንያት ። በይኑ ፡ በይና ፡ በይንከ ፡ ኪ ፡ ክሙ ፡ ክን ፡ እያለ ፡ ይዘረዝራል ።

**እንበይነ** ፤ (**እን** ፡ **በይነ**) ፤ ዝኒ ፡ ከማሁ ፤ ስለ ። እን ፡ ትርፍና ፡ ተውሳክ ፡ አዳማቂ ፡ ነው ፤ ፍች ፡ የለውም ። እንበይነ ፡ ዘኢበልዑ ። እንበይነ ፡ መኑ ፡ ይብል ። እንበይነ ፡ ምጽዋት ። ላሕም ፡ ዘእንበይነ ፡ ኀጢአት ። እንበይነ ፡ ዝንቱ ፡ (ስንክ ፡ ሚያ፱ ። ዮሐ፲፫ ፡ ፳፪ ። ሚራ፳፱ ፡ ፱ ። ዘፀ፳፱ ፡ ፴፮ ። ቲቶ፩ ፡ ፩) ።

**በበይነ** ፤ (**በ** ፡ **በይን**) ፤ ዝኒ ፡ ዓዲ ፡ ከማሁ ፤ ስለ ። በ ፡ እንደ ፡ እን ፡ አዳማቂ ፡ ነው ፤ ሥራ ፡ የለውም ። በበይነ ፡ ነፍሱ ፡ ለዝንቱ ፡ ብእሲ ። በበይነ ፡ ዚአክሙ ። አኮ ፡ በበይነ ፡ ወርቅ ። በበይነ ፡ እግዚ ። በበይነ ፡ መኑ ። በበይነ ፡ ምንት ፡ (ዮና፩ ፡ ፲፬ ። ሚክ፫ ፡ ፲፪ ። ኢሳ፵፰ ፡ ፲ ። ፳፱ ፡ ፲፩ ። ፩ነገ ፡ ፲፬ ፡ ፴፰ ። ሚል፩ ፡ ፪) ።

**በይን** ፤ ብቻ ፤ ርስ ፡ ራስ ፤ ባለቤት ፤ እኔ ፡ የሚል ፡ የተለየ ፡ አካል ። ፩ ፡ ወገን ፤ ፩ ፡ ክፍል ፤ ፩ ፡ ፈርጅ ፤ ነጠላ ፡ ቀንጃ ።

**በይኑ**፤ ለሊሁ፤ ብቻው፤ ርሱ፤ ራሱ፡ ባለቤቱ።

**በበይኑ**፤ በብቻው፤ በራሱ፡ ወይም፡ ለብቻው፤ ብቻውን። ጳማዊ፡ ወፈጻሜ፡ መልእክት፡ ዘበበይኑ፡ (ስንክ፡ ኅዳ፴)።

**በበበይኑ**፤ (በበ፡ በይኑ)፤ በየራሱ፡ በየብቻው፤ ራስ፡ ራሱ፤ ብቻ፡ ብቻው። በበን፡ ተመልከት። አናብስት፡ መሠጥ፡ ወመንኰራዂራት፡ ዘበበ፡ በይኑ፡ (ስንክ፡ መጋ፴)።

**በይናት**፤ ኹለት፡ ወገን፤ ኹለት፡ ክፍል፤ ጥንድ፤ ዘውግ፡ መንታ፤ እንደ፡ እጅና፡ እግር፡ ያሉ፤ ተባባሮች፡ ተንጻጻሮች፤ ተመሳሳዮች።

**በበይናት**፤ በኹለት፡ ወገን፤ በኹለት፡ ክፍል፤ ኹለት፡ ወገን፡ ኹሞ።

**በበይናቲሁ**፤ ርስ፡ በርሱ፤ አንዱ፡ ካንዱ፡ ጋራ። በበይናቲሃ፡ ከ፡ ቲን፡ እያለ፡ ይዘረዝራል። ተባሀሉ፡ በበይናቲሆሙ። ተኣምኑ፡ በበይናቲክሙ፡ (ዘፍ፵፪፡ ፳፩። ቅዳ)።

**በዪጽ**፤ **ጾት**፤ **(ቤጸ፡ ይበይጽ፡ ይቢጽ። ዕብ፡ ባጻዕ። ዐረ፡ በፀዐ)**፤ መለየት፡ መምረጥ፤ አስተካከሎ፡ መቍረጥ። ወቤጸ፡ ያዕቆብ፡ አባግዒሁ። እበይጽ፡ እምውስቴትክሙ፡ ኃጥኣነ። ዘይበይጽ፡ በክናፍሪሁ፡ ዡሎ፡ እኩየ፤ ለየ፡ (ዘፍ፴፡ ፵። ሕዝ፳፡ ፴፰። ምሳ፲፯፡ ፴)።

—፤ መንጣት፡ መገርጣት፤ ብጭጭ፡ ማለት፤ ዕንቍላል፡ ወይም፡ የበሰለ፡ ቅጠል፡ መምሰል።

**በያጺ**፤ **(ጺት፡ ጽያን፡ ያት)**፤ የሚለይ፤ መራጭ፤ ቈራጭ።

**ተበይጸ**፤ ተለየ፤ ተመረጠ፤ ተገለለ።

**ብዩጽ**፤ **(ጻን፡ ጻት፡ ይጽት)**፤ የተለየ፤ ልዩ፡ ምርጥ።

**ቢጽ**፤ **(ዐረ፡ ጻሕብ፤ ቀሪብ፤ ሺሪክ። ዕብ፡ ሐቤር፤ ሬዕ)**፤ ባልንጀራ፤ እኩያ፡ አምሳያ፤ ወንድም፡ መንቲያ፤ ወዳጅ፡ ዘመድ፤ ወገን፡ ጎረ፡ ቤት፤ ጓደኛ፡ ባልደረባ፡ አቻ፡ ሚስት፤ ዘማች፡ ወታደር፡ ሰራዊት፤ ኅብረት፡ አንድነት፡ ትክክልነት፡ ያለው፡ ማናቸውም፡ ኹሉ። ባለመጣፎች፡ መጣፋቸውን፡ ተከትለው፤ ቢጽ፡ እንደ፡ ሰብእ፡ ውስጠ፡ ብዙና፡ አስተጋባኢ፡ ነው፤ ላንድም፡ ለብዙም፡ ለወንድም፡ ለሴትም፡ ይነገር፡ ይላሉ፤ ባለቅኔዎች፡ ግን፡ ቢጽና፡ ፀር፡ ላንድ፡ ብቻ፡ እንጂ፡ ለብዙ፡ አይኾንም፡ ይላሉና፡ ፀርን፡ ተመልከት። አፍቅር፡ ቢጸከ፡ ከመ፡ ነፍስከ። ኢኮንኩ፡ አነ፡ እግዚእከ፡ አላ፡ ቢጽከ። ዘያፈቅር፡ ቢጾ፡ ውስተ፡ ብርሃን፡ ይነብር፤ ወዘሰ፡ ይጸልእ፡ ቢጾ። ብእሲ፡ እምቢጹ። ንግበር፡ ሎቱ፡ ቢጸ። ቢጸ፡ እስራኤል፡ ወቢጸ፡ ይሁዳ፡ (ዘሌ፲፱፡ ፲፰። ዕር፡ ኢሳ፰፡ ፭። ፩ዮሐ፡ ፪፡ ፲፡ ፲፩። መክ፬፡ ፬። ዘፍ፪፡ ፲፰። ፩ነገ፡ ፲፭፡ ፴)።

**አብያጽ**፤ ባልንጀሮች፡ (ዳን፯፡ ፳። ማቴ፲፩፡ ፲፯። ዘካ፫፡ ፰)። ኢይትፈለጥ፡ እምአብያጽየ። አጥሪ፡ አግዋሪ፡ እምቅድመ፡ ትሕንጽ፡ አብያተ፤ ወአብያጸ፡ እምቅድመ፡ ትሑር፡ ፍኖተ። አብያጺከ፡ እለ፡ መርቆሬ፡ (አፈ፡ ድ፳፯። ፈላስ። ደራሲ)። በአብያጽ፡ ፈንታ፤ ይከይድዎ፡ ቢጹ፤ ለቢጹ፡ አርዳእ፤ ቢጽ፡ ወራዙት፤ ቢጽ፡ እኩያን፤ ቢጽ፡ ሐሳውያን፤ ኀምስቱ፡ ምእት፡ ቢጽ፡ እያለ፡ ይገኛል፤ የጣፊና፡ የመላሽ፡ ስሕተት፡ ነው። እሬኢ፡ በሰላተ፡ ቢጸ፤ ኹለት፤ ዐይነት፡ በለስ፡ ክፉና፡ መልካም፡ (ኤር፳፬፡ ፫)። ቢጽ፡ የግእዝ፡ ተውሳክ፡ ነው፤ በሌላ፡ አይገኝም።

**ተበየጸ**፤ ባልንጀራ፡ ኾነ፤ ተመሳሰለ፤ ተካከለ፤ ተዋደደ፤ ተሰማማ፤ ተሳተፈ። ውእቱ፡ መነኮስ፡ ዘተባየጸከ። ይትባየጸሙ፡ ለልዑላን። ዘይትባየጾ፡ በማኢድ። በእንተ፡ ዘኀሠሠ፡ ተባይጾተ፡ (ስንክ፡ ሐም፳፰። አፈ፡ ድ፩። ፈ፡ መ፡ ፪፡ ፲፩። ፍ፡ ነ፡ ፬)።

**አስተባየጸ**፤ አመሳሰለ፤ አወዳጀ፤ አቀናጀ፤ አሰማማ። እንዘ፡ ያስተባይጸሙ፡ ምስሌሁ፡ (መጽ፡ ምስ)።

**መስተባይጽ**፤ **(ጽት፡ ጻን፡ ጻት)**፤ የሚያሰማማ፤ የሚሰማማ፤ ስምም፤ ፍቅረኛ። ሰሐቡ፡ ሰኰናሁ፤ ወኮኑ፡ ሎቱ፡ መስተባይጻነ፡ በተጋንዮ፡ ብዙኅ፡ (ስንክ፡ ታኅ፯)።

**ቤጻ**፤ **ብጻ**፤ ብጫ፤ ብጫቴ፤ ዐይነቱ፡ የንቍላል፡ አስኳል፡ ዐደይ፡ የሚመስል፤ አስፈርን፡ እይ።

**ቤቃ**፤ ስመ፡ አምላክ፤ እንደ፡ አካዕ፡ ያለ። ቤ፡ ኹለተኛ፡ አካል፤ ቃ፡ ቃል፡ ቀዳማዊ፤ በሌላው፡ አንቀጽ፡ መቅድመ፡ ቃል፡ ብሎ፡ ይፈታዋል፡ (ሔኖ)።

**ቢራ**፤ **ባሬ**፤ **(ዕብ፡ ቢራህ። ጽር፡ ባሬ)**፤ ስመ፡ ሀገር፤ መዲና፤ የንጉሥ፡ ከተማ፤ ታላቅ፡ ሕንጻ፤ ጽኑ፡ አንባ፤ ዕርድ፡ ምሽግ፡ (ዳን፰፡ ፪። ፩ዕዝ፡ ፯፡ ፪)።

**በይረሙን**፤ **(ዐረ፡ በይራም)**፤ ቅድሳት፤ ዕለተ፡ ቅድሳት፤ አስተርእዮ፡ ጥምቀት፡ (ስንክ፡ ጥቅ፲)።

**ቢስ**፤—**በቍሙ**፤ **ንፉግ**፤ **ጨባጭ**፤—**ብእሰ፡ ብኢስ**።

**በዪት**፤ **ቶት**፤ **(ቤተ፡ ይበይት፡ ይቢት። ሱር፡ ቡት፤ ባት። ዐረ፡ ባተ)**፤ ማደር፤ ባሉበት፡ ቦታ፡ ከሠርክ፡ እስከ፡ ነግህ፡ መቈየት፤ የትም፡ ውሎ፡ ወደ፡ ቤት፡ መመለስ፤ መግባት፡ መከተት፤ ከሰው፡ መጠጋት። መኖር፤ ባንድ፡ አገር፡ መወሰን፤ ቦታ፡ መያዝ፡ ቤት፡ መሥራት፤ አጽንዖ፡ በኣት። ቤትኩ፡ ወወዐልኩ፡ እንዘ፡ እጼብት። ቤቱ፡ ክልኤሆሙ፡ በይእቲ፡ ሌሊት። ትበይት፡ ሌሊተ፡ ውስተ፡ ፆም። አልቦ፡ ንብረት፡ ዘኀበ፡ መስየ፡ ይበይት። ኀቤየ፡ ትበይት፡ ዮም፤ ዐደረ፡ ገባ፡ ተኛ፡ (፪ቆሮ፡ ፲፩፡ ፳፯። ጦቢ፰፡ ፱። ኢሳ፳፩፡ ፲፫። ሚራ፴፯፡ ፴፩። ዘፍ፴፡ ፲፮)። ይበ

ይት ፡ ውስተ ፡ በኣታተ ፡ ኵሉሙ ። በጸጋሁ ፡ ተፈጥረ ፡ ዅሉ ፡ ወበኂሩቱ ፡ ይበይት ፤ ኖረ ፡ (ኢዮ፴፱ ፡ ፳፯ ፡ ፳፰ ። ቅዳ ፡ ግሩ) ።

**በያቲ** ፤ (ቲት ፡ ትያን ፡ ያት) ፤ የሚያድር ፡ ዐዳሪ ፤ ነዋሪ ፤ ቤት ፡ ሠሪ ።

**ቤት** ፤ (ብ ፡ አብያት ። ዕብ ፡ ባይት ። ሱር ፡ ቤታ ። ዐረ ፡ በይት) ፤ በቁሙ ፡ ማደሪያ ፡ መኖሪያ ፤ ሥራ ፡ መሥሪያ ፤ በደንጊያ ፡ በብረት ፤ በጡብና ፡ በንጨት ፤ በኖራ ፡ በጭቃ ፡ በሣር ፡ በጨፈቃ ፡ የሚሠራ ። ውስጠ ፡ ክፍትነት ፡ ያለው ፡ ዕቃ ፡ ቦታ ፤ ዋሻ ፡ ፍርኵታ ፤ ጕሬ ፡ ጕድጓድ ፤ ታላቁም ፡ ታናሹም ፡ ማናቸውም ፡ ኹሉ ። እቀትሎ ፡ ለቤተ ፡ ምክራም ፡ ወለቤተ ፡ ሐጋይ ፤ ይትሀጐሉ ፡ አብያት ፡ ዘቀርነ ፡ ነጌ ፡ ወይተከሉ ፡ አብያት ፡ ካልኣን ። ይቀሥፎ ፡ ለዐቢይ ፡ ቤት ፡ በድቀት ፡ ወለንኡስ ፡ ቤት ፡ በንፅቃት ። ባእ ፡ ቤተከ ። ቤት ፡ ምሩግ ፡ (ዓሞ፫ ፡ ፲፭ ። ፮ ፡ ፲፩ ። ኢሳ ፳፯ ፡ ፳ ። ምሳ፳፭ ፡ ፱) ።



ቤት ፡

—፤ ወገን ፡ ነገድ ፤ ዘር ፡ ትውልድ ፤ ጉባኤ ፡ ማኅበር ፤ ጭፍራ ፡ ወታደር ፡ በያለቃው ። ርስዒ ፡ ሕዝበከ ፡ ወቤተ ፡ አቡከ ። ቤተ ፡ ያዕቆብ ፤ ቤተ ፡ ዳዊት ፤ ቤተ ፡ እስራኤል ፤ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፤ ቤተ ፡ ክህነት ፤ ቤተ ፡ መንግሥት ።

**ቤት** ፤ ገንዘብ ፤ ዘመድ ፤ ቤተ ፡ ሰብ ፡ (ማቴ፳፫ ፡ ፲፱ ። ዘፀ፩ ፡ ፳፩) ።

**ቤተ ፡ እግር** ፤ መጫሚያ ፤ ሹራብ ፤ ሱሪ ፡ ገንባሌ ፤ ድርማንቅ ፡ ቦለሌ ።

**ቤተ ፡ እግዚ** ፤ የሙሴ ፡ ድንኳን ፤ መቅደስ ፡ ሰሎሞን ፤ ቤተ ፡ ክሲያን ፤ ጉባኤ ፡ ምእመናን ፡ (ቀሌ) ።

**ቤተ ፡ እድ** ፤ እጅጌ ፡ እጀ ፡ ጠባብ ፤ የእጅ ፡ ቤዛ ፤ ሹራብ ። የዕቃ ፡ ገሮ ፤ ቀለብት ፡ (ዘፀ፳ ፡ ፳፭) ።

**ቤተ ፡ አማልክት** ፤ የጣዖታት ፡ ቤት ፤ ብዙ ፡ ዐይነት ፡ ጣዖት ፡ ያለበት ፡ መስጊድ ።

**ቤተ ፡ አንስት** ፤ ጥሩ ፡ ዕልፍኝ ፡ የተሸለመ ፤ የተጌጠ ፤ የተንቈጠቈጠ ፡ (አስቴ፪ ፡ ፱ ፡ ፲፫) ።

**ቤተ ፡ አፈው** ፤ የሽቱ ፡ መደብ ፡ የበቀለበት ፡ የተተከለበት ፡ (ማሕ፮ ፡ ፪) ።

**ቤተ ፡ ብሉይ** ፤ የውሽባ ፡ ቤት ፤ መታጠቢያ ፤ ሽቱ ፡ መዝገቢያ ፡ (ቀሌ) ።

**ቤተ ፡ ግብእ** ፤ የድግስ ፡ የመሸታ ፡ ቤት ፤ ሣቅ ፡ ጨዎት ፡ ስካርና ፡ ዝሙት ፡ ያለበት ፡ (መክ፯ ፡ ፪) ።

**ቤተ ፡ ድዉያን** ፤ በሽተኞች ፡ እስኪድኑ ፡ የሚተኙበት ፤ ሕኪምና ፡ ፈውስ ፡ ያለበት ፡ ንጹሕ ፡ ቦታ ፡ (ቀኖ ፡ ኒቅ) ።

**ቤተ ፡ ወይን** ፤ የጠጅ ፡ ቤት ፤ የወይን ፡ ጠጅ ፡ በበርሚል ፡ በጋን ፡ የሚሸምበት ፡ (ማሕ፪ ፡ ፬) ።

**ቤተ ፡ ዝሙት** ፤ የዝሙት ፡ መደብር ፤ ያመንዝሮች ፡ ቤት ፡ ከንፍረት ፡ በቀር ፡ ሌላ ፡ ነገር ፡ የማይሸጥበት ፡ (ሕዝ፲፮ ፡ ፴፱) ።

**ቤተ ፡ ሐኖት** ፤ ቤተ ፡ ዝሙት ፤ የገበያ ፡ ቤት ፡ መብል ፡ መጠጥ ፡ የሚሸጥበት ፡ (ስንክ ፡ ግን፲፪) ።

**ቤተ ፡ ጣዖት** ፤ የሰይጣን ፡ ቤት ፤ ሰይጣን ፡ በጣዖቱ ፡ ዐድሮ ፡ የሚመለክበት ፡ (ኩፋ ፡ ፲፪) ።

**ቤተ ፡ ክሣድ** ፤ ዐንገትጌ ፡ የቀሚስ ፡ አፍ ፤ ራስ ፡ ማግቢያ ።

**ቤተ ፡ ልብስ** ፤ ጋን ፡ ሣጥን ፤ ዕቃ ፡ ቤት ፡ የቤተ ፡ ክሲያን ፡ ልብስ ፡ የሚከተትበት ፡ (ትእ ፡ ጴጥ) ።

**ቤተ ፡ ላሕ** ፤ የሐዘን ፡ ቤት ፤ ማልቀሻ ፡ እንባ ፡ ማፍሰሻ ፡ (መክ፯ ፡ ፪) ።

**ቤተ ፡ ልሔም** ፤ ስመ ፡ ሀገር ፤ ቤተ ፡ ኅብስት ፡ (ዘፍ፴፭ ፡ ፲፱) ።

**ቤተ ፡ መበስላን** ፤ የወጥ ፡ የንፍሮ ፡ ቤት ፤ ማብሰያ ፡ መቀቀያ ።

**ቤተ ፡ መዋጽሕት** ፤ ማረፊያ ፤ መክደኛ ፡ ጐባባ ፡ (ዘፀ፳፭ ፡ ፳፱) ።

**ቤተ ፡ ሞቅሕ** ፤ የግዞት ፡ ቤት ፤ ወንጀለኞች ፡ የሚታሰሩበት ፡ (መክ፬ ፡ ፲፬) ።

**ቤተ ፡ ሙታን** ፤ መቃብር ፤ የመቃብር ፡ ቤት ፤ ሲኦል ፡ (ስንክ ፡ የካ፰) ።

**ቤተ ፡ መዛግብት** ፤ ዕቃ ፡ ቤት ፡ ግምጃ ፡ ቤት ፡ ዕቃና ፡ ልብስ ፡ በሣጥን ፡ መልቶ ፡ የሚቀመጥበት ፡ (ዳን፩ ፡ ፪) ።

**ቤተ ፡ መጥበሕት** ፤ አሮት ፤ ሰገባ ፡ ሽፋፍ ፡ ድርቄ ፡ (ማቴ፳፮ ፡ ፶፪) ።

**ቤተ ፡ ማይ** ፤ ሠገራ ፤ ዐዘቅት ፡ ሾበሕ ፡ (ስንክ ፡ የካ፳፩) ።

**ቤተ ፡ መያሲ** ፤ የመሸታ ፡ ቤት ፤ ክዚያው ፡ እየጠጡ ፡ የሚሰክሩበት ፡ (ኢሳ፭ ፡ ፲፩) ።

**ቤተ ፡ መምሀራን** ፤ ታላቅ ፡ የተማሪ ፡ ቤት ፡ የፈላስፎች ፡ ትምርት ፡ ያለበት ፡ (ስንክ ፡ ግን፲፪) ።

**ቤተ ፡ ምሥያጥ** ፤ ሱቅ ፡ መደብር ፤ የንግድ ፡ ቤት ፡ (ዮሐ፪ ፡ ፲፮) ።

**ቤተ ፡ መጻሕፍት** ፤ የመጣፍ ፡ ቤት ፡ መጣፍ ፡ ኹሉ ፡ በያይነቱ ፡ የሚገኝበት ፤ (ቢብሊዮቴክ) ፡ ትርጓሜ ፡ የሚነገርበት ፤ የመጣፍ ፡ መክተቻ ፡ ሣጥን ፡ ማኅደር ፤ ዕቃ ፡ ቤት ፡ ዋሻ ፡ (ገድ ፡ አዳ) ።

**ቤተ፡ መቅደስ፤** በቁሙ፤ ቤተ፡ እግዚ፤ መ ቅደስ፡ ኦሪት፤ መቅደስ፡ ወንጌል፤ ቤተ፡ ክሲያን ።

**ቤተ፡ ምርፋቅ፤** የምግብ፡ ቤት፤ ዳስ፡ ደጀ፡ ሰላም፤ ቤተ፡ ልሔም ።

**ቤተ፡ ምሳሕ፤** አዳራሽ፤ ግብር፡ ማግቢያ፤ ምሳ፡ ማቅረቢያ፡ (ዳን፩፡ ፲) ።

**ቤተ፡ ነግድ፤** እንግዳ፡ የሚያርፍበት፤ ሰተት፡ ብሎ፡ የሚገባበት፤ ልኳንዳ፤ ሆቴል፡ (ስንክ፡ ነሐ፲፩) ።

**ቤተ፡ ፍንዱቅ፤** ዝኒ፡ ከማሁ፤ ቤተ፡ ነግድ፡ (ትእ፡ ጴጥ) ።

**ቤተ፡ ፍሥሓ፤** የሰርግ፡ የመሸታ፡ ቤት፡ (መ ክ፯፡ ፭) ።

**ቤተ፡ ጸሎት፤** ታናሽ፡ ምኵራብ፤ የሥዕል፡ ቤት፤ ከጸሎት፡ በቀር፡ መሥዕት፡ የማይቀርብበት፤ ወ ይም፡ ታላቅ፡ መቅደስ፤ ቤተ፡ ክሲያን፡ (ኢሳ፶፮፡ ፯) ።

**ቤተ፡ ርእስ፤** ቆብ፡ ባርኔጣ፤ የከባ፡ የበርኖስ፡ ቍንጮ ።

**ቤተ፡ ስምዕ፤** ደብተራ፡ ስምዕ፤ የሙሴ፡ ድ ንኳን፤ (፩ዜና፡ ፮፡ ፴፪ ። ፪ዜና፡ ፩፡ ፫) ።

**ቤተ፡ ስታይ፤** የድግስ፡ የመሸታ፡ ቤት፤ ያ ረቄ፡ መደብር፡ መጠጥ፡ ኹሉ፡ በያይነቱ፡ የሚገኝበት፡ (ሚራ፴፩፡ ፮) ። ቤት፡ በነገር፡ ኹሉ፡ እየተናበበ፡ በዚህ፡ አምሳል፡ እንደ፡ ዘርፉ፡ ስልት፡ ይፈታል፤ ዘርፍና፡ ቅ ጽል፡ ባለቤትን፡ ወይም፡ ስምና፡ ግብርን፡ እንዲገልጥ፡ አስተውል ።

**ቤታዊ፡ አብያታዊ፤** የቤት፤ ቤታም፡ ባለ ቤት፤ ቤት፡ አባት፤ አዛዥ፡ መጋቢ፤ ቤተ፡ ሰብ፡ ዘመድ፤ የቤት፡ ውልድ ። ገብረ፡ ንጉሥ፡ ሰብእ፡ አብያታዊ፡ (ዮሐ፬፡ ፵፮፡ ፵፱) ።

**አቤተ፤** አሳደረ፤ እስከ፡ ነግህ፡ አቈየ፤ አኖረ፤ አስጠጋ ። ወኢያሠነዩ፡ ማኅትቶሙ፡ ለአቢቶ ። ወለ ብዙኃን፡ ዕሩቃን፡ አቤትዎሙ፡ ዘእንበለ፡ ልብስ ። ወኢያቤተ፡ ምንተኒ ። ተዘሳተ፡ ዐረብ፡ እለ፡ ኢያበ ይቱ፡ ለነግህ፡ (፩ነገ፡ ፫፡ ፫ ። ኢዮ፳፬፡ ፯ ። ሶፎ፫፡ ፫) ።

**ምብያት፤** ማደሪያ፤ ማሳደሪያ፤ መኖሪያ፤ ቦታ፡ ቤት፡ በረት ። ከመ፡ መርዔት፡ ውስተ፡ ምብያ ቲሁ ። ምብያቲከ፡ (ሚክ፪፡ ፲፪ ። ኢሳ፴፯፡ ፳፰) ።

**ተበየተ፤** ተዳደረ፤ ተዋገነ፤ ተጎራበተ፤ ተከታ ተመ ።

**አስተበየተ፤** አስተዳደረ፤ አዋገነ፤ አጎራበተ ።

**መስተበይት፤** ተዳዳሪ፤ አስተዳዳሪ ።

**ቤት፤** ስመ፡ ፊደል፡ ካልእ፤ በ፡ ቅርጹ፡ ቤ ትና፡ ደጅ፡ አፍ፡ የሚመስል፡ (መዝ፡ ፻፲፰፡ ፱—፲፮ ። ሰቈ፩፡ ፪ ። ፪፡ ፪ ። ፫፡ ፭ ። ፬፡ ፪) ። ስሙንና፡ መል ኩን፡ ከቤት፡ ወስዷል ።

**ብኮ፤—ብኩይ፤—በከየ ።**
**ቦክ፤—መባከን፤—በዊክ ።**

**በኲሕ፤ ሖት፤ (በኰሐ፡ ይበኵሕ፡ ይ ብኳሕ ። ዕብ፡ ፉዋሕ፤ ያፉሕ፤ ናፉሕ፤ ነፍኀ)፤** መንፋት፤ እፍ፡ ማለት፤ እሳትን፡ በአፍ፡ ወይም፡ በወ ናፍ ። ከአፍ፡ እሳት፡ ማውጣት፤ ነበልባል፡ መትፋት፤ በምትሀት ። መጽሐፍ፡ ግን፡ በበኰሐ፡ ፈንታ፡ አብኰሐ፡ ይላል፤ አያስኝም፤ አ፡ ያማርኛ፡ ነው ። (ሕዝ፳፪፡ ፳፡ ፳፩) ። ዙሎሙ፡ ያበዙሑ፡ እሳተ፡ እምአፉሆሙ፡ (ገድ፡ ተክ) ። መለምለም፡ መርጠብ፤ ከነፋስ፡ ከውሃ፡ ጠል፡ መንማት ።

**አብኰሐ፤** አናፋ፡ አስነፋ፤ አስተነፈሰ፤ እፍ፡ እፍ፡ አሰኘ ። ዘያበዙሕ፡ ምብኳሐ፡ እሳት፡ (ኤር፮፡ ፳፱) ።

**መብኰሕ፤ (ሕት፡ ሓን፡ ሓት)፤** ቅጽልና፡ ጥሬ ። የሚያናፋ፤ አናፊ ። ማናፊያ፡ ወናፍ ።

**ምብኳሕ፤ (ሓት)፤** አጉደ፡ ማናፊያ፤ ወ ናፍ ። ምብኳሐ፡ ነሃቢ፡ ሥጡቅ ። በብዙኅ፡ ምብ ኳሕ፡ (ኢዮ፡ ፵፪፡ ፲፱ ። አርጋ፡ ፫) ።



ምብኳሕ፡

»ኩሓ፤ (ሓት)፤ እፍታ፡ አክታ፤ ትንፋሽ፡ የሚያነድ፡ የሚያበርድ፤ ወይም፡ ልምላሜ፤ ርጥበት፡ ርጥብነት ። ስመ፡ ዕፅ፡ ሓያ፡ አሓያ፡ የሚባል፤ በወንዝ፡ ዳር፡ በውሃማ፡ ቦታ፡ የሚበቅል ። ከመ፡ ኩሓ፡ ዘኅበ፡ ሙሓዘ፡ ማይ ። ውስተ፡ ኩሓቲሃ፡ (ኢሳ፵፬፡ ፬ ። መዝ፡ ፻፵፫) ።

**በክይ፤ ዮት፤ (በከየ፡ ይበኪ፡ ይብኪ ። ዕብ፡ ባካ ። ሱር፡ ብካ ። ዐረ፡ በከ)፤** ማልቀስ፤ እንብ፡ ማፍሰስ፤ ዋይ፡ ማለት፡ መጮኽ፤ መንሰቅሰቅ ። ኀደገት፡ በክየ ። ብክዮ፡ ለዘሞተ ። ኢይበክይዎሙ ። በእንተ፡ ዙሉ፡ ምንዱብ፡ እበኪ፡ (ጦቢ፯፡ ፭ ። ሚራ ፳፪፡ ፲፭ ። ኤር፳፫፡ ፪ ። ኢዮ፴፡ ፳፭) ።

**በካዪ፤ (ዪት፡ ይያን፡ ያት፤ በከይት)፤** የሚያለቅስ፡ አልቃሽ፤ እንብ፡ አፍሳሽ፤ ልቅሶኛ ። ብፁ ዓን፡ እንተ፡ ትብህለት፡ ለሕዙናን፡ ወለበካይያን፡ (ፊልክ፡ ፸፱ ። ገድ፡ አዳ) ።

**መብክይ፤** ዝኒ፡ ከማሁ፤ አልቃሽ፤ ወይም፡ አስለቃሽ ። ወበዊአ፡ ቤተ፡ ርእየ፡ መብክያነ፡ (ማቴ፱፡ ፳፫ ። መጽ፡ ምስ) ።

**ብኩይ፤ (ያን፡ ያት፡ ኪት)፤** ያለቀሰ፡ አል ቃሽ፤ ሐዘንተኛ ።

(ጕ) ብከ፤ ብኰ፤ (ዕብ፡ በኬ)፤ ስመ፡ ሰብእ፤ ዳዊት፤ በካዪ፡ ብኩይ፡ አልቃሽ፡ እንባማ፡ ማለት፡ ነው። ባኀር፡ ወልደ፡ ብኰ፡ (ጥበ፩። መዝ፳፡ ፯—፰)። የባኀርን፡ ፍች፡ ትመልከት።

**ብካይ**፤ (ያት)፤ ልቅሶ፤ ዋይታ፡ ፍጅጅት፤ መራራ፡ ጩኸት፡ ከእንባ፡ ጋራ። በከየ፡ ብካየ፡ ዐቢየ። ብካየ፡ ኢያዜር። ብካይ፡ ወላሕ። ቃለ፡ ብካይ፡ ወቃለ፡ ዐውያት፡ (ኤርም፴፡ ፫። ኢሳ፲፭፡ ፱። ፳፱፡ ፲፱። ፳፭፡ ፲፱)።

**አብከየ**፤ አስለቀሰ፤ አሳዘነ፤ አስጮኸ፡ ዋይ፡ አሰኘ፤ እንባ፡ አስፈሰሰ። በከየ፡ ብካየ፡ መሪረ፡ እስከ፡ አብከየ፡ እለ፡ ሀለዉ፡ ህየ። ለእመ፡ ኢበከይኑ፡ በፈቃድኑ፡ በዝየ፡ ያበክዩኑ፡ በህየ፡ ዘእንበለ፡ ፈቃድኑ። እለ፡ አብከዩ፡ ዕቤረ፡ ወዕጓለ፡ ማውታ። ምንት፡ ያበክየኪ፡ (ዮሴፍ። መቃ። ግንዘ። ፩ነገ፡ ፩፡ ፰)።

**ተባከየ**፤ ተላቀሰ፤ ተለቃቀሰ፤ ተፋጀ። ሰብ፡ ተኣምኑ፡ ወተባከዩ፡ በበይናቲሆሙ፡ ወተሳዐሙ፡ (ተረ፡ ባሮ)።

**አስተባከየ**፤ አላቀሰ፤ አለቃቀሰ። ስሕልት፡ ሰይፍከ፡ ብእሲ፡ ልዑል፤ ለሰብአ፡ ሞረት፡ ወመርሐ፡ ቤቴ፡ አምኃ፡ ኢየሱስ፡ መስተጋድል። የተሳለች፡ ሰይፍኸ፡ ታላቅ፡ ሰው፡ (ያማርኛ፡ ግእዝ)።

**በኪክ**፤ ኪት፤ (በከ፡ ይበክክ፡ ይብክክ። ዕብ፡ ባቃቅ። ዐረ፡ በቀ፤ በካእ)፤ ማብክክ፤ ማብኪት፤ ባዶ፡ ጠፍ፡ ብላሽ፡ ከንቱ፡ ማድረግ፤ ወይም፡ መኾን። እባክኸ፡ ማለት፡ ከዚህ፡ የወጣ፡ ነው። መጽሐፍ፡ ግን፡ በበከከ፡ ፈንታ፡ በከየ፡ ይላል፤ የተሳሳተ፡ ነው። ኢይሬኢኑ፡ ፀጓየ፡ ዘያበርህ፡ ወይጠፍእ፤ ወወርኃኒ፡ ትበኪ፡ (ኢዮ፴፩፡ ፳፮)።

**በክ**፤ በክት፤ ሙቱ፡ ያደረ። ባዶ፡ ጠፍ፡ ብቻ፤ ከንቱ፡ ብላሽ፤ ዋዛ፡ ፈዛዛ፤ እንዲያው፤ የዝም፡ ብሎ። ዙሉ፡ ክበቡ፡ በክ። ትንበር፡ በከ። ነበሩ፡ እስራኤል፡ በበክ። አብድ፡ ያፈደፍድ፡ ነቢበ፡ በክ። እኮ፡ በከ፡ በከመ፡ ትሬእይዎ፡ ለዝንቱ፡ ኅብስት፡ (ሔኖ፸፫፡ ፭። ፯ቆሮ፡ ፯፡ ፲፭። ስንክ፡ የከ፳፯። ሆሴ፫፡ ፬። መክ፪፡ ፲፭። ቅዳ፡ ሕር)።

**በከ**፤ በከንቱ፤ በብላሽ፤ እንዲያው፤ ወይም፡ ለ፡ ኹኖ። በከ፡ ጻመውኩ። ኢትክዐው፡ ደመ፡ በከ፡ ዘእንበለ፡ ዙነኔ። ነሀብከ፡ በከ። ኢነሥአ፡ እምኔሆሙ፡ በከ። በከ፡ ለሊኑ፡ ተፈጠርኑ፡ (ኢሳ፵፱፡ ፬። ኩፋ፡ ፳፭፡ ፲፱። ጥበ፪፡ ፪)።

**በኵር**፤ ሮት፤ (በኰረ፡ ይበኵር፡ ይብኵር። ዕብ፡ ባኬር)፤ መብኵር፡ መበከር፤ መዠመሪያ፡ መውለድ፡ ማፍራት፤ መውለድንና፡ ማፍራትን፡ መዠመር፤ በኩር፡ መኾን። መጽሐፍ፡ ግን፡ በበኰረ፡ ፈንታ፡ ተበኵረ፡ ይላል፤ አያስኬም። ዕጕላት፡ እለ፡ ተበዙራ። አባግዐ፡ እለ፡ ተበዙራ። መካን፡ ተበዙረት፡ ዮሐንስሀ፡ (፩ነገ፡ ፮፡ ፯። ክብ፡ ነገ፸፫። መዋሥ)።

—፤ በኵር፡ ማድረግ፤ ማላቅ፡ ማብለጥ፤ የብኵርና፡ ክብር፡ መስጠት፤ ወልድየ፡ ዘበኵርየ፡ ማለት፡ (ዘፍ፳፯፡ ፳፱። ፵፱፡ ፫። ዘፀ፬፡ ፳፪። ዕብ፩፡ ፭፡ ፯። መዝ፹፰፡ ፳፯፡ ፳፰)።

—፤ ማብከር፤ ማስታጐል፤ ማቆም፡ ማቋረጥ፡ መተው። መጽሐፍ፡ ግን፡ በበኰረ፡ ፈንታ፡ አብኰረ፡ ይላል፤ አ፡ ያማርኛ፡ ነው። ሰማይኒ፡ ለእመ፡ አብኰረት፡ ዝናመ፡ (፪ዜና፡ ፯፡ ፳፮)።

**በኳሪ**፤ (ሪት፡ ርያን፡ ያት)፤ በካር፡ ዠማሪ፤ በኵር፡ አድራጊ፤ አስታጓይ።

**አብኰረ**፤ አስበከረ፤ በካር፡ በኵር፡ አስደረገ፤ አስተወ፤ ከለከለ።

**ተበኵረ**፤ ተበኰረ፤ በኵር፡ ኾነ፡ በኵር፡ ተባለ፤ የበኵርነት፡ ክብር፡ ተቀበለ። ዮሐንስ፡ እምክርሥ፡ መካን፡ ዘተበዙረ፡ (ድጓ)።

—፤ ታጐለ፤ ቀረ። እምይትበኵር፡ በዓሉ፡ ለቅዱስ፡ ሚካኤል፡ (ድር፡ ሚክ)።

**ብኩር**፤ (ራን፡ ራት፡ ኵርት)፤ የተበኰረ፤ በኵር፡ የኾነ፡ የተባለ፤ የቀረ፡ የታጐለ።

**በኵር**፤ (ራት፤ አብኳር። ዕብ፡ ብኮር። ሱር፡ ቡክራ። ዐረ፡ ቢክር)፤ በቁሙ፤ መዠመሪያ፡ ልጅ፤ ፍሬ፤ ቀዳማዊ፤ ታላቅ፡ አለቃ፡ ሹም፤ አንጋፋ፡ ግንባር፡ ቀደም፤ ፊት፡ የተወለደ፡ የበሰለ፤ መብሰል፡ የፍሬ፡ ነው። ሙፍራ፡ የሌለው፡ አለቃ፡ እንዳይባል፤ ታናሽ፡ ተከታይ፡ የሌለውም፡ ዋሕድ፡ እንጂ፡ በኵር፡ አይባልም። እፎ፡ አሐደ፡ ወሊዳ፡ ውእቱ፡ ይቤ፡ ዘበዙራ፤ አላ፡ እስመ፡ ኢወለደት፡ እምድኅሬሁ፡ (ቄር)። ዙሉ፡ በዙር። በዙረ፡ ወልድከ። በዙሩ፡ ለላሕም፤ በዙሩ፡ ለበግዐ፡ ወለአድግ። ደቂቀ፡ ዳዊት፡ አብኳር፡ ቀደምት። አብኳረ፡ እስራኤል። በዙረ፡ በለስ። በዙራት፡ ይሰዐሩ። ዓሥራት፡ ወበዙራት፡ (ዘፀ፲፭፡ ፭። ፳፱፡ ፳፰። ፴፱፡ ፲፱፡ ፳። ፩ዜና፡ ፲፰፡ ፲፯። ክብ፡ ነገ። ሆሴ፱፡ ፲። ስንክ፡ ታኅ፳፰። ፍ፡ ነ፡ ፲፰)።

**በኵርና**፤ ብኵርና፤ (ናት)፤ በኵርነት፤ በኵር፡ መኾን፤ በፊት፡ መወለድ፤ ልቅና፡ ቅድምና። ተማየጠ፡ እምኔሁ፡ ብዙርናሁ። ብፅዕናት፡ ወብዙርናት፡ (ስንክ፡ ነሐ፳፰። ቀሌ። ዕብ፲፪፡ ፲፮። አፈ፡ ድም፭)። በብኵርና፡ ፈንታ፡ ያንዱን፡ በብዙ፤ ብኵርናት፡ ይላል፤ አያስኬም። አውፅአ፡ ለሮቤል፡ እምኍልቈ፡ አኀዊሁ፡ ወጸገዎ፡ ብዙርናት፡ ለዮሴፍ፡ (ግንዘ)።

**በኬሴል**፤ (ዕብ፡ ባሴቤል)፤ ባ፡ በ፤ ሴቤል፡ ሸከም፤ በሸከም፡ በመሸከም፡ ወይም፡ ተሸከመው፡ (ነሐ፱፡ ፲፯)።

**በል**፤—ትእዛዝ፤—ብሀለ፤ ቤለ፡ ይቤ። ቤልከ፡ ትቤ፡ ትበል፡ በል።

**ቤል ፤—የባቢሎን፡ክፊል ፤—በዪል ።**

**በልበለ ፤—አረጀ ፤—በሊል፡በለ ። በልየ ።**

**በልግ፤(ዐማርኛ)፤** የበጋ ፡ ዝናም ፤ ጸደይ ።

**በለድ፤(ትግሬ ፡ ወዐረ)፤** የተወለዱበት ፡ አገር ።

**በለዝ፤(ጽር ፡ በሎዝ ። ዕብ ፡ በዐዝ)፤** የዐምድ ፡ ስም ፤ ሰሎሞን ፡ በመቅደሱ ፡ ደጅ ፡ አፍ ፡ በበረንዳው ፡ በደጀ ፡ ሰላሙ ፡ ካቆማቸው ፡ ከኹለቱ ፡ አዕማድ ፡ አንዱ ፡ በስተሰሜን ፡ ያለው ፡ የግራው ፡ ዐምድ ። ቦ ፡ ዐዘዝ÷ሎ ፡ ዐዘዝ÷ኀይሉ ፡ ወጽንዑ ፡ ዐዘዙ ፡ ለመቅደስ ፡ ማለት ፡ ነው ፤ ባለብሉዮች ፡ ግን ፡ ርትዕ ፡ ይሉታል ፡ (፫ነገ ፡ ፯ ፡ ፳፩) ።

**በልሐ ፤—ተሳለ ፤—በልኀ ።**

**ባልሐ፤ሖት፤(ባልሐ ፡ ይባልሕ ፡ ይባልሕ ። ዕብ ፡ ባሎሕ ፤ መዝለል ፤ መንጐራደድ)፤** ማዳን ፡ ማውጣት ፤ መታደግ ፡ መቤዠት ፤ ከተያዙ ፡ ከገቡ ፡ በኋላ ። ይባልሖ ፡ ለንጹሕ ። ኢይክልኑ ፡ ባልሖ ። አልቦ ፡ ዘያድኅን ፡ ወዘይባልሕ ። ለባልሖትየ ፡ (ኢዮ፳፪ ፡ ፴ ። ኢሳ፶ ፡ ፪ ። መዝ ፡ ፯ ። ስንክ ፡ ጥቅ፳፬) ።

**ባላሒ፤መባልሒ፤** የሚያድን ፤ አዳኝ ፡ ታዳጊ ። ባላሔ ፡ ሠልጡ ። ባላሒ ፡ ለዕጓለ ፡ ማውታ ። መባልሒት ፡ (ቅዳ ። ኪዳ ። አርጋ) ።

**ተባልሐ፤** ዳነ ፤ ወጣ ፡ አመለጠ ። ኢይትባላሕ ፡ ዘተመንደበ ። ዘይትባላሕ ፡ እምኔሃ ። ሠለስቱ ፡ ደቂቅ ፡ እለ ፡ ተባልሑ ፡ እምእቶነ ፡ እሳት ፡ (ኢሳ፰ ፡ ፳፱ ። መክ፯ ፡ ፳፯ ። መዋሥ) ።

**ብሉሕ፤(ሓን ፡ ሓት ፡ ልሕት)፤** የዳነ ፡ የወጣ ፡ ያመለጠ ። ብሉሕ ፡ እመቅሠፍት ፡ (አዋል) ።

**አስተባልሐ ፤ (አስደራጊና ፡ አደራራጊ)፤** አስዳነ ፡ አስቤዠ ፤ አስወጣ ። አዳዳነ ፡ አዋጣ ፤ ዐገዘ ፡ ረዳ ፤ ለማዳን ፡ ለማውጣት ። እስመ ፡ ኢያስተባልሐከ ፡ እግዚ ፡ (መቃ ፡ ፲፳፩) ።

**ቤልሖር፤(ጽር ፡ ቤሊአር ። ዕብ ፡ ብሊያዐል)፤** ሰይጣን ፤ የሰይጣን ፡ ስም ፤ ለሰውም ፡ ይኾናል ። ክፉ ፡ ጥፉ ፤ ልክስክስ ፡ ምናምንቴ ፤ ሕገ ፡ ወጥ ፡ ቀንበር ፡ ሰበር ፤ ዳንደ ፡ ወንበዴ ፡ ቀማኛ ፡ ሽፍታ ፡ ማለት ፡ ነው ። መኑ ፡ ዘያኀብሮ ፡ ለክርስቶስ ፡ ምስለ ፡ ቤልሖር ። ወኢይኩንኖሙ ፡ መንፈስ ፡ ቤልሖር ፡ (፪ቆሮ ፡ ፮ ፡ ፲፭ ። ኩፋ ፡ ፩) ።

(ሳ) **በሊኅ፤ኆት፤(በልኀ ፡ ይበልኅ ፡ ይብላኅ)፤** መብላት ፤ መስላት ፤ መሾል ፤ መፍጠን ፤ ስል ፡ ሹል ፡ ፈጣን ፡ መኾን ። ይበልኅ ፡ እምሰይፍ ። ሚ ፡ ይበልኅ ፡ እምሠርት ። በልኀት ፡ ኵናት ፡ (ዕብ፬ ፡ ፲፪ ። ፊላስ ። ሕዝ፳፩ ፡ ፲፩) ። ይበዝኅ ፡ ይጸንዕ ፡ በማለት ፡ ፈንታ ፡ ይበልኅ ፡ ይላል ፡ (ዘፀ፲፱ ፡ ፲፱) ።

—፤ መበለኅ ፤ ብልኅ ፡ ዐዋቂ ፡ መኾን ፤ መባል ፡ እገሌ ፡ ምላጭ ፡ ነው ፡ እንዲሉ ፡ (ዐማርኛ) ።

(ጥ) **በሊኅ፤(ኃን ፡ ኃት ፡ ላኅ)፤** የበላ ፡ የሰላ ፡ የሾለ ፤ ስል ፡ ሹል ፤ ትብ ፤ ደፋር ፡ ጩካኝ ፤ ፈጣን ፡ ብልኀተኛ ፤ ጽሩይ ፡ ረቂቅ ። መላጺ ፡ በሊኅ ። ሰይፍ ፡ በሊኅ ። ቀኖት ፡ በሊኅ ። ሠያንው ፡ በሊኃን ። ስባራተ ፡ ማህው ፡ በሊኃት ። በበሊኅ ፡ ልሳን ። ብእሲ ፡ በሊኅ ፡ በምግባሩ ። በሊኅ ፡ እገሪሆሙ ፡ ለክዒወ ፡ ደም ። በበሊኅ ፡ ዐይነ ፡ ልብክን ፡ ትነጽራ ፡ (መዝ ፡ ፶፩ ። ራእ፩ ፡ ፲፯ ። ግብ፱ ፡ ፩ ። አርጋ ። ሚራ፵፫ ፡ ፱ ። ስንክ ፡ መጋ፱ ። ምሳ፳፪ ፡ ፳፱ ። መዝ ፡ ፩ ። ቄር) ። በበላኅ ፡ ፈንታ ፡ ብልኅት ፡ ይላል ፤ አያስኼም ። ዘሩን ፡ መስሎ ፡ የሚገኝ ፡ ቅጽል ፡ ኀጺር ፡ ነዊኅ ፤ ገዚፍ ፡ ጸሊም ፤ ጠቢብ ፡ ሐኪም ፤ ጸቢብ ፡ ርሒብ ፤ ረቂቅ ፡ ቀጢን ፤ ይህን ፡ የመሰለ ፡ ኹሉ ፡ መንገዱ ፡ አንድ ፡ ነው ፤ ከብዙዎች ፡ በቀር ፡ ላንዲቱ ፡ ሴት ፡ ምእላድ ፡ የላትም ። ቅጽልነቱም ፡ ማልስና ፡ ሳድስ ፡ ያለበት ፡ ቱሱሕ ፡ ውስጠ ፡ ዘ ፡ ስለ ፡ ኾነ ፤ ኀጻሪ ፡ ነዋኂ ፡ ገዛፊ ፡ ጸላሚ ፡ ጠባቢ ፡ ረቃቂ ፤ ወይም ፡ ነዊኅ ፡ ጥቡብ ፡ ርቁቅ ፡ ቅጡን ፡ አያስኼም ። አንዳንድ ፡ ጊዜ ፡ ግን ፡ ማልስ ፡ ትቶ ፡ በሳድስ ፡ ብቻ ፤ ኅጹር ፡ ግዙፍ ፡ ጽሉም ፡ እያለ ፡ ይገኛል ።

**ብልኅ፤(ኃት)፤** ስለት ፡ ሹለት ፤ የሰይፍና ፡ የጦር ፡ አፍ ፡ አንደበት ። ብልኀ ፡ ሰይፍ ፡ ትነድድ ። ቅትሎሙ ፡ በብልኀ ፡ ሰይፍ ። በብልኀ ፡ ሰይፍ ፡ እሙንቱ ፡ ረከቡ ፡ አክሊለ ። ብልኀ ፡ ኲናት ፡ ዘተረግዘ ፡ ቦቱ ፡ እግዚእነ ። በብልኀ ፡ ኲናት ፡ ገቦሁ ፡ ደጐጸ ፡ (ፍ ፡ ነ ፡ ፵፯ ። አፈ ፡ ተ፲፩ ። ስንክ ፡ ኅዳ፳ ። ግን፳፳) ።

**ብልኅ፤(ዐማርኛ)፤** በቁሙ ፤ አስተዋይ ፡ ዐዋቂ ።

**ብልኀት፤** በቁሙ ፤ መስላት ፤ መሾል ፤ መፍጠን ፡ አስባል ፤ አሿሿል ፡ አፈጣጠን ፤ ስለት ፡ ሹለት ፡ ፍጥንት ፤ ብልኅነት ፡ ፈጣንነት ። ወእምቅድመ ፡ ያስተርኢ ፡ ብልኀተ ፡ መብረቅ ፤ ስለቱ ፡ ፍጥንቱ ፡ ብልጭታው ፡ (ቅዳ ፡ ግሩ) ።

**አብልኀ፤** አበላ ፤ አሰላ ፡ አሾለ ፤ አፈጠነ ፤ አስፈጠነ ፡ ብልኅ ፡ አደረገ ። ኀጺን ፡ ለኀጺን ፡ ያበልኆ ። አብልኀ ፡ ጸራቢ ፡ ኀጺነ ። ያበልኅ ፡ መዐቶ ፡ ሰይፈ ፡ መታሬ ። አብልኁ ፡ ልሳኖሙ ፡ (ምሳ፳፯ ፡ ፲፯ ። ኢሳ፵፬ ፡ ፲፪ ። ዘካ፩ ፳፩ ። ጥበ፭ ፡ ፳፩ ። መዝ ፡ ፻፫) ።

**መብልኂ ፤ ኅ ፤ (ኂት ፡ ኅያን ፡ ያት)፤** የሚስል ፡ የሚያሾል ፤ ሳይ ፡ አሿይ ።

**መብልኅ ፤ ት ፤ (ብ ፡ መባልኅት)፤** የብረት ፡ መሣሪያ ፤ ስለትና ፡ ሹለት ፡ ጥርስ ፡ ሌላም ፡ ብዙ ፡ ዐይነት ፡ ያለው ። ካራን ፡ ቢላዎ ፡ ማለት ፡ ከዚህ ፡ የወጣ ፡ ነው ። ወእምዝ ፡ አዘዞ ፡ ንጉሥ ፡ ለነሃቤ ፡ ኀጺን ፡

አስረገጠ፡ አስጠቀጠቀ። ማበራየት፡ ያውድማ፤ ማረባየት፡ የጤፍ፡ ዕርሻ፡ ነው፤ መሬቱ፡ እንዲጠብቅ፡ ክብት፡ ይነዱበታል። በሬ፡ በረት፡ ባሪያ፡ ባሬታ፡ ማለት፡ ዐማርኛው፡ ከዚህ፡ ወጥቷል፤ በዐረን፡ እይ። የወዲያኛው፡ ትግሬ፡ ሐባብም፡ ክሕደ፡ ሲል፡ በረየ፡ ይላል፤ ምስጢሩ፡ ፈራ፡ ደነገጠ፡ ከለው፡ ይገባል።

**በርዮድስ፤(ጽር፡ ፔሪዎዶስ)፤** ቀመር፤ የቀመር፡ ስም፤ የጨረቃ፡ ቢኾን፡ ፲፱፤ የፀሓይ፡ ቢኾን፡ ፳፰፡ ዓመት። ሲያበዛ፡ በርዮድሳት፡ ይላል፡ (አቡሻ፡ ፳፭)።

**ብርያል፤(ጽር፡ ቤሪያል)፤** የሰይጣን፡ ስም፤ ቤልሖርን፡ እይ፤ ከዚህ፡ ጋራ፡ አንድ፡ ነው፡ (ዕር፡ ኢሳ፩፡ ፰። ፪፡ ፱። ፫፡ ፲፭፡ ፲፫። ፬፡ ፪፡ ፲፬፡ ፲፯፡ ፲፰። ፭፡ ፩፡ ፲፭)።

**ብርያሚን፤—ሐጹጻን፤—ድርያሚን።**

**በሪክ፤ ኮት፤(በረከ፡ ይበርክ፡ ይብርክ። ዕብ፡ ባራኽ። ሱር፡ ብሬኽ። ዐረ፡ በረከ)፤** መብረክ፤ መብረክረክ፤ መንበርከክ፤ ጕልበትን፡ ማጠፍ፡ በጕልበት፡ መቆም፤ መስገድ፤ ትንበርክኮ፡ መኼድ፤ ተጣጥፎ፡ መተኛት፡ (ጥኰ) መኰድኰድ፡ (ዘኍ፳፬፡ ፳፯)። ሶበ፡ በጽሐ፡ ገመል፡ ኀበ፡ ውእቱ፡ መካን፡ በረከ፡ በብረኪሁ፡ ወኢተንሥአ፡ (ስንክ፡ ነሐ፲፱)።

**ብሩክ፤(ካን፡ ካት፡ ርካት)፤** የበረከ፡ የተንበረከከ፡ እንብርክ።

**ብርክ፤(ብ፡ ብረክ፤አብራክ)፤** ጕልበት፡ ጭን፤ ማቀፊያ፤ መታጠፊያ፡ መንበርከኪያ። አዕደወኒ፡ እስከ፡ ብርክ። ወደክመኒ፡ ብረክየ፡ በጾም። አብራኪክ፡ እለ፡ አውተራ፡ ስግደተ። ሐቂፍ፡ በአብራክ። በእንተ፡ አብራኪሃ፡ እለ፡ ሐቀፋክ፡ (ሕዝ፵፯፡ ፬። መዝ፡ ፻፰። ደራሲ። አርጋ፡ ፩። ሳታት)። ብራኳ፡ ብርኩማ፡ ማለት፡ ከዚህ፡ የወጣ፡ ነው።

**አብረከ፤** አበረከ፡ አብረከረከ፤ አንበረከከ፡ አስገደ፡ በጕልበት፡ አቆመ፤ ራሱን፡ ሰውነቱን፡ ወይም፡ ሌላውን። መጽሐፍ፡ ግን፡ በበረከና፡ በአብረከ፡ ቦታ፤ ይልቁንም፡ በበረከ፡ ፈንታ፡ አስተብረከ፡ ይላል፤ እያስኘም። አስተብረከ፡ በብረኪሁ፡ ከመ፡ ይስተይ። አስተብረከ፡ ወአስተብቍዖ። ሰገደ፡ ሎቱ፡ ወአስተብረከ። አስተብርኩ፡ እለ፡ መነና፡ (መሳ፯፡ ፭። ማር፩፡ ፵። ቀሌ። ደራሲ)። ዳግመኛም፡ በአብረከ፡ ፈንታ፡ አቤተ፡ ይላል፡ ስሕተት፡ ነው፡ (ዘፍ፳፱፡ ፲፩)።

**ባርክ፤ኮት፤(ባረከ፡ ይባርክ፡ ይባርክ)፤** ማመስገን፤ ከመንበርከክ፡ ጋራ፡ ወይም፡ ትንበርክኮ፡ ምስጋና፡ ማቅረብ። ባርኮና፡ በሪክ፡ በሴም፡ ቋንቋ፡ ኹሉ፡ አንድ፡ ዘር፡ ነው፤ የዱሮ፡ ሰዎች፡ አበው፡ ቀደምት፡ ነቢያት፡ ካህናት፡ የፈጣሪን፡ ስም፡ ሲጠሩ፡ ሲጸልዩ፡ ሲያመሰግኑ፡ ስግደው፡ ትንበርክከው፡ ነበረና፤ ባረከ፡ ማለት፡ የኹሉንም፡ ስልት፡ ያሳያል። ይባርክዎ፡ ሡሉ፡ ግብረ፡ እግዚ፡ ለእግዚ። ወባረኩ፡ ዘ፡ ቡራኬ። ባርኩ፡ ለስሙ፡ በሡሉ፡ ጊዜ፡ (ዳንኛ፡ ፶፯—፹፰። ዘፀ፲፭፡ ፩። ሚራ፴፱፡ ፴፭)።

**ባረከ፤** በቁሙ፤ አማተበ፤ ጸሎት፡ ቡራኬ፡ ደገመ። አእኰተ፡ (አኰተ)፡ ባረከ፡ ወፈተተ። ኀቡረ፡ ይባርኩ፡ ማእደ፡ በውስተ፡ ጸሎት። ኢይባርኩ፡ ላዕለ፡ በጸል፡ (ቅዳ። ግብ፪፡ ፵፪። ፍ፡ ነ፡ ፲፯)።

—፤ መረቀ፤ መልክም፡ ስጦታን፡ ስለ፡ ሰው፡ ተመኘ፡ ተናገረ፤ አዘዘ፡ ሰጠ። አከበረ፡ ሾመ፤ አበዛ፡ አበረከተ፡ (ዘፀ፩፡ ፳፪፡ ፳፰። ፲፪፡ ፪፡ ፫። ፲፯፡ ፲፯)። ወዘእን በለ፡ ካሕድ፡ ዘየዐቢ፡ ይባርክ፡ ለዘይንእስ። ብሔር፡ ኀበ፡ በልዑ፡ ኅብስተ፡ ዘባረከ፡ እግዚእ፡ (ዕብ፯፡ ፯። ዮሐ፮፡ ፳፫)።

—፤ ሰደበ፡ አዋረደ፤ ዐማ፡ ነቀፈ፤ ረገመ፡ ካደ። ውስተ፡ ገጽከ፡ ይባርከከ። ባርኮ፡ ለእግዚ፡ ወሙት። ባረካሁ፡ ለእግዚ፡ ወለንጉሥኒ፡ (ኢዮ፩፡ ፲፪። ፪፡ ፭፡ ፱። ፫ነገ፡ ፳፩፡ ፲፡ ፲፫። ስንክ፡ ታኅ፩)።

**አባረከ፤** አስባረከ፡ አስመረቀ፤ አስመሰገነ፡ ቡሩክ፡ አሰኘ።

**ተባረከ፤(ተደራጊና፡ ተደራራጊ)፤** በቁሙ፤ ተመሰገነ፡ ተመረቀ፤ ቡራኬ፡ ምስጋና፡ ተቀበለ፤ በዛ፡ በረከተ። ይትባረክ፡ እግዚ። ሰገደ፡ ሎቱ፡ ወተባረከ፡ እምኔሁ፡ (ሩት፬፡ ፲፬። መዋሥ)። ተበራረከ፡ ተመራረቀ፤ ተመሰጋገነ፡ ርስ፡ በርሱ። ይትባረኩ፡ ቦቱ፡ አሕዛብ፡ ምድር። ተባረኩ፡ በበይናቲሆሙ፡ (መዝ፡ ፸፩፡ ፲፰። ስንክ፡ የካ፱)።

**ቡሩክ፤(ካን፡ ካት፡ ርካት)፤** በቁሙ፤ የተባረከ፡ የተመሰገነ፤ ክቡር፡ ምስጉን፡ ምሩቅ። ሙሴ፡ ዘቡሩክ፡ ዝክሩ። ቡሩክ፡ አንተ፡ አምላክነ። ቡርክት፡ አንቲ፡ እምአንስት፡ ወቡሩክ፡ ፍሬ፡ ከርሥኪ። ቅብዕ፡ ቡሩክ፤ ቅዱስ፡ (ሢራ፵፭፡ ፩። ዮዲ፲፫፡ ፲፯። ሉቃ፩፡ ፵፪። ዘፀ፳፱፡ ፳፩)።

**ቡራኬ፤(ክያት)፤** ሳቢና፡ ጥሬ፡ ዘር። መባረክ፤ (ጥባ) መባረክ፤ አበራረክ፤ በቁሙ፡ ቡራኬ፤ ምስጋና፡ ምርቃት። ባርከኒ፡ አባ፡ ለወልድከ፡ ዝኬ፤ እስመ፡ ልማዱ፡ ለመምህር፡ ቡራኬ። ጸሎተ፡ ቡራኬ። ቡራኬሁ፡ ለሴም። ቡራኬ፡ ወመርገም። ትጽናስ፡ ኮነ፡ መርገመ፡ ወብዕልስ፡ ኮነ፡ ቡራኬ፡ (ደራሲ። ቅዳ። ያዕ፫፡ ፲። አፈ፡ ተ፲፰)።

—፤ የመከፈልት፡ ወግ፤ ታላቅ፡ ዕድል፡ ለባለወገች፡ የሚሰጥ። እሊሁም፡ መሪጌታና፡ ቄስ፡ ዐቃቢ፡ ናቸው።

**በረከት፤(ታት)፤** በቁሙ፤ ማበርከት፤ መበርከት፤ አበረካከት፤ ብርከታ፡ ብዛት። ምስጋና፡ ምርቃት፤ ቡሩክ፡ መባል፤ ጸጋ፡ ሀብት፡ ድልብ፡ ዐባባ፤ መልክም፡ ነገር፡ ኹሉ። በረከተ፡ ኅብስት። በረከተ፡ አሮን፡ ፈኑ፡ ላዕለ፡ ሕዝብከ። ክብር፡ ወስብሐት፡ ወ

በረከት ። ዙሉ ፡ በረከት ፡ እለ ፡ ባረከኒ ፡ እግዚ ። በረከተ ፡ ግብጽ ። ትበልዑ ፡ በረከተ ፡ (ትር ፡ ወን ። ሚራ ፴፮ ፡ ፳፱ ። ራእ ፳ ፡ ፲፱ ፡ ፲፫ ። ኩፋ ፡ ፲፱ ። ዘፍ ፵፭ ፡ ፲፰ ። ኢሳ ፶፭ ፡ ፪) ።

**አስተባረከ** ፤ አበራረከ ፡ አመራረቀ ፤ አመስጋገን ። ዳግመኛም ፡ አባረከ ፡ በማለት ፡ ፈንታ ፡ አስተባረከ ፡ ይላል ፤ ምክንያቱም ፡ የባረከ ፡ ቤት ፡ ተደራጊው ፡ ከተደራራጊው ፡ እንዲደረብ ፤ አስደራጊውም ፡ ከደራራጊው ፡ ይደረባልና ፤ ስለዚህ ፡ ነው ። መደረቡም ፡ ሥርወ ፡ ቀለሙ ፡ ራብዕ ፡ ስለ ፡ ኾነለት ፡ ነው ፤ ተቃተለ ፡ አስተቃተለ ፡ እንደ ፡ ማለት ፤ አስተን ፡ እይ ።

**ብርኩት** ፤ የደንጊያ ፡ ግርንቡድ ፤ ወይም ፡ የብረት ፡ ዙሖ ፡ ከባድ ። ወቦኡ ፡ ክልኤቱ ፡ እምአግብርቲሁ ፡ በሌሊት ፡ ወአንበሩ ፡ ዲበ ፡ ገጹ ፡ ለሰምከር ፡ ንጉሥ ፡ ፋርስ ፡ ብርኩተ ፤ ወነበረ ፡ አሐዱ ፡ እምኔሆሙ ፡ ዲበ ፡ ርእሱ ፡ ወካልኡ ፡ ዲበ ፡ እገሪሁ ፡ እስመ ፡ ውእቱ ፡ አረጋዊ ፡ ዐቢይ ፡ ወሞተ ፡ ሰቤሃ ፡ (ጊ ፡ ወ ፡ ሐ ፡ ገ፵፰) ።

**ብርኩታ** ፡ (ዐማርኛ) ፤ በቁሙ ፤ በፍም ፡ የሚበስል ፡ ርሚጦ ፡ ቂጣ ፤ ሲበሉት ፡ የሚያጠግብ ፡ የሚመክት ፡ የሚበረክት ፤ የጭብጦ ፡ ዐይነት ። ኪመ ፡ በላዕሌሁ ፡ ያስተርኢ ፡ ግብረ ፡ በሲታ ፤ ዘዕውሩ ፡ ተወልደ ፡ ብርኩታ ፡ (ቅኔ) ።

**ቢረሌ** ፤ (ልያት ። ጽር ፡ ቢሬሊዎን) ፤ ዕንቍ ፡ ፈርጥ ፤ የብርሌ ፡ የብርጭቆ ፡ ደንጊያ ፡ (ዘፀ ፳፰ ፡ ፳ ። ጦቢ ፲፫ ፡ ፲፯) ። ሳምን ፡ በቢረሌ ፡ ወታለዕ ፡ በወራውሬ ። አናቅጽኪ ፡ ዘቢረሌ ፡ (ራእ ፳፩ ፡ ፳ ። ኢሳ ፶፬ ፡ ፲፪) ። በቁሙ ፤ ብርሌ ፡ ብርጭቆ ፡ ነጭ ፡ ጥሩ ። ይሰትዩ ፡ ወይነ ፡ በማህው ፡ ወቢረሌ ። ምስኪ ፡ ዘውስተ ፡ ቢረሌ ። ቢረልያት ፡ ብዙኃት ፡ (ዓሞ ፯ ፡ ፯ ። ፍ ፡ ነ ፡ ፴፫ ፡ ፬ ። ፊልክ ፡ ፪፻፯) ።

**በርሙዳ** ፤ (ቅብጥ) ፤ የወር ፡ ስም ፡ ሚያዝያ ፤ በጽርእ ፡ ፈርሙ(ቲ)ኒ ፡ ይባላል ፡ (ገድ ፡ አዳ ። አርጋ ፡ ፬ ፡ ፮) ። በርሙዳ ፡ ይሰመይ ፡ ፈርሙኒ ፡ (አቡሻ ፡ ፳ ። ተረ ፡ ቄር) ።

**በረምሃት** ፤ (ቅብጥ) ፤ ዝኒ ፡ ከማሁ ፤ ስመ ፡ ወርኅ ፡ መጋቢት ። በጽርእ ፡ ፋሚኑት ፡ ይባላል ። በረምሃት ፡ ይሰመይ ፡ ፋሚኑት ፡ (አቡሻ ፡ ፳ ። ተረ ፡ ቄር ፳፩) ።

**በርሞስ** ፤ አስቈጥስ ፡ የነመክሲሞስ ፡ የናርሳንዮስ ፡ ገዳም ፤ ደብረ ፡ ሮም ፡ ገዳመ ፡ ሮም ፡ ማለት ፡ ነው ፡ (ስንክ ፡ መጋ፳፯) ።

**ብርኒ** ፤ ድመት ፡ የጽርኒ ፡ ዐይነት ። ዐይነ ፡ ብር ፡ ዐይናማ ፡ ማለት ፡ ነው ፤ ለድመት ፡ እያበሩላት ፡ እንዲሉ ።

**ብራና** ፤ (ዐማርኛ ። ጽር ፡ ሜምብራና) ፤ በቁሙ ፤ ብርሃና ፤ በርሀን ፡ ተመልከት ። ኀልፍ ፡ አሐደ ፡ ብራና ፡ ወእምዝ ፡ ኅሊፈከ ፡ ስመንተ ፡ አዕማደ ፡ ወዐሥርተ ፡ ወሠለስተ ፡ መሥመራተ ፡ ትረክብ ፡ መትልወ ፡ ዝንቱ ፡ ቃል ፡ (አዋል) ።

**በረዐ** ፤ ዖት ፤ (በርዐ ፡ ይበርዕ ፡ ይብራዕ ። ዐረ ፡ የረዐ ። ዕብ ፡ ያራዕ) ፤ መራድ ፡ መንቀጥቀጥ ፤ መታወክ ፡ መናወጥ ፤ መገፋት ፡ መናጥ ፤ መወዛወዝ ፤ ከፍርሀት ፡ ከነፋስ ፡ የተነሣ ፡ (ማቴ ፲፩ ፡ ፯) ።

**ብርዕ** ፤ (ብ ፡ አብራዕ) ፤ ሸንበቆ ፤ የጕሽ ፡ መቃ ፤ የሸንበቆ ፡ ዐይነት ፡ ውስጠ ፡ ክፍት ፤ አገዳ ፡ ቅልጥም ። በቁሙ ፡ የጸሐፊ ፡ ብር ፤ የገብስ ፡ የስንዴ ፡ ብር ፤ ገለባ ፡ ማር ፡ ቂሻሻ ። በትረ ፡ ብርዕ ። ብርዐ ፡ ባሕሩስ ። አብትር ፡ ፀቡሳን ፡ ወአብራፅ ፡ ቅጥቁጣን ። ዐምደ ፡



ብርዕ ፡

ወአብራዊሃ ፡ (ኢሳ ፴፯ ፡ ፯ ። ፩ ፡ ፴፩ ። መጽ ፡ ምስ ። ዘፀ ፳፩ ፡ ፴፩—፴፯) ። ሱብዐቱ ፡ ሱብል ፡ ዘሥዊት ፡ ዘሠረጹ ፡ እምአሐዱ ፡ ብርዕ ። ብርዐ ፡ ይመስሎ ፡ መናፍጽሐ ። ማዕር ፡ ወብርዕ ፡ ዘይየብስ ። እሳት ፡ እንተ ፡ ትበልዕ ፡ ብርዐ ፡ (ዮሴፍ ። ኢዮ ፵፩ ፡ ፳ ። ፲፫ ፡ ፳፩ ። ዮኤ ፪ ፡ ፭ ። ዓብድ ፡ ፲፰ ። ዘፀ ፭ ፡ ፲፪ ። ፲፭ ፡ ፯) ። ብርእ ፡ ተብሎ ፡ እንደ ፡ ዕብራይስጡ ፡ በአልፍ ፡ ሲጣፍ ፡ ግን ፤ የማግስኛ ፡ ፍጥረት ፡ ያሰኛል ፡ (ዘፍ ፩ ፡ ፲፩ ፡ ፲፪) ።

**ብርፎሬከን** ፤ (ጽር ፡ ፕሮፎሬኮስ) ፤ የትንቢትና ፡ የስብከት ፡ የተግሣጽ ፡ ቃል ፡ ጩኸ ፡ ጉንትቶ ፡ አሰምቶ ፡ የሚናገሩት ። ወብርፎሬከንኒ ፡ ውእቱ ፡ ቃል ፡ ዘሰምዕዎ ፡ ነቢያት ፡ እምእግዚ ፡ ወውእቱ ፡ ቃለ ፡ ትንቢት ፡ (ሃይ ፡ አበ ፡ ጎር) ።

**በሬጽ** ፤ ጾት ፤ (በረጸ ፡ ይበርጽ ፡ ይብርጽ ። ዕብ ፡ ባራጽ ፤ ዐለፈ ፡ ተረፈ ፤ ፈልቶ ፡ ገንፍሎ) ፤ ማንጸብረቅ ፡ ማሸብረቅ ፤ ማወልወል ፡ ማጽደልደል ፤ የመልክ ፡ የፊት ።

**ተበረጸ** ፤ ተብለጨለጨ ፤ ብልጭልጭ ፡ ቊልጭልጭ ፡ አለ ። እምቅድመ ፡ ይትባረጹ ፡ ከዋክብት ፡ (ቅዳ ፡ አፈ) ።

**በረጽ** ፤ (ዐረብ) ፤ ለምጽ ፤ ነጭ ፡ የሚብለጨለጭ ።

**በሬቅ** ፤ ቆት ፤ (በረቀ ፡ ይበርቅ ፡ ይብርቅ ። ዕብ ፡ ባራቅ ። ሱር ፡ ብራቅ ። ዐረ ፡ በረቀ) ፤ መብረቅ ፡ ብልጭ ፡ ማለት ፤ መፍለቅ ፡ ማንጸብረቅ ፤ መወርወር ፡ መመዘዝ ፤ የመብረቅ ፡ የሰይፍ ። ብርቅ ፡ ድንቅ ፡ ታይቶ ፡ የማያውቅ ፡ መኾን ፤ መታየት ፡ መገለጥ ። በሬጽና ፡ በሬቅ ፡ አንድ ፡ ዘር ፡ ናቸው ፤ በሬጽ ፡

ከበሬቅ ፡ ወጥቷል ። በዕጠሱ ፡ ይበርቅ ፡ ብርሃን ። ወላ ትው ፡ ይበርቅ ። በረቀ ፡ ሥጋሆሙ ። ግብተ ፡ በረቀ ፡ መብረቅ ፡ ዲቤሁ ፡ እምሰማይ ፡ (ኢዮ፴፮ ፡ ፴ ። ናሖ ፡ ፫ ። መቃ ፡ ፲፪ ። ድጓ ። ግብ፱ ፡ ፫) ። መበርቋት ፡ መገር ጣት ፤ ያዝመራ ።

**አብረቀ** ፤ አበረቀ ፡ አባረቀ ፤ አብረቀረቀ ፤ መብ ረቅ ፡ ጣለ ፡ ወረወረ ፤ አበራ ፡ ገለጠ ፤ ብልጭ ፡ አደረገ ። እግዚ ፡ አብረቀ ፡ መብረቀ ። አብርቅ ፡ መባርቅቲከ ። ፀሓየ ፡ ጽድቅ ፡ ዘሞአ ፡ ሰሞት ፡ ያበርቅ ፡ ጸዳሉ ፡ ላዕ ሌነ ። አራዊት ፡ እለ ፡ እምውስተ ፡ ዐይኖሙ ፡ ፀዋገ ፡ ቀለምጺጸ ፡ ያበርቁ ፡ (፪ነገ ፡ ፳፪ ፡ ፲፭ ። መዝ ፡ ፻፲፫ ። አፈ ፡ ድ፱ ። ጥበ፲፩ ፡ ፲፱) ።

**መብረቅ** ፤ (ብ ፡ መባርቅት) ፤ በቁሙ ፤ የ እሳት ፡ ሰይፍ ፡ የእሳት ፡ ፍላጻ ፡ በዝናም ፡ ጊዜ ፡ ከደመና ፡ አፎት ፡ የሚመዘዝ ፡ የሚወረወር ። ብልኀተ ፡ መብረቅ ። መብረቅ ፡ ወፀዓዕ ፡ ወነጐድጓድ ። ይረውጽ ፡ መብ ረቅ ፡ ቅድመ ፡ ነጐድጓድ ። ገብረ ፡ መባርቅተ ፡ ለዝ ናም ፡ (ቅዳ ፡ ኤጲ ። ራእ፬ ፡ ፭ ። ሢራ፴፭ ፡ ፲ ። ኤር፲ ፡ ፲፫) ።

—፤ የክብር ፡ ብርሃን ፤ ጮራ ፡ ምዕዛር ። ሰላም ፡ ለሥ ንኪ ፡ ዘአዋከየ ፡ መብረቃ ፡ ለብሔረ ፡ ጽልመት ፡ ወ ጣቃ ። መብረቅ ፡ ለሥጋሁ ፡ ክለላ ፡ (ስንክ ፡ መጋ፳ ። ሚያ፴) ።

**በረቅ** ፤ በቁሙ ፤ ነጭ ፡ ዐፈር ፡ ደንጊያ ፤ ብሕክ ፡ ጠመኔ ፡ የኖራ ፡ ዐይነት ።

**ብርቅ** ፤ በቁሙ ፤ ወትሮ ፡ የማይታይ ፡ በኹሉ ፡ የማይገኝ ፡ ድንቅ ፡ ሥራ ፡ ጕድ ፡ ታምራት ፡ መንከራት ።

**በራቂኒም** ፤ (ዕብ ፡ ባርቃኒም) ፤ ነጣጭ ፡ እሾኾች ፡ ኵሸሽሎች ፤ ወይም ፡ ግራሮች ፡ የግራር ፡ ዐይ ነቶች ፤ አንዱን ፡ ባርቃን ፡ ይላል ። አርቆሚንን ፡ እይ ፤ ከዚህ ፡ ጋራ ፡ አንድ ፡ ነው ፡ (መሳ፰ ፡ ፲፯) ።

**በሬር ፤ ሮት ፤ (በረ ፡ ይበርር ፡ ይብርር ። ዕብ ፡ ባራር ። ሱር ፡ ባር ። ዐረ ፡ በረ ፤ በሬረ)** ፤ መምረጥ ፡ መለየት ፤ መልቀም ፡ ማጥራት ፤ ጽሩይ ፡ ጸዐዳ ፡ ማድረግ ፤ የማዕደናት ። በርበረን ፡ እይ ።

**ተበረ ፤ (ይትበረር)** ፤ ተለቀመ ፤ ጠራ ፡ ጥሩ ፡ ኾነ ። ብርትና ፡ ብረት ፡ የዚህ ፡ ዘር ፡ ነው ።

**ብሩር ፤ (ራን ፡ ራት ፡ ርርት)** ፤ የተመረጠ ፡ የተለየ ፤ ልቅም ፡ ጥሩ ፡ ነጭ ፡ ማዕደን ።

**ብሩር ፤ (ብ ፡ በራውር ፤ ብሩራት)** ፤ ብር ፤ ከቡር ፡ ገንዘብ ፡ የወርቅ ፡ ምክትል ። ብሩር ፡ ጽሩይ ። ብሩር ፡ ኅሩይ ። ሠላሳ ፡ ብሩር ። ህየንተ ፡ ወርቅ ፡ ወ ብሩር ፡ ጸፀዳ ፡ (መዝ ፡ ፲፩ ። ምሳ፰ ፡ ፲፱ ። ማቴ፳፯ ፡ ፲፭ ። ደራ.ቢ) ።

**በረረ ፤ (ሰረረ)** ፤ በቁሙ ፤ ሮጠ ፡ ክንፈ ፡ ተጣ ደፈ ። ዐለፈ ፡ ዘለቀ ፤ በሳ ፡ ነደለ ። ወፅአ ፡ ኀጺኑ ፡ በሬሮ ። ረገዘ ፡ ለአሐዱ ፡ ውስተ ፡ ሰንብዑ ፡ ወወፅአት ፡ ኩ ናት ፡ በሬራ ፡ እንተ ፡ ዘባኑ ፡ ወወግአቶ ፡ ለካልኡ ። በ ረረ ፡ ቅትራት ፡ ውስተ ፡ እገሪሁ ። በረሮ ፡ እስከ ፡ ዘባኑ ። ኢይበርሮ ፡ ቀስተ ፡ ብርት ፡ (፪ነገ ፡ ፪ ፡ ፳፪ ። ገድ ፡ ተክ ። ስንክ ፡ ነሐ፲፬ ። መሳ፫ ፡ ፳፪ ። ኢዮ፳ ፡ ፳፬) ።

**በራሪ ፤ (ሪት ፡ ርያን ፡ ያት)** ፤ በቁሙ ፤ የ ሚያልፍ ፡ የሚዘልቅ ።

**በር** ፤ በቁሙ ፤ ደጅ ፡ አፍ ፡ መውጫ ፡ መግቢያ ፡ መዝለቂያ ፡ ማለፊያ ፡ (ዐማርኛ) ። ነቅጸን ፡ ተመልከት ።

**ቤሩሽ ፤ (ዕብ ፡ ብሮሽ ። ጽር ፡ ኪፓሪሶስ)** ፤ ጥድ ፤ የጥድ ፡ ዐይነት ፡ ዛፍ ፡ ወፍራም ፡ ረዥም ፡ መለሎ ። ለየዐውዩ ፡ ቤሩሽ ፡ እስመ ፡ ወድቀ ፡ ዘግባ ፡ (ዘካ፲፩ ፡ ፪) ።

**ቤሩሲም ፤ በርሲም ፤ (ዕብ ፡ ብሮሽም)** ፤ ዝኒ ፡ ከማሁ ፤ ጥዶች ። ዕፀወ ፡ በርሲም ፡ (፫ነገ ፡ ፭ ፡ ፭) ።

**ቤርሳቤሕ ፤ (ዕብ ፡ ብኤር ፡ ሻባዕ)** ፤ ዐዘ ቅተ ፡ መሐላ ፤ የመሐላ ፡ ጕድጓድ ፡ (ዘፍ፳፩ ፡ ፴፩) ።

**ቤርሴክታን ፤ (ጽርእ)** ፤ ሣጥን ፤ ታቦት ፤ የገ ንዘብ ፡ የሬሳ ። ኤርጋብን ፡ እይ ፡ (፩ነገ ፡ ፮ ፡ ፰) ።

**ብርስኔ ፤—ባርሰነት ፤—ምርስኔ ።**

**ብርስን ፤ (ዐረ ፡ ቡልስን ፤ ዐደስ ። ዕብ ፡ ዐዳሽ)** ፤ ምስር ፤ ጥሩ ፡ ያበባ ፡ እኽል ፡ ወጥ ፡ የሚኾን ፤ ቅንጣቱ ፡ ታናናሽ ፡ ክኩ ፡ ቀይ ። ምስራዊ ፡ ዘእምስር ፡ ማለት ፡ ነው ፤ የግብጥ ፡ ብርስን ፡ ካገር ፡ ኹሉ ፡ ብርስን ፡ የሚያምር ፡ የሚበልጥ ፡ በውድ ፡ የሚሼጥ ፡ ስለ ፡ ኾነ ፡ የሻም ፡ ዐረብ ፡ ዐደስ ፡ መስሪ ፡ እንዲል ፡ ምስራዊ ፡ ሲል ፤ ተርሙስ ፡ ግብጦ ፡ እንዲባል ፡ ብርስንም ፡ ምስር ፡ ይባ ላል ፤ ጥንተ ፡ ስሙ ፡ ዐደስ ፡ በምርስኔና ፡ በብርስኔ ፡ ሞ ክሼ ፡ ወደ ፡ ባርሰነት ፡ ኺዷል ። ፪ኛም ፡ ስለ ፡ ቅላቱ ፡ ግብጥ ፡ ይባላል ፤ ግብጥ ፡ ምስር ፡ እንዲሉ ። ልባም ፡ ሴት ፡ በጥሩ ፡ ዐዋዜ ፡ ሠርታ ፡ ስታቀርበው ፡ በቅላት ፡ ላይ ፡ ቅላት ፡ ተጨምሮለት ፡ መልኩ ፡ ጿሕ ፡ ጃዊ ፡ እን ድኪ ፡ ፍሕሶ ፤ ዐረብ ፡ አንቀልባ ፡ የሱፍ ፡ አበባ ፡ ይመስ ላልና ፤ የምሥራች ፡ ለሚል ፡ ምስር ፡ ብላ ፡ ማለት ፡ ስለ ዚህ ፡ ነው ፤ የምሥሬች ፡ ቅሉ ፡ ከምስር ፡ ወጥ ፡ መጥቷል ። ሽማግሎችም ፡ የምስር ፡ ወጥ ፡ ብዙርና ፡ የሚያሼጥ ፡



ብርስን ፡

ይሉታል ፡ (ዘፍ፳፭ ፡ ፴፬ ። ኩፋ ፡ ፳፱) ። ዐተረ ፡ ወብር ስነ ። ገራህት ፡ ዘምሉእ ፡ ብርስነ ፡ (፪ነገ ፡ ፲፯ ፡ ፳፰ ። ፳፫ ፡ ፲፩ ። ሕዝ፬ ፡ ፱) ። የምስር ፡ ዐይነት ፡ ፫ ፡ ነው ፤

ከዚህ ፡ ሌላ ፡ ያይጥ ፡ ምስር ፡ የገመል ፡ ምስር ፡ የሚባል ፡ አለ ። ይበልዕ ፡ ሠለስተ ፡ ብርስነ ፡ (ስንክ ፡ ኅዳ፲፫) ።

**ቡራት ፤ ቡራቴ ፤ (ጽር ፡ ብራቲ ። ዕብ ፡ ብሮት) ፤** ስመ ፡ ዕፅ ፤ ብርቱ ፡ ጠንካራ ፡ ዕንጨት ፡ የጥድ ፡ የደቅማ ፡ ዐይነት ፡ እንዳዝጋሮ ፡ ያለ ፡ ምዑዝ ፡ ዐዚዝ ። ወይም ፡ ርሱው ፡ ራሱ ፡ ጥዱ ፡ ደቅማው ፤ ቤሩሽን ፡ እይ ፡ ዕብራይስጡ ፡ ብሮሽን ፡ ሲያበዛ ፡ ብሮት ፡ ይላልና ፤ ቡራቴ ፡ ውስጠ ፡ ብዙ ፡ ነው ፤ ምስጢሩም ፡ ከብሩርና ፡ ከብርት ፡ ይስማማል ።

**ብርት ፤ (ታት ። በሪር ፡ በረ ፤ ብሩር) ፤** በቁሙ ፤ የብረት ፡ ወገን ፡ የብር ፡ ምክትል ፤ ብርቱ ፡ ማዕደን ፤ መዳብ ፤ ንሐስ ፤ መዳብ ፡ ቀዩ ፤ ንሐስ ፡ ብጫው ። ግብረ ፡ ብርት ፡ ወንጺን ። ብርት ፡ ርሱን ። ብርተ ፡ ሊባኖስ ። ፍጽምከ ፡ ዘብርት ፡ (ዘፍ፬ ፡ ፳፪ ። ሕዝ፵ ፡ ፫ ። ራእ፩ ፡ ፲፭ ። ኢሳ፵፰ ፡ ፬) ።

**ብረት ፤ (ዐማርኛ) ፤** በቁሙ ፤ ኀጺንን ፡ ተመልከት ። ብርቱ ፡ ማለት ፡ ከዚህ ፡ ወጥቷል ።

**ብርትኳን ፤ (ዐረብ) ፤** በቁሙ ፤ በዡረ ፡ ሎሚ ፤ ጥሩ ፡ ጥፍጥ ፡ ተክል ።

**በስብሶ ፤ ሶት ፤ (በስበሰ ፡ ይበሰብስ ፡ ይበስብስ ። ዐረ ፡ በጸ ፤ በጽበጸ ። ዕብ ፡ ባጻጽ ፡ ባጽቤጽ ፤ ፈለቀ ፡ መነጨ) ፤** መከፈት ፡ መግለጥ ፡ ማቍለጭለጭ ፤ የዐይን ። መነስነስ ፡ መቍላት ፡ ማወዝወዝ ፤ የኸራት ። በቁሙ ፡ መበስበስ ፤ መራስ ፡ መርጠብ ፤ መበላሸት ፡ (ዐማርኛ) ። በኍበኍን ፡ እይ ። ዘሩ ፡ በሲስ ፡ በስ ፤ በሰሰ ፡ ነው ።

**አንበስበሰ ፤** አገለባበጠ ፤ ተገለባበጠ ፤ አርገበገበ ፤ ተርገበገበ ፤ የዐይን ፡ የቅንድብ ፤ ለእጅም ፡ ይኾናል ። አንበስብሶ ፡ ዐይን ። አንበስብሶ ፡ ቀራንብቲሆን ፡ (ቀሌ ። ፈ ፡ መ ፡ ፴፬ ፡ ፳) ።

—፤ አራመደ ፡ አሻገረ ፡ ወረወረ ፤ ተራመደ ፡ ተወረወረ ፤ የዐይን ፡ የእግር ፡ የመብረቅ ። ያንበሰብስ ፡ ዲበ ፡ አውግር ። እምቅድመ ፡ ያንበስብስ ፡ ፀዓዕ ። ያንበሰብሱ ፡ መባርቅት ፡ እምፀአተ ፡ ቃሉ ፡ (ማሕ፪ ፡ ፳ ። ቅዳ ፡ አፈ ። አርጋ) ።

—፤ አመሳለሰ ፡ ተመሳለሰ ፤ ብልጭ ፡ ድርግም ፡ ከፍት ፡ ክድን ፡ አለ ፤ የሰማይ ፡ የዐይን ። ወከመ ፡ ፀሓይ ፡ አንበስበሰት ፤ ተመሳለሰች ፡ (ቅዳ ፡ አት) ።

**ነበስባስ ፤** የዐይን ፡ የሸፋሽፍት ፡ አገላለጥ ፤ አስተያየት ፡ ጥቅሻ ። ዐይንን ፡ ማፍጠጥ ፡ ማጕረጥ ፡ መበልጠጥ ፤ ክፍ ፡ ዝቅ ፡ ቈለል ፡ ቈለል ፡ ከብለል ፡ ከብለል ፡ ማድረግ ፤ በዐይን ፡ ዐለንጋ ፡ መግረፍ ፡ መሸንቈጥ ፡ መገርመም ፡ መግጠጥ ፡ መገላመጥ ። አልቦ ፡ ቀዲመ ፡ ህላዌ ፡ ለአብ ፡ እምወልድ ፡ ኢመጠነ ፡ ቅጽበተ ፡ ዐይን ፡ ወኢመጠነ ፡ ነበስባሰ ፡ ቀራንብት ። ሰላም ፡ ለቀራንብቲከ ፡ ዘነባስባሶን ፡ ይዋሄ ፡ (መጽ ፡ ምስ ። ደራሲ) ።

—፤ ነፋስ ፡ እስትንፋስ ፤ ሽው ፡ ሽው ፤ እፍ ፡ እፍ ፡ ማለት ፤ ሽውታ ፡ እፍታ ። አንብቦ ፡ መጻሕፍት ፡ ከመ ፡ ነበስባሰ ፡ ነፋሳት ፡ ውስተ ፡ አፉሁ ፡ ለአብድ ፤ ይትሜካሕ ፡ በአንብቦታ ፡ ወኢየአምር ፡ ዘውሳጢታ ፡ (መጽ ፡ ምስ) ።

**አንበሳ ፤ (ብ ፡ አናብስት) ፤** በቁሙ ፤ ግርማ ፡ ያለው ፡ አውሬ ፤ ኀይለኛ ፡ ተፈሪ ፤ ነጣቂ ፡ ሰባሪ ፤ ዘላይ ፡ ተወርዋሪ ፤ ዐዳኝ ፡ ግሩመ ፡ ዐይን ፡ የድመት ፡ ወገን ። ድመትን ፡ ብስ ፡ ማለት ፡ ከዚህ ፡ የወጣ ፡ ነው ። አንበሳ ፡ ዘጽኑሕ ፡ ለመሚጥ ። ረከቦ ፡ አንበሳ ፡ በፍኖት ፡ ወቀተሎ ። ፈነወ ፡ አናብስተ ፡ ወበልዕዎሙ ። ግበ ፡ አናብስት ፡ (መዝ ፡ ፲፮ ። ፫ነገ ፡ ፲፫ ፡ ፳፬ ። ፬ነገ ፡ ፲፯ ፡ ፳፭ ። ዳንኤ ፡ ፯) ።



አንበሳ ፡

**አንበሳዊ ፤ (ዊት ፡ ውያን ፡ ያት) ፤** ያንበሳ ፡ ወገን ፡ ዐይነት ፤ አንበስማ ፤ አንበሳም ፡ ባላንበሳ ። ሰላም ፡ ኢብል ፡ ለአንበሳዊ ፡ አውሎግ ፡ (ስንክ ፡ የካ፲፩) ።

**አንበሳዊት ፤** አንበሲት ፤ እንስት ፡ አንበሳ ። ጣሕረ ፡ አንበሳ ፡ ወንቃወ ፡ አንበሳዊት ። እምከ ፡ አንበሳዊት ። ከመ ፡ አንበሳዊት ፡ (ኢዮ፬ ፡ ፲ ። ሕዝ፲፱ ፡ ፪ ። ዳንኤ ፡ ፬) ።

**አንበሰ ፤ አው ፡ ተአንበሰ ፤** አንበሳ ፡ ኾነ ፤ አንበሳ ፡ ተባለ ፡ በጠባይ ፡ በግብር ።

**አንበሳ ፤ ዕጓለ ፡ አንበሳ ፤** ታላቅ ፡ የታላቅ ፡ ልጅ ፤ ንጉሥ ፡ ወልደ ፡ ንጉሥ ፤ ኀያል ፡ ወልደ ፡ ኀያል ።

**እንበሳ ፤ (ዐማርኛ) ፤** በቁሙ ፤ ጥጃ ፡ የሚዘል ፡ የሚፈነጭ ። (ተረትና ፡ ምርቃት) ፤ ወተት ፡ ለንቦሳ ፤ ሥጋ ፡ ላንበሳ ። ቤት ፡ ለንቦሳ ፤ እስር ፡ እንቦሳ ።

**በሰከ ፡ (ዐማርኛ) ፤** በቲከ ፡ በተከ ፤ በጠሰ ። ሰና ፡ ተ ፡ ይዋረሳሉ ፤ ይልቁንም ፡ በዐረብ ፡ በቡርስት ፤ ሶር ፡ ቶር ።

**በሲል ፤ ሎት ፤ (በሰለ ፡ ይበስል ፡ ይብስል ። ዕብ ፡ ባሻል ። ሱር ፡ ብሼል) ፤** መብሰል ፤ መሻከክ ፡ መንደርከክ ፤ በእሳት ፡ በፀሓይ ፡ መለስለስ ፤ ተጋግሮ ፡ ተነፍሮ ፡ ታምሶ ፡ ተጠብሶ ፡ ለመበላት ፡ መድረስ ፤ ለጥርስ ፡ መግራት ፤ መሸት ፡ መጕምራት ። ኢበልዐት ፡ ምንተኒ ፡ በእሳት ፡ ዘበሰለ ። ሠዊት ፡ ዘበሰለ ። ዘእንበለ ፡ ይብስል ፡ (ስንክ ፡ ጥቅ፩ ። ኢሳ፲፮ ፡ ፩ ። ኤር ፴፩ ፡ ፴፪) ።

**ተበስለ፤** ተቀቀለ፤ ተጋገረ፤ ተቈላ፤ ተነፈረ። ሰላም፡ ለአሮን፡ ዕጓላተ፡ ርግብ፡ ዘአስረረ፤ በእሳት፡ ወማይ፡ ድኅረ፡ ተበስሉ፡ ኅቡረ፡ (ስንክ፡ ግንቦ፩)።

**ብሱል፤** (ላን፡ ላት፡ ስልት)፤ የበሰለ፤ የተቀቀለ፤ ቅቅል። ረከቦ፡ ለውእቱ፡ ጸብኅ፡ ፍሉሐ፡ ወብሱለ፡ (ስንክ፡ ታኅ፲፩)። ኢብሱል፡ በማለት፡ ፈንታ፡ ብሱል፡ ይላል፡ (ዘፀ፲፪፡ ፱፪)።

**ብስሎ፤** ብስል፡ ቅቅል፡ አንፊላ። ብስሎን፡ ቅቅሉን። ጥራዩ፡ ወኢብስሎ፡ በማይ፡ (ዘፀ፲፪፡ ፱፪)።

**ተብሲል፤** ንፍሮ፤ የኽል፡ ወጥ። ተብሴለ፡ ብርስን፡ (ዘፍ፳፭፡ ፳፱። ዳን፲፫፡ ፴፫)።

**አብሰለ፤** አበሰለ፤ አስበሰለ፤ ተኵስ፡ ጠበሰ። ያበስሉክሙ፡ በጽህርት። ያበስሉ፡ ሥጋ። ንጥፋሕ፡ ግንፋለ፡ ወናብስሎ፡ በእሳት፡ (ዓሞ፱፡ ፪። ፩ነገ፡ ፪፡ ፲፫። ዘፍ፲፩፡ ፫)።

**አብሳሊ፤** መብሰሊ፤ መበስል፤ (ላን፡ ላት)፤ የሚያበስል፡ አብሳይ፤ ጋጋሪ፡ ቀቃይ፤ ሊጥ፡ አፍሳሽ፡ ወጭት፡ ጠባሽ፤ ፀበዛ፡ ወጥ፡ ቤት። ሊቀ፡ መበስላን። ለመበስላት። ወለንባዝያት። ይቤሎ፡ ለመበስል፡ (ዘፍ፴፯፡ ፴፮። ፩ነገ፡ ፰፡ ፲፫። ፱፡ ፳፫)።

**መብሰል፤** (ላት)፤ ማብሰያ፡ መቀቀያ። መብሰለ፡ ብርት፡ ዘውዑይ፡ ፍልሐቱ። በመብሰለ፡ ብርት፡ ርሱን፡ (ስንክ፡ ንሐ፳። ጥበ፡ ጠቢ)።

**መብስል፤** የበሰለ፡ ምግብ፤ ትኩስ፡ ለስላሳ፤ የላመ፡ የጣመ። ኢይብልዑ፡ መብስላተ፡ አባ፡ ኅብስተ፡ ይቡስ፡ ወጼወ፡ ወማየ፡ (ቄድር)።

**ባሲላዊ፤** (ጽር፡ ባሲሌፍስ)፤ ንጉሣዊ፤ የንጉሥ፡ ወገን። ባሲላውያን፡ (ቀሌ)።

**ባሲልያ፤** መንግሥት፤ ጌትነት፡ ንጉሥነት። መጽሐፍ፡ ግን፡ ባሲልያሱ፡ በማለት፡ ፈንታ፡ ፋሲልያሱ፡ ይላል፤ ሱ፡ ዝርዝር፡ ነው፡ ከ። አምንስቲቲን፡ እይ።

**ባስልዮስ፤** የሰው፡ ስም፤ ንጉሥ፡ ንጉሣዊ፡ ማለት፡ ነው።

**ቢሶም፤** (ዕብ፡ በሼም፤ ባሳም)፤ የሽቱ፡ ዕንጨት፡ ዛፍ፤ መልካም፡ ሽታ፡ ያለው፡ ማናቸውም፡ ኹሉ፤ በየስሙና፡ በያይነቱ። ባለብሉዮች፡ ግን፡ ለይተው፡ ሾላ፡ ብሳና፡ ይሉታል፡ (ኩፉ፡ ፳፩)።

**በሶንስ፤ በሸንስ፤ ብሸንሶ፤** (ቅብጥ፡ ፓሾንስ)፤ የግብጦች፡ ወር፡ ግንቦት። ብሸንሶ፡ ይሰመይ፡ በሰንጹስ፤ ወካዕበ፡ ይሰመይ፡ ማኹን፡ (አቡሻ፡ ፳)።

**ብስራት፤** ባሶር፤—በሢር፡ በሠረ፤ ብሥራት፤ ባሦር፤

**በሲስ፤ ሶት፤** (በሰ፡ ይበስስ፡ ይብስስ)፤ መበሰስ፡ ማደን፤ በሳስ፡ መኾን፤ የወፊ፡ ያውፊ። በስ በሰን፡ እይ፤ የዚህ፡ ዲቃላ፡ ነው። ማለዘብ፡ ማለስለስ፤ የነገር፡ የልብስ።

**ቢሶስ፤ ቢሶን፤** (ጽር፡ ቢሱስ። ዕብ፡ ቡጽ። ሱር፡ ቡጺ። ዐረ፡ በዝ)፤ ከታን፡ ልብስ፡ ከታን፡ ልዝብ፡ ለስላሳ፤ ወይም፡ ነደው፡ ፈትሉ። ቢሶስ፡ ክዑብ፡ (ዘፀ፳፭፡ ፬። ፳፯፡ ፭፡ ፴፩፡ ፴፯። ሉቃ ፲፯፡ ፲፱)። ቢያበዛ፡ ቢሶሳት፡ ይላል። አልባበ፡ ቀጠንት፡ ወቢሶሳት፡ ወሚራያት፡ (መቃ፡ ገ፳፪)።

(ጥ) **ባት፤** (ዕብራ)፤ የርጥብ፡ መስፈሪያ፤ የዘይት፡ ገንቦ፡ ማድጋ። መስፈርተ፡ ባት። ባተ፡ ጽድቅ፡ (፫ነገ፡ ፲፩፡ ፲፩። ሕዝ፵፭፡ ፲፡ ፲፩)።

**ቤት፤—በቈሙ፤** ስመ፡ ፊደል፤—በዪት፡ ቤተ፤ በ።

**በቲክ፤ ኮት፤** (በተከ፡ ይበትክ፡ ይብትክ። ዐረ፡ በተከ። ዕብ፡ ባቴቅ፤ ናታቅ)፤ መበተክ፤ መበስከ፤ መቍረጥ፡ መበጠስ፤ አባላ፡ መምታት፤ መንቀል፡ መፈንቀል፤ መናድ፡ ማፍረስ፤ መስበር፡ መሠንጠር። እበትክ፡ ማኅሜከ። በተከ፡ ማእሰረ፡ (ንሐ፩፡ ፲፫። ኤር፳፡ ፳)። በበተከ፡ ፈንታ፡ አብተከ፡ ይላል፤ አያሰኝም። ታበትክ፡ ቃሎሙ፡ በኀበ፡ እግዚ፡ (ዘፀ፲፰፡ ፲፱)። ዕብራይስጡ፡ ግን፡ ውሂቤእታ፡ ይላል፤ ታበውእ፡ ታበጽሕ፡ ታቀርብ፡ ማለት፡ ነው። መብተክ፡ መብተክተክ፤ መብስክስክ፤ መበላሸት፡ ከንቱ፡ መኾን፤ የግብር፡ የነገር፡ (ዐማርኛ)።

**አብተከ፤** አበተከ፡ አብተከተከ፤ አስበተከ፡ አስቈረጠ፡ አስበጠሰ።

**ተበትከ፤** ተበተከ፤ ተቈረጠ፤ ተበጠሰ፤ ተነቀለ፡ ተፈነቀለ። ይትበተክ፡ ፈትል። ኢይትበተክ፡ ቶታነ፡ አሣእኒሆሙ። ይትበተክ፡ መሣግሪሆሙ። ተበትከ፡ እብን፡ እምደብር፡ (መሳ፲፮፡ ፱። ኤር፳፡ ፳፯። ሉቃ፩፡ ፯። ዳን፪፡ ፴፱፡ ፵፭)።

**ብቱክ፤** (ካን፡ ካት፡ ትክት)፤ የበተከ፤ የተበተከ፡ የተቈረጠ፡ የተበጣጠሰ፤ ብጥስጥስ። መሥገርት፡ ብቱክ። አሣእን፡ ብቱክ፡ (ኢሳ፡ ፲፱፡ ፱። ኢያ፱፡ ፫)።

**ብትክ፤** አባላ፡ የተመታ፤ ጥንብ፡ ውዳቂ፤ ታርዶ፡ የሰነበተ፡ (ዘሌ፲፱፡ ፯። ግብ፳፩፡ ፳፭)።

**ብትከት፤** መቍረጥ፤ መቈረጥ፡ መበጠስ፤ አበጣጠስ፡ ብጠሳ፤ ብጥስነት። በይብሰት፡ ፈንታ፡ ብትከት፡ ይላል፤ ስሕተት፡ ነው። እሰ፡ አልቦሙ፡ ብትከት፡ (መሳ፲፮፡ ፯፡ ፰)።

**ባተለ፤** (ዐማርኛ)፤ በቈሙ፤ ባተሌ፡ ኾነ፤ ደነገለ።

**ባቱል፤** (ዕብ፡ ብቱላ)፤ ድንግል፤ ወንድ፡ ያላወቃት፡ ሴት፡ ልጅ፤ ልጃገረድ፡ (አዋል)።

**ብቱል፤** (ላን፡ ላት። ዐረብ)፤ ድንግል፤ ሴት፡ ያላወቀ፡ ወንድ። ባተሌ፤ ፈት፡ መዐስብ፤ ሚስቱ፡

ሙታ፡ ወይም፡ በነውር፡ ተፈታ፡ ብቻውን፡ የሚኖር፤ ድንግላይ፡ ማለት፡ ነው።

**በተነ፤(ይበትን፤ ሀማርኛ)፤** በቁሙ፡ በተነ፡ በታተነ፤ ዘረወ፡ ዘርዐ።

**በቲር፤ ሮት፤(በተረ፡ ይበትር፡ ይብትር። ትግ፡ በትረ። ዕብ፡ ባታር)፤** መቍረጥ፡ መከርከም፤ ማረቅ፡ ማቅናት፤ ቀጥ፡ ለጥ፡ ማድረግ፤ የንጨት። መምታት፡ መውቃት፤ መነረት። መተረኘ፡ ተመልከት፤ የዚህ፡ መንቲያ፡ ነው።

**በትር፤(ብ፡ አብትር)፤** በቁሙ፤ ዘንግ፡ ሽመል፡ ምርኵዝ፡ ዱላ፡ ጕመድ፡ ክንተሮ፡ መንደርቆ፡ ለበቅ፡ ጨንገር። ትወፅእ፡ በትር፡ እምሥርወ፡ እሴይ። አብትረ፡ ልብኔ። ቍስለ፡ አብትር። በትርከ፡ ወቀስታምከ። ዘይምህክ፡ በትሮ፡(ኢሳ፲፩፡ ፩። ኢዮ፴፡ ፲፯። ሚራ፳፰፡ ፲፯። መዝ፡ ፳፪። ምሳ፲፫፡ ፳፬)።

—፤ ሥልጣን፡ አገዛዝ፡ ቀንበር። በትር፡ እንተ፡ ዲበ፡ ክሣዱ። በትረ፡ መንግሥትከ፡(ኢሳ፱፡ ፬። አስቴ፬፡ ፲፩። መዝ፡ ፵፬)።

**በትረ፡ ብርዕ፤** የሸንበቆ፡ ምርኵዝ፤ ጎለት፡ ውስጠ፡ ክፍት፡(ሕዝ፳፱፡ ፯። ኢሳ፴፮፡ ፯)።

**በትረ፡ ወርቅ፤** ከወርቅ፡ የተሠራ፡ በወርቅ፡ የተጌጠ፡ የጳጳስና፡ የንጉሥ፡ በትር፡(አስቴ፭፡ ፪። ፰፡ ፬)።

**በትረ፡ ኀጺን፤** የብረት፡ ዘንግ፤ ባለብረት፡ ጅንፎ፤ ጅንፎም፡ በትር፡(መዝ፡ ፪። ራእ፪፡ ፳፯)።

**በትረ፡ መሃፒል፤** ዐጭር፡ ወፍራም፡ መንደ፤ እንደ፡ ጩንቻ፡ እንደ፡ መሮ፡ መምቻ፡ ያለ፤ ዐጣቢ፡ ቀለም፡ አግቢ፡ ልብስ፡ የሚመታበት፡(ስንክ፡ ጥቅ፳፯)።

**በትረ፡ መዐት፤** መቅጫ፤ ለበቅ፡ ጨንገር፤ ረኃብ፡ ጦር፤ ዐባር፡ ቸነፈር፡(ኢሳ፲፡ ፭)።

**በትረ፡ ነገድ፤** የነገድ፡ አለቃ፡ በኵር፡ ሹም፤ ግንባር፡ ቀደም፡(፩ነገ፡ ፱፡ ፳። ስንክ፡ ግን፲)።

**በትር፤** ወገን፡ ነገድ፤ ዘር፡ ትውልድ። በበ፡ በትርክሙ፡ ወበበ፡ ሕዝብክሙ። በትረ፡ ይሁዳ፡ ወብንያም፡(፩ነገ፡ ፲፡ ፲፱። ፫ነገ፡ ፲፪፡ ፳)።

**በትረ፡ ያርክ፤(ጽር፡ ፓትሪአርኽ)፤** ሊቀ፡ ጳጳስ፤ አብ፡ ቀዳማዊ፤ ወይም፡ መዠመሪያ፡ ታላቅ፡ ደገኛ፡ አባት፡ ማለት፡ ነው፡(ስንክ፡ መጋ፲፫። ታኅ፩)።

**በታሮን፤(ጽር፡ ፓቴሮን)፤** አበው፤ ከአዳም፡ እስከ፡ ኖኅ፡ ያሉ፡ ዐሥሩ፡ አባቶች፤ ወይም፡ ሌሎች። ደብረ፡ በታሮን፤ ዘውእቱ፡ ብሂል፡ ደብረ፡ አበው፡(ስንክ፡ ሠኔ፲፰)።

**በቲት፤ ቶት፤(በተ፡ ይበትት፡ ይብትት። በልየ)፤** መበተት፤ ብትቱ፡ መኾን፡ ማለቅ፡ ማርጀት፤ የልብስ። በልበለን፡ ተመልከት።

**በትበተ፤(ይበተብት)፤** በቁሙ፤ በተበተ፤ ቦጠቦጠ፡ ፈለፈለ፤ ውስጥ፡ ውስጡን፡ በላ፡ አቃጠለ፤ የውሻና፡ የዥብ፡ የእሳት፡ አበላል። መቦጥቦጥና፡ መፈልፈል፡ የእሸትና፡ የዳቦ፡ በሊታ።(ተረት)፤ በገዛ፡ ዳቦዬ፡ ልብ፡ ልቡን፡ ዐጣኹት። ኹሉም፡ ዐማርኛ፡ ነው፤ ያማርኛ፡ ቃል፤ ከግእዝ፡ ሲደቀል፡ ተቀጥላም፡ ኹኖ፡ ሲነገር፤ አበቃቀሉና፡ አወጣጡ፡ እንዲህ፡ እንደ፡ ኾነ፡ አስተውል። ሥረ፡ ነገሩ፡ ከሣበት፡ ቅንጣት፡ ፊደል፡ አይበልጥም፡ አያንስም፤ ቋንቋነቱ፡ ሴማዊ፡ ነውና፤ ፩ኛ፡ ዕር፡ ፲ቀ፡ ተመልከት።



**ገ፤** ሦስተኛ፡ ፊደል፤ በግእዝ፡ አልፍ፡ ቤት፡ በአበገደ፤ ስሙ፡ ገምል፡ ቍጥሩ፡ ፫፤ አኃዝ፡ ሲኾን፡ ገ፡ ሠለስት፡ ቱ፡ ይባላል። ዕብራውያን፡ ግን፡ ሦስትን፡ መደብ፡ አድርገው፡ በራሱ፡ ላይ፡ ነቍጣ፡ እየጨመሩ፡ ሦስት፡ እልፍ፡ ይሉታል። ምስጢሩ፡ ሠሉስንና፡ የሠሉስን፡ ፍጥረት፡ መደብ፡ አድርጎ፡ ፫ኛውን፡ አካል፡ መንፈስ፡ ቅዱስን፡ የመንፈስ፡ ቅዱስን፡ ሀብትነት፡ ፍሬ፡ ጸጋውን፡ ያሳያል፤ ገመልን፡ እይ፡(ዘፍ፩፡ ፲፩፡ ፲፪)።

**ጋ፤** እን፡ ሲጨመርበት፡(እንጋ፡ እንጃ)፡ ደቂቅ፡ አገባብ፡ ይኾናል።

**ጓ፤(ንኡስ፡ አገባብ)፤** እኮን፡ ቢያ፤ ማ፡ እንኳ፡ ስንኳ። አንተሂጓ፡ ተሠገርከ፡ ከማነ። አንተሰጓ፡ ሀሎከ፡ ምስሌየ። ክለባትኒጓ፡(ኢሳ፲፬፡ ፲። ሉቃ፲፰፡ ፴፩። ፊልክ፡ ፫። ማቴ፲፰፡ ፳፯)።

**ጌ፤(ጽር፡ ጊ)፤** ምድር፡ ሀገር፤ ርስት። ባለጌ፡ ሐፄጌ፡ እተጌ፡ እንዲሉ። ሐፀየን፡ እይ።

**ግኢዝ፤ዘት፤(ግእዘ፤ አው፡ ገእዘ፡ ይግእዝ፡ ይግአዝ። ሱር፡ ግዓጽ፤ ጋየጸ)፤** ማዘን፡ መቈጣት፤ መበሳጨት። መንቀፍ፡ መጥላት፡ መጣላት፤ መውቀሥ፡ መክሰስ። ገአዝኩ፡ ሕይወትየ። ለምንት፡ እንከ፡ ትግእዝ፡ ፈቃደ፡ እግዚ። ወዳእነ፡ ግእዝናሆሙ። ወግእዘ፡ ጽንዐ፡ ልቦሙ። ምንተ፡ ረከቡ፡ በላዕሌየ፡ በዘይግእዙኒ። ሶበ፡ ይግእዘከ፡ ዐርክከ። ግእዘ፡ ሕዝብ፡ ለሙሴ፡(ኩፋ፡ ፳፯። ሚራ፵፩፡

፱ ። ሮሜ ፫ ፡ ፱ ። ማርጀ፮ ፡ ፲፱ ። ኤር ፪ ፡ ፩ ። ምሳሽ፩ ፡ ፰ ። ዘፀ፲፮ ፡ ፱ ፡ ፮) ።

—፤ ማጋዝ ፡ ከግዞት ፡ ቤት ፡ ማግባት ፤ ግእዝ ፡ መማር ፡ እየቈጠሩ ፡ ማንበብ ።

ገአዚ ፤ (ዚት ፡ ዝያን ፡ ያት ፤ አዝት) ፤ የሚነቅፍ ፡ ነቃፊ ፤ ወቃሽ ፡ ከሳሽ ፤ ፈራጅ ፡ (ያዕ፬ ፡ ፲፩) ።

መግእዝ ፤ (ዝት ፡ ዛን ፡ ዛት) ፤ ዝኒ ፡ ከማሁ ፤ ንዝናዚ ፡ ዘብዛባ ፤ ጓረኛ ፡ ነገረኛ ። ጕጉእ ፡ ወመግእዝ ። ዐርክ ፡ መግእዝ ። ብእሲት ፡ መግእዝት ፡ (ምሳሽ፩ ፡ ፳፱ ። ፳፪ ፡ ፳፱ ። ፱ ፡ ፲፫ ። ዲድ ፡ ፫) ።

አግአዘ ፤ አስጠላ ፡ አስነቀፈ ፤ አስጋዘ ፡ አስጕ ተተ ፤ ከግዞት ፡ አስገባ ፤ ግእዝ ፡ አስተማረ ።

ተግእዘ ፤ ተጠላ ፡ ተነቀፈ ፤ ተጋዘ ።

ግኡዝ ፤ (ዛን ፡ ዛት ፡ እዝት) ፤ የተጋዘ ፡ የ ተጠላ ፤ የተነቀፈ ፡ ንቁፍ ።

ግእዘት ፤ ማጋዝ ፡ መጋዝ ። መንቀፍ ፡ መነቀፍ ፤ አንቃቀፍ ፤ ንቀፋ ፡ ነቀፌታ ፤ ወቀሣ ፡ ክሰሳ ። በእንተ ፡ ግእዘት ፡ ዘግእዝዎ ። እንበለ ፡ ተካሕዶ ፡ ወግእዘት ፡ (ዘፀ፲፮ ፡ ፮ ። ደራሲ) ።

ተጋአዘ ፤ ተነቃቀፈ ፡ ተጣላ ፤ ተከራከረ ። አልቦ ፡ ዘትትጋአዙ ፡ በፍኖት ። ደናግለ ፡ ቀተለ ፡ ዮልያኖስ ፡ በተጋእዞ ። እለ ፡ ይትጋአዙ ። ተጋአዝኩ ፡ ምስሌሃ ። ኢይክል ፡ ተጋእዞ ፡ ምስለ ፡ ዘይጸንዕ ፡ (ዘፍ፵፭ ፡ ፳፬ ። ስንክ ፡ ኅዳ፲ ። ምሳ፲ ፡ ፲፪ ። ጦቢ፪ ፡ ፲፬ ። መክ፯ ፡ ፲) ።

ተጋአዚ ፤ ተጣይ ፡ ተፃራሪ ፤ ተሟጋች ፡ ተከራ ካሪ ፤ ባለጋራ ። ዘይፈትሕ ፡ ማእከለ ፡ ተጋአዝያን ። ኮኑ ፡ ተጋአዝያኒ ፡ ምስለ ፡ ሐዋርያት ፡ (ፍ ፡ ነ ፡ ፵፫ ፡ ፪ ። አቡሻ ፡ ፲፪) ።

አስተጋአዘ ፤ አጣላ ፤ አሟገተ ፡ አከራከረ ።

መስተጋእዝ ፤ የሚያጣላ ፡ የሚያሟግት ፤ የሚ ሟገት ፡ ተሟጋች ፡ ተከራካሪ ። ለእመ ፡ ይቤለከ ፡ አሐዱ ፡ መስተጋእዝ ። መስተጋእዛን ፡ በበይናቲሆሙ ፡ (ፈ ፡ መ ፡ ፪ ፡ ፲ ። አፈ ፡ ድጓ ፡ ፳፱) ።

ጋእዝ ፤ (ዛት) ፤ ጠብ ፡ ክርክር ፡ ሙግት ፤ ንዝ ንዝ ፡ ስድብ ፡ ውዝግብ ፡ ጭቅጭቅ ። ሰደም ፡ ደቀድሞ ፡ ላኳ ፡ ወጋእዝ ። ጋእዘሙ ፡ ስራሕ ፡ ለዘይሰምዖ ። ነ ገረ ፡ ጋእዝ ። ሰይጣን ፡ አብአ ፡ ፍልጠተ ፡ ወጋእዘ ፡ ውስተ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ። መቲረ ፡ ጋእዛት ፡ (ሚራ ፡ ፳፪ ፡ ፳፱ ። ፳፮ ፡ ፲፩ ። ፩ጢሞ ፡ ፮ ፡ ፱ ። ዲድ ፡ ፴፪ ። ፍ ፡ ነ ፡ ፬) ። በቁሙ ፡ ጋዝ ፡ ላንባ ፡ ሽታውና ፡ ጢሱ ፡ እንደ ፡ ከፋ ፡ ነገር ፡ የሚያስቀይም ፤ ነፍጥን ፡ እይ ።

ግእዝ ፤ የቋንቋ ፡ ስም ፤ ሴማዊ ፡ አዳማዊ ፡ ቋ ንቋ ፡ የዕብራይስጥ ፡ ወንድም ፤ ከዐረብ ፡ ከሱርስት ፡ የሚ ገጥም ። ዘይቤው ፡ አልፍ ፡ እንደ ፡ ማለት ፡ አንድ ፡ መጀ መሪያ ፤ ምክጢሩ ፡ ጥንታዊ ፡ አዳማዊ ፡ ልሳን ፡ ማለት ፡ ነው ፡ (ዘፍ፲፩ ፡ ፩) ። ፪ኛም ፡ እንደ ፡ ሌላው ፡ ቋንቋ ፡ ብዙ ፡ ድካም ፡ ስለሌለበት ፡ ቅን ፡ ገር ፡ ብለው ፡ ይፈቱ ታል ። ተተርጐመ ፡ እምልሳነ ፡ ቅብጢ ፡ ለዐረብ ፡ ወ እምዐረቢ ፡ ለግእዝ ፡ (ሃይ ፡ አበ ፡ ፩) ።

ግእዝ ፤ የፊደል ፡ ስም ፤ አንድ ፡ ወጣት ፡ አንድ ፡ ቅንጣት ፡ አንድ ፡ በቀል ፤ ዕዝል ፡ ቅጥል ፡ ነቍጣ ፡ ምክ ትል ፤ ዋየል ፡ አጣማጅ ፡ ኹለተኛ ፡ ፈርጅ ፡ የሌለው ፡ ቀንጃ ፡ ነጠላ ፡ ፊደል ፡ (ኮንሶን) ፡ ከአ ፡ እስከ ፡ ፐ ፡ ያለ ፤ አ ፡ በ ፡ ገ ፡ ደ ፡ ሀ ፡ ወ ፡ ዘ ። ከስላሜ ፡ በፊት ፡ ከካዕብ ፡ እ ስከ ፡ ሳብዕ ፡ ድረስ ፡ ሳይኖረው ፡ ርሱው ፡ ራሱ ፡ ግእዙ ፡ ብቻ ፡ ነበረና ፤ ቋንቋውን ፡ ግእዝ ፡ ያሰኘው ፡ ይህ ፡ ነው ፡ ይባላል ። ከዚያ ፡ ወዲህ ፡ ግን ፡ ከካዕብ ፡ እስከ ፡ ሳብዕ ፡ ላሉት ፡ በሆር ፡ ግንባር ፡ ቀደም ፡ ባለኇ ፡ ወንድም ፡ ስለ ፡ ኾነ ፡ አንደኛ ፡ ወይም ፡ መዠመሪያ ፡ ይባላል ። አ ፡ ግእዝ ፤ ቡ ፡ ካዕብ ፤ ጊ ፡ ሣልስ ፤ ዳ ፡ ራብዕ ፤ ሄ ፡ ኃምስ ፤ ው ፡ ሳድስ ፤ ዞ ፡ ሳብዕ ፡ እንዲሉ ። ግእዝ ፡ አንድ ፡ አንደኛ ፡ መባሉ ፡ በእ ፡ ምክንያት ፡ ነው ።

ግእዝ ፤ የንባብ ፡ ስም ፤ መዠመሪያ ፡ ንባብ ፤ ሕፃናት ፡ የፊደልን ፡ ቍጥር ፡ እጅ ፡ እግሩን ፡ ከለዩ ፡ በ ኋላ ፡ ከንቍጥ ፡ እስከ ፡ ነቍጥ ፡ እየጕተቱ ፡ የሚያግ ዙት ፡ ማጋዝ ። ለንባብ ፡ ትምርት ፡ በየስልቱ ፡ ፱ ፡ ስም ፡ አለው ፤ ግእዝ ፡ ወርድ ፡ ዐቢይ ፡ ድጋም ።

ግእዝ ፤ የዜማ ፡ ስም ፤ አንደኛ ፡ ስልት ፡ መዠ መሪያ ፡ ዜማ ፤ ፪ኛው ፡ ዕዝል ፡ ፫ኛው ፡ አራራይ ፡ ይባላል ። ሠለስቱ ፡ ዜማ ፡ ዘውእቱ ፡ ግእዝ ፡ ወዕዝል ፡ ወአራ ራይ ። ወእምዝ ፡ ትብል ፡ ጸሎተ ፡ ዘእምዳዊት ፡ በ ዜማ ፡ ግእዝ ። ህየንተ ፡ ዕዝል ፡ ዘነግህ ፡ ግእዝ ፡ (ስንክ ፡ ግን፲፩ ። ግንዘ ። ድጓ) ።

ግእዘ፤—ተጓዘ ፤ ነጻ ፡ ወጣ፤—ግዒዝ ፡ ግዕዘ ።

ገአረ፤—ጋረ ፡ ጣረ ፡ ጮኸ፤—ግዒር ፡ ገዐረ ።

ገአተ፤—ገነፎ፤—ግዒት ፡ ገዐተ ።

ገበ ፤—ጕን ፤—ገቢእ ፡ ገብአ ።

ግብ ፤—ጕድጓድ ፡ ጕሬ ፤—ገብበ ፡ ገበበ ።

ገቢእ ፤ አት ፤ (ገብአ ፡ ይገብእ ፡ ይግ በእ ። በአ ፤ መጽአ ። ገብአ ፡ ትግ ፡ ከነ ፡ ይከ ውን) ፤ መግባት ፡ መጥለቅ ፡ መዝለቅ ፤ ወደ ፡ ውስጥ ። መመለስ ፡ ወደ ፡ ኋላ ፡ መዞር ፡ መታጠፍ ፡ ተመልሶ ፡ መ ምጣት ። ገቢኦትክ ፡ ውስተ ፡ ሥጋ ። ይትመየጥ ፡ ለገ ቢእ ። ገብአ ፡ ቤቶ ። እገብእ ፡ ውስተ ፡ ምድር ። ገ ብኡ ፡ እምፍኖት ፡ እኩይ ፡ (ዕር ፡ ኢሳ፰ ፡ ፳፮ ። መክ ፩ ፡ ፲፱ ። ጦቢ፰ ፡ ፲፩ ። ኢዮ፩ ፡ ፳፩ ። ኤር፵፪ ፡ ፲፩) ።

—፤ መኾን ፤ መያዝ ፡ መሰጠት ። ገብኡ ፡ ታሕተ ፡ እደ ፡ ትሑት ። ገብኡ ፡ ከመ ፡ ዘኢተወልዱ ። ደኃርት ፡ ይ ገብኡ ፡ ቀዳምተ ፤ ኮኑ ፡ ይከውኑ ። ገባእኒ ፡ ውስተ ፡

እደ፡ጸላእትነ ። ይግባእ ፡ ውስተ ፡ እደ ፡ ሰብእ ፡ (ሚ ራ ፲፭ ፡ ፮ ። ሣ፱ ፡ ፱ ። ማር፲ ፡ ፴፭ ። ሱቱ ፡ ዕገዝ፲ ፡ ፴፮ ። ሉቃ፳፬ ፡ ፯) ።

**ገባኢ** ፤ (ኢት ፡ እያን ፡ ያት ፤ እት) ፤ ቅጽ ልና ፡ ጥሬ ፤ የሚገባ ፡ ገቢ ፤ ተመላሽ ፤ ተመላላሽ ። ገበሬ ፡ ዐራሽ ፤ የሰት ፡ ምንደኛ ፡ ሙያተኛ ፤ ዐራሚ ፡ ቈፋሪ ፤ አሽ ከር ፡ ወታደር ፡ አገልጋይ ፡ ሎሌ ። ገባኢ ፡ ዘይጸምሙ ፡ በተገብሮታ ፡ ለምድር ። ገባኢ ፡ ዘይሴፎ ፡ ዐስቦ ። ይትዓሰብ ፡ ገባእተ ። ገባኢሁ ፡ ለኤፍሬም ፡ (ጥበ፲፯ ፡ ፲፯ ። ኢዮ፯ ፡ ፪ ። ማቴ፳ ፡ ፩ ። ዮዲ፯ ፡ ፱) ።

**ግቡእ** ፤ (ኣን ፡ ኣት ፡ ብእት) ፤ የገባ ፤ የተ መለሰ ፤ ምልስ ፡ ቅልስ ።

**ግብአት** ፤ መግባት ፡ መመለስ ፤ አገባብ ፡ አመ ላለስ ፤ ግቢ ፡ ምለሳ ፤ መያዝ ፡ መሰጠት ። ግብአተ ፡ መን ጦላዕት ። ሑረት ፡ ወግብአት ። ግብአትከ ፡ ውስተ ፡ ርስትከ ። ዜና ፡ ግብአቱ ፡ ለአግሪጳስ ፡ ኀበ ፡ ሮሜ ። እፈድየከ ፡ በግብአትየ ። በእንተ ፡ ግብአቱ ፡ ለክርስ ቶስ ፡ (ቅዳ ። ዘካ፯ ፡ ፲፬ ። ቀሌ ። ዮሴፍ ። ሉቃ፲ ፡ ፴፭ ። ማቴ፳፯ ፡ ፵፯) ።

**ምግባእ** ፤ (እት) ፤ መግቢያ ፤ መመለሻ ፤ ተመ ልሶ ፡ መምጫ ፡ ቦታ ። ኅቤየ ፡ ምግባኢሁ ። ውስተ ፡ ምድር ፡ ምግባኢሆሙ ። የሐውር ፡ ውስተ ፡ ፍኖት ፡ እንተ ፡ አልባቲ ፡ ምግባእ ፡ ለዓለም ፡ (ማሕ፯ ፡ ፲፭ ። ሚራ፲፯ ፡ ፴ ። ግንዘ ። ዘፍ፫ ፡ ፲፯ ። ፱ ፡ ፯) ።

**አግብአ** ፤ አገባ ፡ ከተተ ፡ አስገባ ፤ መለሰ ፡ አስ መለሰ ፤ አግባ ፡ መልስ ፡ አለ ። አግብኣ ፡ ለመጥባሕትከ ፡ ውስተ ፡ ቤታ ። ያገብኦሙ ፡ ድኅሬሆሙ ፡ ለጠቢ ባን ። ወያገብእ ፡ ድኅረ ፡ ዘባኑ ። እመ ፡ አእተተ ፡ መኑ ፡ ያገብእ ። ወአግብአት ፡ ባሕርኒ ፡ ዙሎ ፡ ሙታነ ፡ (ሜቴ፳፯ ፡ ፶፪ ። ኢሳ፵፬ ፡ ፳፭ ። ሚራ፳፮ ፡ ፲፭ ። ኢዮ፱ ፡ ፲፪ ። ራእ፳ ፡ ፲፫) ።

—፤ አሳልፎ ፡ ሰጠ ፤ ከተቀባይ ፡ እጅ ፡ አገባ ፤ አስያዘ ፡ አስጨበጠ ፤ አመጣ ፡ አቀረበ ፡ አስረከበ ፤ ፈረደ ፡ ፍርድ ፡ አቀና ። ወኢያገብኦ ፡ ውስተ ፡ እደ ፡ ጸላኢሁ ። ይሁዳ ፡ ዘአግብኦ ። እለ ፡ አግብኡ ፡ ነፍሶሙ ፡ ለከ ። አግብኡ ፡ ቀርኖሙ ፡ ለባዕድ ፡ ወክብሮሙኒ ፡ ለካልእ ። እለ ፡ ያገብኡ ፡ ጸባሕተ ። አግብአ ፡ ፍትሐ ፡ ለዘሩባቤል ፡ (መዝ ፡ ፴፱ ። ማቴ፲ ፡ ፬ ። ቅዳ ፡ ዮሐ ። ሚራ፵፱ ፡ ፭ ። ፪ነገ ፡ ፰ ፡ ፪ ። አርጋ) ።

**ተጋብአ** ፤ ተመላለሰ ፤ ወጣ ፡ ገባ ፡ ምልስ ፡ ቅ ልስ ፡ አለ ። መጽሐፍ ፡ ግን ፡ በተጋብአ ፡ ፈንታ ፡ ተገባብአ ፡ ይላል ፤ አያሰኝም ። ወተገባብአ ፡ ኀበ ፡ አረጋዊ ፡ (ፈ ልክ ፡ ፪፳፰) ።

**አስተጋብአ** ፤ በቁሙ ፤ አስተጋባ ፤ የገደል ፡ የተራራ ፡ (ዐማርኛ) ።

**ገቦ** ፤ (ብ ፡ ገበዋት ። ሱር ፡ ጋበአ ። ዐረ ፡ ጀንብ ፤ ጃኒብ) ፤ ጐን ፡ ጐድን ፡ ወገብ ፤ ወገን ፡ ማእ ዝን ፤ ቅርብ ፡ አጠገብ ። ግንቦት ፡ ማለት ፡ ከዚህ ፡ ወጥ ቷል ፤ ገቦ ፡ ክረምት ፡ ማለት ፡ ነው ፤ ከጻደ ፡ ጋራ ፡ ይስ ማማል ። ትሰክብ ፡ በገቦከ ፡ ዘፀጋም ። ለገብር ፡ እ ኩይ ፡ ሥትሮ ፡ ገበዋቲሁ ። ይትዐጸፍ ፡ ርትዐ ፡ ውስተ ፡ ገቦሁ ። ወልድከ ፡ ዘወፅአ ፡ እምገበዋቲከ ። በገቦ ፡ መስዕ ። ወእምገበዋቲሁ ፡ ለውእቱ ፡ መንበር ። አዝ ማድ ፡ እለ ፡ ገበዋት ። ገዳም ፡ ዘገቦ ፡ ዮታይም ። ኖመት ፡ በገቦሁ ፡ (ሕዝ፬ ፡ ፬ ። ሚራ፵፪ ፡ ፭ ። ኢሳ፲፩ ፡ ፭ ። ፫ነገ ፡ ፰ ፡ ፲፯ ። መዝ ፡ ፵፯ ። ራእ፬ ፡ ፯ ። ፍ ፡ ነ ፡ ፳፬ ፡ ፱ ። ዮዲ፬ ፡ ፯ ። ስንክ ፡ ሠኔ፴) ።

**ዘገቦ** ፤ የገቦ ፡ በጐን ፡ የሚወጣ ፡ የሚያፈጠፍጥ ፡ ቅጥይ ፤ የማሽላ ። ወይም ፡ ሳይዘሩት ፡ የሚበቅል ፡ ወፈ ራሽ ። የገቦ ፡ ማለት ፡ ኀባቡም ፡ ምስጢሩም ፡ ከሔዋን ፡ ተፈጥሮ ፡ መጥቷል ፡ (ዘፍ ፡ ፪ ፡ ፳፩) ።

**አግቦ** ፤ (ዐማርኛ) ፤ ሸውራራ ፡ ስድብ ፤ በ ራሱ ፡ እኔ ፡ እንዲህ ፡ አይደለኹ ፡ ብሎ ፡ ወይም ፡ በሌላ ፡ አስመስሎ ፡ ጠላትን ፡ ለመንካት ፡ የሚነገር ። (ተረት) ፤ ወይ ኖን ፡ ግረፈው ፡ ፈንዘን ፡ እንዲሰማው ።

**ጋብአ** ፤ አት ፤ (ጋብአ ፡ ይጋብእ ፡ ይጋ ብእ ። ዐረ ፡ ጀባእ ፤ ተቀበለ ። ሱር ፡ ግባእ) ፤ መሰብሰብ ፡ ማከብ ፤ ማጋበስ ፡ ማግበስበስ ፡ ማከማቸት ፤ መልቀም ፡ ማጠራቀም ፡ መከተት ። ማጠፍ ፡ መኰርተም ፤ የሕዋስ ። መጽሐፍ ፡ ግን ፡ በጋብአ ፡ ፈንታ ፡ አስተጋብአ ፡ ይላል ፤ በሳተፈና ፡ በባረየ ፡ ፈንታ ፡ አስተሳተፈ ፡ አስተባ ረየ ፡ እንዲል ። መራዕየከ ፡ አስተጋብአ ። አስተጋብአ ፡ ንዋየ ፡ ብዙኀ ። ያስተጋብእ ፡ ሥርናየ ፡ ውስተ ፡ መዝ ገቡ ። ያስተጋብኡ ፡ ክነፊሆሙ ። ታስተጋብእ ፡ እ ዴከ ፡ (ኩፋ ፡ ፴፭ ። ስንክ ፡ ሠኔ፲፫ ። ማቴ፫ ፡ ፲፪ ። ሕዝ፩ ፡ ፳፬ ። ምሳ፮ ፡ ፲) ።

**አጋብአ** ፤ አሰበሰበ ፤ ሰብስቡ ፡ አለ ፡ (አስደራጊ) ።

**አስተጋብአ** ፤ አሰበሰበ ፤ አሰባሰበ ፡ (አስደራ ጊና ፡ አደራራጊ) ። ልማዱ ፡ ግን ፤ ሰበሰበ ፡ ነው ።

**አስተጋባኢ** ፤ መስተጋብኢ ፤ የሚያሰበ ስብ ፡ አሰብሳቢ ፤ አሰባሳቢ ። ልማዱ ፡ ግን ፡ ሰብሳቢ ፡ ነው ። ይቤ ፡ አስተጋባኤ ፡ መጽሐፍ ። መስተጋብኤ ፡ ነፍ ሳት ፡ (ፈላስ ። ቢኖደ) ።

**መስተጋብእ** ፤ ኢ ፤ ዝኒ ፡ ከማሁ ፤ የሚሰበ ስብ ፡ ሰብሳቢ ፤ መሰብሰቢያ ፡ ቦታ ። መስተጋብአ ፡ ጸጋ ፡ ተግሣጻት ፡ ውእቱ ። አ ፡ ከርሥ ፡ መስተጋብኢተ ፡ ዙሉ ፡ ርስሐተ ፡ ኀጢአት ፡ (ፈላስ ። ግንዘ) ።

**ተጋብአ** ፤ ተሰበሰበ ፤ ተሰባሰበ ፤ ተከማቸ ፡ ተከ መቻቸ ፤ ተወሰነ ፡ ተጨበጠ ፡ ተኰረኰመ ። ተጋብኡ ፡ ዙሎሙ ፡ አሕዛብ ፡ ኅቡረ ። ህየ ፡ ይትጋብኡ ፡ አንስ ርት ። ፀነስኪዮ ፡ እንዘ ፡ ኢይትጋባእ ፡ (ኢሳ፵፫ ፡ ፱ ። ማቴ፳፬ ፡ ፳፰ ። ቅዳ) ። በገብአ ፡ ፈንታ ፡ ተጋብአ ፡ ይላል ፤ አያሰኝም ። ማይ ፡ እምከመ ፡ ተክዕወ ፡ ኢይትጋባእ ። ይትጋባእ ፡ ማይ ፡ ዲበ ፡ ግብጽ ። ትትጋባእኑ ፡ መሥ ገርት ፡ ዘእንበለ ፡ ተአኀዝ ፡ (፪ነገ ፡ ፲፬ ፡ ፲፬ ። ዘፀ፲፬ ፡ ፳፯ ። ዓሞ፫ ፡ ፲፭) ።

**ጉቡእ፤ እስትጉቡእ፤ (አን፡ አት፡ ብእት)፤** የተያዘ፡ የተሰበሰበ፤ ስብስብ፡ ክምቹ። ቅምም፡ ጥርቅም። ጉቡእ፡ በኢድ። ሎሉ፡ እስራኤል፡ ምስሌሁ፡ ጉቡኣን። እለ፡ ጉቡኣን፡ ውስተ፡ ኢየሩሳሌም፡ (ምሳ፲፩፡ ፱። ፩ዜና፡ ፯፡ ፰። ፲፪፡ ፩)። እስትጉቡእ፡ ዝንቱ፡ መጽሐፍ፡ እመጻሕፍት፡ አምላካውያት፡ ወቀኖናት። ወእምዝ፡ አትለወ፡ በዝንቱ፡ ከመ፡ ተግሣጽ፡ እስትጉቡእ። ወዝንቱ፡ ውእቱ፡ ዘእስትጉቡእ፡ ለሎሉ፡ (ፍ፡ ነ፡ መቅ። አፈ፡ ድ፵፫። ተ፴፱)። በእስትጉቡእ፡ ፈንታ፡ ምስትጉቡእ፡ ይላል፤ ስሕተት፡ ነው። ምስትጉቡኣት፡ አእላፍ፡ እምነ፡ መላእክት፡ (አፈ፡ ድ፴፪)።

**ጉባኤ፤ (እያት)፤** መሰብሰብ፤ (ጥስ) መሰብሰብ፤ አሰባሰብ፤ ስብሰባ፡ እከባ፤ አንድነት። መሰብሰቢያ፡ (ጥስ) መስብስቢያ፤ መሰባሰቢያ፡ መገናኛ፡ ጊዜ፡ ቦታ፤ ገበያ፡ ሸንጎ፡ አደባባይ፡ ገዳም፡ ቤተ፡ ክሲያን፡ የትምርትና፡ የሰርግ፡ የልቅሶ፡ ቤት፤ የመሰለው፡ ኹሉ። ወይም፡ በቁሙ፤ የተሰበሰበው፡ ማኅበር፡ እንግልጋ፤ ገበያተኛ፡ የሰው፡ መንጋ። በጉባኤክ። ጉባኤ፡ ቀኖናት። በመካነ፡ ጉባእያት፡ ዘከመ፡ መራሕብት፡ ወምሥያጣት፤ ቦታ፡ (ዘፀ፳፫፡ ፲፯። ፈ፡ መ፡ ፩፡ ፱። ፍ፡ ነ፡ ፵)። ተጋብኡ፡ ላዕሌሆሙ፡ እምሮም፡ ጉባኤ፡ ብዙኅ። ጉባኤ፡ ፀርየ፡ ዝኑ። ጉባኤ፡ ሐራ። ጉባኤ፡ ኤጲስቆጶሳት። ጸሐፈ፡ መጽሐፈ፡ ጉባኤ። ቤተ፡ ክርስቲያን፡ እንተ፡ ላዕለ፡ ሎሉ፡ ጉባኤ፡ ዘሐዋርያት፤ ብዙ፡ ሰው፡ (ዮሴፍ። ስንክ፡ ነሐ፲፱። አርጋ። ቀኖ፡ ኒቅ። ቅዳ)።

**ጉባኤ፡ ቃና፤** የቅኔ፡ ስም፤ መዠመሪያ፡ ቅኔ፡ ባለ፱፡ ቤት። የስሙ፡ ንባብና፡ ምስጢር፡ ከወንጌል፡ መጥቷል፡ (ዮሐ፪፡ ፲፩)።

**ምጕባእ፤ (ኣት)፤** መሰብሰቢያ፡ መከማቻ፤ መጠራቀሚያ፡ ቦታ። ወበይእቲ፡ ዕለት፡ ፈጠረ፡ ላቲ፡ ልጕታተ፡ ዘአብሕርት፡ በበ፡ ምጕባኣቲሆሙ፡ ወሎሎ፡ አፍላገ፡ ወምጕባኣቲሆሙ፡ ለማያት፡ ውስተ፡ አድባር፡ ወውስተ፡ ሎሉ፡ ምድር፡ ወሎሎ፡ ምዕቃላተ፡ (ኩፉ፡ ፪)።

**ምስትጕባእ፤** ዝኒ፡ ከማሁ። ቤተ፡ ምስትጕባአ፡ ዚኣሁ። ምስፋሕ፡ ወምስትጕባእ፡ (ሔኖ፶፫፡ ፯)። አንዳንድ፡ መጽሐፍ፡ ግን፡ ጥሬውን፡ በቅጽል፡ ለውጦ፤ ምስትጕቡእ፡ ይላል፤ አያስኼም፡ (ቅዳ፡ ሕር)።

**ገብበ፤ ቦት፤ (ገበበ፡ ይጌብብ፡ ይገብብ። ዕብ፡ ጋባብ)፤** መሰብሰብ፤ ማግባት፡ መክተት። መቈፈር፤ መቅበር። ማጓበብ፡ መንጓበብ፤ ጕብ፡ ጕባባ፡ መኾን፤ እንደ፡ ቀስት። ጕብ፡ መስጠት፡ መቀበል።

**ግብ፤ (ብ፡ ግበብ፤ ባት፤ አግባብ። ዕብ፡ ጎብ። ሱር፡ ጉባ። ዐረ፡ ጉብ)፤** መክተቻ፡ መክተቻ፤ ጕድጓድ፡ ዐዘቅት፤ ዋሻ፡ ጕሬ፡ መቃብር፡ የምድር፡ ቤት፤ የመሰለው፡ ኹሉ። ዘከረየ፡ ግበ፡ ለቢጹ፡ ይወድቅ፡ ውስቴቱ። ግበበ፡ ምድር። ይድፍኑ፡ ግበባተ። እለ፡ አብያቲሆሙ፡ ውስተ፡ ግበበ፡ ኰኵሕ። ግበበ፡ አራዊት። እለ፡ ይወርዱ፡ ውስተ፡ ግብ፡ (ሚራ፳፯፡ ፳፯። ዕብ፲፩፡ ፴፰። ዮሴፍ። ኢዮ፴፡ ፮። ኤር፱፡ ፲፩። ሕዝ፴፱፡ ፲፰)። ጕብ፤ ጕብ፡ ማለት፡ ዐማርኛው፡ ከዚህ፡ ወጥቷል።

**ግበ፡ ዐይን፤** ያይን፡ ጕድጓድ፡ ዋሻው፡ ሠርጓዳው፡ ምዕቃሉ፤ ብርንደው፡ እንደ፡ ፈርጥ፡ የተሰካበት፤ ወይም፡ እንደ፡ ውሃ፡ የመላበት፡ (ምሳ፳፱፡ ፶፪። ዘካ፲፬፡ ፲፪)።

**ገብገብ፤ ገብገቦ፤** አዳራሽ፡ ሰቀላ፡ በረንዳ። ሸንጎ፡ አደባባይ፤ ዐውደ፡ ምቅታል። ወወፅአ፡ ውስተ፡ ገብገብ። አዘዘ፡ ይሰድዋ፡ ኀበ፡ ገብገቦ፡ ወይምትርዋ፡ ከማደ፡ (ዮዲ፲፡ ፳፪። ስንክ፡ ታኅ፯)።

(ጥ) **ጋብ፤ (ዕብራ)፤** ረዥም፡ ቤት፤ ሰገነት፡ የደርብ፡ ደርብ፤ ዕንቍላል፡ ግንብ። ወያንኀሉ፡ ጋቤኪ፡ (ሕዝ፲፯፡ ፴፱)።

**ገቢዝ፤ ዘት፤ (ገበዘ፡ ይገብዝ፡ ይግብዝ)፤** መለካት፡ መወሰን፤ ዙሪያውን፡ መቍረጥ፡ መክለል፤ የመሬት፡ የሕንጻ። መጕበዝ፤ መገበዝ፤ ጕበዝ፡ ግብዝ፡ መኾን። መጋበዝ፡ (ዐማርኛ)።

**ገበዝ፤** ዳር፡ ዳርቻ፤ ጠረፍ። ተቀበሎ፡ ዲበ፡ ገበዘ፡ ተከዚ፡ (ዘፀ፯፡ ፲፭)።

—፤ ብርቱ፡ ጠባቂ፡ ዘበኛ፤ በረኛ። እምነ፡ ጽዮን፡ ገበዘ፡ አሡስም። ሰደድዎ፡ እምሀገር፡ እለ፡ ገበዘ፡ አሡስም፤ ዕጣና፡ ለገበዝ። ቦአ፡ ውስተ፡ ቤተ፡ ክርስቲያን፡ ዘገበዘ፡ አሡስም። ገበዝ፡ የጽዮን፡ ቅጥል፡ ነው፡ (ሥር፡ አኵ፡ ገ፹፱። መዋሥ። ስንክ፡ ግን፲፭)።

—፤ የሹመት፡ ስም፤ የቤተ፡ ክሲያን፡ ሹም፡ አስተንታኝ፤ የሰሞነኞች፡ አለቃ። ምስጢሩ፡ ያው፡ ጠባቂነት፡ ነው። ቀይሰ፡ ገበዝ። ኢይትለአክ፡ ከመ፡ ካህናት፡ ወኢይኩን፡ ሊቀ፡ ካህናት፡ ወኢይቀድስ፡ ከመ፡ ገበዝ፡ (ሥር፡ አኵ። ቄድር፡ ገ፹፰)።

—፤ መሐንድዝ፤ ሊቀ፡ ነደቅት። ገበዝ፡ አንባ፡ እንዲሉ።

**ገበጣ፤** በቁሙ፤ የጠጠር፡ ጨዋታ፤ ልቅምሽ፡ ቅልምሽ፤ ግብጦች፡ ወይም፡ ጠጠር፡ ጣዮች፡ ያወጡት። (ተረት)፤ ገበጣ፡ ላዋቂ፡ ወሬ፡ ለጠያቂ። ኢይትላሀዩ፡ ግብረ፡ ሰንጠረዥ፡ ወገበጣ፡ (ፈ፡ መ፡ ፴፱፡ ፯)።

**ግብጦ፤** ያበባ፡ እኽል፡ መኼ፡ የሚመስል፡ ተርሙስ፤ ግብጣዊ፡ ማለት፡ ነው።

**ገብጥ፤** የሆድ፡ በሽታ፤ ብስና፡ ጓታ፡ እህታ፤ የሚቈርጥ፡ የሚጕራብጥ፡ የሚያስቀምጥ። ቅንጣዌ፡ ወገብጥ። ያበዝኖ፡ ለገብጥ፡ ሥሥዕት፡ (ሚራ፴፩፡ ፳። ፴፯፡ ፴)።

**ተግቢጥ፤** ሽታ፤ ሽንት፡ ቅዘን፤ ቀጭን፡ ዐይነ፡ ምድር። በረዘንና፡ ተብሪዝን፡ እይ።

**ገበጥባጥ፤** የሆድ፡ ትል፤ ወስፋት፡ ሹጥ፤ ሥራይ። ዘከመ፡ ዝንቱ፡ ደዌ፡ ወገበጥባጥ፡ (ኩፋ፡ ፳፫)።

**ገበይ፤(ትግሬ)፤** መንገድ፡ ጐዳና፤ ገበያ። ዘሩና፡ ሥሩ፡ ጉባኤ፡ ነው።

**ገበያዊ፤** መንገደኛ፤ ነጋዴ፡ ገበያተኛ።

**ገበለ፤(ዕብ፡ ጋቤል)፤** ለወሰ፡ አቦካ፡ አላቄጠ፤ የደቄት፡ የጭቃ።

**ገብላ፤(ላት)፤** ገንዳ፤ ከግንድ፡ ከደንጊያ፡ የሚሠራ፡ ማቡኪያ፡ ማላቈጫ፤ የከብቶች፡ ውሃ፡ ማጠጫ፤ እንደ፡ ገበታ፡ የተጠረበ፡ የተፈለፈለ። ዘየአምር፡ ወኢይገብር፡ ይመስል፡ ገብላ፡ ዘምሉእ፡ ማየ፡ ዘእምኔሁ፡ ይሰትዩ፡ ብዙኃን፡ ወያነጽሕ፡ ብዙኃነ፡ እምርስሐቲሆሙ። ገብላተ፡ እብን፡ ዘያሰትዩ፡ ባቲ፡ አፍራሰ፡ (ፊልክ፡ ፶፱። ስንክ፡ መስ፩። ዘፍ፴፡ ፴፰፡ ፵፩። ዘፀ፪፡ ፲፯)።

**ጌባል፤(ጽርእ። ዕብ፡ ዔባል)፤** የተራራ፡ ስም፤ የገሪዛን፡ ወንድም፡ ቅርብ፡ አጠገብ፤ የርግማን፡ ቃሎች፡ የሚነገሩበት፡ ከገሪዛን፡ በስተሰሜን፡ ያለ፡ ፀጋማይ፡ ተራራ። ኹለቱም፡ በኤፍሬም፡ ዕፃ፡ ውስጥ፡ ናቸው፡ (ዘዳ፲፩፡ ፳፱። ፳፯፡ ፲፫)።

**ገበነ፤(ዕብ፡ ጋቤን)፤** አረጋ፡ ዐየበ፤ ዐይብ፡ አደረገ፤ ወተቱን።

**ግብን፤ ግብነት፤(ዕብ፡ ግቢና። ሱር፡ ግቤንታ። ዐረ፡ ጁብን)፤** ጅብና፤ ርጎ፡ ዐይብ፤ ያይብ፡ ልጥልጥ፤ በሚዛን፡ የሚሼጥ። ከመ፡ ሐሊብ፡ ሐለብከኒ፡ ወአርጋዐከኒ፡ ከመ፡ ግብነት። የሐልቦሙ፡ ለእንስሳ፡ ወይገብር፡ ግብነተ። ግብነት፡ ዘላሕም፡ (ኢዮ፲፡ ፲። ስንክ፡ መስ፲፰። ሥር፡ ጻኸ)።

**ግብጽ፤(ጽር፡ ኤጊብት። ዕብ፡ ሚጽራይም። ዐረ፡ ሚጽር)፤** ግብጥ፤ ስመ፡ ነገድ፡ ስመ፡ ሀገር፡ የካም፡ ዕፃ። መካነ፡ ጻዕር፡ ልሳነ፡ ባሕር፤ የእስያና፡ ያፍሪቃ፡ ወሰን፡ ደንበር፡ ማለት፡ ነው። በግብጽ፡ ፈንታ፡ ቅብጥ፡ ይላል፤ ፍችው፡ አንድ፡ ነው። ብሔረ፡ ግብጽ። ልሳነ፡ ቅብጥ፡ (መዝ፡ ፸፱። ሃይ፡ አበ)።

**ገቢር፤ሮት፤(ገብረ፡ ይገብር፡ ይግበር። ዕብ፡ ጋበር፤ ኀየለ፡ ጸንዐ)፤** መሥራት፡ ማድረግ፡ መፍጠር፤ ያልነበረ፡ ነገር፡ ማስገኘት፤ የነበረውን፡ ማዘጋጀት፤ ፍጥረትን፡ ከፍጥረት፡ ጨምሮ፡ ሌላ፡ ሀላዌ፡ ማቆም፤ እንደ፡ ሥጋና፡ እንደ፡ ሸክላ፡ እንደ፡ ቤት፡ እንደ፡ ምንጣፍ። በሚሠሩት፡ ሥራ፡ ማየል፡ መበርታት፡ መሠልጠን፤ ከሃሊ፡ መኾን። ሰዱሰ፡ ዕለተ፡ ትገብር፡ ግብረ። ገቤረ፡ ግበር፡ በከመ፡ አዘዝኩ። ዘገብረ፡ ሰማየ፡ ወምድረ። ወገብሮ፡ እግዚ፡ ለሰብእ፡ መሬተ፡ እምድር። ገብረ፡ ወይነ፡ እምፍሬ፡ (ዘሌ፳፫፡ ፫። ዮሐ፪፡ ፲፫። መዝ፡ ፺፭፫። ዘፍ፪፡ ፯። ኩፋ፡ ፯)። ገብረ፡ ዐሥራ፡ ኹሉ፡ እየገባ፡ እንደ፡ ሥራው፡ ስልት፡ ይፈታል። ይግበሩ፡ ውስተ፡ ማኅቶት፡ ቅብዐ፤ ይደዩ። ግበር፡ እዴከ፡ ዲበ፡ ዘቲ፡ ዓሕል፤ ሚያም፡ አንብር፡ ያሰኛል፡ (ስንክ፡ ጥቅ፳። ቅዳ)።

**ገባሪ፤(ሪት፡ ርያን፡ ያት፤ በርት)፤** የሚሠራ፡ ሠሪ፤ አድራጊ፡ ፈጣሪ፡ ፈጻሚ። አሐዱ፡ ገባሪ፡ በማለት፡ ፈንታ፡ አሐዱ፡ ግብር፡ ይላል፡ የጣፊ፡ ስሕተት፡ ነው፡ (ሃይ፡ አበ፡ ጎር። ብን)። ግብር፡ ምስለ፡ ገባሪሁ። ጥበብ፡ ገባሪተ፡ ዥሉ። ገባርያነ፡ ብርት። ገበርተ፡ ዐመፃ፡ (ጥበ፲፬፡ ፲። ፳፡ ፭። ፲፭፡ ፱። መዝ፡ ፭)። ገብረ፡ በመላላቱ፡ የቀተለ፡ ሰርዌ፡ ሺኾን፡ በመጥበቁ፡ ቀደሰን፡ ይመስላል፤ መምስሉም፡ ይህ፡ ነው።

(ጥ) **ገብሮ፤ሮት፤(ገበረ፡ ይጌብር፡ ይገብር)፤** (ጥገ) መገበር፡ ማረስ፡ መ ኰፈር፤ ገበሬ፡ መኾን፤ መነገድ፡ ንግድ፡ ማድረግ። (ጥበ) መገበር፤ ግብር፡ መስጠት፤ በግድ፡ መሥራት፤ ባሪያ፡ ገባር፡ ዜጋ፡ መኾን። መጽሐፍ፡ ግን፡ በገብረና፡ በገበረ፡ ፈንታ፡ ተገበረ፡ ይላል፤ አያሰኝም። ተገበሩ፡ ጽድቀ። እለ፡ ይትጌበሩ፡ ሜላተ። ዘይትጌበራ፡ ለምድር። ዘይትጌበር፡ ገራህተ። ሐመር፡ እንተ፡ ትትጌበር፡ እምርሑቅ። ተገበሩ፡ እንከ፡ እስከ፡ አአቱ። ንትጌበር፡ ወንረብሕ፡ (ዕብ፲፩፡ ፴፫። ኢሳ፲፱፡ ፱። ምሳ፲፪፡ ፲፩። ፳፰፡ ፲፱። ፳፱፡ ፴፱። ሉቃ፲፱፡ ፲፫፡ ፲፭። ያዕ፬፡ ፲፫)።

**ገባር፤(ራት። ዕብ፡ ጊቦር፤ ብርቱ)፤** በቁሙ፤ ገበሬ፡ ሠራተኛ፤ በግድ፡ የሚሠራ፤ ጕልበቱን፡ ገንዘቡን፡ ለሹም፡ የሚያፈስ፡ ሹማምት፡ እንደ፡ ወደዱ፡ የሚያደርጉት፡ ባለርስት፡ ባሪያ። (ግጥም፤ ቡልጌ፡ ያበቡት፡ ባለጌ፡ ጤፍ፡ ሲወቃ)፤ የየጀርሳ፡ ዝሞ'ን፡ የከረመ፡ እንደኾን፤ ስንኳን፡ ገባር፡ ጢሰኛም፡ ሰው፡ አይኾን። መጽሐፍ፡ ግን፡ በገባራት፡ ፈንታ፡ ገባር፡ ይላል፤ አያሰኝም። ወገባሩ፡ ኅዳጥ፤ ከመ፡ ይወስክ፡ ገባረ። ናሁ፡ ዐስቦሙ፡ ለገባር። ወሚመ፡ ዲቤሆሙ፡ ሊቃነ፡ ገባር፡ ከመ፡ ይማቅይዎሙ፡ በግብር። ነዳእተ፡ ገባር፡ (ማቴ፱፡ ፴፯። ያዕ፭፡ ፬። ዘፀ፩፡ ፲፩። ፫፡ ፯)። ገባረ፡ ሪፍ። ገባራት። አምጽአ፡ ገባራተ፡ ከመ፡ ያንኅሉ፡ አረፍተ፡ ቤት፡ (ታም፡ ማር። ስንክ፡ ነሐ፩። አዋል)።

**ገባራዊ፤** ዝኒ፡ ከማሁ፤ ገበሬ፤ የነገር፡ የሥራ፡ (፪ጢሞ፡ ፪፡ ፲፭። ክብ፡ ነገ። ስንክ፡ ኅዳ፲)።

**ገብር፤(ብ፡ አግብርት)፤** ባሪያ፡ ተገዥ፤ አገልጋይ፡ ሰው፤ የተማረከ፡ ወይም፡ የተገዛ፡ ግዝ፤ ውላጅ። ገብር፡ ከመ፡ እግዚኡ። ቦኑ፡ ውእቱ፡ ገብር፡ ያዕቆብ፡ አው፡ ልደ፡ ቤት። ነሥአ፡ አርኣያ፡ ገብር። ከመ፡ ኪያነ፡ ይቤዙ፡ እግዚእ፡ ኮነ፡ ገብረ። አግብርትየ፡ ወአእማትየ። አግብርተ፡ ኀጢአት፡ (ኢሳ፳፬፡ ፪። ኤር፪፡ ፲፬። ፊልጵ፪፡ ፯። ድጓ። ግብ፪፡ ፲፰። ሮሜ፮፡ ፲፯)።

**ግብርናት፤** ባርነት፡ ገባርነት፤ ተገዥነት። ግዕዝከሙ፡ እምግብርናት። ገብር፡ ለእመ፡ ግዕዘ፡ እምግብርናቲሁ። ዔወዎሙ፡ ወወሀቦሙ፡ ለግብርናት፡ (ዲድ፡ ፴፫። ዮሴፍ። ስንክ፡ ኅዳ፳፯)።

**አግበረ** ፤ አሠራ ፤ አስደረገ ። አግበሩነ ፡ ዕጹብ ፡ ግብረ ። እለ ፡ ይቀውሙ ፡ ወያገብሩ ፡ ወያስተፋጥኑ ፡ ግብረ ፡ እግዚ ። ፍቅር ፡ ኢታገብር ፡ እኩየ ፡ ወኢታኄሊ ፡ ሕሡመ ፡ ላዕለ ፡ ቢጽ ። አግቢሮ ፡ ኀዳውንተ ። ማሕረስክሙ ፡ አግብሩ ፡ ሑያንወ ፡ ወማዕጺደክሙ ፡ አግብሩ ፡ ረምሐ ፡ (ዘዳ፳ ፡ ፲ ፡ ፲ ። ፩ዜና ፡ ፳፫ ፡ ፬ ። አፈ ፡ ተ፲፱ ። ገድ ፡ ላሊ ። ዮኤ፬ ፡ ፲) ።

**አግባሪ** ፤ አሠሪ ፡ አስደራጊ ፤ አዛዥ ።

**አገበረ** ፤ በቁሙ ፤ ግድ ፡ አለ ፡ አስገደደ ፡ በግድ ፡ አሠራ ። መፀቱ ፡ ለብእሲ ፡ ጽድቀ ፡ እግዚ ፡ ኢያጌብሮ ። ዛቲ ፡ መጽሐፍ ፡ ኢታጌብረከ ፡ ግብረ ፡ ዘኢትክል ። ሰብእ ፡ እኩያን ፡ ያጌብሩኒ ፡ ዘንተ ። ምንትኑ ፡ ዘአገበረከ ፡ ላዕለ ፡ ዝ ። አገበሩነ ፡ ንግበር ። እመኒ ፡ አገበሩከ ፡ ትብላዕ ። ኢያገበርኩከ ፡ ከመ ፡ ትሡዕ ፡ (ያዕ፩ ፡ ፳ ። ፈላስ ። ስንክ ፡ ሠኔ፳፰ ። ዮሴፍ ። ዮዲ፰ ፡ ፵ ። ሚራ፴፱ ፡ ፳ ። ኢሳ፵፫ ፡ ፳፫) ።

**አገባሪ** ፤ በቁሙ ፤ የሚያስገድድ ፡ አስገዳጅ ፡ (ፍ ፡ ነ ፡ ፴፭) ።

**አስተገበረ** ፤ (አግበረ ፡ አገበረ) ፤ አሠራ ፡ አስደረገ ፤ አሳረሰ ፡ አስነገደ ። ነፍስነ ፡ ትፈቅድ ፡ ረድኤተ ፡ ጽኑዐ ፡ ዘያስተጌብራ ፡ ለኃሊናነ ። ኢያስተገበረ ፡ ኃሊናሁ ፡ በምንትኒ ፡ ዘይክልእ ፡ አብጽሖ ፡ ኀበ ፡ እግዚ ። ወያስቱጌብሮሙ ፡ ለኬነውት ። መጺእየ ፡ እምአስተገበርከዎ ፡ (አፈ ፡ ተ፴፬ ። ፊልክ ፡ ፩ ። ግብ፲፱ ፡ ፳፬ ። ማቴ፳፭ ፡ ፳፯ ። ሉቃ፲፱ ፡ ፳፫) ።

**መስተገብር** ፤ (ርት ፡ ራን ፡ ራት) ፤ አግባሪ ፡ አገባሪ ፡ መገብር ፤ የሚያሠራ ፡ አሠሪ ፡ አስደራጊ ። ልማዱ ፡ ግን ፡ እንደ ፡ ተገበረ ፡ አድራጊነት ፡ ነው ፤ አስተገበረን ፡ አይመስልም ። መስተገብር ፡ ውእቱ ፡ ዘይትጌበር ፡ ዘልፈ ። ንህብ ፡ መስተገብርት ፡ ይእቲ ። መስተገብራነ ፡ ማህው ። መስተገብራነ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ። መስተገብራነ ፡ ምድር ፡ (ፈ ፡ መ ፡ ፳፫ ፡ ፩ ። ምሳ፮ ፡ ፰ ። ገድ ፡ ላሊ ። ዲድ ፡ ፲፫) ።

**መስተገብራዊ** ፤ ዝኒ ፡ ከማሁ ፤ አሠሪ ፡ ባለ ሥራ ። ሠሪ ፡ ሠራተኛ ፡ (ፊልክ ፡ ፪፮) ። ተግባር ፡ ረባሕ ፡ በማለት ፡ ፈንታ ፡ ምስትግባር ፡ መስተገብር ፡ ይላል ፤ ስሕተት ፡ ነው ፡ (ኢሳ፳፫ ፡ ፲፰) ።

**ተገብረ** ፤ (ይትገበር) ፤ ተሠራ ፡ ተደረገ ፤ ተፈጠረ ፤ ተበጀ ፡ ተዘጋጀ ። እንተ ፡ ተገብረት ፡ በወርቅ ፡ ወበዕንቍ ። ይትገበር ፡ ሎቱ ፡ በዓል ፡ ዐቢይ ። ተገቢሮ ፡ ሠሐቅዎ ፡ መላእክት ። ዘበአማን ፡ ተወልደ ፡ ወኢተገብረ ። ተገብረ ፡ ዝንቱ ፡ ኵሉ ፡ በእዴከ ፡ (ራእ ፲፰ ፡ ፲፮ ። ስንክ ፡ ሚያ፳፱ ። ኢዮ፵ ፡ ፲፱ ። ቄር ። ዮዲ ፲፭ ፡ ፲) ።

**ተገበረ** ፤ (ይትጌበር) ፤ ዝኒ ፡ ከማሁ ፤ በግድ ፡ ተሠራ ፤ ተደረገ ፡ ታረሰ ፡ ተነገደ ። ልማዱ ፡ ግን ፡ አድራጊነት ፡ ነው ፤ በጣም ፡ ተሳስቷል ፤ መዝመሪያውን ፡ እይ ። ተገባሬ ፡ ምድር ፡ (ዘካ፲፫ ፡ ፭ ። ፍ ፡ ነ ፡ ፴፰) ።

**ግቡር** ፤ (ራን ፡ ራት ፡ ብርት) ፤ የተሠራ ፡ የተደረገ ፤ ፍጡር ። ግቡር ፡ በጽድቅ ፡ ወበርትዕ ። ኀጺን ፡ ግቡር ። ማእሰ ፡ በግዕ ፡ ግቡረ ፡ መሓን ። ለግቡራንሂ ፡ ይቤልዎሙ ፡ ኢኮኑ ፡ ግቡራነ ፡ ወኢተፈጥሩሂ ፤ አላ ፡ ሀለዉ ፡ ዘእንበለ ፡ ጥንት ፡ (መዝ ፡ ፻፲ ። ሕዝ፳፯ ፡ ፲፱ ። ዘፀ፴፭ ፡ ፯ ። አፈ ፡ ድ፳፪) ።

**ግብረት** ፤ ማድረግ ፤ መደረግ ፡ መሠራት ፡ መፈጠር ፤ አሠራር ፡ አደራረግ ፤ ሥራ ። ከመ ፡ ግብረተ ፡ ግንፋል ። ግብረተ ፡ ዕጣን ። ግብረተ ፡ ፍትሎ ። ለኵሉ ፡ ግብረቱ ፡ ለደብተራ ። እምቅድመ ፡ ግብረተ ፡ ሰማያት ። ወሥናይ ፡ ግብረቱ ። ወግብረቶንሂ ፡ ግብረተ ፡ እግዚእ ፡ (ዘፀ፳፬ ፡ ፲ ። ፴ ፡ ፴፭ ። ፴፯ ፡ ፳፪ ። ፴፭ ፡ ፳፩ ። ቅዳ ፡ ግሩ ። ዮሴፍ ። አርጋ ፡ ፫) ።

**ግብር** ፤ (ብ ፡ ግበር ፡ ግብራት) ፤ ሥራ ፡ ድርጊያ ፡ ፍጥረት ፤ ነገር ፤ የተደረገ ፡ ወይም ፡ የሚደረግ ። ኢትትማከር ፡ ምስለ ፡ ሀካይ ፡ በእንተ ፡ ግብር ። ንዋየ ፡ ግበሪሆሙ ። ኵሉ ፡ ግብረ ፡ እግዚእ ። ግብራተ ፡ ሰማይ ። በእንተ ፡ ሠላስ ፡ ግብራት ፡ (ሢራ፴፯ ፡ ፲፩ ። ዕብ፱ ፡ ፳፩ ። ዳን፫ ፡ ፴፬ ። ሔኖ፫፭ ፡ ፯ ። ፊልክ ፡ ፲፩) ።

**ግብር** ፤ ኵርህ ፤ ግድ ፡ ግዴታ ። በግብር ፡ ዘእንበለ ፡ ፈቃዱ ። በግብር ፡ ይከውን ፡ ዘነበበ ፡ ዮናስ ። ግብረ ፡ ይመጽእ ፡ መንሱት ፡ (ፈ ፡ መ ፡ ፭ ፡ ፲፪ ። ጦቢ ፡ ፲፬ ፡ ፰ ። ሉቃ፲፯ ፡ ፩ ። ዕብ፱ ፡ ፲፯) ። እወ ፡ አማን ፡ በማለት ፡ ፈንታ ፡ ግብር ፡ ይላል ፤ አያሰኝም ፡ (ሉቃ፬ ፡ ፳፫) ።

**ግብር** ፤ በቁሙ ፤ ጸባሕት ፡ አምኃ ፡ ድኻ ፡ ለመንግሥት ፡ የሚሰጠው ። ከመ ፡ የሀቡ ፡ ግብረ ። እለ ፡ ይቀውሙ ፡ ላዕለ ፡ ግብር ። ርሑብ ፡ ግብር ። ይሁብዎ ፡ ግብረ ፡ በበ ፡ ዓመት ፡ (፪ዜና ፡ ፰ ፡ ፰ ፡ ፲ ። ፲ ፡ ፲፰ ። ፳፯ ፡ ፭) ።

**ተግባር** ፤ በቁሙ ፤ ፍጥረት ፡ ሥራ ፤ ዕርሻ ፡ ቍፋሮ ፡ ንግድ ፤ ጥበበ ፡ እድ ፡ በየስሙና ፡ በያይነቱ ። ኵሉ ፡ ተግባረ ፡ እግዚ ፡ ሠናይ ፡ ወአልቦ ፡ ግዱፍ ። ተግባረ ፡ ምድር ። ወሰምረ ፡ ሎቱ ፡ ተግባሩ ። በንዋየ ፡ ብርት ፡ ረሰዩ ፡ ተግባረኪ ። ሜጥ ፡ ወተግባር ። ተግባረ ፡ እደው ። ምንት ፡ ተግባርክሙ ፡ (፩ጢሞ ፡ ፬ ፡ ፬ ። ኤር ፲፴ ፡ ፬ ። ሉቃ፲፱ ፡ ፲፯ ። ሕዝ፳፯ ፡ ፲፫ ። ሢራ፳፯ ፡ ፪ ። ፯ ፡ ፲፯ ። ዘፍ፵፯ ፡ ፴፫) ።

—፤ ጕዳይ ፡ ግዳጅ ፡ ባሕርያዊ ፡ ሥራ ። ኀይል ፡ ብዕል ፡ የንግድ ፡ ዕቃ ፡ መናገጃ ። እምብዝኀ ፡ ተግባርኪ ። አምጽኡ ፡ ዓሣኒ ፡ ወባዕደኒ ፡ ብዙኀ ፡ ተግባሮሙ ፡ (ሕዝ ፳፯ ፡ ፲፰ ። ነሐ፲፫ ፡ ፲፯) ።

**ትግብርት** ፤ ሥራነት ፤ አሠራር ፡ አደራረግ ። ሥራ ፤ የሥራ ፡ ስልት ፡ መልክ ። ትግብርቶሙ ። ትግብርተ ፡ ንህብ ፡ (ኩፋ ፡ ፲፭ ። ምሳ፮ ፡ ፰) ። ግርድ ፡ ዕንፋጭ ፡ በማለት ፡ ፈንታ ፡ ትግብርት ፡ ይላል ፡ (ዓሞ፰ ፡ ፮) ።

**መግበር** ፤ ት ፡ (ብ ፡ መጋብርት) ፤ መሥሪያ ፡ መሣሪያ ፤ ዕቃ ። ኵሉ ፡ ግብሩ ፡ ወኵሉ ፡ መጋብርቲሁ ። ለመጋብርት ፡ (ዘፀ፳፯ ፡ ፲፱ ። ፴፱ ፡ ፲ ፡ ፳፩ ። ሕዝ፲፭ ፡ ፫) ።

**ምግባር ፤ (ራት) ፤** በቁሙ ፤ ሥራ ፤ የሚገባ ፥ የማይገባ ፤ በሕግ ፥ የታዘዘ ፥ ወይም ፥ ያልታዘዘ ፥ ማናቸ ውም ፥ ኹሉ ። ለዅሉ ፡ ሰብእ ፡ ይፈድዮ ፡ በከመ ፡ ምግባሩ ። ምግባረ ፡ ወሀብናሁ ። ዅሉ ፡ ምግባሮሙ ፡ ርኩስ ። ንጹሕ ፡ አነ ፡ በምግባርየ ። ሰበሰ ፡ አብርሃም ፡ በምግባሩ ፡ ጸድቀ ። ዘይበቀዐ ፡ ለምግበ ፡ ምግባራቲሁ ፡ ወንዋዩ ። (ሢራ ፴፪ ፥ ፳፬ ። ኩፋ ፥ ፫ ። ፳፩ ። ኢዮ ፲፩ ፥ ፬ ። ሮሜ ፬ ፥ ፪ ። ፍ ፥ ነ ፥ ፴፪) ።

**ምግባር ፤** መሥሪያ ፥ ማድረጊያ ፥ ቦታ ፥ መሣሪያ ፤ ወይም ፥ ባሕርይ ፤ አካል ፥ ሥራውን ፥ የሚፈጽምበት ። ምግባር ፡ ይመርሕ ፡ ኀበ ፡ ጥያቄ ፡ አስማት ፡ ወምግባርኒ ፡ ይትፌጸም ፡ በህላዌ ፡ (ሃይ ፥ አበ) ።

**ገቢስ ፤ ሶት ፤ (ገበሰ ፥ ይገብስ ፥ ይግብስ ። ዕብ ፥ ጋባሽ ፤ መላ ። አው ፥ ገብስሶ ፤ ሶት ፤ ገብሰሰ ፥ ይገበስስ ፥ ይገብስስ) ፤** ማጋበስ ፥ መሰብሰብ ፤ የማር ፥ የንጨት ፥ የሾረት ፤ መምላት ፥ ማስተከክል ፤ መምረግ ፥ መለሰን ፥ መቅባት ፥ መለቅለቅ ፤ የግድግዳ ፥ የግንብ ። መምላት ፥ ውስጡን ፥ በሾረት ፤ መለሰን ፥ አፍኣውን ፥ በጭቃ ፤ መለቅለቅ ፥ በኖራ ፥ በበረቅ ። ገየረን ፥ እይ ።

**ገብሳሲ ፤ (ሲት ፥ ስያን ፥ ያት ፤ ሰስት) ፤** የሚለስን ፥ ለሳኝ ፤ ቀቢ ፥ ለቅላቂ ።

**ተገብሰሰ ፤** ተመረገ ፥ ተለሰነ ፤ ተካከለ ፥ የተላሰ ፥ ነገር ፥ መሰለ ፤ ኖራ ፥ ተቀባ ።

**ግብሱስ ፤ (ሳን ፥ ሳት ፥ ስስት) ፤** የተመረገ ፥ የተለሰነ ፤ ምርግ ፥ ልስን ፥ ቅብ ፥ ልቅልቅ ። አረፍት ፡ ግብስስት ። መቃብር ፡ ግብሱሳን ፡ (ግብ፳፫ ፥ ፫ ። ማቴ፳፫ ፥ ፳፯) ።

**ግብስስ ፤ (ጽር ፥ ጊብሶስ ። ዕብ ፥ ሲድ) ፤** ኖራ ፥ በረቅ ፤ የደንጊያ ፥ ፀመድ ፥ ነጭ ፥ ደቃቅ ። አውዐዩ ፡ አዕፅምቲሁ ፡ ለንጉሥ ፡ ለግብስስ ። ዐጥንቱ ፥ ፀመድ ፥ እስኪኾን ፥ ኖራ ፥ እስኪመስል ፥ ማለት ፥ ነው ፤ ባለብሉዮች ፥ ግን ፥ ግብስስ ፥ ለሚባል ፥ ጣዖት ፥ ይሉታል ፥ (ዓሞ ፪ ፥ ፩) ። አምጽኡ ፡ ግብስሰ ። ከመ ፡ ግብስስ ፡ ድቁቅ ፡ (ሄርማ ፥ ገ፹፩ ። ኢሳ፳፯ ፥ ፱) ።

—፤ ልስናት ፥ ልቅልቃት ። የተላጠ ፥ የተቀረፈ ፥ ምርጊት ፤ የፈረሰ ፥ የተናደ ፥ ቤት ።

**ገብስ ፤** በቁሙ ፤ ሰገም ፥ የብር ፥ እኽል ፤ ነጭ ፥ ነጫነጭ ፥ ማለት ፥ ነው ። ገብስማ ፥ ደሮ ፥ እንዲሉ ።

**ግብት ፤—ድንገት ፤— ወጊብ ፥ ወገበ ።**

**ገበታ ፤ (ብ ፥ ገባትው) ፤** በቁሙ ፤ የንጨት ፥ ለገን ፥ ወጭት ፤ ማቡኪያ ፥ ማሻ ፥ መለወሻ ፥ ቆሬ ፤ ወይም ፥ ማሣሻ ፥ ዝርግ ፥ ጠፍጣፋ ፤ ሉሕ ፤ ሰደቃ ። ዋልታም ፥ ይኸናል ። ወደበ ፡ ገባትው ፡ በዘይገብሩ ፡ ናእተ ፡ (፩ዜና ፥ ፳፫ ፥ ፳፱) ።

**ገበታ ፤ (ዕብ ፥ ጋብታ ። ጽር ፥ ጋባታ) ፤** የቦታ ፥ ስም ፤ ከፍታና ፥ ሜዳነት ፥ ያለው ፥ (ዮሐ፲፱ ፥ ፲፫) ።

**ገበታ ፥ ሐዋርያ ፤ (ዐማርኛ) ፤** የመጽሐፍ ፥ ስም ፤ ገበታዋሪያ ፥ ት ፥ ሰባቱ ፥ የሐዋርያት ፥ መልእክታት ፥ ከያዕቆብ ፥ እስከ ፥ ይሁዳ ፥ ያሉት ። መጽሐፉን ፥ ገበታ ፥ ያሰኘው ፥ ዕንጨቱ ፥ ነው ፤ ፍችውም ፥ ማእድ ፡ ማእደ ፥ ትምህርት ፥ ዘሠርዐዎ ፥ ሐዋርያት ፥ እንደ ፥ ማለት ፥ ነው ።

**ገቦታ ፤** የሰው ፥ ስም ። ምስለ ፡ ገቦታ ፡ ወታራ ፡ (አስቴ፩ ፥ ፲፪) ።

**ጉጋ ፤ ጕጋ ፤** ጉጕት ፤ የጕጕት ፥ ዐይነት ፥ አሞራ ። ባለብሉዮች ፥ ቍንጫ ፥ ይሉታል ፥ (መዝ ፥ ፻፩ ። ዘሌ፲፩ ፥ ፲፯ ። ዘዳ፲፬ ፥ ፲፯) ። ቆቃሕ ፥ በማለት ፥ ፈንታ ፥ ጉጋ ፥ ይላል ፤ ስሕተት ፥ ነው ፥ (፩ነገ ፥ ፳፮ ፥ ፳) ።

**ጓጓ ፤** ጋጋኖ ፤ እጎወ ፥ ቀቆኖ ። የጥንብ ፥ አሞራ ፤ እንደ ፥ ጋጋኖ ፥ በዝቶ ፥ ተንጋግቶ ፥ የሚኼድ ።

**ጋግ ፤ ጋጋ ፤ (ብ ፤ ጋጋት ። ዕብ ፥ ጋግ ፤ ጠፈር ፥ መዋቅር ፥ ባጥ) ፤** መንቈር ፥ ቀንበር ፥ ዘንጅር ፤ የቅጣትና ፥ ያገዛዝ ፥ መሣሪያ ፥ (ዘዳ፳፰ ፥ ፵፰ ። ፫ነገ ፥ ፲፪ ፥ ፬ ፥ ፱ ፥ ፲ ። ሢራ፯ ፥ ፳፬ ፥ ፳፱ ። ዕን፪ ፥ ፯) ። ግድፊ ፡ ጋጋ ፡ እምክሣድኪ ። አንትሙ ፡ እሱራን ፡ በሰናስል ፡ ወበጋጋ ፡ ወበመዋቅሕት ። ያከብዱ ፡ ለነ ፡ ጋጋተ ፡ ውስተ ፡ ክሣውዲነ ፡ ዘኢንክል ፡ ጸዊሮቶ ። ወደዩ ፡ አርባዕተ ፡ ጋጋተ ፤ አሐደ ፡ ውስተ ፡ ክሣዱ ፡ ወአሐደ ፡ ውስተ ፡ ገቦሁ ፡ ወአሐደ ፡ ውስተ ፡ ሐቌሁ ፡ ወአሐደ ፡ ውስተ ፡ አብራኪሁ ፡ (ኢሳ፶፪ ፥ ፪ ። ዮሴፍ ። ቀሌ ። ስንክ ፥ የካ፲፫) ።

—፤ ያንገት ፥ ጌጥ ፥ ሽልማት ፤ ልሻን ፥ ማርዳ ፥ ድሪ ። ጋጋ ፡ ዘወርቅ ፥ (ስንክ ፥ ጥር፲፯) ።

**ጐጕአ ፤ አት ፤ (ጐጕአ ፥ ይጔጕእ ፥ ይጐጕእ ፤** መጓጓት ፥ መመኘት ፤ ተስፋ ፥ ማድረግ ፤ መሠየት ፥ መጕምዠት ፤ ከዚህ ፥ የተነሣ ፥ መቸኰል ፥ መጣደፍ ፤ መፍጠን ፥ መቀልጠፍ ፥ መጣር ፥ መፍጨርጨር ፤ መትጋት ። ጐጕአ ፡ ከመ ፡ ይፃእ ፡ እምህየ ። ጐጕአ ፡ ከመ ፡ ይዕርግ ። ይጔጕእ ፡ ዘተነድፈ ፡ ይምላኅ ፡ ሐጸ ። እስመ ፡ ቦ ፡ ዘይጔጕእ ፡ ወይበርሕ ። ይጔጕእ ፡ ይብዐል ፡ (፪ዜና ፥ ፳፮ ፥ ፳ ። ፲ ፥ ፲፰ ። ሢራ፲፱ ፥ ፲፪ ። ፲፩ ፥ ፲፩ ። ምሳ፳፰ ፥ ፳፪ ። ፪ጴጥ ፥ ፩ ፥ ፲ ፥ ፲፩ ። ፫ ፥ ፲፬) ።

**ጐጓኢ ፤ (ኢት ፥ እያን ፥ ያት) ፤** የሚቸኵል ፥ ቸኳይ ። አንተ ፡ ብእሲ ፡ ጐጓኢ ፡ (ሄርማ) ።

**ጕጉእ ፤ (አን ፥ አት ፥ ጕእት) ፤** የጓጓ ፥ ጕጉ ፤ የቸኰለ ፥ ችኵል ፤ ፈጣን ፥ ቀልጣፋ ፥ ትጉ ። አፍ ፡ ጕጉእ ። ለሰማዐት ፡ ጕጉእ ። ጕጉእ ፡ በከናፍሪሁ ። እመ ፡ ርኢከ ፡ ብእሴ ፡ ጕጉአ ፡ በቃል ፡ (ምሳ፲ ፥ ፲፬ ። ፲፪ ፥ ፲፱ ። ፲፫ ፥ ፫ ። ፳፱ ፥ ፳) ።

**ጕጓኤ ፤** መጓጓት ፤ ጕጕት ። መቸኰል ፥ አቸኳኰል ፤ ችኰላ ፥ ችኵልነት ፥ (ዮሴፍ) ። በጕጓኤ ፥ ፈንታ ፥ ጕጕአት ፥ ይላል ፤ አያሰኝም ። እምብዝኀ ፡ ጕጕአት ፡ (ስንክ ፥ ጥር፲፯) ።

**ጕጕአ፤** ችኰላ፤ ጥድፊያ፡ ቅልጠፋ፤ ትጋት፡ ጥረት፤ ድንጋፄ። ፈነዎሙ፡ በብዙኅ፡ ጕጕኣ። ኀለፈ፡ በጕጕኣ። ጕጕኣ፡ ገቢረክሙ። ቃል፡ ወሁከት፡ ወነ ጐድጓድ፡ ወድልቅልቅ፡ ወጕጕኣ፡ ባዕለ፡ ምድር፡ (ጥበ፲፱፡ ፱። መዝ፡ ፸፯። ፱ኤጥ፡ ፩፡ ፭። አስቴ፩፡ ፲፱። ሔኖ፴፱፡ ፱)።

**አጎጕአ፤** አስቸኰለ፤ አቻኰለ፤ አጣደፈ፤ አስ ደነገጠ፡ (ዘፍ፲፱፡ ፲፭። ዘፀ፭፡ ፲፫። ሔኖ፲፱፡ ፰)። ያጔጕእዎ፡ ለሐማ፡ ውስተ፡ በዓል። መላእክት፡ ያ ጔጕኡኒ። እግዚ፡ አጕጕአኒ፡ (አስቴ፮፡ ፲፬። ሔኖ፷፱፡ ፲። ኢዮ፳፫፡ ፲፮)።

**አጎጓኢ፤ መጎጕእ፤** የሚያጓጓ፤ የሚያስቸ ኵል፡ አስቸኳይ፤ መደንግፅ።

**ገግጸ፤ ጸት፤ (ገገጸ፡ ይጌግጽ፡ ይገግጽ)፤** መገገጽ፤ ተግ፡ ማለት፡ መቆም፡ መገታት፤ ማፈግፈግ፡ ማሸግሸግ፡ ወደ፡ ኋላ፡ ማለት፤ ዐፍሮ፡ ፈርቶ፡ ደንግጦ። ኢይጌግጽ፡ እመዋቲ። ኢይጊግጽ፡ እምገጸሙ። ኢ ይጌግጽ፡ እምጸብእ፡ ወቀትል። ገገጹ፡ እምንዳሬ፡ ሞት። እንዘ፡ ይጌግጹ። ሰላም፡ ለአዕይንቲከ፡ እለ፡ ኢገገጻ፡ እምርእይ፡ (ኢዮ፴፱፡ ፴፩። ፴፱፡ ፲፱። ዮ ሴፍ። አፈ፡ ድ፬። ሄርማ። ደራ.ሲ)። ገጽን፡ ተመልከት፡ የዚህ፡ ዘር፡ ነው።

**ግጋጼ፤** ማፈግፈግ፤ ኀፍረት፡ ፍርሀት፤ ድን ጋጤ፡ ሽሽት። ቀርበት፡ ለመዊት፡ እንበለ፡ ግጋጼ። በማዕታተ፡ ክርስቶስ፡ እንበለ፡ ግጋጼ፡ (ዮሴፍ። ስ ንክ፡ ነሐ፲)።

**ግግጽና፤** ገዘኒ፡ ከማሁ፤ አፈግፋጊነት። ሖረ፡ ምስሌሆሙ፡ እንበለ፡ ግግጽና፡ (ስንክ፡ ሚያ፱)።

**አገገጸ፤** አስፈገፈገ፤ አስፈራ፡ አሳፈረ፤ ተግ፡ አ ሰኘ፡ አሸታገሠ።

**ጋዳ፤ ጋድ፤—በቁሙ፤—ገዲው፡ ገ ደወ።**

**ጎድአ፤—መቃ፡ ደሰቀ፤—ጎዲዕ፡ ጎ ድዐ።**

**ጎዲብ፤ ቦት፤ (ጎደበ፡ ይጎድብ፡ ይ ጕድብ)፤** መጎደብ፡ ማረድ፤ መቈፈር፡ ማጎድጎድ፤ መቆረጥ፤ የመሬት። መመንደብ፡ መጕረድ፡ መጕመድ፤ መጨፍጨፍ፡ መመንጠር፡ መለበድ፤ ካንቻ፡ መምታት፤ የንጨት። መገደብ፡ መወደብ፤ መክተር፡ ማገድ፡ የውሃ። የሦስቱ፡ ኹሉ፡ ስልት፡ አንድ፡ ነው፤ ምስጢሩ፡ ከመ ቍረጥ፡ አይወጣም፤ ገዘመንና፡ ገመደን፡ ይመስላል፤ አንቀጹ፡ ከማርኛ፡ በቀር፡ በግእዝ፡ ቃላት፡ አይገኝም።

**ጕድበ፤** በቁሙ፤ የታረደ፡ የተቈረጠ፤ ዕርድ፡ ምሽግ። ማንሾት፡ ፈፋ፤ ውሃ፡ የበላው፡ መሬት።

**ጕድብ፤ (ብት። ዕብ፡ ጋርዜን፤ ቃር ዱም። ዐረ፡ ፋስ)፤** ምግዘም፤ ገዠሞ፤ የብረት መሣሪያ፤ መጥረቢያ፡ ምሣር። ኹለት፡ አፍ፡ ብረት፡ ምሣርና፡ ዶማ፤ የሚቈርጥና፡ የሚቈፍር፤ እጀታው፡ አንድ፡ ምላሱ፡ ጥንድ፡ በኹለት፡ ወገን፡ የሚሠራ፡ (ዘዳ፲፱፡ ፭። መሳ፱፡ ፲፰። ፩ነገ፡ ፲፫፡ ፳። ኢሳ፲፡ ፲፭። መዝ፡ ፸፫። ሉቃ፫፡ ፱። ሕዝ፱፡ ፪)። ከመ፡ ምሣር፡ ዘይሜጽር፡ ወከመ፡ ጕድብ፡ ዘይሰብር፡ (ዲድ፡ ፲። አዋል)።

ጕድብ፡

**ገድገደ፤ (ገዲድ፡ ገደ። ገዘ)፤** በቁሙ፤ ገደ ገደ፡ አቆመ፡ አጸና፡ ተከለ፤ የይሎ፡ የድንኳን።

**ገድገድ፤** ግድግዳ፤ ካብ፡ ቅጥር፤ የድንኳን፡ ከ ስማ፡ አውታር፤ የሸማ፡ ዐጥር። በዐውደ፡ ገድገደ፡ ቤቱ። በዐጸደ፡ ገድገዱኒ፡ ሊደብተራ፡ (መቃ፡ ገ፩። ፲፰)። አንገደገደ፡ ተንገደገደ፤ ገድጋዳ፡ ማለት፡ ከዚህ፡ ወጥቷል።

**ገዲድ፤ ዶት፤ (ገደ፤ ገደደ፡ ይገድድ፡ ይግድድ። ዕብ፡ ጋዳድ። ዐረ፡ ጀደ)፤** (ጥገ) መገደድ፡ በግድ፡ መያዝ፤ ማስገደድ፡ ግድ፡ ማለት፤ የዳኛ፡ የባለዳ። መወንበድ፡ መሸፈት፡ መጨከን፤ የስራ ዊት። መባስ፡ መታደስ፤ ማገርሸት፤ የደዌ፡ የክፋት። መግደድ፡ ማግደድ፤ መወላገድ፤ መጥመም፡ መጣመም፤ የመልክ፡ የጠባይ፤ ኹሉም፡ የክፉ፡ ነው።

(ጥ) **ግዱድ፤ (ዕብ፡ ግዱድ፤ ወራሪ፡ ዘራፊ)፤** በግድ፡ የተያዘ፤ ወይም፡ የሚይዝ፡ የሚያስገድድ፡ ጨ ካኝ፡ ወንበዴ፡ ሽፍታ። ወኀይላኒ፡ ከመ፡ ብእሲ፡ ግዱድ፡ (ሆሴ፯፡ ፱)።

—፤ የባሰ፡ የጸና፤ የበረታ፡ ብርቱ። እስመ፡ ኀጢአቶሙ፡ ዐቢይ፡ ወግዱድ፡ በኀበ፡ እግዚ፡ (ቄድር)።

**ግድ፤** በቁሙ፤ ውድና፡ ፈቃድ፡ የሌለበት መጽሐፍ፡ ግን፡ በግድ፡ ፈንታ፡ ግዱድ፡ ይላል፤ አያስ ኝም። አዘዘ፡ ይጥዐምዎ፡ በግዱድ፡ (ግንዘ)።

**ግደት፤** መገደድ፤ ማስገደድ፤ ግዴታ፡ ግድ፡ ግዳጅ፤ ጥናት፡ ብርታት። እመ፡ ወድቀ፡ ብሑት፡ ውስተ፡ እከይ፡ እመ፡ አከ፡ በእንተ፡ ድካመ፡ ሥጋ፡ አው፡ በእንተ፡ ግደተ፡ ገድል፡ (ፊልክ፡ ፱)።

**ጎዲድ፤ ዶት፤ (ጎደ፤ ጎደደ፡ ይጎ ድድ፡ ይጕድድ)፤** መጓደድ፡ መቈነን፤ ያካኼድ፡ ያ ረማመድ፤ የታቦት፡ የዑደት።

**ጎደዳ፤ (ዐማርኛ)፤** ያዘባ፡ ጡብ፤ የሾበት፡ ጠገራ፡ ከባድ፡ ጥፍጥፍ፤ ሲማገድ፡ ከእሳት፡ ሲዋሐድ፡ የሚጓደድ፡ ብርቱ፡ ጠንካራ። (ተረት)፤ ሆድ፡ ዕዳ፡ ያስ በላል፡ ጕደዳ።

**ጎድጎደ፤ (ጎዲዕ፡ ጎድዐ)፤** ደጅ፡ መቃ፡ ቀበቀበ፤ እጅ፡ ጸፋ፡ አጨበጨበ፤ ለማስከፈት። ግስንቱ፡

ከጕዲዕና ፡ ከገዲድ ፡ ከኹለቱ ፡ የተደቀለ ፡ ነው ። ሶበ ፡ ጕድጕደ ፡ ኆኅተ ። ነሥአ ፡ እብነ ፡ ወጕድጕደ ፡ ቦቱ ፡ አንቀጸ ። ቦአ ፡ ወጕድጕደ ፡ በኆበ ፡ ዐጸድ ፡ ዘቅድመ ፡ ደብተራ ። ወለዘኒ ፡ ጕድጕደ ፡ ይትረኀዎ ፡ (ፊልክ ፡ ፶፭ ። ስንክ ፡ የካ፪ ። ዮዲ፲፱ ፡ ፲፱ ። ማቴ፯ ፡ ፰) ።

**ጐድጐደ** ፤ ከተተ ፤ ከቤት ፡ ከጓዳ ፡ ከጕድጓድ ፡ አገባ ። ጕደጐደ ፡ ጕድጓድ ፡ ኾነ ፡ (ዐማርኛ) ።

**አንጐድጐደ** ፤ አንጕደጕደ ፡ አሰማ ፤ ተንጕደጕደ ፡ ተሰማ ፡ (፩ነገ ፡ ፯ ፡ ፲፱ ። መዝ ፡ ፲፯) ። ያንጕደጕድ ፡ ኀይል ፡ በፀዓዐ ፡ መደንግፀ ። ዘበላዐሉ ፡ አንጕድጕደ ፡ (ኢዮ ፡ ፴፯ ፡ ፫ ፡ ፬ ። ቅዳ ፡ ግሩ) ።

**ነጐድጓድ** ፤ (ዳት) ፤ በቁሙ ፤ የመብረቅ ፡ ጓታ ፡ ነጕዳ ፤ ታላቅ ፡ ግሩም ፡ ድምፅ ፤ የሚያስፈራ ፡ የሚያስደነግጥ ፤ የሚያርድ ፡ የሚያንቀጠቅጥ ፡ (መዝ ፡ ፸፯ ። ፻፫ ። ኢዮ፵ ፡ ፬ ። ማር፫ ፡ ፲፯) ። መብረቅ ፡ ወፀዓዐ ፡ ወነጕድጓድ ። ወሰማዕኩ ፡ ቃሎ ፡ ከመ ፡ ነጕድጓድ ። ነጕድጓዳት ፡ ወመባርቅት ፡ (ራእ፬ ፡ ፭ ። ፯ ፡ ፭ ። ኩፋ ፡ ፪) ።

**ገዲው** ፤ ዎት ፤ (ገደወ ፡ ይገዱ ፡ ይግዱ) ፤ መስጠት ፡ ማቅረብ ፡ ማስረከብ ። መጋዳት ፡ መከልከል ።

**ጋዳ** ፤ (ዳት) ፤ እጅ ፡ መንሻ ፡ በረከት ፡ መተያያ ፡ በፈቃድ ፡ የሚሰጥ ። ነገሥት ፡ ሳባ ፡ ወዐረብ ፡ ጋዳ ፡ ያመጽኡ ። ጸባሕት ፡ ወጋዳ ። አስትዓ ፡ ወጋዳ ። የሀበነ ፡ ሰላመ ፡ ጋዳ ፡ (መዝ ፡ ፸፩ ። ማቴ፲፯ ፡ ፳፭ ። ሔኖ ፶፫ ፡ ፩ ። ድጓ) ።

**ጋድ** ፤ የሰው ፡ ስም ፤ ገድ ፡ ብዕል ፡ በረከት ፡ ማለት ፡ ነው ፡ (ዘፍ፴ ፡ ፲፩) ።

**ጎድ ፤—ጎይል ፤—ገወድ ።**

**ገዲል** ፤ ሎት ፤ (ገደለ ፡ ይገድል ፡ ይግድል ፤ ቀተለ ። ዕብ ፡ ጋዳል ፤ ዐብየ) ፤ መግደል ፡ ማቍሰል ፤ ማረድ ፡ መቅተል ፤ ማነቅ ፡ ገደል ፡ መጣል ። ፈነወ ፡ ሐጾ ፡ ወነደፎ ፡ ለዔሳው ፡ እኁሁ ፡ ወገደሎ ። ወገደሎ ፡ ዳቤላ ፡ ጠሊ ፡ (ኩፋ ፡ ፴፰ ። ዳን፰ ፡ ፯) ። በጠብሐ ፡ ፈንታ ፡ ገደለ ፡ ይላል ። ወገደለ ፡ ንጉሥ ፡ እምጥሪተ ፡ ዚአሁ ፤ ወመላእክቲሁ ፡ ገደሉ ፡ ለሕዝብ ። እገድላ ፡ ለዛቲ ፡ ዶርሆ ፡ ለተዝካረ ፡ አቡየ ፡ (፪ዜና ፡ ፴፭ ፡ ፯ ። ገድ ፡ ተክ ፡ ታም) ።

**ገዳሊ** ፤ (ሊት ፡ ልያን ፡ ያት) ፤ የሚገድል ፡ ገዳይ ፡ ዐራጅ ፤ ገደል ፡ ሰዳጅ ።

**አግደለ** ፤ አስገደለ ፤ ገደል ፡ አስጣለ ።

**ተገድለ** ፤ ተገደለ ፡ ታረደ ፡ በሰው ፡ እጅ ፡ ሞተ ፤ ተጣለ ፡ ወደቀ ፡ ገደል ፡ ገባ ።

**ግዱል** ፤ (ላን ፡ ላት ፡ ድልት) ፤ የተገደለ ፡ የተጣለ ፤ ገደል ፡ የገባ ።

**ገደላ** ፤ (ላት) ፤ ውዳቂ ፡ ሬሳ ፡ ጥንብ ፤ ገደል ፡ ገብ ፡ (ዘፀ፳፩ ፡ ፴፱—፴፮) ። ኀበ ፡ ሀሎ ፡ ገደላ ፡ ህየ ፡ ይትጋብኡ ፡ አንስርት ፡ (ማቴ፳፬ ፡ ፳፰ ። ሉቃ፲፯ ፡ ፴፯) ።

**ገደል** ፤ (ዕብ ፡ ጋዶል ፤ ዐቢይ) ፤ በቁሙ ፤ ጸድፍ ። (ተረት) ፤ ዛፍና ፡ ወፍ ፤ ገደልና ፡ አፋፍ ። በሬ ፡ ሆይ ፡ በሬ ፡ ሆይ ፡ ሣሩን ፡ አየኽና ፡ ገደሉን ፡ ሳታይ ።

**ተጋደለ** ፤ በቁሙ ፤ ታገለ ፡ ተናነቀ ፤ ተማታ ፡ ተቋሰለ ፤ ተጋ ፡ ተዋጋ ፡ ተሳለፈ ፤ ተቃወመ ፡ ተከራከረ ፡ ተደባደበ ፤ በጕልበት ፡ ባንደበት ፤ በመሰለው ፡ ኹሉ ። ወተጋደሎ ፡ ብእሲ ፡ እስከ ፡ ጸብሐ ። ረከበ ፡ ክልኤተ ፡ ዕደወ ፡ እንዘ ፡ ይትጋደሉ ። ንትጋደል ፡ ለጸቢአቶሙ ፡ እስከ ፡ ንመውት ። ይትጋደል ፡ አበ ፡ ምኔት ፡ ለአድኅኖቱ ። ተጋድሎታ ፡ ለፍትወት ። ተጋደልዋ ፡ ለኀጢአት ። ተጋደለ ፡ በንስሓ ። ተጋደሉ ፡ በማዕተ ፡ በጻማ ፡ ወበምንዳቤ ፡ (ዘፍ፴፪ ፡ ፳፬ ፡ ፳፭ ። ዘፀ፪ ፡ ፲፫ ። ዮሴፍ ። ፍ ፡ ነ ፡ ፲ ። ፳፬ ፡ ፭ ። ዕብ፲፪ ፡ ፬ ። መቃ ፡ ገ፲፭ ። መዋሥ) ።

**ተጋዳሊ** ፤ የሚጋደል ፤ ተጋዳይ ። (ተረት) ፤ አልሞት ፡ ባይ ፡ ተጋዳይ ። ገድለኛ ፤ መንፈሳዊ ፡ ዐርበኛ ። ይቤ ፡ አሐዱ ፡ እምተጋዳልያን ፡ ክቡር ፡ ሞቶሙ ፡ ለሰማዕታት ፡ (ፊላስ ፡ ገ፸፱) ።

**ገድል** ፤ (ላት) ፤ በቁሙ ፤ ትግል ፡ ፈተና ፤ ውጊያ ፡ ሰልፍ ፤ ድልና ፡ አክሊል ፡ እስኪገኝ ፡ ድረስ ፡ የሚደክሙት ፡ ድካም ፤ የሚሠሩት ፡ ሥራ ፤ የሚቀበሉት ፡ መከራ ። ገድለ ፡ መዊእ ። ገድል ፡ ጽኑዕ ። ነበረ ፡ በዝንቱ ፡ ገድል ፡ ሠለስተ ፡ ዓመተ ። እለ ፡ ተጋደሉ ፡ ሠናየ ፡ ገድለ ፡ ወሞቱ ፡ በእንተ ፡ ክርስቶስ ። ዕሴተ ፡ ገድላቲሆሙ ፡ ወድካማቲሆሙ ። ለሰማዕታት ፡ ገድላቲሆሙ ፡ ተጽሕፈ ፡ ለነ ፡ ንትመሀር ፡ ሃይማኖቶሙ ። ገድላቲሆሙ ፡ ለቅዱሳን ፡ (ጥበ፬ ፡ ፪ ። ፲ ፡ ፲፪ ። ገድ ፡ ተክ ። ዲድ ፡ ፳፭ ። ፈ ፡ መ ፡ ፩ ፡ ፪ ። መዋሥ ። አፈ ፡ ድ፳፰) ።

—፤ መንፈሳዊ ፡ ዜና ፤ ወግ ፡ ታሪክ ፤ የቅዱሳንን ፡ መከራና ፡ ጻጋ ፡ ተጋድሏቸውን ፡ የሚናገር ፡ መጽሐፍ ። ገድለ ፡ አዳም ፤ ገድለ ፡ አብርሃም ፤ ገድለ ፡ ሐዋርያት ፤ የመሰለው ፡ ኹሉ ።

**አስተጋደለ** ፤ አጋደለ ፤ አስታገለ ፤ አስተጋገለ ።

**መስተጋድል** ፤ (ልት ፡ ላን ፡ ላት) ፤ የሚጋደል ፡ የሚታገል ፤ ተጋዳሊ ። የሚያጋድል ፡ የሚያስታግል ፤ አጋዳይ ። ወእመኒ ፡ መስተጋድል ፡ ኢይከውኖ ፡ ምዝጋና ፡ እመ ፡ ዘበሕጉ ፡ ኢተጋደለ ። መስተጋድልት ፡ ተሐራሚት ፡ ወንጽሕት ፡ ማርታ ። ሰማዕት ፡ ወጻድቃን ፡ መስተጋድላን ፡ ለሠናይ ፡ (፪ጢሞ ፡ ፪ ፡ ፭ ። ስንክ ፡ ሠኔ፫ ። ቅዳ) ።

**ጐዲል** ፤ ሎት ፤ (ጐደለ ፡ ይጐድል ፡ ይጕድል ፤ ዐማርኛ) ፤ ሐጺጽ ፡ ነቲግ ፡ ንኢስ ፤ መጕደል ፡ ማነስ ፤ ሕጹጽ ፡ መኾን ። ለእመ ፡ ከነት ፡ ምግባራቲከ ፡ ሕጽጽተ ፡ እምጸብአ ፡ ሰይጣናት ፡ አላ ፡ ኅሊናከሰ ፡ ርትዕት ፡ ወኢጕ●ለት ፡ (ፊልክ ፡ ፵፯ ። ፶፱) ።

**ጐደሎ** ፤ በቁሙ ፤ ጕዱል ፡ ያነሰ ፡ የጕደለ ፤ ሕጹጽ ። ዘርቍዐ ፡ ግዕዝ ፡ ወሥርዐቱ ፡ ጕደሎ ፡ በእንተ ፡ ልኅላኄ ፡ ኅሊናሁ ፡ (ፊልክ ፡ ፪)

**ጐደላዊ ፤ (ዊት ፡ ውያን ፡ ያት) ፤** ገዢ ፡ ከማሁ ፤ ያነሰው ፡ የጐደለው ። ጐደላውያን ፡ እምው ስተ ፡ ትምህርት ፡ ዘበእንተ ፡ አእምሮ ፡ ወጽንዐ ፡ ወ ሙቀተ ፡ ፍቅር ። ጐደላውያን ፡ ንሕነ ፡ እምአበው ፡ (ፊልክ ፡ ፵፭ ። ፪፻፲፯) ።

**ጕድለት ፤** በቁሙ ፤ መጕደል ፡ አጕዳደል ፤ ጕ ደሎነት ። በጕድለት ፡ ፈንታ ፡ ጕደሎ ፡ ይላል ፤ አያስኝም ። አቡነ ፡ ምሉእ ፡ ዘአልቦ ፡ ጕደሎ ፡ (ገድ ፡ ኪሮ) ።

**አጕደለ ፤** በቁሙ ፤ አጕደለ ፤ አሳነሰ ፤ አስጕደለ ፡ አስቀነሰ ።

**ገዲም ፤ ሞት ፤ (ገደመ ፡ ይገድም ፡ ይግ ድም ። ዕብ ፡ ጋዳም ፤ ገዘመ) ፤** መጋደም ፤ መተ ኛት ። (ጥደ) መገደም ፡ መደበር ፡ መከለል ፤ ዳሩ ፡ እ ሳት ፡ ማኽሉ ፡ ገነት ፡ ይኹን ፡ ማለት ። መንየን ፡ ተመል ከት ፤ የዚህ ፡ ጎር ፡ ነው ።

**ገዳሚ ፤ (ሚት ፡ ምያን ፡ ያት) ፤** የሚጋ ደም ፡ ተጋዳሚ ፤ ጋድም ። ገዳሚ ፡ ደባሪ ፤ ገዳም ፡ ሠሪ ።

**ግድም ፤ (ብ ፡ ግደም ፤ ግድማት) ፤** በቁሙ ፤ አግድሞ ፤ ወርድ ፡ ስፋት ። ወእመኒ ፡ ሖር ክሙ ፡ ግድመ ፡ አነኒ ፡ አሐውር ፡ ግድመ ፡ ምስሌ ክሙ ። ወግድሙ ፡ ስድስቱ ፡ በእመት ። አልብነ ፡ ኑኅ ፡ ወግድም ። ኢይትአመር ፡ ኑኃ ፡ ወግድማ ፡ ወኢቀማ ። እምግደሚሁ ፡ ለደብተራ ፡ (ዘሌ፳፮ ፡ ፳፩—፳፬ ። ዳን፫ ፡ ፩ ። ቀሌ ። ዘፀ፳፯ ፡ ፲፫) ።

**ግዳሜ ፤** ጋድም ፤ የመስቀል ፡ ክንፍ ። በትረ ፡ ከርካዕ ፡ ውእቱ ፡ ዕፀ ፡ መስቀል ፡ ወበትረ ፡ ለውዝ ፡ ይትሜሰል ፡ በግዳሜሁ ፡ (መጽ ፡ ምስ ። ኤር፩ ፡ ፲፩) ።

**ገዳም ፤ (ማት ። ዕብ ፡ ሚቅላጥ) ፤** በቁሙ ፤ ምኔት ፡ ደብር ፡ የመነኮሳት ፡ ሰፈር ፤ ታላቅ ፡ ቤተ ፡ ክሲ ያን ፤ በደለኛ ፡ ሸሽቶ ፡ የሚጠጋበት ፡ ደውሎ ፡ የሚማ ጠንበት ፡ ደብረ ፡ ምስካይ ፡ (ኢያ፳ ፡ ፩ — ፱) ። ዱር ፡ ጫካ ፡ ወማ ፡ በረሓ ፡ ምድረ ፡ በዳ ፤ ከሀገር ፡ ከመንደር ፡ የራቀ ፡ የአራዊት ፡ ክፍል ። ውስተ ፡ ገዳም ፡ ዐቢይ ። አራዊተ ፡ ገዳም ። ገዳም ፡ ውእቱ ፡ ብሔር ። ገዳማት ፡ ወአድ ባራት ። ቦአ ፡ ውስተ ፡ ውሳጤ ፡ ገዳማት ፡ በድው ፡ (ዮዲ፩ ፡ ፭ ። ዘፍ፱ ፡ ፳ ። ማቴ፲፱ ፡ ፲፭ ። ስንክ ፡ ጥር፳፱ ። የካ፲፭) ።

**ገዳማዊ ፤** የገዳም ፡ ሰው ፡ በረኸኛ ፤ ዐዳኝ ፡ መነ ኰሴ ፡ ባሕታዊ ።

**አግደመ ፤** አጋደመ ፡ አስተኛ ፤ አግድሞ ፡ ወ ሰደ ። ያጸንንዎሙ ፡ ለፍጹማን ፡ እምዘክሮ ፡ እግዚ ኣበ ፡ ኀልዮ ፡ ፍጥረቱ ፡ ከመ ፡ ያግድምዎሙ ፡ እመ ልዕልት ፡ ኀበ ፡ ርሡሰት ፡ (ፊልክ ፡ ፹፭) ።

**አግደምደመ ፤** አፋተለ ፤ አጣመረ ። ኢታግ ደምድም ፡ እገሪከ ፡ ሶበ ፡ ትቀውም ፡ ለጸሎት ። ወ ታግደመድም ፡ እገሪከ ፡ (አዋል ። አረጋ) ።

**መግድም ፤ (ምት ፡ ማን ፡ ማት) ፤** የሚ ያገድም ፡ አግድሞ ፡ የሚያይ ፤ ጠማማ ፡ ፀዋግ ፤ አግድሞ ፡ አደግ ። ወሶበ ፡ ትናገረ ፡ ምስሌሆሙ ፡ ረከቦሙ ፡ ዓለ ማውያነ ፡ መግድማነ ፡ (ፊልክ ፡ ፸፱) ።

**አመግደመ ፤** አግድሞ ፡ አየ ፤ የተንኰል ፡ የክ ፋት ፡ የንቀት ፡ የስርቆት ፡ አተያይ ።

**ጐዳና ፤ ጐድን ፤ (ዐማርኛ) ፤** በቁሙ ፤ አ ውራ ፡ መንገድ ፤ ገበ ፡ ዐፅመ ፡ ገበ ።

**ጐዲዕ ፤ ዖት ፤ (ጐድዐ ፡ ይጐድዕ ፡ ይጕ ዳዕ ። ዕብ ፡ ጋዳዕ) ፤** መጕዳት ፡ መንካት ፡ መጕነጥ ፤ መምታት ፡ መደስቅ ፤ መሰባበር ፡ ማድቀቅ ። መውጋት ፤ መውገጥ ፡ መለጥለጥ ። ጕድዖ ፡ ገቦሁ ። ጕድዐ ፡ እን ግድዓሁ ። ጕድዖ ፡ ነፋስ ፡ ለቤት ። ለሊሃ ፡ ትጕድዕ ፡ ወለሊሃ ፡ ትኬልሕ ። አንዘ ፡ ይጕድዕዎሙ ፡ ለእልኩ ፡ አባግዕ ። ኢይጕድዖ ፡ ዐይነ ፡ እኩይ ። ቅብዐ ፡ ንሒጕ ፡ ንጕዳዕ ፤ ወጕድዑ ፡ በተባርዮ ፡ (ግብ፲፪ ፡ ፯ ። ሉቃ፲፰ ፡ ፲፫ ። ፳፫ ፡ ፵፰ ። ኢዮ፩ ፡ ፲፱ ። ሚራ፲፫ ፡ ፪ ። ሔኖ፹፭ ፡ ፬ ። ደራሲ ። ድር ፡ መድ) ።

**ጐዳዒ ፤ (ዒት ፡ ዕያን ፡ ያት) ፤** የሚጐዳ ፡ የሚነካ ፤ ጕዳት ፡ የሚያመጣ ።

**ተጐድዐ ፤** ተጐዳ ፡ ተመታ ፤ ተነካ ፡ ተጐነጠ ፡ ተሰበረ ፤ ተፈተነ ። ተጕድዐ ፡ ብረኪሁ ። መጽአ ፡ ድ ምፅ ፡ ከመ ፡ ዘጽኑዕ ፡ ነፋስ ፡ ወመሰሎሙ ፡ ከመ ፡ ዘተጕድዐ ፡ ገበዋቲሁ ፡ ለቤት ። ይትጕድዑ ፡ አዕማ ዲክሙ ። ብእሲ ፡ ዘበሥሉ ፡ ተጕድዐ ። ወዘሰ ፡ ኢተ ጕድዐ ፡ አልቦ ፡ ዘየአምር ፡ (ዳን፭ ፡ ፮ ። ሕዝ፮ ፡ ፮ ። መጽ ፡ ምስ ። ሢራ፴፩ ፡ ፳፱ ። ፴፬ ፡ ፲) ።

**ጕዱዕ ፤ (ዓን ፡ ዓት ፡ ድዕት) ፤** የተጐዳ ፡ የተነካ ፡ ንክ ፤ ሰባራ ፡ ከሻዋ ፡ ኰሳሳ ።

**ጕድዐት ፤** መጕዳት ፡ መጐዳት ፡ አጐዳድ ፡ አን ካክ ፤ ጕዳት ፡ ንኪት ፡ ስብራት ።

**ተጓድዐ ፤** ተጓዳ ፤ ተማታ ፡ ተጋጨ ፡ ተጻፋ ፡ (ተ ዋጋ ፡ ተሳበረ ፡ ተቀራሸመ ፤ የበሬ) ። እንዘ ፡ ይትጓድዑ ፡ ምስለ ፡ ክንፍ ፡ ክንፈ ። ይደነግፁ ፡ ሠረገላት ፡ ወይ ትጓድዑ ፡ በፍኖት ፡ (ስንክ ፡ ግን፲፱ ። ናሖ፪ ፡ ፭) ።

**ግድዓ ፤ እንግድዓ ፤ (ዓት) ፤** ደረት ፡ እንቢያ ፤ ፍርእንቢያ ። እን ፡ ምልአተ ፡ ንባብ ፡ ነው ፤ ከአንጕድጕደ ፡ መጥቷል ። ግድዓ ፤ ደረት ፡ በሐዘን ፡ ጊዜ ፡ የሚመታ ፡ የሚ ደሰቅ ። ድጕዳን ፡ እይ ። እንግድዓሁ ፡ ዘብሩር ። ልብሰ ፡ እንግድዓ ። በጕዲዐ ፡ እንግድዓ ፡ ንጕዳዕ ፡ እንግድዓ ቲነ ። አ ፡ እምኔከ ፡ ሞት ፡ እስመ ፡ ኬድከ ፡ በሰኰናከ ፡ እንግድዓቲሆሙ ፡ ለካህናት ፡ (ዳን፪ ፡ ፴፪ ። ዘፀ፳፰ ፡ ፬ ። አፈ ፡ ተ፳፯ ። ፊልክ ፡ ፪፲ ። ግንዘ) ። ልብ ፡ ሆድ ፡ ትዕ ግሥት ፡ አእምሮ ። ሑሪ ፡ በእንግድዓኪ ። ለብእሲ ፡ ጸቢበ ፡ እንግድዓ ፡ በግዕዙ ፡ ይጸልእዎ ፡ ሰብእ ። አ ጥሪ ፡ ትዕግሥተ ፡ ወርሐበተ ፡ እንግድዓ ። ብእሲ ፡ ድኩመ ፡ ኅሊና ፡ ወጸቢበ ፡ እንግድዓ ፡ አብድ ፡ ው እቱ ፡ (ዘፍ፲ ፡ ፲፬ ። ፈላስ ፡ ገ፶፯ ። ሃ፯ ። አፈ ፡ ተ፲፱) ።

**ገዲፍ ፤ ፎት ፤ (ገደፈ ፡ ይገድፍ ፡ ይግ ድፍ ። ዐረ ፡ ጀደፈ ። ዕብ ፡ ጋዴፍ ፤ ሰደበ ፡**

**አረከሰ)** ፤ መግደፍ ፤ መጣል ፡ መተው ፤ መርሳት ፤ ማጥፋት ፤ የጣፈ ፡ የተማሪ ፤ ለጢሚም ፡ ይኾናል ፤ ገዳፍ ፡ ዘኢያገድፍ ፡ እንዲሉ ፡፡ መወርወር ፡ ማሽቀንጠር ፤ ጥሎ ፡ መኼድ ፤ የጕድፍ ፡ የሸክም ፤ የመሰለው ፡ ኹሉ ፡፡ ገደፊቶ ፡ ለሕፃን ፡ ታሕተ ፡ ዕፀ ፡፡ ንግድፎ ፡ ውስተ ፡ ግብ ፡፡ ይግድፉ ፡ ውሉዶሙ ፡ ውስተ ፡ ፈለግ ፡፡ ግድፋ ፡ ውስተ ፡ ምድር ፡፡ አስተዋፅኡ ፡ ወገደፉ ፡ ውስተ ፡ ባሕር ፡ ንዋዮሙ ፡ (ዘፍ፴፯ ፡ ፲፰ ፡፡ ፀ፯ ፡ ፳ ፡፡ ኩፋ ፡ ፵፯ ፡፡ ዘፀ፩ ፡ ፫ ፡፡ ዮና፩ ፡ ፭) ፡፡

**ገዳፊ** ፤ **(ፊት ፡ ፍያን ፡ ያት)** ፤ በቊሙ ፤ የሚገድፍ ፡ የሚጥል ፤ መናኒ ፡፡ ገዳፍያነ ፡ ዓለም ፡ (ፊልክ ፡ ፫) ፡፡

**አግደፈ** ፤ አስገደፈ ፡ አስጣለ ፤ አስተወ ፡ አስረገፈ ፡፡ አገድፈከ ፡ ቀስተከ ፡፡ ያገድፎሙ ፡ ሖ ያንዊሆሙ ፡ (ሕዝ፴፱ ፡ ፫ ፡፡ ኢሳ፵፩ ፡ ፱) ፡፡

**ተገድፈ** ፤ ተገደፈ ፤ ተጣለ ፡ ወደቀ ፤ ተተወ ፡ ተረሳ ፤ ቀረ ፤ ጠፋ ፡ ታጣ ፡፡ ትትገደፍ ፡ አፅት ፡ እምካህን ፡፡ ይትገደፍ ፡ አብድንቲሆሙ ፡፡ ከመ ፡ አባግዐ ፡ ተገደፍነ ፡፡ ተገድፈ ፡ ወአልቦ ፡ ዘተረክበ ፡፡ በእንተ ፡ ረኪበ ፡ ዘተገድፈ ፡ (ሕዝ፷ ፡ ፳፯ ፡፡ ኢሳ፴፬ ፡ ፫ ፡፡ ፶፫ ፡ ፯ ፡፡ ኩፋ ፡ ፵፫ ፡፡ ፍ ፡ ነ ፡ ፵) ፡፡

**ግዱፍ** ፤ **(ፉን ፡ ፉት ፡ ድፍት)** ፤ የተገደፈ ፤ የተጣለ ፡ የወደቀ ፡ የተኛ ፡ የተጋደመ ፤ የጠፋ ፡ የታጣ ፤ የረከሰ ፡ የተናቀ ፡፡ ከመ ፡ ፀፍዐ ፡ ግዱፍ ፡ ከማሁ ፡ ሀካይ ፡ በንበ ፡ ሰከበ ፡፡ ረከበ ፡ በድኖ ፡ ግዱፈ ፡ ውስተ ፡ ምድር ፡፡ ግዱፍ ፡ ውስተ ፡ ዴዴሁ ፡፡ ግዱፋነ ፡ ይርከብ ፡፡ ሖሉ ፡ ተግባረ ፡ እግዚ ፡ ሠናይ ፡ ወአልቦ ፡ ግዱፍ ፡ ወኢምንትኒ ፡ (ሢራ፳፪ ፡ ፱ ፡፡ ዮዲ፲፬ ፡ ፲፭ ፡፡ ሉቃ፲፮ ፡ ፳ ፡፡ ኪዳ ፡፡ ፩ጢሞ ፡ ፬ ፡ ፬) ፡፡

**ግድፈት** ፤ በቊሙ ፤ መግደፍ ፡ መጣል ፤ መገደፍ ፡ አገዳደፍ ፡ ገደፋ ፡ ርሳታ ፡ ዝንጋታ ፤ ገዳፍነት ፡፡ ግድፈተ ፡ ቃል ፡ (ፍ ፡ ነ ፡ መጨረሻው) ፡፡

**ጕድፍ** ፤ **(ፉት)** ፤ በቊሙ ፤ ጥራጊ ፡ ውዳቂ ፡ ገዘብል ፡ ተጠርጎ ፡ የሚጣል ፡፡ ከመ ፡ ሖሉ ፡ ይኩስትር ፡ ቤቶ ፡ አው ፡ መሬተ ፡ አው ፡ ጕድፈ ፡ ይገር ፡ ውስተ ፡ መቃብሪሁ ፡፡ ወኮነ ፡ ወግረ ፡ ዐቢየ ፡ ውእቱ ፡ ጕድፍ ፡ (ስንክ ፡ መስ፲፯ ፡፡ መጋ፲) ፡፡

**ጕደፈ** ፤ በቊሙ ፤ አደፈ ፡ ተዥለፈለፈ ፡፡ እድፋም ፡ ጕድፋም ፡ ኾነ ፡ (ዐማርኛ) ፡፡

**ጌዴር** ፤ **(ዕብ ፡ ጋዴር)** ፤ ዐጥር ፡ ቅጥር ፡ ካብ ፡ ግንብ ፡ መከበቢያ ፡ (ሕዝ፵፱ ፡ ፯) ፡፡

**ጌዶር** ፤ **(ጽር ፡ ጌዱር ፡፡ ዕብ ፡ ግዱድ)** ፤ ወራሪ ፡ ዘራፊ ፡ ፋኖ ፡ ወያኔ ፤ የሽፍታ ፡ ሰራዊት ፡ የወንበዴ ፡ ጭፍራ ፡፡ ገዲድን ፡ እይ ፡፡ እዴግኖሙኑ ፡ ለእሉ ፡ ጌዶር ፡ (፩ነገ ፡ ፴ ፡ ፰) ፡፡

**ጊደር** ፤ **(ዐማርኛ)** ፤ በቊሙ ፡ ያልሸረረችና ፡ ያልተጠቃች ፡ ዕጕልት ፡፡

**ጎህ ፤—ወገግታ ፤—ገዊሕ ፡ ጎሐ፤ጎሕ፡፡**

**ገሀግሀ** ፤ **(ዕብ ፡ ጋሃሀ ፡፡ ሱር ፡ ግሃአ ፡፡ ዐረ ፡ ጀሀጀሀ)** ፤ አራቀ ፡ አስገለለ ፤ ለየ ፡ ከላ ፡ ከለከለ ፡፡ ኀጢአት ፡ እንተ ፡ አልባቲ ፡ ዘይገሀግሃ ፡ (፪ጴጥ ፡ ፪ ፡ ፲፬) ፡፡ ዘሩ ፡ ግሂሀ ፡ ነው ፤ ገሀሀን ፡ እይ ፡፡

**ግሂድ** ፤ **ዶት** ፤ **(ግህደ ፡ አው ፡ ገሀደ ፡ ይግህድ ፡ ይግሀድ ፡፡ ዐረ ፡ ጀሀደ ፤ ጀሀረ)** ፤ (ጥጋ) መጋድ ፡ መገለጥ ፡ መታየት ፤ ግልጥ ፡ ገሃድ ፡ መኾን ፤ መታወቅ ፡ መረዳት ፡፡ መጽሐፍ ፡ ግን ፡ በገሀደ ፡ ፈንታ ፡ ተግህደ ፡ ይላል ፤ አያሰኛም ፡፡ ተግህደ ፡ ሃይማኖተ ፡ ክርስቶስ ፡፡ ደትገሀድ ፡ ተአምሪከ ፡ አሜሃ ፡፡ ለእመ ፡ ጸንዐት ፡ ዛቲ ፡ ወተግህደት ፡፡ ዘተግህዱ ፡ በወዒአ ፡ እምትእዛዛት ፡ (መጽ ፡ ምስ ፡፡ ስንክ ፡ ሐም፴ ፡፡ ፈ ፡ መ ፡ ፱ ፡ ፲፩ ፡፡ ፍ ፡ ነ ፡ ፲፰) ፡፡

**ገሃድ** ፤ **ገሃዲ** ፤ **(ዲት ፡ ድያን ፡ ያት)** ፤ በቊሙ ፤ የሚጋድ ፡ የሚገለጥ ፤ ተገላጭ ፡ ተገላላጭ ፡ ግልጥ ፡፡ ሖሉ ፡ ዘገሃድ ፡ ብርሃን ፡ ውእቱ ፡፡ ኢኮኑ ፡ ገሃደ ፡ ይእዜ ፡ ከመ ፡ ኮነ ፡ አማነ ፡፡ ወብዙኅ ፡ ይጌሥጸሙ ፡ ከመ ፡ ገሃደ ፡ ኢይረስይዎ ፡ (ኤፌ፭ ፡ ፲፫ ፡፡ ቄር ፡፡ ማር፫ ፡ ፲፱) ፡፡

**ገሃደ** ፤ ገልጠ ፡ ተገልጠ ፤ ግልጥ ፡ ኹኖ ፤ በግልጥ ፡ በገሃድ ፡፡ ዘገሃደ ፡ ተነበይኩ ፡፡ ገሃደ ፡ ይመጽእ ፡፡ ዐርገ ፡ ጽሚተ ፡ ወአኮ ፡ ገሃደ ፡ (ዕር ፡ ኢሳ፬ ፡ ፳ ፡፡ መዝ ፡ ፵፱ ፡፡ ዮሐ፯ ፡ ፲) ፡፡

**ግሁድ** ፤ **(ዳን ፡ ዳት ፡ ሀድ** ፤ የተጋደ ፤ የተገለጠ ፡ ግልጥ ፡ የታየ ፡ የጐላ ፡ የተረዳ ፡ ጕልሕ ፡፡ ሖሉ ፡ ክሡት ፡ ቅድሜከ ፡ ወግሁድ ፡፡ ምግባርየ ፡ ዘዐመፃ ፡ ግሁድ ፡ ቅድሜየ ፡፡ ለሖሉ ፡፡ ዕዉቅ ፡ ወግሁድ ፡ ከመ ፡ . .) ወበእንተ ፡ ዝ ፡ ግህደ ፡ ኮነት ፡ ከመ ፡ ወላዲተ ፡ አምላክ ፡ ይእቲ ፡ (ሔኖ፱ ፡ ፭ ፡፡ ግንዘ ፡፡ ቄር ፡፡ ውዳ ፡ ማር፭) ፡፡

**ግህደት** ፤ መገለጥ ፡ አገላለጥ ፤ ግልጥነት ፡ ገሃድነት ፡፡ አብአ ፡ በግህደት ፡ ውስተ ፡ መንግሥተ ፡ ሰማያት ፡፡ አሜሃ ፡ ይቀውም ፡ ጻድቅ ፡ በብዙኅ ፡ ግህደት ፡ (ግንዘ ፡፡ ጥበ፭ ፡ ፩) ፡፡

**ግህድና** ፤ ዝኒ ፡ ከማሁ ፤ ገሃድነት ፤ መገለጥ ፡፡ ረከብነ ፡ ንሕነሂ ፡ ቦቱ ፡ ግህድና ፡ ፍኖት ፡ ኀበ ፡ እግዚ ፡፡ ብነ ፡ ግህድና ፡ ውስተ ፡ በዊአ ፡ ቅዱሳን ፡ (ቄር ፡ ጸላ) ፡፡

**ገሀድ** ፤ **ገሃድ** ፤ በቊሙ ፤ የልደት ፡ የጥምቀት ፡ ዋዜማ ፤ እንዳርብና ፡ ረቡ ፡ የሚጦም ፡፡ ሰላም ፡ እብል ፡ ለጾመ ፡ ዕለት ፡ ዋሕድ ፤ ዘስሙ ፡ ገሀድ ፡ (ስንክ ፡ ጥር፲) ፡፡

**አግሀደ** ፤ አጋደ ፡ ገለጠ ፤ አስገለጠ ፤ አሳየ ፡ አስረዳ ፤ ገልጦ ፡ ነገረ ፡፡ አግህድ ፡ ሎቱ ፡ ፍዳሜ ፡ ዘይመጽእ ፡፡ እስመ ፡ በዛቲ ፡ ዕለት ፡ አግሀደ ፡ እግዚእነ ፡ ኢየ ፡ ክር ፡ ርእሶ ፤ እስመ ፡ ውእቱ ፡ ኢያግሀደ ፡ ርእሶ ፡ ለመኑሂ ፡ መጠነ ፡ ሠላሳ ፡ ዓም ፡፡ ጳውሎስ ፡ ያግህድ ፡ ለነ ፡ ምስጢረ ፡፡ ወይእዜሰ ፡ አግሀደ ፡ በብሂሎቱ ፡፡ ስመ ፡ ክርስቶስ ፡ አግሀዱ ፡ (ሔኖ፲ ፡ ፱ ፡፡ ስንክ ፡ ጥር፲፩ ፡፡ ቄር ፡ ጸላ ፡ አፈ ፡ ድ፫ ፡፡ ስንክ ፡ መስ፳፰) ፡፡

**አግሃዲ፤ መግሀዲ፡ ህድ፤** የሚያግድ፡ የሚገልጥ፤ ገላጭ፡ አስረጅ።

**ምግሃድ፤** መግለጫ፤ መገለጫ፤ ማስረጃ፡ (በታ፡ መግሪያ፡ ቃል)።

**ግሂህ፤ ሆት፤(ገሀሀ፡ ይግህሀ፡ ይግሀሀ)፤** መብራት፡ ማብራት፡ መጽደል፤ መምላት፡ መተካከል፤ ምሉእ፡ ፍጹም፡ መሆን፤ መድመቅ፤ ገሃ፡ ብሕካ፡ በረቅ፡ መምሰል፤ የወርኅ።

**ገሃህ፤ ገሀሀ፤** የጨረቃ፡ ምላት፡ ብርሃኗ፤ በተወለደች፡ ወይም፡ በበቀለች፡ ባ፲፭ኛ፡ ቀን፡ መልቶ፡ ተካክሎ፡ ዐውድማ፡ መስሎ፡ የሚታየው። **ከመ፡ ወርኅ፡ ምልእት፡ በዕለተ፡ ገሃህ። ወርኅ፡ ተፈጥረ፡ ምሉአ፡ ብርሃን፡ ከመ፡ ዕለተ፡ ገሃሁ። ሥኑ፡ ለወርኅ፡ ገሀህ። በቀዳሚ፡ ወርኅ፡ አመ፡ ገሃሁ። ወርኅ፡ ዘአሜ፡ ገሀህ፡**(ሚራ፺፡ ፯። አቡሻ፡ ፲፫። አርጋ፡ ፯። ሕዝ፴፪፡ ፲፯። ደራሲ)።

**ጕሂን፤ ኖት፤(ጕሀነ፡ አው፡ ጐሀነ፡ ይጕህን፡ ይጕሀን)፤** መሰወር፡ መደበቅ። መጮኽ፡ ማዜም፡ ማጕረምረም። ገንሐንና፡ ገነየን፡ ተመልከት፤ የዚህ፡ ጎር፡ ናቸው። መኳን፤ ማኳን፡ ወደ፡ ላይ፡ (ዐማርኛ)።

**ጐሃኒ፤(ኒት፡ ንያን፡ ያት፤ ሀንት)፤** የሚሰውር፡ ደባቂ፤ ጯኺ። የሚጕን፤ የሚያጕን።

**ጕሀን፤ ጉሃን፤** ስዋሬ፤ ስውር፡ ድብቅ፤ ስወራ፡ ድበቃ፤ ስርቆሽ። **ወሀብዎ፡ በዓላተ፡ በጕሃን፡ ወመሥዋዕተ፡ በምስጢር፡**(ጥበ፲፬፡ ፲፭)።

**ጕሀን፤(ናት)፤** ኅቡእ፡ ነገር፤ ረቂቅ፡ ምስጢር፤ በትምርትና፡ በብቃት፡ የሚገኝ። **ጳውሎስ፡ ዘበዙሉ፡ ጠቢብ፡ መጋቤ፡ ጕህናቲ፡ ለክርስቶስ፡**(ቄር፡ ጸላ)። ኅቡኣቲሁ፡ ምስጢራቲሁ፡ ማለት፡ ነው፤ አንዳንድ፡ መጽሐፍ፡ ጕህነት፡ ይላል፤ አያስኬድም።

**ጕህና፤** በቁሙ፤ ዐቢይ፡ ዜማ፤ ስልት፡ ያለው፡ ጩኸት፡ ጉማ፡ ተመማ፤ ወፍራም፡ ድምጥ። **ዝማሬ፡ ዘበልሳን፡ ወጣዕመ፡ ቃል፡ ዘበጕህና። ወሕንጻቲሂ፡ ይእቲ፡ ዘታቀርበነ፡ ኀበ፡ እግዚ፡ በአእዙቶ፡ ማሕሌቱ፡ ውስቴታ፡ በዘይደምፅ፡ ጕህና፡ ኀቤነ፡**(አረጋ፡ ድ፯። ዮሴፍ)።

**ተጓሀነ፤ ተጓሀነወ፤** ተጓጓነ፤ ተጯጯኸ፡ ተዚያዚያመ፡ ተናናረ።

**አስተጓሀነወ፤** አጓጓነ፡ አጯጯኸ፤ አዚያዚያመ። **ጸዋዕክዎሙ፡ ለነቢያት፡ ከመ፡ ያስተጓሀንዉኒ፡ በቃለ፡ ትንቢቶሙ፡**(መጽ፡ ምስ)።

**ገሀነም፤ ገሃነም፤(ጽር፡ ጌሄና። ዕብ፡ ጌይሂኖም። ዐረ፡ ጀሀነም)፤** የቦታ፡ ስም፤ ከደብረ፡ ጽዮን፡ የተያያዘ፤ የተራራው፡ እግር፤ የቄድሮንና፡ የግዮን፡ ወንዝ፡ ማየ፡ ሰሊሖም፡ የሚወርድበት፤ የኢየሩሳሌም፡ ቅርብ፡ አጠገብ፡ በስተደቡብ፡ ያለው፡ ጕድጓዳ፡ ቈላ፡ ሸለቆ፡ ወንዛወንዝ፡ መቀራቅርት፤ እስራኤል፡ ልጆቻቸውን፡ ለሞሎኽ፡ ይሠዉበትና፡ ይጠብሱበት፡ ያቃጥሉበት፡ የነበረ፤ የከተማው፡ ኵስ፡ ውስጥ፡ ለውስጥ፡ ወደ፡ ርሱ፡ የሚጕርፍበት፡ የጥንብና፡ የጕድፍ፡ መጣያ፡ ርኩስ፡ ቦታ፤ የውነተኛው፡ ገሃነም፡ ምሳሌ። ሄኖም፡ የሚባል፡ ሰው፡ ያቀናው፡ የወረሰው፡ የሄኖም፡ ወንዝ፤ ወይም፤ ከሄኖም፡ ልጆች፡ ላንዱ፡ የደረሰ፡ ያንደኛው፡ ልጁ፡ ክፍል፡ ማለት፡ ነው። ጣፌጥን፡ እይ፤ ከዚህ፡ ጋራ፡ አንድ፡ ነው፡ (ኢያ፲፭፡ ፰። ኤር፯፡ ፴፩፡ ፴፪። ፪ነገ፡ ፲፯፡ ፫። ፳፫፡ ፲)። በቁሙ፡ ሲኦል፡ መቃብር፤ የእሳት፡ ጕድጓድ፡ ዐዘቅት፤ መካነ፡ ኃጥኣን፡ ከሞቱ፡ በኋላ፡ የሚኖሩበት፡ የሥቃይ፡ ቦታ፤ እሳቱና፡ ትሉ፡ የማይጠፉ፡ የማያንቀላፉ፡ (ምሳ፩፡ ፲፪። ፲፭፡ ፲፩። መክ፱፡ ፲)። **እቶነ፡ ገሃነም። እሳተ፡ ገሃነም። ሥቃያት፡ ዘገሃነም። ወሞትሰ፡ ዳግም፡ ገሃነም፡ ዘእሳት፡**(ሉቃ፡ ዕዝ፯፡ ፩። ማቴ፭፡ ፳፪። ዕር፡ ኢሳ፩፡ ፫። ራእ፳፡ ፲፬። ማር፱፡ ፵፫። ኢሳ፷፯፡ ፳፬)።

**ገሃነማዊ፤** የገሃነም፤ ሥቃይ፡ እሳት፡ ጭፍራ፡ ሰራዊት። **ላህብ፡ ገሃነማዊ፡**(ጥበ፡ ጠቢ)።

**ጋሀረተ፤—ተጋ፤—ሀጊር፡ ሀገረ፤ ሀግረተ።**

**ኀግዎ፤ ዎት፤(ኀገወ፡ ይኅጉ፡ ይኅጉ፤ ገዊግ)፤** መሳት፡ መሳሳት፤ ከሕግ፡ ከሥርዐት፡ ከመንገድ፡ መውጣት፤ ከጽድቅ፡ መራቅ። ጌገየንና፡ ሳኰየን፡ ጠዐወን፡ እይ፤ የዚህ፡ ጎሮች፡ ናቸው።

—፤ መንጋጋት፡ መርባት፡ መብዛት፤ መንጋ፡ መኾን፤ የሰው፡ የከብት። መንጋ፡ ማለት፡ ቅሉ፡ ከዚህ፡ ወጥቷል።

**አንኀገወ፤** አባከነ፡ አባዘነ፤ አዞረ፡ አንከረተተ፤ አናወዘ፡ አቅበዘበዘ፤ የዐይን፡ የእግር፡ የኅሊና። **አነ፡ ኣንጎግዋ። ኣንጎግወከ፡ ምስለ፡ ሰራዊትከ። እንዘ፡ ታሐምሙ፡ ልበክሙ፡ ወታንጎግዉ። ኣንጎግዎሙ፡ ውስተ፡ አድባር፡**(ሆሴ፪፡ ፲፬። ሕዝ፴፰፡ ፬። ኤር፶፡ ፲፰። ፳፯፡ ፯)። ባከነ፡ ባዘነ፡ ዞረ፡ ተንከረተተ። **ያንጎግዉ፡ በካልእ፡ ሥርዐት። አንጎግዎ፡ ዘስሒት። የዐቅቡ፡ አልባቢሆሙ፡ እምአንጎግዎት፡ ውስተ፡ ኅሊናት፡ እኪት። ያንጎጉ፡ አልባቢሆሙ፡ እምሀገር፡ ኀበ፡ ሀገር፡**(ጥበ፲፬፡ ፳፫። ሃይ፡ አበ። ፊልክ፡ ፺፩። ፻፪)።

**አንኀጋዊ፤ መንኀግው፤(ውት፡ ጉት፤ ዋን፡ ዋት)፤** የሚያባክን፡ የሚባክን፡ በካና፡ በከንካና፡ ዘዋሪ፡ ቀላዋጭ። **ፍልጠት፡ ማእከለ፡ ፈላሲ፡ ወመንጎግው፤ እስመ፡ ፈላሲ፡ የዐውድ፡ ውስተ፡ ምኔታት፡ ከመ፡ ይርባሕ፡ ወያርብሕ፡ ግብራተ፡ መንፈሳውያተ፤ ወመንጎግውሰኬ፡ ይረብሕ፡ ግብራተ፡ ሥጋውያተ፡**(ፊልክ፡ ፷፩)።

**እንጕግው፤** የባከነ፡ ብኩን፤ ዝርው፡ እንቡዝ፡ ቅብዝብዝ። **እስመ፡ እምርእይ፡ ወሰሚዐ፡ ነገር፡ ብዙኅ፡ ትከውን፡ እንጕግወ፡ ኅሊና። ኅሊናቲ**

ሆሙ ፡ እንጕግውት ፡ ድኅረ ፡ ዘይረክብዎ ፡ (ፊልክ ፡ ፵፰ ። ፶፩) ።

**እንጕጋዌ** ፤ መባከን ፡ ብክነት ፤ በክንነት ፤ የ ልቡና ፡ ሁከት ። እንጕጋዌ ፡ በእንተ ፡ ቃል ፡ ንእስት ፡ (ፊልክ ፡ ፺፫) ።

**ነጎጋው** ፤ ዝኒ ፡ ከማሁ ፤ ብክነት ፡ ሁከት ፡ ቅብ ዝብዝታ ፤ ቍጣ ፡ ብስጭት ፡ የቅለት ፡ ሥራ ። መፍትው ፡ ለነ ፡ ንሑር ፡ በህድአት ፡ ሰሲለነ ፡ እምነጎጋው ፡ ከመ ፡ ኢንደቅ ። ዘእንበለ ፡ ፍርሀት ፡ ወነጎጋው ፡ (አፈ ፡ ተ፴፬) ። እበድ ፡ ውእቱ ፡ ነጎጋው ፡ አመ ፡ መዐት ፤ ወ ተቀይሞ ፡ እምድኅረ ፡ ዕርቅ ። ኂሩቱ ፡ ለልቡና ፡ ት ዕግሥት ፡ ወሕሠሙሂ ፡ ነጎጋው ፡ ወጕጕኣ ፡ (ፈላስ) ።

**ጎግ** ፤ ሰራዊት ፡ መንጋ ፡ በዝቶ ፡ የሚኼድ ፡ የ ሚንጋጋ ።

**ማጎግ** ፤ ጎጋዊ ፡ የጎግ ፡ ወገን ። ወያስተጋብ እሙ ፡ ለጎግ ፡ ወለማጎግ ፡ (ራእ፳ ፡ ፰) ።

**ጎግ ፡ ማጎግ** ፤ ጎግ ፡ ስመ ፡ ሀገር ፤ ማጎጋውያን ፡ የወረሱት ፡ (ቃውቃዝ) ። ማጎግ ፡ ስመ ፡ ነገድ ፡ የያፌት ፡ ልጅ ፤ የመስኮቦች ፡ አባት ፡ (ሕዝ፴፰ ፡ ፪ ። ራእ፳ ፡ ፰ ። ዘፍ፲ ፡ ፪) ። ኹለተኛም ፡ ጎግ ፡ ብዙ ፤ ማጎግ ፡ የብዙ ፡ ብዙ ፤ ወይም ፡ ጎግ ፡ ጀርመን ፤ ማጎግ ፡ መስኮብ ፡ ይባላል ፤ ም ስጢሩ ፡ ብዛት ፡ ነው ። አይሁድ ፡ ግን ፡ ከኦሪት ፡ ዘዳግም ፡ (፴፪ ፡ ፰ ፡ ፱) ፡ አያይዘው ፡ ፸ ፡ ቋንቋ ፡ ፸ ፡ ነገድ ፡ ብለው ፡ በፊደል ፡ ቍጥር ፡ ይፈቱታል ፤ አፈታታቸውም ፡ እንዲህ ፡ ነው ። ገ ፡ ሳብዕ ፡ መኾኑ ፡ ወን ፡ ጕርደ ፡ ነውና ፡ ሲጥፉ ፡ ገወግ ፡ ማገወግ ፤ ሲያነቡ ፡ ግን ፡ እንደኛ ፡ ጎግ ፡ ማጎግ ፡ ይሉታል ። ገወግ ፡ ፲፪ ፤ ማገወግ ፡ ፶፪ ፤ ፷፬ ። በዚህ ፡ ላይ ፡ ደግሞ ፡ ገወግ ፡ ማገወግ ፡ ፮ ፡ ብለው ፡ ነጠላ ፡ ቍጥር ፡ ይ ቈጥሩና ፡ ከ፷፬ ፡ ጋራ ፡ ሲገጥሙት ፡ ፸፩ ፡ ይኾናል ። ፸ው ፡ ወይም ፡ ፸፩ዱ ፡ አሕዛብ ፤ ፸፪ኛው ፡ እስራኤል ፡ ይላሉ ፤ ይህ ፡ ደግሞ ፡ (ዘፍ፩ ፡ ፳፰) ። ብዝኍ ፡ ወተባዝኍ ፡ ወ ምልእዋ ፡ ለምድር ፡ ያለውን ፡ ያዳምን ፡ ዘር ፡ ኹሉ ፡ ያሳያል ።

**መግዌ** ፤ (ዕብ ፡ ግዊያ ፤ ገላ ፡ በድን ፡ ሬሳ) ፤ ጥራዝ ፡ የመጽሐፍ ፡ ነደ ፡ ገና ፡ ያልተሰፋ ፡ ያል ተጠረዘ ። በውኁድ ፡ መግዌ ፡ (አዋል) ።

**ጎድ** ፤ (የግዱድ ፡ ከፊል) ፤ ኀይል ፡ ሰራ ዊት ። ይመጽእ ፡ በጎድ ፡ (መቃ) ፡ በንግሊዝ ፡ ቋንቋ ፡ ግን ፡ አምላክ ፡ ማለት ፡ ነው ።

## ጎሀ ፤—ነጋ ፡ በራ ፤—ገዊሕ ፡ ጎሐ ።

**ገውዛ** ፤ (ዐረ ፡ እልጀውዛ) ፤ ኮከብ ፤ ስመ ፡ ኮከብ ፡ ከ፲፪ ፡ መናዝል ፡ አንዱ ። ዕጥፍ ፡ ጥንድ ፡ መንታ ፡ ኹለት ፡ ማለት ፡ ነው ፤ መልኩ ፡ በሥዕል ፡ ሲያዩት ፡ ባ ልና ፡ ሚስት ፡ ወንድና ፡ ሴት ፡ ይመስላል ። ኮከብነቱም ፡ የግንቦት ፡ ነው ፤ ከፀሓይ ፡ ጋራ ፡ ፴፩ ፡ ዕለት ፡ ፴ ፡ ኬክ ሮስ ፡ ይመግባል ፡ (አቡሻ ፡ ፬) ።

**ገውዝ** ፤ (ዕብ ፡ ኤጎዝ ። ሱር ፡ ጋውዛ ። ዐረ ፡ ጀውዝ) ፤ በቁሙ ፤ የታወቀ ፡ የተክል ፡ ዛፍ ፡ ስም ፤ የፍሬው ፡ ዐጥንት ፡ ደረቅ ፡ ጠንካራ ፤ ውስጡ ፡ የ ሚበላ ፡ መንታንት ፡ ያለው ፡ ዘይት ፡ የሚኾን ፤ ሌላውም ፡ የገውዝ ፡ ዐይነት ፡ ኹሉ ። ገውዝ ፡ ወለውዝ ። እመ ፡ ተከልከ ፡ ገውዘ ፡ ይበቍልኑ ፡ ወይን ፡ (ሆሴ፬ ፡ ፲፫ ። መቃ ፡ ገ፳) ።

**ገዊሕ** ፤ **ሖት** ፤ (ጎሐ ፡ ይገውሕ ፡ ይጉሕ ። ዕብ ፡ ጊያሕ) ። መጎሕ ፤ መውገግ ፡ መፍገግ ፤ ወገግ ፡ ፈገግ ፡ ማለት ፤ የንጋት ፡ ምልክት ፡ ማሳየት ፤ ሐመድ ፡ ያ ህያ ፡ ሆድ ፡ መምሰል ፤ የሰማይ ። ሶበ ፡ ይገውሕ ። እ ንዘ ፡ ይገውሕ ፡ ጽባሕ ። ኮከበ ፡ ጽባሕ ፡ ዘይሠርቅ ፡ ሶበ ፡ ይገውሕ ። ወይገውሕ ፡ ሶቤሃ ፡ ብርሃንከ ፡ (ኢያ፮ ፡ ፲፭ ። ፪ነገ ፡ ፲፯ ፡ ፳፪ ። ኢሳ፲፬ ፡ ፲፪ ። ፶፰ ፡ ፰) ።

**ጎሕ** ፤ ወገግታ ፤ ውጋጋን ፡ ፈገገን ፤ የንጋት ፡ ብ ርሃን ፤ ከጽባሕ ፡ በፊት ፡ የሚታይ ፡ ያጥቢያ ፡ ኮከብ ፡ ዘ መን ። ከንግሀ ፡ ጽባሕ ፡ እንዲቀድም ፡ ከጽባሕ ፡ ደግሞ ፡ ጎሕ ፡ ይቀድማል ፤ ጨርሶ ፡ እስኪታይ ፡ ጎሕ ፡ ይባላል ፤ ከታየ ፡ በኋላ ፡ ፀሓይ ፡ እስክቶጣ ፡ ጽባሕ ፡ ይባላል ፤ ን ግሀ ፡ ከዚያ ፡ በኋላ ፡ ነው ። የሦስቱ ፡ ኹሉ ፡ ዘራቸውና ፡ አንቀጻቸው ፡ የተለየ ፡ ነው ። ሶበ ፡ ዐርገ ፡ ጎሕ ። እም ጊዜ ፡ የዐርግ ፡ ጎሕ ። ከመ ፡ ጎሕ ፡ ድልው ፡ ሰወሊደ ፡ ፀሓይ ። ርእየ ፡ ጎሐ ፡ ወኢርእየ ፡ ጽባሐ ፡ (መሳ፲፱ ፡ ፳፭ ። ነሐ፬ ፡ ፳፩ ። አርጋ ፡ ፪ ። ፱) ።

**ተጋውሐ** ፤ ተገለጠ ፤ ተጋለጠ ፤ በራ ፡ አበራ ፤ የብርሃን ። እምቅድመ ፡ ይትጋውሑ ፡ ብርሃናት ። ይሬኢ ፡ ደመናተ ፡ ብርሃን ፡ እንዘ ፡ ይትጋውሑ ። ጸ ዳለ ፡ መባርቅት ፡ እንዘ ፡ ይትጋዋሕ ፡ (ቅዳ ፡ አፈ ። አ ረጋ ፡ መል፴፪ ። መጽ ፡ ምስ) ። ሸሸ ፡ ጠፋ ፤ ራቀ ፡ ወ ገደ ፤ ተሰደደ ፤ የጽልመት ። ዘያቀድም ፡ ውሂበ ፡ ምጽ ዋት ፡ እንዘ ፡ ሀሎ ፡ በሕይወቱ ፡ ይትጋዋሕ ፡ ሎቱ ፡ ጽ ልመተ ፡ ኀጣውኢሁ ፡ በብርሃነ ፡ ማኅቶት ፡ ዘውሂበ ፡ ምጽዋት ፡ (መጽ ፡ ምስ) ።

**ገዊል** ፤ **ሎት** ፤ (ገወለ ፡ ይገውል ፡ ይ ጉል ። ዐረ ፡ ጃል ፡ ጋል) ። ማጠር ፡ መቅጠር ፡ ዘ ለሳ ፡ መጣል ፤ መከብ ፡ መከበብ ፡ ዙሪያውን ፡ መዝጋት ፤ የበረት ፡ ያታክልት ፤ ገዘዘንና ፡ ጸቈነን ፡ ተመልከት ።

**ጎል** ፤ (ብ ፡ አግዋል ፡ ላት) ፤ በረት ፡ የከብ ቶች ፡ ማደሪያ ፡ መቃጕሪያ ። ወአልሕምትኒ ፡ ኢይት ረከቡ ፡ በውስተ ፡ ጎል ። አግዋላት ፡ ለእንስሳሁ ፡ (ዕ ንባ ፡ ፲፯ ። ፪ዜና ፡ ፴፪ ፡ ፳፰) ።

**ጎል** ፤ (ዐረ ፡ ማዝወድ ። ዕብ ፡ ኤቡስ) ፤ ግርግም ፤ በዚያው ፡ በበረቱ ፡ ውስጥ ፡ ዙሪያውን ፡ ወ ይም ፡ ባንድ ፡ ወገን ፡ እንደ ፡ ገንዳ ፡ ኹኖ ፡ የሚሠራ ፡ የእንስሳት ፡ ማእድ ፡ ገለባ ፡ ደፈጫ ፡ የሚቀመጡበት ። አስ ከበቶ ፡ እሙ ፡ ውስተ ፡ ጎለ ፡ እብን ። በጎለ ፡ እንስሳ ፡ ተወድየ ፡ (ድጓ ። ቅዳ ፡ ዲዮ) ። በግርግም ፡ ውስጥ ፡ ማ ለት ፡ ነው ።

**ጎልጎል** ፤ (ዕብ ፡ ጊልጋል) ፤ ስመ ፡ ሀገር ፤ (ዘዳ፲፩ ፡ ፴) ።

**ኀልኀል ፤ (ዕብ ፡ ጕልጎሌት)** ፤ የራስ ፡ ቅል ፤ የራስ ፡ ዐጥንት ፤ መላው ፡ ክንንት ፡ በላይ ፡ ያለው ። ናላን ፡ አንጎል ፡ ማለት ፡ ከዚህ ፡ የወጣ ፡ ነው ።

**ኀልኀታ ፤ (ዕብ ፡ ጎልጎልታ)** ፤ መካን ፡ ርእስ ፤ መካን ፡ ድማኅ ። ይኸውም ፡ የአዳም ፡ ራስ ፡ ቅል ፡ የተቀበረበት ፤ ዳግማይ ፡ አዳም ፡ የተሰቀለበት ፡ ቀራንዮ ፡ ናት ፡ (ዮሐ፲፱ ፡ ፲፯) ።

**ኀን ፤ (ዕብራ)** ፤ መልክ ፡ ሕብር ፡ ዐይነት ፤ አንጻር ፡ አርኣያ ፡ አምሳል ። በቁሙ ፡ ጕን ፤ ገበ ፡ (ዐማርኛ) ።

**ገውሣን ፤ (ዐረ ፡ ገውሽን)** ፤ የሰልፍ ፡ ልብስ ፡ ጌዋ ፡ ሸልማት ፤ ድርዕ ፡ ጥሩር ፤ የመሰለው ፡ ኹሉ ። ወከነ ፡ ላዕሌሁ ፡ ገውሣን ፡ ዘወርቅ ፡ ዘንኩር ፡ ግበሪሁ ፡ (ዮሴፍ) ።

**ኀፍ ፤ (ትግ ። ዕብ ፡ ጕፍ)** ፤ ሀላዌ ፡ ጠባይዕ ፤ ገላ ፡ ግዘፍ ፤ ሥጋ ፡ ሬሳ ፤ የሚታይና ፡ የሚዳሰስ ፡ ማናቸውም ፡ ግዙፍ ፡ ነገር ፡ ኹሉ ። ገፋፋ ፡ ጕፋፋ ፡ ጕፋያ ፡ ማለት ፡ ከዚህ ፡ ወጥቷል ።

**ገዊር ፤ ሮት ፤ (ጎረ ፡ ይገውር ፡ ይጕር ። ዕብ ፡ ጋር)** ፤ መቅረብ ፡ መጠጋት ፤ ቅርብ ፡ አጠገብ ፡ ጥገኛ ፡ መኾን ፤ በቤት ፡ በቦታ ። ጕር ፡ ጕሬ ፡ ማለት ፡ ከዚህ ፡ ወጥቷል ።

**ጎር ፤ (ዐረ ፡ ጃር ። ዕብ ፡ ሽኬን)** ፤ ጓሮ ፡ የቤት ፡ ኋላ ። በቁሙ ፡ ጎረ ፡ ቤት ፤ ቤቱ ፡ የቤት ፡ ቅርብ ፡ ጕን ፡ ሕፅን ፡ አጠገብ ፡ የኾነ ፤ የርስት ፡ የመሬት ፡ የቦታ ፡ አዋሳኝ ፡ ደንበረተኛ ፤ በዙሪያ ፡ ላለ ፡ ለቅርብ ፡ ኹሉ ፡ ይነገራል ። ካልእ ፡ ዘጎሩ ። ወቤቱ ፡ ጎረ ፡ ምኵራብ ። በኀበ ፡ ጎርየ ። ጎር ፡ እኩይ ፡ እለ ፡ ይገስሱ ፡ ርስትየ ። ወቦ ፡ ዐጺደ ፡ ሐምል ፡ ጎረ ፡ ቤቱ ፡ (ዘፀ፲፪ ፡ ፬ ። ግብ ፲፰ ፡ ፯ ። መዝ ፡ ፴ ። ኤር፲፪ ፡ ፲፬ ። ዳን፩ ፡ ፩) ።

**አግዋር ፤ (ራት)** ፤ ጎረ ፡ ቤቶች ፤ ቅርቦች ፡ አጠገቦች ። አክብር ፡ አግዋሪከ ፡ ወአንዋዊከ ። ግዕዙ ፡ እምአግዋሪሁ ፡ ለእግዚ ፡ ወመላእክቲሁ ፡ ኀበ ፡ አግዋሪሆሙ ፡ ለአጋንንት ። እስመ ፡ ግዕዝነ ፡ እምአግዋሪሁ ፡ ለገነት ፡ ወገባእነ ፡ ውስተ ፡ ምድር ፡ ርግምት ፡ (ፈላስ ፡ ገ፷፪ ። ቀሌ ፡ ገ፲፯ ። ፷፫) ።

**ተጋወረ ፤** ተጎራበተ ፤ ተቃረበ ፡ ተቀራረበ ። ኢይትጋወርዎ ፡ ለአንስት ። ጸልአ ፡ ተጋውሮ ፡ እንኍሁ ። ወአርሐቀ ፡ እምተጋውሮ ፡ መላእክት ። በሓውርት ፡ እለ ፡ ይትጋወራ ፡ ምስለ ፡ ከተታ ፡ (ፍ ፡ ነ ፡ ፲ ፡ ፮ ። ዮሴፍ ። ፈ ፡ መ ፡ ፫ ፡ ፪ ። ገድ ፡ ተክ) ።

**ጕር ፤ ጎር ፤ (ዕብራ)** ፤ ያንበሳ ፡ ግልገል ፤ የኹብ ፡ የተኵላ ፡ የውሻ ፡ ቡችላ ፡ የናቱን ፡ ጡት ፡ አጥብቆ ፡ የሚመጥ ፡ የሚመጠምጥ ።

**ኀርየመ ፤ (ይኀረይም ፡ ይኀሪም)** ፤ ዐገመ ፡ ዐከመ ፤ ጠባ ፡ ሳበ ፡ መጠመጠ ፤ ደምን ፡ እንደ ፡ ወተት ፡ ለማውጣት ። ሐገመን ፡ እይ ።

**ኀሬም ፤ (ብ ፡ ኀራይም)** ፤ ዐጋሚ ፡ ሐኪም ፤ ባለዋገምት ። ማገሚያ ፡ ዋገምት ፤ የቀንድ ፡ የብርጭቆ ።

**ጕዛ ፤ (ዕብ ፡ ጋዝ ፤ ጋስ)** ፤ ነጣቂ ፡ ወፍ ፡ አሞራ ፤ ጭላት ፡ የጭላት ፡ ዐይነት ፡ (ዘሌ፲፩ ፡ ፲፯ ። ዘዳ፲፬ ፡ ፲፯) ። በንስር ፡ ፈንታ ፡ ጕዛ ፡ ይላል ፤ ስሕተት ፡ ነው ። ከመ ፡ ክንፈ ፡ ጕዛ ፡ (ዘፀ፲፱ ፡ ፬) ።

**ጋዛ ፤ ጊዛን ፤ (ጽር ፡ ጋዛ ፡ ጋዚስ ። ዕብ ፡ አጻር ። ዐረ ፡ ኀዛኢን)** ፤ የቃ ፡ ቤት ፡ ግምጃ ፡ ቤት ፡ ጕተራ ፡ የብዕል ፡ የገንዘብ ፡ መከተቻ ፡ ማድለቢያ ፡ መሰብሰቢያ ፤ ቤት ፡ መዛግብት ። ቤት ፡ ዘጋዛ ። እምቤተ ፡ መንግሥትየ ፡ ዘጋዛ ። ለዙሉ ፡ ጋዛ ። ንዋየ ፡ ቤተ ፡ ጊዛን ፡ (ዕዝ፩ ፡ ፲፯ ። ፯ ፡ ፳ ፡ ፳፩ ። ኢሳ፴፱ ፡ ፪) ።

**ጋዛ ፤ (ጽር ፡ ጋዛ ። ዕብ ፡ ዐዛ)** ፤ ስመ ፡ ሀገር ፡ የይሁዳ ፡ ክፍል ፤ ከምስቱ ፡ አህጉረ ፡ ኢሎፍሊ ፡ አንዲቱ ፡ የፍልስጥኤም ፡ ደቡብ ፤ እንደ ፡ ዘጌ ፡ እንደ ፡ ቈሬጣ ፡ በባሕር ፡ ጠረፍ ፡ ያለች ፡ (ኢያ፲፭ ፡ ፵፯ ። ግብ፰ ፡ ፳፮) ።

**ገዚእ ፤ እት ፤ (ገዝአ ፡ ይገዝእ ፡ ይግዛእ ። ዐረ ፡ ጀዘአ ፤ ሰጠ ፡ ዐደለ)** ፤ መግዛት ፡ መቆጀት ፤ መጌትየት ፤ ጌታ ፡ መኾን ፤ በገንዘብ ፡ በዜጋ ፡ መሠልጠን ። መቍረስ ፡ መክፈል ፤ መስጠት ፡ ማደል ፤ ማሳለፍ ፡ ማገልገል ፤ በጌትነት ፡ ወይም ፡ ባሽከርነት ። ማብላት ፡ መቀለብ ፡ መከባከብ ፡ ለማሳደግና ፡ ለማሥባት ፤ የሕፃን ፡ የከብት ። መጽሐፍ ፡ ግን ፡ በገዝአ ፡ ፈንታ ፡ አመግዝአ ፡ ይላል ። ይእት ፡ አሚረ ፡ ያመገዝእ ፡ ሰብእ ፡ ዕጉልተ ፡ ወክልኤተ ፡ አባግዐ ፡ (ኢሳ፯ ፡ ፳፩) ። ግዕዘን ፡ እይ ፤ የዚህ ፡ ጎር ፡ ነው ።

**ገዛእ ፤ ገዛኢ ፤ (ኢት ፡ እያን ፡ ያት ፤ እት)** ፤ የሚገዛ ፤ ገዥ ፡ ጌታ ፤ ሹም ፡ ባለቤት ። የሚሰጥ ፡ የሚናኝ ፤ ቀጅ ፡ አሳላፊ ፡ ዐዳይ ፤ የድግስ ፡ አገልጋይ ። ደቂቀ ፡ ገዛእየ ። በወይነ ፡ ማሕሌት ፡ እንተ ፡ ይቀድሕ ፡ ገዛኢ ። ደቀ ፡ ጽርሕ ፡ ወገዛእት ። ቦእት ፡ ይእቲ ፡ ወክልኤ ፡ ገዛእቲሃ ። ወገዛእትሰ ፡ እለ ፡ ቀድሕዎ ፡ (ኢዮ፲፱ ፡ ፲፯ ። ስንክ ፡ ታኅ፳፱ ። ኢሳ፴፱ ፡ ፯ ። ዳን፩ ፡ ፴፯ ። ዮሐ፪ ፡ ፱) ።

**መግዝእ ፤ (እት ፡ አን ፡ አት)** ፤ ዝኒ ፡ ከማሁ ፤ ገዥ ፡ ዐዳይ ፡ ቀላቢ ፤ ሐፃኒ ፡ መጋቢ ፡ ሞግዚት ።

**መግዝእ ፤ እት ፤ (ብ ፡ መጋዝእ ፡ እት ፤ መጋዝእት ፡ ታት)** ፤ ፍሪዳ ፤ ሰንጋ ፡ ድልብ ፡ ቅልብ ፤ ኰርማ ፡ ገች ፡ ሙክት ፤ የሥጋ ፡ ከብት ። አምጽኡ ፡ መግዝአ ፡ ላሕም ፡ ወጥብሑ ። አልሕምት ፡ መጋዝእ ፡ ወመጋዝእ ፡ ደዋርህ ። ጠባሕኩ ፡ መጋዝእትየ ፡ (ሉቃ፲፭ ፡ ፳፫ ። ፫ነገ ፡ ፩ ፡ ፳፫ ። ማቴ፳፪ ፡ ፬) ።

**አግዝአ ፤** አስገዛ ፡ አጌተየ ፤ ጌታ ፡ አደረገ ፤ ሾመ ፡ አሠለጠን ፤ ራሱን ፡ ወይም ፡ ሌላውን ።

**እግዚእ ፤ (አን ፡ አት ፡ ዝእት)** ፤ ቅጽልና ፡ ጥሬ ። የግብርና ፡ የክብር ፡ የማዕርግ ፡ ስም ፤ ጌታ ፡ ገዥ ፡ አዛዥ ፡ ሹም ፡ ባለቤት ፡ መምህር ፡ አያት ፤ ታላቅ ፡ ወንድም ። ጎይታይ ፡ እንዲል ፡ (ትግሬ) ። ገብር ፡ ከመ ፡ እግዚኡ ። ሙኑ ፡ ውእቱ ፡ እግዚእነ ። እግዚአ ፡ አጋዕዝት ፡

(ኢሳ፳፱፥፱። መዝ፥፲፩። ፶፬፭)። እግዚእ፥ ብሎ፥ በአልፍ፥ አጋእዝት፥ ማለት፥ ስሕተት፥ እንደ፥ ኾነ፥ አስተውል። አጋዕዝት፥ የአግዓዚ፥ ብዥ፥ ነው፥ እንጂ፥ የእግዚእ፥ ብዥ፥ እንዳይመስልኽ፥ ግዕዘንና፥ አግዐዘን፥ ተመልከት። የእግዚእስ፥ ብዥ፥ ቢኾን፥ አጋዝእት፥ ይልልኽ፥ ነበር።

**እግዝእት፤(ታት)፤** እመቤት፥ ወይዘሮ፤ ሴት፥ እያት፥ ታላቅ፥ እኅት። እመይተይ፥ እንዲል፥ (ትግሬ)። አዘዘ፡ ኢይስምይዋ፡ ለረሲስ፡ እግዝእተ። አመት፡ ለእመ፡ አውፅአት፡ እግዝእታ። ለኅሪት፡ ወለእግዝእት፡ (ዮሴፍ። ምሳ፳፱፥፶፰። ፱ዮሐ፥፩)።

**እግዝእተ፥ ጌ፤** እትጌ፤ የንጉሥ፥ ሚስት፥ ንግሥት፥ ምድር፤ ሐፄጌን፥ እይ። (ግጥም፥ ስለ፥ ራስ፥ ዐሊ፥ እናት)፤ እኛስ፥ እንላለን፥ እትጌ፥ መንን፤ ዐሊ፥ ማን፥ ይላታል፥ ሲጠራ፥ እናቱን።

**እግዚአዊ፤(ዝእታዊ፥ ይ)፤** የጌታ፤ የግዜር፤ ጌትኛ። አምሳላት፡ እግዚኣውያት፡ (ፍ፥ ነ፥ ፲፱)።

**እግዚእና፤** ሥልጣን፥ ሹመት፥ መብት። በቁሙ፤ ገዥነት፥ ጌትነት፥ እግዜርነት። መንግሥት፡ ወእግዚእና። ወይትአመን፡ በእግዚእናሁ። እግዚእናሁ፡ ላዕሌሃ፡ (ቄር። ፍ፥ ነ፥ ፲፱። ፶፩)።

**እግዚእ፤** የጨዋትና፥ ያቤቱታ፥ የምልጃ፥ የልመና፥ ቃል፤ በቅርብ፥ ባጠገብ፥ ፊት፥ በፊት፥ ላለ፥ ለሚያይ፥ ለሚሰማ፥ የሚነገር፤ አቤቱ፥ ቶ፤ እግዜር፥ ሆይ፥ ጌታ፥ ሆይ፥ ጌቶ። እግዚኦ፡ መሐረነ፡ ክርስቶስ። ሙያው፥ እንደ፥ እግዚእ፥ ነው፤ ቅጽልና፥ በቊ፥ ይኾናል። እግዚአብሔር፡ እግዚኦ። እግዚኦ፡ ኢየሱስ፡ ክር፤ ቅጽል። ስምዐኒ፡ እግዚኦ፡ ጸሎትየ፤ እግዚኦ፡ ጸራሕኩ፡ ኀቤከ፤ በቊ።

**እግዚአብሔር፤(ዕብ፥ ይሆዋ። ሱር፥ ይያ። ዐረ፥ ረብ። ጽር፥ ወቅብ፥ ኪሪዮስ። ሮማይ፥ ዶሚኑስ)፤** ስመ፥ አምላክ፤ እግዚእ፥ ብሔር፤ እግዚእ፥ ጌታ፤ ብሔር፥ ዓለም፤ በተገናኝ፥ የዓለም፥ ገዥ፥ የዓለም፥ ጌታ፤ ዓለም፥ ሳይፈጠር፥ የነበረ፤ ዓለምን፥ ፈጥሮ፥ የሚገዛ፤ ርሱ፥ ኹሉን፥ ቢያስገኝ፥ ኹሉን፥ ቢገዛ፥ እንጂ፥ ለርሱ፥ አስገኝና፥ ጌታ፥ የሌለው፤ አበ፥ ዓለም፥ ንጉሠ፥ ዓለም፥ ወይም፥ እግዚአ፥ ኵሉ፥ ንጉሠ፥ ኵሉ፥ ማለት፥ ነው፤ ባማርኛ፥ እግዜር፥ ተብሎ፥ በ፫፥ ቅንጣት፥ ፊደል፥ ይጣፋል፤ የአልፋ፥ ምስጢር፥ አለበት፤ ብሔርን፥ እይ። እግዚእ፥ እንደ፥ አደናይ፥ ማእከላይ፥ ስም፥ ነው፤ ለኹሉ፥ ይኾናል፤ ብሔር፥ ሲጨመር፥ ግን፥ እንደ፥ ይሆዋና፥ እንደ፥ መለኮት፥ ነው፤ ከፈጣሪ፥ በቀር፥ ለማንም፥ ፍጡር፥ አይሰጥም፤ ፍጡር፥ ምንም፥ ቢነግሥ፥ ምንም፥ ቢጌተይ፥ በታናናሽ፥ ክፍል፥ ነውና፤ ያው፥ ቅሉ፥ የፈጣሪ፥ ገንዘብ፥ ነውና፤ የዓለም፥ ጌታ፥ ሊኾን፥ ወይም፥ እግዜር፥ ሊባል፥ አይቻልም። ጸባኦት፥ በሚልበት፥ ግን፥ ዕብራይስጡ፥ ይሆዋ፡ ጽባኦት፡ እንደሚለው፥ እግዚኦ፡ ጸባኦት፡ ቢያሰኝ፥ እንጂ፥ እግዚአብሔር፡ ጸባኦት፡ አያሰኝም፤ ፍጹም፥ ጸያፍ፥ ነው። የጸባኦት፥ ፍች፥ ኀይላት፥ ሰራዊት፥ ነውና፤ ከዘርፍ፥ በቀር፥ ቅጽል፥ አይኾንም። ዳግመኛም፥ ዕብራይስጥና፥ ዐረብ፥ ጽርእ፤ አምላክ፥ አምላክ፥ የሚሉትን፥ ኹሉ፥ ግእዝ፥ በብዙ፥ ቦታ፥ እግዚአብሔር፥ ይላል፥ (ዘፍ፩፥ ፩—፲፩። ዮሐ፩፥ ፩፥ ፱፥ ፯፥ ፲፱፥ ፲፫)። ይህን፥ የመሰለ፥ ብዙ፥ አለ፤ ይህም፥ ጥንቱን፥ ሲመለስ፥ ቃል፥ በቃል፥ አለመተርጐሙን፤ ኋላም፥ አለመታረሙን፥ ያስረዳል።

**እግዚአብሔርና፤** እግዜርነት፥ አምላክነት፤ እግዜር፥ መኾን። አመ፡ ጽሕቀ፡ ለከዊነ፡ ዕጓለ፡ መሕያው፡ ኢኀደገ፡ እግዚአብሔርናሁ፡ (መጽ፥ ምስ)።

**እግዚአብሔራዊ፤** የግዜር፤ ግብር፥ ባሕርይ፥ ወይም፥ ወገን፥ እግዜራም፥ ባለግዜር። ገቢረ፡ መንክራት፡ እግዚአብሔራዊ። ሐውጽዎሙ፡ በሕዋጼ፡ እግዚአብሔራዊት። በዓላት፡ እግዚአብሔራውያት፡ (መጽ፥ ምስ። ፍ፥ ነ፥ ፳። አቡሻ፥ ፩)።

**ተገዝአ፤** ተገዛ፤ ተገዥ፥ ኾነ። ታደለ፥ ተሰጠ፤ ምግቡ።

**ግዙእ፤(ኣን፥ ኣት፥ ዝእት)፤** ግዙ፥ ግዝ፤ የተገዛ፥ ተገዥ፥ ዜጋ፤ ገብር፥ ገባር።

**ግዝአት፤** መግዛት፥ መገዛት፤ አገዛዝ፥ ግዙነት፤ ግዛት፥ ይዞታ፥ ርስት፥ ጕልት። እስመ፡ እሙንቱ፡ ቅኑያቲ፡ ወምልክናሁ፡ ወግዝአት፡ ሎቱ። አሐዱ፡ ግዝአት፡ (ቅዳ፥ ሕር። አዋል)።

**ግዝእ፤(ኣት)፤** ጋሬዳ፥ ድግስ፥ መሰናደ፤ ፍሪዳ፥ ያለበት፥ የመብል፥ የመጠጥ፥ የምሳ፥ በዓል። ወገብረ፡ ግዝአ፡ ዐቢየ። ቤተ፡ ግዝእ። መዋዕለ፡ ግዝእ፡ (ኩፋ፥ ፲፯። መክ፯፥ ፱። ኢዮ፩፥ ፭)።

**ጊዜ፤(ብ፥ ጊዝያት)፤** በቁሙ፤ የተለየ፥ የተወሰነ፥ ሰዓት፥ ዕለት፥ ወርኅ፥ ዓመት፥ ዘመን፥ ዕድሜ፤ ሰው፥ እስኪሞት፥ እስኪሻር፥ የሚኖርበት፤ የሚያርፍበት፥ የሚሠራበት፥ ሌትና፥ መዓልት፤ ፳፱፥ ሰዓት። (ሙሾ፥ ያጤ፥ ቴ፥ ዘመን፥ ስለ፥ በዛ)፤ እስኪ፥ ቀደም፥ ብለኽ፥ ጥቂት፥ እኽል፥ ቅመስ፤ ሰዉ፥ ያልቅ፥ የለሞይ፥ ያንተ፥ ጊዜ፥ እስኪደርስ። ቦ፡ ጊዜ፡ ለኵሉ። በጊዜ፡ እምጊዝያት። ጊዝያቲሆሙ፡ ለአውራኅ፤ በኵሉ፡ ጊዜ፡ (መክ፫፥ ፩—፱። ዮሴፍ። ኩፋ፥ ፳፱)።

**ጊዜ፤** ዐቢይና፥ ደቂቅ፥ አገባብ፥ ቅጽል፥ ይኾናል፤ አመና፥ ሶበ፥ ሰዓትና፥ ዕለት፥ በሚገቡበት፥ እየገባ፥ ጊዜነቱን፥ ሳይለቅ፥ ይፈታል። ዐቢይ፥ ሲኾን፥ በኀላፊ፤ ጊዜ፡ ሖረ። ቅጽል፥ ሲኾን፥ በትንቢት፤ ጊዜ፡ ይመጽእ። ደቂቅ፥ ሲኾን፥ በጥሬ፤ ጊዜ፡ ቀትል፡ ጊዜ፡ ሞት፡ እያለ፥ ይገባል፤ አመንና፥ ሶበን፥ ተመልከት።

**ገዝአ፤—ገዘገዘ፤—ገዝዐ።**

**ጐዝጐዘ፤(ዐማርኛ። ገለደ፥ ነጸፈ)፤** በቁሙ፤ ጐዘጐዘ፥ አነጠፈ፤ አመቻቸ።

**ጐዝጐዝ፤(ብ፥ ጐዛጕዝ፤ ዛት)፤** ዐልጋ፤ በቁሙ፥ ጕዝጓዝ፥ ሰርፍ፤ ስጋጃ፥ ምንጣፍ፤ የሌት፥

ልብስ ፡ ለሐፍ ። አምጽኡ ፡ ዐሥርተ ፡ ዐራታተ ፡ ወጒዛ ጒዛተ ፡ (፬ነገ ፡ ፲፯ ፡ ፳፱) ።

**ገዚዝ፤ዞት፤(ገዘ ፤ ገዘዘ ፡ ይገዝዝ ፡ ይግዝዝ ። ዕብ ፡ ጋዘዝ ፤ ጊዛሀ)፤** መግዛዝ ፤ መሸለት ፡ መቍረጥ ፡ መቈጥቈጥ ፤ ማጨድ ፡ መጨርገድ ፡ የጠጒር ፡ የፀምር ፡ የማር ፡ የቅጠል ። የተቈረጠውን ፡ መጀጐል ፤ ማጠር ፡ መቅጠር ፡ መጋረድ ፡ መከለል ፡ የቡቃያ ፡ የተክል ፤ ገድገደን ፡ ተመልከት ። መጽሐፍ ፡ ግን ፡ በገዘዘ ፡ ፈንታ ፡ አግዘዘ ፡ ይላል ፤ አያሰኝም ። አግዘዝኩ ፡ ሎቱ ። በክንፍክሙ ፡ ዐውድየ ፡ አግዝዞ ፡ (ኢሳ፩ ፡ ፱ ። ስንክ ፡ ኅዳ፳፱) ።

**ገዛዚ ፤ መግዝዝ ፤** የሚቈርጥ ፤ የሚጀጕል ፤ ጀጕል ፡ ሠሪ ።

**መግዝዝ ፡ ት ፤ (ብ ፡ መጋዝዝ) ፤** መጋረጃ ፡ ዐጥር ፡ ቅጥር ፤ ከለላ ፡ ጀጕል ፤ ጋሬ ፡ ተራራ ፡ ገመገም ። መገዝዝ ፡ ማለት ፡ ከዚህ ፡ የወጣ ፡ ነው ። (ግጥም) ፤ ጣርማ ፡ በር ፡ ኹኙ ፡ ታየኝ ፡ መገዝዝ ፤ ልቤ ፡ ለቡልጋ ፡ ዐደር ፡ ሲ.ጋበዝ ።

**አግዘዘ ፤** አስቈረጠ ፤ አስጀጐለ ፡ ጀጐል ፡ አሠራ ።

**ገዚም ፤ሞት ፤ (ገዘመ ፡ ይገዝም ፡ ይግዝም ። ዕብ ፡ ጋዛም ። ሱር ፡ ግዛም ። ዐረ ፡ ጀዘመ) ፤** መግዛም ፡ መቍረጥ ፤ መጕንደብ ፡ መመንደብ ፤ መመልመል ፡ መጨፍጨፍ ፤ ድል ፡ መንሣት ፡ ማሸነፍ ። ጕደበን ፡ እይ ፤ የዚህ ፡ ጎር ፡ ነው ። ግዝሙ ፡ ዕፀዊሃ ። ይገዝም ፡ በጕድብ ፡ ሾሎ ፡ መሠንየ ፡ አርዝከ ። ገዘማ ፡ ከመ ፡ ዕፀ ፡ ለሕይወትየ ፡ (ኤር፮ ፡ ፮ ። ፳፪ ፡ ፯ ። ኢዮ፲፱ ፡ ፲) ።

**ገዛሚ ፤ (ሚት ፡ ምያን ፡ ያት ፤ ዘምት) ፤** የሚገዝም ፡ የሚቈርጥ ፡ ቈራጭ ።

**ገዝም ፤ (ማት) ፤** በቁሙ ፤ ቃዳ ፡ ተለላ ፤ ፈፋ ፡ እመም ፤ መዛሪያ ፡ ትልም ፤ በዘርና ፡ ባረም ፡ ባጨዳ ፡ ጊዜ ፡ ሠራተኞች ፡ ከዳር ፡ እስከ ፡ ዳር ፡ የሚያወጡት ፡ ከፍል ።

**አግዘመ ፤** አስገዘመ ፤ አስቈረጠ ። አግዘመ ፡ አዕዋመ ። በአፈ ፡ መጥባሕት ፡ ክሣዶ ፡ አግዘመ ፡ (፪ዜና ፡ ፴፬ ፡ ፬ ። ፫ነገ ፡ ፲፭ ፡ ፲፫ ። ስንክ ፡ የካ፲፩) ።

**መግዝም ፤** መቍረጫ ፡ ገዥሞ ፡ ጕድብ ። ገዛሚም ፡ ይኾናል ።

**ተገዝመ ፤** ተቈረጠ ፡ ተቈራረጠ ፤ ተጨፈጨፈ ። ዕፀው ፡ ነዊኃን ፡ ይትገዘሙ ። ዕፀ ፡ እንተ ፡ ተገዝመት ። ተገዚሞ ፡ ደግመ ፡ ይፈሪ ፡ (ሔኖ፹፫ ፡ ፬ ። ዲድ ፡ ፳፭ ። ኢዮ፲፬ ፡ ፯ ። ማቴ፫ ፡ ፲) ።

**ግዙም ፤ (ማን ፡ ማት ፡ ዝምት) ፤** የተቈረጠ ፡ የተጨፈጨፈ ፤ ቍርጥ ፡ ምልምል ። ዕፀው ፡ ግዙማን ፡ (መጽ ፡ ምስ) ።

**ግዝመት ፤** መግዘም ፡ መገዘም ፡ አገዛዘም ፤ አቈራረጥ ፤ ቈረጣ ፡ ምልመላ ፡ ጭፍጨፋ ።

(ጥ) **ግዝም ፤ (ማት) ፤** ጕማጅ ፤ ቍራጭ ፡ ጭፍጫፊ ፤ ዝንጣፊ ።

**ጊዛን ፤—የዕቃ ፡ ቤት ፤—ጋዛ ።**

**ገዝዐ ፤ (ዕብ ፡ ጋዛዕ ። ዐረ ፡ ጀዘዐ) ፤** ከረከረ ፡ ገዘገዘ ፤ ቈረጠ ፡ ገረዘዘ ፤ የመጋዝ ። አዘዘ ፡ መኩንን ፡ ይቀንውዎ ፡ ወይሥትሩ ፡ ሥጋሁ ፡ ወይዝሕቁ ፡ አምእስቲሁ ፡ ወይግዝዕዎ ፡ በመጋዝዕ ፡ እደዊሁ ፡ ወእገሪሁ ፡ (ስንክ ፡ ጥቅ፳፩) ።

**መግዝዕ ፤ (ብ ፡ መጋዝዕ ፡ ዓት) ፤** መጋዝ ፤ መገዝገዣ ፡ መቍረጫ ፡ መተርተሪያ ። አዘዘ ፡ ይሥትርዋ ፡ በመጋዝዕ ፡ ወተሰብረ ፡ መጋዝዕ ፡ (ስንክ ፡ ጥር፳) ።

(ጥ) **ግዛዕ ፤ (ዓት ። ዕብ ፡ ጊዛዕ ። ዐረ ፡ ጂዝዕ) ፤** ጕንደ ፡ ዕፅ ፤ ክሥር ፡ በላይና ፡ ከዐጽቅ ፡ በታች ፡ በመካከል ፡ ያለው ፤ አዕጹቅን ፡ እንደ ፡ ዐምድ ፡ ኹኖ ፡ የሚሸከም ። በትግርኛ ፡ ግን ፡ አንዳች ፡ ማለት ፡ ነው ።

**ገዚፍ ፤ ፎት ፤ (ገዝፈ ፡ ይገዝፍ ፡ ይግዝፍ) ፤** መግዘፍ ፡ መወፈር ፡ መደንደን ፤ መዳጕስ ፡ መሥባት ፤ ወፍራም ፡ ደንደሳም ፡ መኾን ። አጽባዕትየ ፡ ይገዝፍ ፡ ወይጸንዕ ፡ እምሐቌ ፡ አቡየ ። ናሁ ፡ ገዝፋ ፡ አልባቢክሙ ፡ ወከና ፡ ከመ ፡ አእባን ። ከመ ፡ ኢይግዝፍ ፡ ልቡ ፡ ወኢይጽልም ፡ አእምሮቱ ፡ (፪ዜና ፡ ፲ ፡ ፲ ። ዮሴፍ ። ፍ ፡ ነ ፡ ፳) ።

—፤ ማጕራት ፡ መጮኽ ፡ መጨፈር ፤ ሂያ ፡ ሂያ ፡ ማለት ፡ የዘራም ።

(ጥ) **ገዚፍ ፤ (ፋን ፡ ፋት ፡ ዛፍ) ፤** የገዘፈ ፡ ወፍራም ፡ ደንሳ ፡ ደንዳና ፤ ጕልሕ ፡ ሥጋዊ ። ገዚፈ ፡ አባል ። ለምንት ፡ አውሰብከ ፡ ብእሲተ ፡ ንእስተ ፡ ወአንተኒ ፡ ብእሲ ፡ ገዚፍ ፡ ወዐቢይ ። ገዚፍ ፡ ዐምድ ። ልብስ ፡ ገዚፍ ። አምእስተ ፡ ገዚፋን ። አብትር ፡ ዘኀጺን ፡ ገዚፋት ። ምክር ፡ ገዚፍ ፡ (ፊላስ ፡ ገ፺፫ ። ቈ፩ ። ስንክ ፡ ጳግ፩ ። ፍ ፡ ነ ፡ ፳፫ ። ፲ ፡ ፮ ። ገድ ፡ ተክ ። ማር ፡ ይሥ ፳፱ ፡ ፩) ።

**ግዙፍ ፤ (ፋን ፡ ፋት ፡ ዝፍት) ፤** በቁሙ ፤ ዝኒ ፡ ከማሁ ። ይኩን ፡ ልብሰሙ ፡ እምፀምር ፡ ግዙፍ ። ግዙፈ ፡ ክሣድ ። ግዙፋነ ፡ ልብ ፡ (ፍ ፡ ነ ፡ ፲ ፡ ፮ ። ዘዳ፱ ፡ ፲፫ ። አርጋ ፡ ፯) ።

**ግዝፈት ፤** መግዘፍ ፡ መወፈር ፡ አወፋፈር ፤ ወፍራምነት ፤ ውፈራ ፡ ወፍር ፤ ውፋሬ ፡ ድንዳኔ ። በግዝፈተ ፡ ልብከ ፤ በግዝፈተ ፡ ክሣድከ ፡ (መቃ ፡ ገ፮ ። ፲፬ ። ስንክ ፡ ታኅ፮) ።

**ግዝፍ ፤ ግዘፍ ፤** በቁሙ ፤ ወፍር ፡ ድንዳኔ ። ግዝፈ ፡ ምድር ። ግዝፈ ፡ ልብ ። ግዝፈ ፡ ደመናት ። ግዝፈ ፡ ዕፀ ። ግዝፊሆን ፡ ለአልባቢከ ፡ (መዝ ፡ ፻፵ ። አርጋ ፡ ፯ ፡ ፩ ። ሕዝ፴፩ ፡ ፳፩ ። ዮሴፍ) ።

**አግዘፈ ፤** አገዘፈ ፡ አወፈረ ፤ አደነደነ ።

**መግዘፊ ፤ ዝፍ ፤** የሚያገዝፍ ፡ አግዛፊ ፤ አሥቢ ፡ አወፋሪ ።

**መግዝፍ ፤** መግዘፊያ ፡ ማግዘፊያ ፤ ማወፈሪያ ። ግዝፍ ፤ ወፍር ። ሲናበብ ፡ የቅጽል ፡ አፈታት ፡ ይፈታል ።

በመግዘፈ፡ምድር፤ከመ፡ግዝፈ፡ምድር፤ግዙፍ፡(፪ዜና፡፬፡፲፯)።

**ገዚር፤ሮት፤(ገዘረ፡ይገዝር፡ይግዝር። ሱር፡ግዛር። ዕብ፡ጋዛር፤ናማል። ዐረ፡ጀዘረ፤ኀተነ)፤** መግዘር፡መግረዝ፤የብልትን፡ሸንኰፍ፡ቈርጦ፤መጣል፤ወይም፡በጭራሽ፡መስለብ፡(ዘፍ፲፯፡፲፡፲፬፡፳፫። ሉቃ፩፡፶፱። ፪፡፳፩)። ዘገዘረ፡ወልዶ፡በእንተ፡ደዌ። ግዝሩ፡እከየ፡ልብክሙ፡(ፊ፡መ፡፴፫፡፭። ኤር፬፡፬። ዘዳ፲፡፲፮)።

**ገዛሪ፤(ሪት፡ርያን፡ያት፤ዘርት)፤** በቁሙ፤የሚገዝር፤ገራዥ፡ባለወግ። ትቤሎ፡ማርያም፡ለዮሴፍ፡አምጽእ፡ሊተ፡ገዛሬ፡ጠቢበ፡(ስንክ፡ጥር፳)።

**አግዘረ፤** አስገዘረ፤አስገረዘ። እምድኅረ፡ሰቡዕ፡መዋዕል፡ታግዝር፡ወልዳ፡(ፊ፡መ፡፲፡፭። ዘሌ፲፪፡፫)።

**ተገዝረ፤** ተገዘረ፡ተቈረጠ፤ተከረከመ፡(ዘፍ፲፯፡፲፬፡፳፬—፳፯)። ተገዘሩ፡ለአምላክክሙ። ዘተገዝረ፡በምክንያተ፡ደዌ፡ወአዘዝዎ፡ዐቀብተ፡ሥራይ፡(ኤር፬፡፬። ፊ፡መ፡፴፫፡፪)።

**ግዙር፤(ራን፡ራት፡ዝርት)፤** በቁሙ፤የተገዘረ፡ግርዝ፤ብልተ፡ጥሩ፤ይሁዲ፡ፈላሻ፡እስላም፤ቢጽ፡ሐሳዊ፡ወንጌል፡እንበለ፡ኦሪት፡ጥምቀት፡እንበለ፡ግዝረት፤አትረባም፡አትጠቅምም፡አታጸድቅም፡የሚል። ግዙር፡ወቈላፍ። በእንተ፡ኅጽዋን፡ወግዙራን፡(ሮሜ፫፡፴። ፊ፡መ፡፴፫። ግብ፲፭፡፩፡፭፡፳፬)።

**ግዝረት፤** በቁሙ፤መግዘር፡መገዘር፤አገዛዘር፡ገዘራ፤ግዙርነት፤ግዝራት። ወሀበክሙ፡ሙሴ፡ግዝረተ። ወግዝረትሰ፡ግዝረተ፡ጽላሌ፡ልብ፡በመንፈስ። ወምንትኑ፡ስላጤሃ፡ለግዝረት። በእንተ፡ግዝረት፡(ዮሐ፯፡፳፪። ሮሜ፪፡፳፱። ፫፡፩። ፍ፡ነ፡፶፩)።

**ግዝሮ፤** ግዝረት፤ግዝራት። ዝ፡ደመ፡ግዝሮሁ፡ለወልድየ። ኢየሐጽጽ፡ሕማመ፡ግዝሮሁ፡ለአረጋይ፡እምሕማመ፡ሕርደቶሙ፡ለንኡሳን፡(ዘፀ፬፡፳፭። መጽ፡ምስ)። ግዝረት፡የሚገባ፡ለወንድም፡ለሴትም፡ሲኾን፤በወንድ፡ላይ፡ብቻ፡ይነገራል። ሴት፡ልጅ፡ካልተገዘረች፡ጡቷ፡አይገንም፡አይፋፋም፤ታላላቅ፡አይኾንም። የፈላስፎች፡መጽሐፍ፤ጡት፡የሚገዝፍበት፡የሚያብጥበት፡የሚነፋበት፡ምክንያቱ፡ግዝረት፡ነው፡ይላል። አነ፡ቅጽር፡ወአጥባትየ፡ከመ፡ማኅፈድ፡ያለውም፡ይህንን፡ያስረዳል፡(ማሕ፰፡፲)።

**ገዚረት፤(ዐረ፡ጀዚረት)፤** ደሴት፡የየብስ፡ቍራጭ፤ባሕር፡ያጠረው፡የከበበው፡መሬት፡አገር። አፈ፡ወርቅ፡ዘሞተ፡በስደት፡በውስተ፡ገዚረት፡(መጽ፡ምስ)።

**ግዘት፤—በቁሙ፡ውግዘት፤—ወጊዝ፡ወገዘ።**

**ግሕይ፤ዮት፤(ገሐየ፡ይግሒ፡ይግሐይ። ትግ፡ገሔ)፤** መፍራት፡መጨነቅ። መማለድ፤ማለዳ፡መነሣት። ኀሖን፡እይ፤የዚህ፡ኀር፡ነው።

**ገሓይ፤ግሔ፤(ሕያት። ዕብ፡ሻፋን። ዐረ፡ወብር። ጽር፡ኪሮግሊዩ)፤** ሽኮኮ፡አሽኮኮ፡እንደ፡ጥንቸል፡ያለ፡ማር፡ቅጠል፡ቡቃያ፡የሚበላ፤ማለዳ፡ኀሕ፡ሲቀድ፡የሚጮኽ፡የሚያሽካካ። ፈሪ፡



ግሔ፡

ድኩም፡ኀሓዊ፡ማለት፡ነው። ከርሥከሂ፡ጸላዕት፡ምጕያየ፡ግሔ፡ረኃብ። ወግሒያት፡ሕዝብ፡ዘኢኮኑ፡ጽኑዓነ። ቈናጽል፡ወግሒያት፡(ቅኔ። መዝ፡፻፫። ምሳ፴፡፴፮። ሔኖ፲፯፡፪)።

**ጕሐየ፤(ዐረ፡ጀሐ)፤** ዐረመ፤ነቀለ፡መንገለ፡አፈለሰ።

**ምጕሕያ፤** ዐረም፡እሾኽም፡ቅጠል፤ሾርንችት፡ዐቃቅማ፡አሜከላ፡ሙጃ፤የመሰለው፡ኹሉ። ሦክ፡ወምጕሕያ፡(ኢሳ፯፡፳፫—፳፭። መቃ፡ገ፲፪)።

**ጕሒል፤ሎት፤(ጕሕለ፡አው፡ጕሐለ፡ይጕሕል፡ይጕሐል። ዐረ፡ጀሐለ። ዕብ፡ጋሓል፤ጋለ፡ጋመ)፤** ማፍረስ፡መጣስ፤ማቃጠል፡መተኰስ፤የሕግ፡የቅጥር፡የቤት። መስረቅ፡መቀማት፤መውረር፡መዝረፍ።

**ጕሓሊ፤(ሊት፡ልያን፡ያት፤ሐልት)፤ ጕሕልያ፤(ያት)፤** ክፉ፡አድራጊ፤ሌባ፡ቀጣፊ፤ዳንዴ፡ወንበዴ፡ቀማኛ፤የቀን፡ወራሪ፡የሌት፡ሰባሪ፤ቤት፡አቃጣይ፡ነፍስ፡ጓዳይ። ጕሒላ፡እንዲል፡(ትግሬ)። መጽሐፍ፡ግን፤ሰራቂ፡ወጕሕልያ፤ሰረቅት፡ወጕሕልያ፡እያለ፡እንደ፡ፀር፡እንደ፡ቢጽ፡ሳንድም፡ለብዙም፡ያደርገዋል፤የጣፊ፡ስሕተት፡ነው፡(፪ጢሞ፡፪፡፱። ዮሐ፲፡፩፡፰። ዐብድ፡፭። ስንክ፡ኅዳ፲፪)።

**ጓሕለወ፤(ይጓሕሉ፡ይጓሕሉ)፤** ሸነገለ፡አታለለ፤ዋሸ፡ዐበለ፤ከዳ፡ተተነኰለ። ወዘኢጓሕለወ፡በልሳኑ። ወጓሕለዉ፡በልሳናቲሆሙ፡(መዝ፲፬፡፫። ሮሜ፫፡፲፫)። ብዙ፡መጽሐፍ፡ግን፡በጓሕለወ፡ፈንታ፡ተጓሕለወ፡ይላል፡(ዘኊ፳፭፡፲፰። ፍ፡ነ፡፳፱። ፴፯)። አሐውርኑ፡በተጓሕልዎ፡ወበተጠብቦ፡(ዮሴፍ)።

**ጓሕላዊ፤(ዊት፡ውያን፡ያት)፤** የሚሸነግል፡የሚያታልል፤ሸንጋይ፡አታላይ፤ዋሾ፡ዐባይ፤ዐላዊ፡ከዳተኛ፡ተንኰለኛ፡(አፈ፡ተ፳፫)። መጽሐፍ፡ግን፡በጓሕላዊ፡ፈንታ፡ጕሕልያ፡እንደ፡ማለት፡ጕሕላዊ፡ይላል፤አያስኼም። ብእሴ፡ደም፡ወጕሕላዊ። እስመ፡ውእቱ፡ብእሲ፡ጕሕላዊ። ሰይጣን፡ሐሳዊ፡

ወጐሕላዊ፡ ውእቱ። እኩያን፡ ወጐሕላውያን፡ ኖሎት፡ (መገ፡ ፳፮። ዮሴፍ። ፈ፡ መ፡ ፳፫፡ ፩። ዲድ፡ ፮። ሮሜ፩፡ ፳፱)። ፪ኛም፡ በጓሕላዊ፡ ፈንታ፡ ጕሕልው፡ ይላል፤ ስሕተት፡ ነው። መስተመይናን፡ ወጐሕልዋን፡ (አፈ፡ ድ፴፫)።

**ተጐሕለ፤** (ይትጐሐል)፤ ተደራጊ፤ የጐሕለ፡ ተገብሮ።

**ተጓሕለወ፤** (ተደራጊና፡ ተደራራጊ)፤ ተሸነገለ፤ ተሞኘ፡ ተታለለ። ተቃትለ፡ በተምያኔ፡ ነገር፡ ወበተጓሕልዎ። ይትጓሐለዉ፡ በፍቅሮሙ፡ (ዮሴፍ። ፪ጴጥ፡ ፪፡ ፲፫)። ተሸናገለ፡ ተሸነጋገለ፤ ተተናኰለ፡ ተተነኳኰለ፤ ተካዳ፡ ተከዳዳ። ከመ፡ ኢይትጓሕለውክሙ። ተጓሕለወነ፡ እዩ፡ (፩ነገ፡ ፳፫፡ ፳፱። ፱ነገ፡ ፱፡ ፳፫)።

**ጕሕልው፤** (ዋን፡ ዋት፡ ሉት)፤ የተታለለ፡ የተሸነገለ፤ ሸንግል፡ ድልል፤ ሌሎች፡ ያታለሉት፡ የሸነገሉት።

**ጕሕላዌ፤ ጕሕሉት፤** መታለል፡ ማታለል፡ አታላይነት። ሸንገላ፡ ልብለባ፤ ክዳት፡ ተንኰል፤ ሰይጣናዊ፡ ባህል። ልማደ፡ አራዊት፡ ጕሕላዌ። ወገብረ፡ ኢዮአብ፡ ዘንተ፡ ጕሕሉተ። ክዒወ፡ ደመ፡ ሰብእ፡ በጕሕሉት። ወጕሕሉት፡ ቃለ፡ አፉሆሙ። ጕሕሉት፡ ወጽልሑት፡ (ቅኔ። ፪ነገ፡ ፲፱፡ ፰። ቀሌ። ኤር፱፡ ፰። ማር፯፡ ፳፪)።

**አስተጓሕለወ፤** አካዳ፡ አከዳዳ። አስተጓሕለውኪ፡ (ኢሳ፵፯፡ ፱)።

**ግሒሥ፤ ሦት፤** (ግሕሠ፤ ገሐሠ፡ ይግሕሥ፡ ይግሐሥ። የጌሠ፡ ጎር)፤ መግባት፡ ማረፍ፡ ማደር፡ መጠጋት፤ መምጣት፡ መቅረብ፡ (ዘፍ፲፰፡ ፭። ፲፱፡ ፪፡ ፫። መሳ፱፡ ፲፰)። ወይቤሎ፡ ገሐሥ፡ ወንበር፡ ዝየ፡ ንትናገር፤ ወግሕሠ፡ ወነበረ፡ (ሩት፬፡ ፩)።

—፤ ከቦታ፡ ወደ፡ ቦታ፡ መፍለስ፤ ከመንገድ፡ መውጣት፡ መጕዳኘት፤ ማግለል፡ መራቅ፤ ገለል፡ ፈቀቅ፡ ማለት፤ ለማደር፡ ለመስፈር፡ የመንገደኛ፡ (መሳ፲፰፡ ፲፭። ፲፱፡ ፲፭)። እስመ፡ ጕንደየ፡ ግሒሠ፡ ህየ፤ ወግሕሠ፡ ህየ፡ ይብላዕ፡ እክለ፡ (፬ነገ፡ ፬፡ ፰)። ዳግመኛም፡ በግሕሠ፡ ፈንታ፡ ተግሕሠ፡ ይላል፤ አያስኬድም፡ (ሚል፪፡ ፰። ዘፍ፴፰፡ ፲፪። ዘኍ፲፪፡ ፲፭)። ተገሐሥ፡ እምኔ፡ ዐመፃ፡ ወትትገሐሥ፡ እምኔከ፡ ለሊሃ። ተግሕሡ፡ ማያት፡ እምዲበ፡ ገጻ፡ ለምድር፡ ውስተ፡ አሐዱ፡ መካን። ይትገሐሥ፡ መንፈስ፡ ቅዱስ፡ እምብዙኃን፡ (ሚራ፯፡ ፪። ኩፋ፡ ፪። ዕር፡ ኢሳ፸፡ ፳፯)። አንቀጹን፡ ተግሕሠ፡ ካለ፡ ዘንድ፡ ጥሬውን፡ ደግሞ፡ ትግሕሥት፡ ይላል። ትሜንን፡ ትግሕሥቶሙ፡ እምፍኖት፡ ርቱዕ፡ (አፈ፡ ድ፪ና፡ ፱)። አንዳንድ፡ መጽሐፍ፡ ግን፡ ተግሕሦቶሙ፡ ይላል።

**ገሓሢ፤** (ሢት፡ ሥያን፡ ያት፤ ሐሥት)፤ የሚገባ፡ ገቢ፡ መጪ፤ የሚርቅ፡ የሚያገል፤ አግላይ፡ ፈቀቅ፡ ባይ፤ መናኒ።

**ግሑሥ፤** (ሣን፡ ሣት፡ ሕሥት)፤ የገባ፡ የመጣ። የራቀ፡ ያገለለ፤ የተለየ፡ ልዩ፤ ፍጹም፡ ባሕታዊ፡ ከረኸኛ። ትንሣኤ፡ ዘግሑሥ፡ እምሐበት። ልደት፡ ቀዳማዊ፡ ዘግሑሥ፡ እምአዝማን። ዐላውያን፡ እለ፡ ርሑቃን፡ ወግሑሣን፡ እምኔከ። ይኩን፡ ግሑሠ፡ እምቤተ፡ ክርስቲያን። ነበረ፡ ግሑሠ፡ በውሳጤ፡ ገዳም፡ (ፍ፡ ነ፡ ፳፱። ማር፡ ይሥ፲፫። ዳን፫፡ ፰። ቀሌ። ስንክ፡ ሠኔ፳፬)።

**ግሕሠት፤** መግባት፤ መራቅ፡ አራራቅ፡ ርቀት፤ ሽሽት፡ ስደት። ምማቴ፡ ወግሕሠት፡ (ምሳ፳፡ ፴)።

**አግሐሠ፤** አገባ፤ አስገባ። አራቀ፡ አስራቀ፡ አስገለለ፤ አሶገደ፡ ለየ። አግሕሥ፡ እገሪከ፡ እምእሠሮሙ። ፍናወ፡ ሕይወት፡ ያግሕሣ፡ እምእኩይ። አግሐሦሙ፡ እንተ፡ ባሕቲቶሙ። አስተፋጠኑ፡ ወአግሐሡ፡ (ምሳ፩፡ ፲፭። ፲፯፡ ፲፯። ጦቢ፲፪፡ ፮። ዮዲ፲፫፡ ፩)። ዳግመኛም፡ በአግሐሠ፡ ፈንታ፡ አስተግሐሰ፡ ይላል፤ ፍችው፡ አንድ፡ ነው። መጽብበ፡ ቦእኩ፡ ወአልቦ፡ ዘያስተግሕሥ፡ ሊተ። ፈቀድኩ፡ ኣስተግሕሥ፡ ዝኩ፡ መጽብበ፡ (ኢዮ፴፡ ፳፰። ሄርማ)። አስተጋሐሠ፡ ቢል፡ ግን፡ አደራራጊ፡ ኹኖ፡ አራራቀ፡ አለያየ፡ ያሰኛል፤ አስተን፡ ተመልከት።

**አግሓሢ፤ መግሕሥ፤** የሚያገባ፡ አግቢ፤ አራቂ፡ አስገላይ፤ አጋፋሪ፡ ከልካይ።

**ምግሓሥ፤** (ሣት)፤ መግቢያ፡ ማግቢያ፤ ማግለያ፡ ማስገለያ፤ ቦታ፡ ዐዘቅት፡ ሾስሕ። ኀበ፡ አልቦ፡ ምግሓሥ። ምግሓሠ፡ ጽርሑ፡ (ዘኍ፳፱፡ ፳፯። መሳ፫፡ ፳፱)።

—፤ መሣሪያ፤ መዘቂያ፡ ማፈሻ፤ መውሰጃ፡ ማንሻ፡ እንዳከፋና፡ እንደ፡ ላይዳ፡ እንዳስፈሬዳ፡ ያለ። ኢያሚንና፡ ኩከም፡ መስወድ፡ የዚህ፡ ዘውጎች፡ ናቸው። ምግሓሣት፡ (ዘፀ፳፯፡ ፫። ፴፰፡ ፫)።

**ግሒፍ፤ ፎት፤** (ገሐፈ፡ ይግሕፍ፡ ይግሐፍ። ዐረ፡ ጀሐፈ)፤ መጋፍ፡ መጥረግ፤ ማፈሥ፡ መውሰድ፤ ማንሣት፡ ማስገለል። መጋፈፍ፡ ማጋፈፍ፤ አብዝቶ፡ መብላት፡ መጠጣት፡ አለማትረፍ፤ ቢተርፍም፡ በልብስ፡ መታቀፍ፤ በኩፋዳ፡ መክተት፡ መወተፍ። ከመ፡ ጸበል፡ ዘይግሕፎ፡ ነፋስ፡ (ጥበ፭፡ ፲፭። መዝ፡ ፩)

**ገሓፊ፤** (ፊት፡ ፍያን፡ ያት፤ ሐፍት)፤ የሚግፍ፡ የሚጠርግ፤ ጋፊ፡ ጋፋፊ፡ ጠራጊ፤ ሆዳም።

**አግሐፈ፤** አስጋፈ፡ አስጠረገ፤ አስነሣ።

**ተግሕፈ፤** ተጋፈ፡ ተጠረገ።

**ግሑፍ፤** (ፋን፡ ፋት፡ ሕፍት)፤ የተጋፈ፡ የተጠረገ፡ የታፈሠ።

**ግሕፈት፤** መጥረግ፡ መጠረግ፡ አጠራረግ፤ ጠረጋ።

**ገሓፍት፤** (ዐረ፡ ቁፈት። ዕብ፡ ሳል)፤ ቅርጫት፡ መሶብ፡ እንቅብ፤ አገልግል፡ ቅንብቻ፤ ኩፋዳ፡

ግትቻ ። ወታነብሮ ፡ ዲበ ፡ ገሓፍት ፡ (ዘፍ ፡ ፳፱ ፡ ፫ ። ፳፫ ፡ ፴፪) ።

**ምግሓፍ** ፤ (ፋት) ፤ ዝኒ ፡ ከማሁ ፤ መጋፊያ ፡ ማፈሻ ፤ መጥረጊያ ።

**ጋሕፍ** ፤ (ትግ ፡ ጋሕፎ) ፤ የባሕር ፡ ዔሊ ፤ ደንጊያ ፡ ልብሱ ።

**ጕሒቀኈ** ፤ **ቆት** ፤ (**ጕሕቄ ፡ ይጕሕቀኈ ፡ ይጕሐቀኈ ። ዐረ ፡ ጀኃ**) ፤ መጕበጥ ፤ መጕንበስ ፡ መጽነን ፤ እንደ ፡ ደጋን ፡ መኾን ፤ በደዌ ፡ በርግና ፡ (ሉቃ ፲፫ ፡ ፲፩) ። መካን ፡ ዘጕሕቁት ፡ ወሞተ ፡ ማሕፀና ። ዕቤራይት ፡ ዘጕሕቁት ፡ እምአብዝኆ ፡ ውሉድ ፡ (አፈ ፡ ድጽ፩ ። መጽ ፡ ምስ) ።

**ጕሑቀኈ** ፤ (**ቋን ፡ ቋት ፡ ሕቀኈት**) ፤ የጐበጠ ፡ ጉባጣ ፤ ቀላሳ ፡ ተርካሳ ።

**ጕሕቄት** ፤ መጕበጥ ፤ አጕባበጥ ፤ ጉባጥነት ፤ ጉብጠት ።

**አጕሐቄ** ፤ አጕበጠ ፤ አስጕበጠ ፤ ጉባጣ ፡ አደረገ ፡ ዐረቀ ፡ ቀለሰ ፤ አስጕንበሰ ። ፍርግያ ፡ ታጕሕቀኈ ፡ ዘባና ። ትካዝ ፡ ያጕሕቀኈ ፡ አባለ ፡ ወያዐውር ፡ አዕይንተ ፡ (ኪዳ ። ፈላስ ፡ ገ፵፯) ።

**ጋሕር** ፤ (**ትግ ፡ ገሕር ። ዕብ ፡ ጊሖር** ፤ **ፍጹም ፡ ቀይ**) ፤ ፍሕም ፡ ፍም ፤ የእሳት ፡ ምርት ፤ የበሰለ ፡ ዕንጨት ፤ ብስል ፡ በርበሬ ፡ የሚመስል ።

**ጕጥ** ፤ **ጕጥ** ፤ በቁሙ ፤ ዐባጣ ፡ ሸካራ ፤ የምድር ፡ የመሬት ፤ የበትር ፡ የንጨት ፤ ለእጅም ፡ ይኾናል ። እጀ ፡ ጉጥ ፡ አወጣ ፡ ቁንዲሉ ።

**ጕጥይ** ፤ **ዮት** ፤ (**ጕጠየ ፡ ይጕጢ ፡ ይጕጢ**) ፤ መጓጐጥ ፡ መጐጥጐጥ ፤ መሠቀሠቅ ፤ መቈፈር ፡ መሰርሰር ፤ መውጋት ፡ መትከል ። ማጣበቅ ፡ መቈንጠጥ ፤ አጣብቆ ፡ መያዝ ።

**ጕጣዪ** ፤ (**ዪት ፡ ይያን ፡ ያት**) ፤ የሚወጋ ፡ የሚጓጕጥ ፤ የሚያጣብቅ ፡ የሚቈንጥጥ ።

**ምጕጣይ** ፤ (**ያት**) ፤ መውጊያ ፡ መጓጕጫ ፤ መቈንጠጫ ፤ አሸሙር ፡ ቾንካር ፡ አርቃቆ ። ይብእስከ ፡ ረገፅ ፡ ውስተ ፡ ቀኖት ፡ ባለው ፤ ጽኑዕ ፡ ለከ ፡ ምጕጣይ ፡ ወተረግፆ ፡ እንዲል ፡ (ግብ፳፮ ፡ ፲፬) ።

**ጕጠት** ፤ (**ታት**) ፤ በቁሙ ፤ መቈንጠጫ ፤ አጥብቆ ፡ አጣብቆ ፡ መያዣ ፤ እንደ ፡ መቀስ ፡ ፪ ፡ ጣት ፡ ያለው ። ፍሕም ፡ ዘነሥአ ፡ በጕጠት ። መጠዋ ፡ በጕጠተ ፡ እሳት ፡ እምሥጋሁ ፡ ወደሙ ፡ ለክርስቶስ ። ወ



ጕጠት ፤

ደዮ ፡ አፍሓመ ፡ እሳት ፡ ዲበ ፡ እደዊሁ ፡ ወአኀዝዎ ፡ በጕጠት ፡ ብዙኀ ፡ ጊዜ ። ወጕጠታቲሃ ፡ (ኢሳ፮ ፡ ፮ ። ስንክ ፡ ነሐ፲፭ ። ታኅ፳፱ ። ዘኊ፬ ፡ ፱) ።

—፤ ሹካ ፡ ሜንጦ ፡ መጕሥሥ ፤ የሥጋ ፤ ማውጫ ፡ የወጣውን ፡ እየወጉ ፡ ማንሻ ፤ እንደ ፡ መንሽ ፡ ፫ ፡ ፬ ፡ ጣት ፡ ያለው ። ጕጠት ፡ ዘሠላስ ፡ ከተማት ። ጕጠታተ ፡ ሥጋ ፡ (ፊልክ ፡ ፭ ። ፩ዜና ፡ ፳፰ ፡ ፲፯ ። ፪ዜና ፡ ፬ ፡ ፲፩) ።

**ጕይ** ፤ **ዕብ ፡ ጎይ** ፤ ሕዝብ ፤ ያንድ ፡ አገርና ፡ ያንድ ፡ መንግሥት ፡ ሰው ፡ ቋንቋውና ፡ ሕጉ ፡ አንድ ፡ የኾነ ። ሲያበዛ ፡ ጎይም ፡ ይላል ፤ አሕዛብ ፡ ማለት ፡ ነው ፤ ጕይይ ፡ ጕየ ፡ ማለት ፡ ከዚህ ፡ ሥር ፡ ወጥቷል ።

**ገይብ** ፤ (**ዐረ ፡ ጀይብ**) ፤ ጀብ ፡ ኪስ ፤ የጀይብን ፡ ፍቹ ፡ ተመልከት ።

**ገይብ** ፤ (**ዕብ ፡ ጋቢያዕ ። ዐረ ፡ ጣስ**) ፤ ኮራ ፡ ታላቅ ፡ ጽዋ ፡ ረዥም ፡ እግሩም ፤ እንደ ፡ ጕሽ ፡ ዋንጫ ፡ በስተላይ ፡ ሰፊ ፡ ለቃቃ ፤ በስተታች ፡ ጠባብ ፡ ሽልቋቋ ፤ ውሃ ፡ አንጥፈው ፡ ያበባ ፡ ችቦ ፡ የሚያኖሩበት ፤ ወይን ፡ ቀድተው ፡ የሚጠጡበት ። ገይበ ፡ ብሩር ፡ ዘቦቱ ፡ ይሰቲ ፡ እግዚእየ ። ኦ ፡ ገይብ ፡ ወርቅ ፡ ምቅዳሐ ፡ ስብሐት ፡ (ዘፍ፵፬ ፡ ፭ ፡ ፮ ፡ ፲ ፡ ፲፯ ። አርጋ) ። ባለብሉዮች ፡ ግን ፡ አንኮላ ፡ ሸክና ፡ ዐቦሬ ፡ ሸልም ፡ ኈባያ ፡ ኩቦ ፡ ይሉታል ።

**ጌግዮ** ፤ **ዮት** ፤ (**ጌገየ ፡ ይጌጊ ። ጎገወ**) ፤ መስተት ፡ መሳሳት ፤ ከመንገድ ፡ መውጣት ፤ በስሕተት ፡ መበደል ፤ ኀጢአት ፡ መሥራት ። ዮጊ ፡ እጌጊ ፡ እስመ ፡ እንተ ፡ ፍኖተ ፡ ደብር ፡ መጻእኩ ። ይጌግዩ ፡ ዙሉ ፡ ሥርዐተ ፡ ዘዓመታት ። ጌገዩ ፡ በስካር ። አበሱ ፡ ወጌገዩ ፡ (ሉእ ፡ ባሮ ። ኩፋ ፡ ፯ ። ሚራ፵፰ ፡ ፯) ።

**ጌጋዪ** ፤ (**ዪት ፡ ይያን ፡ ያት**) ፤ የሚስት ፡ የሚሳሳት ፡ ተሳሳች ፤ አጥፊ ፡ በዳይ ።

**ጊጉይ** ፤ (**ያን ፡ ያት ፡ ጊት**) ፤ የሳተ ፡ ስሑት ፤ አላዋቂ ፤ በደለኛ ፡ ኃጥእ ። ብእሲ ፡ አብድ ፡ ወጊጉይ ። ጊጉይ ፡ ውእቱ ። ምስለ ፡ ጊጉያን ፡ ተኈለቈ ፡ (ሚራ ፲፯ ፡ ፳፫ ። ፲፱ ፡ ፪ ። ቅዳ ፡ ዮሐ) ።

**ጌጋይ** ፤ (**ያት**) ፤ ስሕተት ፤ በደል ፡ ወንጀል ፤ ኀጢአት ፡ ክፋት ። ዐስበ ፡ ጌጋይ ። ምንት ፡ ጌጋይየ ። ኢይመውቱ ፡ አበው ፡ በጌጋየ ፡ ውሉዶሙ ። መጽሐፈ ፡ ጌጋዩ ። በጌጋየ ፡ ልቦሙ ፡ (ይሁ ፡ ፲፩ ። ኤር፲፯ ፡ ፲ ። ፱ነገ ፡ ፲፱ ፡ ፯ ። ማር፲፭ ፡ ፳፰ ። ኤር፳፫ ፡ ፲፯) ።

**አጌገየ** ፤ አሳተ ፤ ኀጢአት ፡ አሠራ ። ያስሕት ፡ ወያጌጊ ፡ (ቴቶ፫ ፡ ፲፱) ።

**አንጌገየ** ፤ (**አንጎገወ**) ፤ አዞረ ፡ አባከነ ፡ አቅበዘበዘ ። ዞረ ፡ ባከነ ፡ ተቅበዘበዘ ። ታንጌጊ ፡ በገዳም ። እንዘ ፡ እንጊጊ ፡ ውስተ ፡ መራዕይ ። አንጌገዩ ፡ ውስተ ፡ አድባር ። አንጌገዩ ፡ ፍኖተ ፡ በዳ ። ኢያንጌግዩ ፡ ሰፈ ፡ ወሰፈ ፡ ከመ ፡ ሐመር ፡ ዘይዘብጥዋ ፡ መዋግድ ፡ (ኩፋ ፡ ፲፯ ። ማሕ፩ ፡ ፯ ። ዲድ ፡ ፲፪ ። ስንክ ፡ ጥር፴ ። ቀሌ) ።

**አንጊጉይ** ፤ የባከነ ፡ ብኩን ፡ ብክንክን ፡ በክና ፤ እንቡዝ ፡ ቅብዝብዝ ።

**እንጌግይ፤ (ያት)፤** ብክንት፡ ዙረት፤ እንባዜ፡ ቅብዝብዝታ፤ ቅብዝብዝነት። ጸሎት፡ ዘእንበለ፡ ፀርፀት፡ ወኢእንጌግይ፡ (ፊልክ፡ ፩። ፲፫)።

**ገዪድ፤ ዶት፤ (ጌደ፡ ይገይድ፡ ይጊድ። ዐረ፡ ጀይድ፤ ጃደ፤ በረታ)፤** መፍጠን፡ መሮጥ፡ መፈርጠጥ፡ መበርታት።

(ጥይ) **ገይድ፤ (ዳን)፤** ቅጽል። ብርቱ፡ ጮሌ፡ ፈጣን፤ ሯጭ፡ ፈርጣጭ። ፈረስ፡ ገይድ፡ ከመ፡ ዐርክ፡ ኄር። ወገይዳን፡ ከመ፡ እንተ፡ ወይጠል፡ (ሢራ፴፮፡ ፮። ፩ዜና፡ ፲፪፡ ፰)።

**አስተጋየደ፤** አፋጠነ፡ አሯሯጠ፡ (ሽምጥ፡ አስጋለበ)። አስተጋይድ፡ ፈረስከ፡ (ደራሲ)።

**ጐይይ፤ ዮት፤ (ጐየ፤ ጐየየ፡ ይጐይይ፡ ይጕየይ። ዕብ፡ ኀይ፤ ሕዝብ)፤** መሸሽ፡ መኰብለል። መራቅ፡ መሰደድ፤ ካሉበት፡ ከነበሩበት፡ መጥፋት፡ መታጣት፤ ወደ፡ ሌላ፡ ሕዝብ፡ መኼድ፡ መጠጋት፤ ሕግን፡ ባንዲራን፡ መለወጥ፤ ሌላ፡ ሕዝብ፡ መኾን፡ መባል። ፈለስን፡ እይ፤ የዚህ፡ ጎር፡ ነው። ጐየ፡ እምገጸ፡ ዔሳው። ከመ፡ ዘይጐይይ፡ እምአርዌ፡ እኩይ፡ ከማሁ፡ ጐየይ፡ እምኀጢአት። ጕዩ፡ እማእከለ፡ ባቢሎን። ወአይቴ፡ እጐይይ፡ እምቅድመ፡ ገጽከ። ጐየይ፡ ብሔረ፡ ግብጽ፡ (ኩፋ፡ ፴፩። ሢራ፳፩፡ ፪። ኤር፳፰፡ ፮። መዝ፡ ፻፴፰። ማቴ፪፡ ፲፫። ፲፡ ፳፫)።

**ጐያዪ፤ (ዪት፡ ይያን፡ ያት፤ የይት)፤** የሚሸሽ፡ ሸሽታ፤ ኰብላይ፤ ፈሪ፡ ደንባሪ፤ ሯጭ፡ ፈርጣጭ፤ ዐመለኛ። ጐያዪ፡ ከዊኖ። ብእሲ፡ ጐያዪ። እንስሳ፡ ጐያዪ፡ (ቄር። ፈ፡ መ፡ ፳፫፡ ፩። ፍ፡ ነ፡ ፴፫፡ ፫። ፵)።

**ጕዩይ፤ (ያን፡ ያት፡ ይይት)፤** የሸሸ፡ የራቀ፤ የኰበለለ። ተረክቡ፡ ጕዩያኒ፡ እምሥርዐተ፡ መላእክት፡ (አዋል)።

**ጕየት፤** መሸሽ፡ መኰብለል፤ ሽሽት፡ ኵብለላ፡ ስደት፤ ሩጫ፡ ፍርጠጣ። ይጼዕሉ፡ ጕየቶ፡ እለ፡ ኢየአምኑ፡ ትስብእቶ። ነጽር፡ ከመ፡ ጕየተ፡ ሕፃን፡ አጕየዮ፡ ለዲያብሎስ፡ (ተረ፡ ቄር፲)።

**ጕያ፤** ዝኒ፡ ከማሁ፤ ሽሽት፡ ስደት፡ ኵብለላ፡ (ማቴ፳፬፡ ፳። ኢሳ፶፪፡ ፲፪)። ይከውን፡ ዐቢይ፡ ምንዳቤ፡ ወጕያ፡ ወክዕወተ፡ ደም። ዑቁ፡ በሰንበት፡ ኢይኩን፡ ጕያክሙ። ጕያከ፡ እምቤተ፡ ልሔም፡ ደብረ፡ ቍስቋም፡ (ኪዳ። ድጓ። አዋል)።

**ጕያ፤** በቁሙ፤ የጭንና፡ የጭን፡ መካከል፤ የሕፃን፡ መሸሻ፡ መደበቂያ። የናት፡ ጕያ፡ እንዲሉ።

**ኀያ፤** በቁሙ፤ የታወቀ፡ ያበባ፡ እኽል፤ እግርን፡ ከጕልበት፡ በታች፡ የሚሰብር፡ የሚያወጣምድ፤ የሚያስነክስ፡ የሚያሽመደምድ። (ተረት)፤ አህያና፡ ኀያ፡ ባምሳያ።

**አጕየየ፤ (ገባሪና፡ አግባሪ)፤** አሸሸ፤ አራቀ። (ጥሸ) አሸሸ፡ አሰደደ፤ አሳደደ፡ አባረረ። እመ፡ ንእሱ፡ አጕየየቶ፡ እሙ፡ እስከ፡ ምድረ፡ ግብፅ። ኢትንሥኡ፡ ቤዛ፡ ከመ፡ ታጕይይዎ፡ ውስተ፡ ሀገረ፡ ምስካይ። እቁም፡ ላዕሌሁ፡ ወአጕይዮሙ፡ ለሕዝብ፡ እለ፡ ምስሌሁ። አጕየዮ፡ ለንዋም። ወአጕየዮሙ፡ ከመ፡ ሩጸተ፡ ሀየል፡ (አፈ፡ ድ፳፰። ዘኍ፴፭፡ ፴፪። ፪ነገ፡ ፲፯፡ ፪። ስንክ፡ የካ፳፩። መጽ፡ ምስ)።

**አጕያዪ፤ መጕይይ፤** የሚያሸሽ፡ የሚያርቅ፤ የሚያስርቅ።

**ምጕያይ፤ (ያት)፤** መሸሻ፡ መጠጊያ፤ መማጠኛ፡ የሙጥኝ፡ መባያ። ምጕያየ፡ ለግሔ። ኮንከኒ፡ ምጕያየ፡ (መዝ፡ ፸፫። ኪዳ)። ጕያ፡ ጕየት፡ በማለት፡ ፈንታ፡ ምጕያይ፡ ይላል፡ (ናሖ፫፡ ፱)።

**ገዪም፤ ሞት፤ (ጌመ፡ ይገይም፡ ይጊም። ዐረ፡ ዓመ)፤** መጎም፡ መዳመን፤ ደመና፡ መልበስ፡ በጉም፡ መታፈን፡ መሸፈን፤ መጮኽ፡ ማስገምገም፤ ማስተጋባት፤ የሰማይና፡ የተራራ። ገመገም፡ ማለት፡ የዚህ፡ ዘር፡ ነው፤ ጐሀነን፡ እይ።

**ጊሜ፤ (ዐረ፡ ዐይም። ሱር፤ ዓይማ)፤** ጉም፡ ብዙ፡ ደመና፤ ከምድር፡ ወርዶ፡ ተራራ፡ ኰረብታ፡ የሚሸፍን፤ ወዠድ፡ ለወዠድ፡ የሚጐትት፡ የቀን፡ ጨለማ። ከመ፡ ጊሜ፡ ከደንክዋ፡ ለምድር። ወረሰየ፡ ላቲ፡ ደመና፡ ልብሳ፡ ወበጊሜ፡ ጠብለላ። ወከደነ፡ ርእሰ፡ ደብር፡ በጊሜ፡ ወጢስ፡ (ሢራ፵፱፡ ፫። ኢዮ፴፰፡ ፱። ውዳ፡ ማርያ)።

—፤ ብትን፡ በረዶ፤ ውርጭ፤ ጠል፡ ከፊያ። በረድ፡ ወጊሜ። ይዘርዎ፡ ለጊሜ፡ ከመ፡ ሐመድ። ከመ፡ ጊሜ፡ ውስተ፡ ፀምር። ወፈውሰ፡ ሖሉ፡ ፍጡነ፡ ጊሜ፡ (ዳን፫፡ ፵፱። መዝ፡ ፻፵፯። ዘዳ፴፪፡ ፪። ሢራ፵፫፡ ፳፪)።

**ጉማ፤** ታላቅ፡ ጩኸት፤ ጕህና፡ ተመማ፤ የብዙ፡ ሰው፡ ዜማ። ገብርኤል፡ ዘራማ፡ አዕራጊ፡ ስብሐት፡ በጉማ። ጉማ፡ ቃሎሙ፡ ሐዋዝ፡ ወጥዑም። ይመልእ፡ ሖሎ፡ ቤተ፡ ዕበየ፡ ጉማ፡ ቃሎሙ፡ (ደራሲ። ሢራ፵፯፡ ፱። ፶፡ ፲፰)። በቁሙ፤ የነፍስ፡ ዋጋ፤ ያውም፡ የቀንድ፡ ከብት፡ የገዳይ፡ ወገን፡ ቀንበር፡ ተሸክሞ፡ እግዚኦ፡ እያለ፡ ለሟች፡ ወገን፡ የሚሰጠው፡ ካሳ። ገመገመ፡ ግምጋሚ፡ ማለት፡ ከጉማ፡ የወጣ፡ ቃል፡ ነው፤ ርኀራኄና፡ ለውጥ፡ ያሳያል።

**ጉምጉማ፤ (ትግ፡ ሐበ)፤** ርኩም፤ አፈ፡ ረዥም፡ ክንፈ፡ ውዥምዥም፡ ድምጡ፡ እንደ፡ ከበሮ፡ የሚተም፤ እንደ፡ ነጋሪት፡ የሚጐሰም፤ እንደ፡ ሰማይ፡ የሚያስገመግም።

**ግዮን፤ (ጽር፡ ጌዖን። ዕብ፡ ጊሖን)፤** ስመ፡ ፈለግ፤ ካራቱ፡ ዐበይት፡ አፍላጋት፡ ኹለተኛው፡ ወንዝ፡ ነጭ፡ አባይ፤ ከአፍሪቃ፡ ደቡብ፡ ተነሥቶ፡ ወደ፡ ሰሜን፡ ወደ፡ ሱዳን፡ አገር፡ የሚፈስ፡ (ዘፍ፪፡ ፲፫)። ነቁን፡ ባለጂዖግራፎች፡ ፮፡ ያኽል፡ ነው፡ ይሉታል፤ ውሃው፡ ነጭ፡ ኒል፡ ስለ፡ መሰለ፡ ነጭ፡ አባይ፡ ይባላል፤ የአባይን፡ ፍች፡ ተመልከት። ጊሖን፡ ማለት፡ ግን፤ ዘየ

ሐውር ፡ በኀይል ፡ ወይርዕም ፡ ወድምፀ ፡ ማዩ ፡ ዐቢይ ፡ ወግሩም ፡ ማለት ፡ ነው ፤ የውሃውን ፡ ብዛት ፡ የመልካውን ፡ ስፋት ፤ ያከኼዱን ፡ ኀይል ፡ የጩኸቱን ፡ ግርማ ፡ ፏፏቴውንና ፡ ተመማውን ፡ ድምጡ ፡ እንደ ፡ ነጐድጓድ ፡ መኾኑን ፡ ያሳያል ። ከአፍሪቃ ፡ ወንዞች ፡ ተለይተው ፡ ነጭ ፡ ኒል ፡ ጥቍር ፡ ኒል ፡ የሚመስሉ ፡ በኦሪትም ፡ ግዮን ፡ ኤፌሶን ፡ የሚባሉ ፡ ነጭ ፡ አባይና ፡ ጥቍር ፡ አባይ ፡ ናቸው ፡ ይባላል ። እሊህም ፡ ኹለቱ ፡ ወንድማማች ፡ ወንዞች ፤ ከየምንጮቻቸው ፡ በኀይል ፡ ተነሥተው ፡ ግርማቸውን ፡ ለብሰው ፤ ተስልፈው ፤ በየፊታቸው ፡ ያለውን ፡ ሐይቅ ፡ እንደ ፡ መርከብ ፡ ሠንጥቀው ፡ ዐልፈው ፡ ስራዊታቸውን ፡ ከግራና ፡ ከቀኝ ፡ አሰከትተው ፤ እንደ ፡ ኹለት ፡ ንጉሥ ፡ ከርቱም ፡ ሲገናኙ ፡ ኹለትነታቸው ፡ ይቀርና ፡ አንድ ፡ ወንዝ ፡ ብቻ ፡ ይኾናሉ ፤ ከከርቱም ፡ ደግሞ ፡ እስከትበራ ፡ ወርደው ፡ ከተከዚ ፡ ጋራ ፡ ይገጥማሉ ። ከዚያ ፡ በኋላ ፡ ግን ፡ የሌላ ፡ ወንዝ ፡ ውሃ ፡ ሳይጨምሩ ፡ ባንድነት ፡ መላ ፡ ምድረ ፡ ግብጽን ፡ ከላይ ፡ እስከ ፡ ታች ፡ አጠጥተው ፡ አጥግበው ፡ አርክተው ፤ ዐልፈው ፡ ተርፈው ፡ ወደ ፡ ሰሜን ፡ ጐርፈው ፡ ሜዲተራኒ ፡ ከሚባለው ፡ ከታላቁ ፡ ባሕር ፡ ይገባሉ ።

**ግዮን** ፤ የየሩሳሌም ፡ ወንዝ ፤ ሰሊሖም ፡ ሰሎሞን ፡ የነገሠበት ፤ ከከተማዪቱ ፡ በስተደቡብ ፡ ያለ ፡ (፩ነገ ፡ ፩ ፡ ፴፫ ። ኢሳ፰ ፡ ፮) ።

**ገዪሥ ፤ ሦት ፤ (ጌሠ ፡ ይገይሥ ፡ ይጊሥ ። ዕብ ፡ ጋየስ ፤ ሰበሰበ)** ። (ጥሰ) መሰብሰብ ፡ መከተት ፤ መሰለፍ ፡ ሰጠር ፡ ለመንገድ ፡ መዘጋጀት ፤ ከዚህ ፡ በኋላ ፡ መገዝመት ፡ መገሥገሥ ፤ ማልደ ፡ መኼድ ፡ ከንግሀ ፡ አስቀድሞ ፡ ጎሕ ፡ ሲቀድ ፡ ወይም ፡ ዶሮ ፡ ሲጮኽ ፡ መነሣት ። ገዩሠክሙ ፡ በጽባሕ ። አሌሲያ ፡ ገዩሠ ። በሌሊት ፡ ትገይሥ ፡ መንፈስየ ፡ ኀቤከ ። ነቂሀነ ፡ እምንዋም ፡ ንጊሣ ፡ ሰቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ (ዘፀ ፲፱ ፡ ፲፯ ። ሉቃ፳፬ ፡ ፩ ። ኢሳ፳፮ ፡ ፱ ። ድጓ) ። ገሥገሠን ፡ እይ ፤ የዚህ ፡ ድርብ ፡ ነው ።

**ገያሢ ፤ (ሢት ፡ ሥያን ፡ ያት)** ፤ የሚገሠግሥ ፡ ገሥጋሽ ፤ ማላጅ ፡ ማለዳ ፡ ኺያጅ ። (ተረት) ፤ ገበያ ፡ ላርፋጅ ፤ ቤት ፡ ከሲያን ፡ ለማላጅ ።

**ጋይሥ ፤ (ብ ፡ አጋይሥ)** ፤ ዝኒ ፡ ከማሁ ፤ እንግዳ ፡ መንገደኛ ፤ ዐድሮ ፡ ኺያጅ ፡ ገሥጋሽ ፡ (ትግሬ) ።

**ጊሠት** ፤ መገሥገሥ ፤ አገሣገሥ ፡ ገሥጋሽነት ፡ ግሥገሣ ፡ ማለዳ ።

**አጌሠ** ፤ አገሠገሠ ፤ አስገሠገሠ ፤ አማለደ ፡ አስማለደ ፤ ማለዳ ፡ ወሰደ ። አመ ፡ ያገይሥዋ ፡ ለታቦት ፡ ካህናት ፡ አግብእዋ ፡ ውስተ ፡ መካና ። እስከ ፡ አመ ፡ ያገይሥዎ ፡ ኀበ ፡ እስራኤል ። ኢርኩስ ፡ ኀሪስኪ ፤ ለምንትኬ ፡ አጌሥኪዮ ፡ ለፍሬ ፡ ቅድሳት ፡ ውስተ ፡ ቤተ ፡ መቅደስ ፡ (ድጓ ። ሉቃ፩ ፡ ፹ ። መጽ ፡ ምስ) ።

**ጌሠም ፤ (ዕብ ፡ ጌሸም ፤ ብርቱ ፡ ዝናም)** ፤ ነገ ፤ ጢት ፡ ማለዳ ፤ ከርሞ ፡ ላመት ። እስከ ፡ ጌሠም ። ጌሠመ ፡ ዘ ፡ ጊዜ ። ጌሠመ ፡ ንመውት ። አነ ፡ ዮም ፡ ወአንተ ፡ ጌሠም ። ኢትተክዝ ፡ ለጌሠም ፡ እስመ ፡ ጌሠምሰ ፡ ትኄሊ ፡ ለርእሳ ፡ (፩ነገ ፡ ፳ ፡ ፲፩ ። ዘፀ፱ ፡ ፲፰ ። ሚሬ፲ ፡ ፲ ። ፴፰ ፡ ፳፱ ። ማቴ፮ ፡ ፴፬) ። ጌሠም ፡ እንደ ፡ ዮምና ፡ እንደ ፡ ትማልም ፡ ጐልት ፡ ነው ፤ አይፈልስም ፤ መጽሐፍ ፡ ግን ፡ ጌሠመ ፡ ይላል ፤ አያሰኝም ።

**ጋይጸ ፤ ጸት ፤ (ጋየጸ ፡ ይጋይጽ ። ግእዝ)** ፤ መንቀፍ ፡ መስደብ ፡ መገደር ፤ መናቅ ፡ ማጥቃት ፤ ማስጨነቅ ፡ ማስቸገር ። ማጌጥ ፡ መጌጥ ፤ መልበስ ፡ መሸለም ፤ መፀረር ፡ ማማገር ፤ ከዚህ ፡ የተነሣ ፡ መኰራት ፡ መታበይ ። መጽሐፍ ፡ ግን ፡ በጋየጸ ፡ ፈንታ ፡ ተጋየጸ ፡ ይላል ፤ አያሰኝም ። እጸልእ ፡ ጸላኢከ ፡ ወእትጋየጽ ፡ ዘይትጋየጸከ ። ይትጋየጽ ፡ ጎረ ፡ ቤቱ ፡ (ዘፀ፳፫ ፡ ፳፱ ። ኢዮ፳ ፡ ፳፮) ። አይቴ ፡ ሀለዉ ፡ እለ ፡ ይትጋየጹ ፡ በሥን ፡ ወበላሕይ ። ኢርቱዕ ፡ ንትዐበይ ፡ ወንትጋየጽ ፡ በምንትኒ ፡ እምግብር ፡ (ግንዘ ። አፈ ፡ ተ፱) ።

**ተጋየጸ ፤ (ተደራጊና ፡ ተደራራጊ)** ፤ ተነቀፈ ፤ ተናቀ ። ተነቃቀፈ ፡ ተናናቀ ፡ ተገዳደረ ። ተጊያጊያጠ ፡ ተሸላለመ ። ርስ ፡ በርስ ፡ ወይም ፡ በገዛ ፡ እጅ ።

**ጋይጽ ፤ ጌጽ** ፤ ጌጥ ፡ ሽልማት ፤ ልብስ ፡ መሣሪያ ።

**ጕየጸ ፤ (የጌገየና ፡ የጕየ ፡ ጎር)** ፤ ሳተ ፡ ለቀቀ ፤ የሕፃን ፡ የድውይ ። ሸሸ ፡ አመለጠ ፤ ያይን ፡ ምድር ፡ የፈስ ፤ ሬሳ ፡ ሸሸ ፡ እንዲሉ ። ፈሰውን ፡ ተመልከት ።

**ገይሮ ፤ ሮት ፤ (ገየረ ፡ ይጌይር ፡ ይገይር ። ዕብ ፡ ጋየር)** ፤ በፍቅር ፡ በትምርት ፡ መሳብ ፡ ማቅረብ ፡ ማስጠጋት ፤ አሕዛብን ፡ ከጣዖት ፡ ማፍለስ ፡ በኦሪት ፡ ማሳመን ፤ መግዘር ፡ ይሁዲ ፡ ማድረግ ።

—፤ ኖራ ፡ ማውጣት ፤ በኖራ ፡ ጭቃ ፡ መምረግ ፡ መለሰን ፡ መቅባት ፡ መለቅለቅ ። ገብሰስን ፡ እይ ። እሰ ፡ ገየርዋ ፡ ለአረፍት ። ከመ ፡ አረፍት ፡ እንተ ፡ ገየሩ ፡ (ሕዝ፲፫ ፡ ፲፩ ። ኢሳ፲፯ ፡ ፲፩) ።

**ገያሪ ፤ መገይር ፤ (ርት ፡ ራን ፡ ራት)** ፤ አቅራቢ ፡ አስጠጊ ፤ ይሁዲ ፡ አድራጊ ። ኖራ ፡ አውጭ ፡ ሸያጭ ፤ ለሳኝ ፡ ቀቢ ፡ ለቅላቂ ። ለመገይራን ፡ ወለወቀርት ፡ እብን ፡ (፬ነገ ፡ ፲፪ ፡ ፲፪) ።

**ጊር ፤ (ዕብራ ። ዐረ ፡ ጀይር)** ፤ ዐዲስ ፡ ትኩስ ፡ ኖራ ፡ ውሃ ፡ ያልነካው ፡ እሳቱ ፡ ያልጠፋ ፡ ያልበረደ ።

**ተገየረ ፤ (ዕብ ፡ ሂትጋየር)** ፤ ወደ ፡ አይሁድ ፡ መጣ ፡ ተጠጋ ፤ ይሁዲ ፡ ኾነ ፡ በኦሪት ፡ አመነ ፤ የሀደንና ፡ ተይሀደን ፡ እይ ። ተለሰነ ፡ ተቀባ ፤ ተለቀለቀ ።

**ግዩር ፤ (ዕብ ፡ ጌር ። ሱር ፡ ጊዮራ)** ፤ መጤ ፡ መጣተኛ ፡ ስደተኛ ፤ ካገሩ ፡ ከሕጉ ፡ የፈለሰ ፡ ፈላሻ ፡ የአይሁድ ፡ ጥገኛ ፤ በኦሪት ፡ ያመነ ፡ ግዙር ። አሐዱ ፡ ሕግ ፡ ይኩን ፡ ለክሙ ፡ ወለግዩር ፡ ዘማእከሌክሙ ። ግዩራን ፡ ወፈላስያን ፡ (ዘፀ፲፪ ፡ ፵፱ ። ዘሌ፳፭ ፡ ፳፫) ።

—፤ የተለሰነ ፡ ልስን ፤ ቅብ ፡ ልቅልቅ ።

**ግያሬ፤** ኖራ ፡ አወጣጥ ፡ አለሳሰን ፤ ልስና ፡ ልቅስቃ ።

**ግይርና ፤** ስደት ፤ ስደተኛነት ፡ ፈላሽነት ፡ (አርጋ) ።

**ጌራ፤ (ብ ፡ ጌራት) ፤** ቍርዐ ፡ ቍር ፤ ቦርቦርቲ ፡ የራስ ፡ ጋሻ ፡ ከወፍራም ፡ ቈርበት ፡ የሚሠራ ፡ ላዩ ፡ ብረት ፡ ውስጡ ፡ ቈርበት ፡ በጦርነት ፡ ጊዜ ፡ የሚለበስ ፡ (፩ተስ ፡ ፭ ፡ ፰ ። ኤፌ፮ ፡ ፲፯ ። ራእ፱ ፡ ፱ ፡ ፲፯) ። ጌራ ፤ መድኀኒት ። ጌራተ ፤ ኅጺን ፤ (ኢሳ፶፱ ፡ ፲፯ ። ስንክ ፡ ሐም፲፭) ። የራስ ፡ ጌጥ ፡ ሽልማት ፡ ራስ ፡ ወርቅ ፤ ሜትራ ፡ ዘውድ ፡ አክሊል ፡ ሾፌት ፡ ቆብ ፡ ባርኔጣ ፤ የመሰለው ፡ ኹሉ ። ክበበ ፤ ጌራ ፤ ወርቅ ፤ ጽኑይ ። ተቀጸለ ፤ ጌራ ፤ ዐቢየ ፤ ዲበ ፤ ርእሱ ፤ አሕጺጾ ፤ ጌራ ፤ ክህነት ፤ ቅዱስ ። ወገብሩ ፤ ዲበ ፤ ርእሱ ፤ ጌራ ፤ ንጉሥ ፤ ወውስተ ፤ እዴሁ ፤ በትረ ፤ ወርቅ ። ወያአትቱ ፤ ጌራቲሆሙ ፤ እምርእሶሙ ፤ (ደራሲ ። ዮሴፍ ። ሕዝ፳፮ ፡ ፲፮) ።



ጌራ ፤

**ጌራ ፤ (ዕብ ፡ ጌራህ) ፤** የገንዘብ ፡ ስም ፤ ታናሽ ፡ ግርሽ ፡ የሰቅል ፡ ኻያኛ ፤ የአቦሊ ፡ እኩያ ። ወሰቅል ፤ ዕሥራ ፤ ጌራ ፤ (ሕዝ፵፭ ፡ ፲፪) ።

**ጌርዮስ ፤ (ጽር ፡ ኪርዮስ) ፤** እግዚእ ፤ እግዚአብሔር ፡ (ቅዳ) ።

**ጌሰ ፤—ገሠገሠ ፤—ገዩ ፡ ሥ ፡ ጌሠ ።**

**ጋይሶ ፤ (ጽርእ ። ዕብ ፡ ኪዶን) ፤** ጦር ፡ ዘገር ፡ የሚወረወር ፤ ዐጭር ፡ መጠነኛ ። ባለብሉዮች ፡ ግን ፡ ላማርኛ ፡ ስለ ፡ ቀረበ ፡ ጋሻ ፡ ይሉታል ። አልዐል ፤ እዴከ ፤ በጋይሶ ፤ (ኢያ፰ ፡ ፲፰) ። ቢደንን ፡ እይ ።

**ጌተ ፤ (ይገይት ፡ ይጊት ፤ ገዩት ። ገዝአ) ።** ጌተየ ፤ ጌታ ፡ ኾነ ፡ ተባለ ።

(ጥ) **ገት ፤ (ትግሬ) ፤** ብዕል ፡ ሀብት ፤ ጌትነት ።

**ጌት ፤** ስመ ፡ ሀገር ፤ የኢሎፍሊ ፡ ክፍል ። ፈለስት ፤ ታቦተ ፤ እግዚአብሔር ፤ ውስተ ፤ ጌት ፤ (፩ነገ ፡ ፭ ፡ ፰) ። ቤት ፤ ጌትያዊ ፤ (፪ነገ ፡ ፲፰ ፡ ፪) ።

**ጋሌ ፤ (ጽር ፡ ጋሊ ። ዕብ ፡ ሔሴድ) ፤** ፋሮ ፡ ፋደት ፤ መጠማጥ ፡ የዱር ፡ ድመት ፤ ሸላ ፡ ሙጭሙጭላ ፤ ደሮ ፡ የሚያድን ፡ የሚበላ ፤ መሬት ፡ የሚፍር ፡ የሚቈፍር ፤ ታናሽ ፡ ክፉ ፡ አውሬ ። ዐይነቱና ፡ ስሙ ፡ ብዙ ፡ ነው ፤ ባለብሉዮች ፡ ግን ፡ ፪ ፡ አፍ ፡ ያለው ፡ እባብ ፡ ይሉታል ፡ (ዘሌ፲፩ ፡ ፳፱) ።

**ግላ ፤—ጨለማ ፤—ገሊው ፡ ገለወ ።**

**ጎል ፤—በረት ፤—ገዊል ፡ ጎለ ።**

**ገልእ ፤—የሸክላ ፡ ስባሪ ፤—ገሊዕ ፡ ገልዐ ።**

**ገሊብ ፤ ቦት ፤ (ገለበ ፡ ይገልብ ፡ ይግልብ ። ዐረ ፡ ጀለበ ፤ ሳበ) ፤** ማጥመድ ፤ መቃጥን ፡ መስደድ ፡ መረብ ፡ መንዛት ፤ መሳብ ፡ መጐተት ፤ መግለብ ፡ መሥራት ፤ ያሣ ፡ ወጋሪ ። እንዘ ፤ ንገልብ ፤ (ኪዳ) ። መግለብ ፡ መግለጥ ፤ የንፍረት ፡ የቂጥ ። መሸሽ ፡ መሮጥ ፤ መጋለብ ፡ ማምለጥ ፤ መዘራት ፡ መበተን ፡ መቅለል ፡ መንጓለል ፡ ፍሬ ፡ ቢስ ፡ መኾን ፤ የገለባ ።

**ገለብ ፤ መግለብ ፡ ት ፤** መቃጥን ፡ መንጠቆ ፤ መግለቢ ፡ ዘረ ፡ መትር ፡ ያሣ ፡ ወጥመድ ፡ መያዣ ፡ መጋፈፊያ ። ከመ ፤ በመግለብት ፤ ወበመዋቅሕተ ፤ ኅጺን ፤ ተሐውር ፤ (ዐር ፡ ኢሳ፫ ፡ ፮) ። ጀልባ ፡ ታንኳ ፡ ፍልኳ ፡ ዓሣ ፡ ወጋሮች ፡ የሚቀመጡበት ። አንዳንድ ፡ መጽሐፍ ፡ በገለብ ፡ ፈንታ ፡ ጌልያ ፡ ብሎ ፡ መርከብ ፡ ይላል ። ገለባ ፡ ኀፋሽ ፡ እንጕላይ ፡ (ዐማርኛ) ።

**ገለብ ፤ (ትግሬ) ፤** ጋሻ ፡ ፀጋም ፤ በግራ ፡ የሚያዝ ፡ የሚነገብ ፡ አላባሽ ፡ አግሬ ።

**ገለባት ፤** ዝማ ፡ ነጋዴ ፡ ቅፍለት ፤ ማኅበር ፡ ኹኖ ፡ አጋሰሱን ፡ ጭኖ ፡ እንደ ፡ ጕርፍ ፡ የሚኼድ ፡ የሚያረብድ ።

**አግለበ ፤** አሸሸ ፤ አባረረ ። ገለባ ፡ አወጣ ፡ አጓለበ ፤ አንጓለለ ። አስገለበ ፡ አስገለጠ ።

**አግላቢ ፤ መገልብ ፤ (ብት ፡ ባን ፡ ባት) ፤** የሚያሸሽ ፡ አባራሪ ፤ ዓሣ ፡ ወጋሪ ። መግለቢ ፡ ሠሪ ፤ ገለባ ፡ አውጭ ። መጺብሓዊ ፤ ወመገልብ ፤ (መቅ ፡ ወን) ።

**ገልበበ ፤ (ተቀ ፡ ግ ። ዐረ ፡ ጀልበበ ፤ ገለወ) ፤** ሸፈነ ፡ ከደነ ፤ አለበሰ ፡ አከናነበ ፤ ጋረደ ፤ ለበጠ ፡ መረገ ፤ ለሰነ ፡ ቀባ ። ገልበቡ ፤ ርእሶሙ ። ይገልብብ ፤ አፉሁ ። ይገለብብዎ ፤ ገጾ ። ሥብሕ ፤ ዘይገለብብ ፤ ከርሦ ። ዘይገለብቦ ፤ ለሰማይ ፤ በደመና ። ወገልበቡ ፤ ሖሎ ፤ ዘውስቴቱ ፤ እምዕፀ ፤ በነፍጥ ፤ ብዙኅ ። ገልበበታ ፤ ለንፍቅ ፤ ፒሳ ፤ (ኤር፲፱ ፡ ፱ ። ዘሌ፲፫ ፡ ፵፭ ። ሉቃ፳፱ ፡ ፳፱ ። ዘፀ፳፱ ፡ ፳፪ ። መዝ ፡ ፻፵፯ ። ዮሴፍ ። ኩፋ ፡ ፵፯) ።

**ገልባቢ ፤ መገልብብ ፤** የሚሸፍን ፤ ከዳኝ ፡ አልባሽ ፤ ጋራጅ ፡ አከናናቢ ።

**ተገልበበ ፤** ተሸፈነ ፤ ተከናነበ ፤ ተሰወረ ፡ ተደበቀ ፤ በልብስ ፡ ባለባበስ ። ተገልበበት ፤ ገጻ ። ከዳን ፤ በዘይትገለበቡ ፤ እምጣል ። አንስት ፤ ደናግል ፤ ኢይትገልበባ ፤ ርእሶን ፤ በቤተ ፤ ክር ፤ አላ ፤ ሥዕርቶን ፤ ያንጎ ። ወይቤሎ ፤ ንጉሥ ፤ እትገልበብ ፤ ወእባእ ፤ ውስተ ፤ ቀትል ፤ (ዘፍ፴፰ ፡ ፲፭ ። ኢሳ፱ ፡ ፯ ። ኪዳ ። ፫ነገ ፡ ፳፪ ፡ ፴) ።

**ግልቡብ ፤ (ባን ፡ ባት ፡ ብብት) ፤** የተሸፈነ ፤ የተከናነበ ፤ ሽፍን ፡ ሽፍንፍን ። ግልቡብ ፤ ርእሱ ። እንዘ ፤ ግልቡባን ፤ ገጾሙ ። ብእሲ ፤ ዘግልቡብ ፤

ርእሱ ። ግልቡባት ፡ (ሄኖ ፣ ፲፭ ፣ ፴ ። ሔኖ፲፫ ፣ ፱ ። ፩ቆሮ ፣ ፲፩ ፣ ፱ ። ዲድ ፣ ፫) ።

**ግልባብ ፤ ቤ ፤ (ባባት ፣ ብያት) ፤** መሸፈኛ ፣ መጋረጃ ፤ ልብስ ፣ ክዳን ፤ ክንብንብ ፣ ሠርመዲ ፣ ሻል ፤ የሐር ፣ የሻሽ ፣ መንዲል ፤ ጥላ ፣ ቀጸላ ። ክሥቲ ፡ ግልባቢክ ። ፲ሥኡ ፡ ግልባብየ ። ከሠተ ፡ ግልባበ ፡ ገጹ ። ሰብበት ፡ ግልባቤ ። ቀራንብት ፡ ሥዩማት ፡ እማንቱ ፡ ህየንተ ፡ ምስዋር ፡ ወግልባቤ ። እምሐፉረ ፡ መርቄ ፡ ወእምቍረ ፡ ዙሉ ፡ ምንዳቤ ፡ አክናፊክሙ ፡ ይኩናኒ ፡ ግልባቤ ። ግልባቡ ፡ (ኢሳ፵፯ ፣ ፪ ። ማሕ፩ ፣ ፯ ። ስንክ ፣ ሠኔ፩ ። ኩፋ ፣ ፵፩ ። ደራሲ ። ስንክ ፣ ኅዳ፲፫ ። መስ፳፩) ።

**ጐልበተ ፤ (ትግ ፣ ገልበተ ፤ ገለበጠ) ፤** በቁሙ ፤ ጐለበተ ፣ ጐልበታም ፣ ኾነ ፤ ፀየለ ፣ በረታ ፣ (ዐማርኛ) ።

**ጕልበት ፤** በቁሙ ፤ ብርክ ፣ ኀይል ፣ ብርታት ፣ ጥንካሬ ። (ግጥም ፤ ፪ ፣ ደጃዝማቾች ፣ ሲዋጉ ፣ ትቢተኛው ፣ ድል ፣ ስለ ፣ ኾነ) ፤ አሳዋቂ ፣ ስፈ ፣ ሱሪ ፣ አሳጥሮበት ፤ የደጃች ፡ እገሌ ፣ ጕልበቱ ፣ ታየበት ።

(ቀ) **ገልጎ ፤ ጎት ፤ (ገለገ ፣ ይጌልግ ፣ ይገልግ ። ዕብ ፣ ጋላግ) ፤** ማጌጥ ፣ መሸለም ፤ መልበስ ፣ መፀረር ፤ መከናወን ፣ መበጃጀትና ፣ መዘጋጀት ፤ ወደ ፣ ሸንጎ ፣ ወደ ፣ ገበያ ፣ ወደ ፣ ሰርግ ፣ ወደ ፣ ቤተ ፣ ክሲያን ፣ ለመኼድ ።

**አንገለገ ፤ (ያንጌልግ ፣ ያንገልግ) ፤** ሰበሰበ ፣ አከማቸ ፣ ጉባኤ ፣ አቆመ ። ተሰበሰበ ፣ ተከማቸ ፤ ሸንጓ ፣ ከተመ ፤ ተጠራቀመ ፤ ደለተ ፣ መከረ ። አንገለግኒ ፡ ፀቢየ ፡ እንግልጋ ። አንገለጉ ፡ ዙሉ ፡ ሕዝብ ፡ ባዕለ ፡ ኤርምያስ ። ለምንት ፡ አንገለጉ ፡ አሕዛብ ፡ (ነሐ፩ ፣ ፯ ። ኤር፴ ፣ ፱ ። መዝ ፣ ፪ ። ዘኍ፲፯ ፣ ፲፩ ። ግብ፲፭ ፣ ፯ ። ፩ቆሮ ፣ ፭ ፣ ፱) ።

**እንግልጋ ፤** መሰብሰብ ፣ መከማቸት ፤ አሰባሰብ ፣ ስብሰባ ፣ ክምችታ ፤ ክምቹነት ። ሸንጎ ፣ ጉባኤ ፣ ማኅበር ፤ ብዙ ፣ ሰው ፤ የሰው ፣ መንጋ ፣ የሚጎጋጋ ። ልቅሶኛ ፣ ሰርገኛ ፣ ገበያተኛ ፣ ቤተ ፣ ክሲያን ፣ ሳሚ ፤ የመሰለው ፣ ኹሉ ። እንግልጋ ፡ አሕዛብ ። ማእከለ ፡ ማኅበር ፡ ወእንግልጋ ። በላም ፡ ለክሙ ፡ ቅዱሳን ፡ እንግልጋ ። ምስለ ፡ ብዙኃን ፡ እንግልጋ ፤ ሀገረ ፡ ዳዊት ፡ ማርያም ፡ ዐሪጋ ፡ (ሚራ፳፯ ፣ ፳ ። ምሳ፭ ፣ ፲፬ ። ስንክ ፣ መስ፫ ፣ ታኅ፳፰) ።

**ምንግላግ ፤ (ጋት) ፤** መሰብሰቢያ ፣ መከማቻ ፤ ቦታ ። ምንግላጊሆሙ ፡ ለኢሎፍሊ ፡ (፩ነገ ፣ ፲ ፣ ፩ ። ዮዲ፯ ፣ ፲፯) ።

**ገልገለ ፤ (ገሊል ፣ ገል) ፤** ገለገለ ፣ ገላገለ ፤ ለየ ፣ ነጠለ ፣ አላቀቀ ፤ የሰው ። ዘረገፈ ፣ ቀዳ ፣ ገለበጠ ፤ አጋባ ፣ ባዶ ፣ አደረገ ፤ የዕቃ ። ወገልገልዋ ፡ ለሙዳየ ፡ ምጽዋት ፡ (፪ዜና ፣ ፳፬ ፣ ፲፩) ።

**ገልጋሊ ፤** ገልጋይ ፣ ገላጋይ ፤ ዘርጋፊ ፣ ዘራፊ ፤ ወራሪ ፣ በርባሪ ።

**አገልገለ ፤ (ዐማርኛ) ፤** በቁሙ ። አገልግል ፣ ግልጋሎ ፣ ጕልጓሎ ፣ ማለት ፣ ከዚህ ፣ ወጥቷል ።

**ተገልገለ ፤ (ዕብ ፣ ጋላሀ) ፤** ተማረከ ፣ ተዘረፈ ፤ ተበረበረ ። እስመ ፡ ገልገላ ፡ ተገልግሎ ፡ ትትገለገል ፡ (ዓሞ፭ ፣ ፭) ። ተዔውዎ ፣ ትዔወው ፤ ፈሊስ ፣ ትፈልስ ፤ ጠፊአ ፣ ትጠፍእ ፣ ማለት ፣ ነው ።

**ገልገላ ፤ ዕብ ፣ (ጊልጋል) ፤** ስመ ፣ ሀገር ፤ መንኰራኵራት ፣ ማለት ፣ ነው ። እሊሁም ፣ በይሁዳ ፣ ክፍል ፣ ያሉ ፣ ፪ ፣ አህጉር ፣ ናቸው ፤ አንዲቱ ፣ የኢያሪሖ ፣ ቅርብ ፣ አጠገብ ፣ (ኢያ፭ ፣ ፱ ። ፩ነገ ፣ ፯ ፣ ፲፮) ። ፪ኛይቱ ፣ በኬብሮን ፣ ያለች ፣ (ዘዳ፲፭ ፣ ፴ ። ኢያ፲፪ ፣ ፳፫) ።

**ጌልጌል ፤ ጌልጌላ ፤ (ዕብ ፣ ጋልጌል ፣ ጋልጋል) ፤** ዝኒ ፣ ከማሁ ፤ መንኰራኵሮች ፣ የሠረገላ ፣ እግሮች ፣ ተሽከርካሮች ፣ ተንከባላዮች ፣ (ሕዝ፲ ፣ ፪ ፣ ፲፫) ። ባለቅኔዎች ፣ ግን ፣ ሰማይ ፣ ይሉታል ። ደመና ፡ ሰማይ ፡ ብርሀት ፡ እንተ ፡ ይብልዋ ፡ ጌልጌላ ፡ (ደራሲ) ።

**ጐልጐታ ፤—ጎልጎታ ፤—ገዊል ፣ ጎለ ፤ ጎል ።**

(ቀ) **ገልዶ ፤ ዶት ፤ (ገለደ ፣ ይጌልድ ፣ ይገልድ ። ዕብ ፣ ጋላድ ፤ ገልድ ፣ ለበሰ) ፤** መደጕስ ፤ ቍርበት ፣ ማልበስ ። ማንጠፍ ፤ መከፈፍ ፤ ፀልጋን ፣ መኝታን ፣ በዠንዲ ፣ በንት ፣ ወይም ፣ በስርፍ ፣ በሌሐፍ ፣ መሸፈን ፣ ማስጌጥ ። በቀጠንት ፡ ገሊድኩ ፡ ምስካብየ ፡ ወዘርቤታተ ፡ ነጸፍኩ ፡ (ምሳ፯ ፣ ፲፯ ። ዲድ ፣ ፪) ።

**ገላዲ ፤ መገልድ ፤ (ዲት ፣ ዳን ፣ ዳት) ፤** የሚደጕስ ፣ ደጓሽ ፤ ቍርበት ፣ አልባሽ ፤ አንጣፊ ።

**ገልድ ፤ (ዕብ ፣ ጌሌድ ። ፀረ ፣ ጊልድ ። ሱር ፣ ጌልዳ) ፤** ቍዳ ፣ ቍርበት ፤ ዠንዲ ፣ ንት ፤ ፀጥፍ ፣ ዳባ ፤ ሌጦ ፣ አንቀልባ ፤ የባሕር ፣ ዐረብ ፤ ብራና ፣ ቅርፍት ፣ ዕፅ ።

**ገለድ ፤ (ትግሬ) ፤** ኪዳን ፤ ሰላም ፤ ዕርቅ ፣ ፍቅር ፣ ስምምነት ፤ ቅርበት ፣ ልጽቀት ።

**ተገለደ ፤** ተቍረበተ ፤ ቍርበት ፣ ለበሰ ፤ ተደጕሰ ።

**ግሉድ ፤ (ዳን ፣ ዳት ፣ ልድ) ፤** የተገለደ ፤ የለበሰ ፣ የተደጕሰ ። የተነጠፈ ፣ የተጌጠ ፤ ደጓሳ ፣ ወፍራም ።

**ተግሊድ ፤ (ዐረ ፣ ተጅሊድ) ፤** ድጕስ ፣ ድጕስት ፤ አደጓጕስ ፤ አጠራረዝ ፤ የድጕስ ፣ ሥራ ።

**መግለድ ፤ (ብ ፣ መጋልድ) ፤** መድጕስ ፤ መደጕሻ ፤ የድጕስት ፣ ዕቃ ፣ መማሪያ ፤ ፱ ፣ ፀይነት ። ርእስ ፣ መድጕስ ፣ ፫ ። መሳቢያ ፣ የድጕሱ ፣ ኹሉ ፣ መከፈፊያ ፣ ፩ ። ዐይን ፣ ርግብ ፣ ትንሽና ፣ ትልቅ ፣ ፪ ። ቀርን ፣ በግዕ ፣ ፩ ። የውሃ ፣ እናት ፣ ፩ ። ፍየል ፣ ፈለግ ፣ ፩ ። ድሙር ፣ ፱ ። በነዚህ ፣ ላይ ፣ ደግሞ ፣ ፯ ። ጨምረው ፣ ፲፭ ፣ የሚሉ ፣ አሉ ፤ መደበኞቹ ፣ ግን ፣ ዘጠኝ ፣ ናቸው ፤ የቀረው ፣ ትርፍ ፣ ነው ።

**ገለዶ ፤ (ዐማርኛ) ፤** ታላቅ ፣ ቢላዎ ፣ ካራ ፤ የበጎች ፣ ጠጕር ፣ መሸለቻ ፤ ቍርበት ፣ የሚቀፍ ፣ ቍዳ ፣ የሚቀድ ፤ የስፎችና ፣ የፋቆች ፣ መማሪያ ።

**ገሊው ፤ ዎት ፤ (ገለወ ፡ ይገሉ ፡ ይግሉ ። ገለበ ፤ ገለደ)** ፤ መጕለብ ፡ መለጐም ፤ መሸፈን ፡ መጋረድ ፡ ማልበስ ፡ መለበጥ ፤ መጕለብ ፡ የስፌት ፤ መለጐም ፡ የባላፍ ፡ ያታሞ ፡ የከበሮ ፤ መሸፈን ፡ ማልበስ ፡ ለኹሉ ፤ መለበጥ ፡ ከንጨት ፡ ከደንጊያ ፡ ለተሠራ ፡ ለቤት ፡ ለማጥን ። ይገልዎሙ ፡ ልቦሙ ፡፡ ከመ ፡ ከበሮ ፡ ዘገለውዎ ፡፡ ኀሞር ፡ ዘገለውዎ ፡ በቈጽለ ፡ ወርቅ ፡ (፪ቆሮ ፡ ፫ ፡ ፲፭ ። ድጓ ። መጽ ፡ ምስ ። ዘፀ፲፯ ፡ ፴፫ ። ፫ነገ ፡ ፯ ፡ ፲፭) ።

**ገላዊ ፤ መግልው** ፤ የሚጕልብ ፡ የሚሸፍን ፤ ጋራጅ ፡ ለባጭ ።

**ተገልወ** ፤ ተሸፈነ ፤ ተጋረደ ። ዘጠሠቀ ፡ ጽልመት ፡ ተገልወ ፡ (መጽ ፡ ምስ) ።

**ግልው ፤ (ዋን ፡ ዋት ፡ ሉት)** ፤ የተሸፈነ ፡ ሽፍን ፤ ጕልብ ፡ ልጕም ፡ ልብጥ ።

**ግልወት** ፤ መሸፈን ፤ (ጥሸ) መሸፈን ፡ አሸፋፈን ፤ ሽፈና ፡ ልበጣ ። መሸፈኛ ፡ ሽፋን ፤ መጋረጃ ፤ ልባጥ ፡ ስሌዳ ። ግልወታ ፡ በወርቅ ፡፡ አመ ፡ ፂዋዌ ፡ አወፈየ ፡ ኤርምያስ ፡ ዙሎ ፡ ንዋየ ፡ ግበሪሃ ፡ ሲደብተራ ፡ ለሥጠተ ፡ ኲሎሕ ፤ ወተመጢዋ ፡ ከነቶ ፡ ከመ ፡ ግልወተ ፡ ኀጺን ፡ (አዋል ። መጽ ፡ ምስ) ።

**ግላ** ፤ መሸፈኛ ፤ ጥቍር ፡ መጋረጃ ፤ ጨለማ ። ቀላዬ ፡ ግላ ፡፡ አምሳለ ፡ ግላ ፡፡ ጽልመተ ፡ ግላ ፡፡ እስመ ፡ ውእቱ ፡ ግላ ፡ ነበረ ፡ ውስተ ፡ ሕግ ፡ ብሉይ ፡ (ጥበ ፡ ጠቢ ። ስንክ ፡ ሐምሸ ። አርጋ ፡ ፪ ። ፪ቆሮ ፡ ፫ ፡ ፲፭ ፡ ፲፯) ።

**ጕሎ** ፤ ስመ ፡ ዕፅ ፤ ፍሬው ፡ ዘይት ፡ የሚኾን ፡ ቅባታም ፤ ሐኪሞች ፡ ለሆድ ፡ መፈወሻ ፡ ዐበዞች ፡ ለምጣድ ፡ ማሠሻ ፡ ፋቆች ፡ ለቈርበት ፡ ማራሻ ፡ ለማለስለሻ ፡ የሚሹት ፤ ዕንጨቱ ፡ ግብዝ ፡ ውስጠ ፡ ክፍት ። (ተረት) ፤ የጕሎ ፡ ዘንግ ፤ የባሪያ ፡ ደግ ።

**ግላውቃ ፤ (ጽር ፡ ግላፍክ)** ፤ ያሞራ ፡ ስም ፤ ጕጕት ፤ የቀን ፡ ዕውር ፡ የሌት ፡ ዐይን ፡ ብር ። ባለብሉዮች ፡ ግን ፡ ጫት ፡ አሞራ ፡ ይሉታል ፡ (ዘሌ፲፩ ፡ ፲፬ ። ዘዳ፲፬ ፡ ፲፭) ።

**ጐሊሕ ፤ ሐት ፤ (ጐልሐ ፡ ይጐልሕ ፡ ይጕላሕ ። ዕብ ፡ ጋሌሕ ። ትግ ፡ ገልሐ ፡ ላጨ)** ፤ መጕላት ፡ መግዘፍ ፤ መታየት ፡ መገለጥ ፤ እንደ ፡ ልጩ ፡ ራስ ፡ መኾን ። የጥፈት ፡ የሥዕል ፡ የመልክአ ፡ ፊደል ፤ የነገር ፡ የምስጢር ፡ የድምፅ ፡ የቃል ።

**ጕሉሕ ፤ ጕልሕ** ፤ በቁሙ ፤ የጐላ ፤ የተገለጠ ፡ ግልጥ ፤ ፈጽሞ ፡ የሚታይ ፡ የሚሰማ ።

**ጕልሓዊ ፤ (ትግ ፡ ጕልሓይ ። ዕብ ፡ ጋሉሕ)** ፤ ልጭ ፤ ንጭ ፤ ራሱን ፡ ጽሕሙን ፡ ኀፍረቱን ፡ የላጨ ፡ የነጨ ፡ መላጣ ፡ ቡሓ ፤ ጐዳ ፤ ራሰ ፡ በዳ ። (ተረት) ፤ የሴት ፡ ላጪ ፤ የወንድ ፡ ነጪ ።

**ተጓልሐ** ፤ ተዳራ ፡ ተቃበጠ ፤ ተዳለቀ ፡ ተዳሰቀ ፤ በግልጥ ። ወይም ፡ በስውር ፤ ኀፍረት ፡ ለኀፍረት ፡ ተጋለጠ ፤ ተገላለጠ ። ኀፍረት ፡ ተናግሮ ፡ ብእሲት ፡ ባዕድ ፡ ወኢትትጓልሓ ፡ ላቲ ፤ ወኢትኒጣ ፡ ለወለታ ፤ ወኢትቅረብ ፡ ኀበ ፡ ምስካባ ፡ (ሚራ፵፩ ፡ ፳፪) ።

**ጓልሕ** ፤ ድሪ ፤ ቅንጥ ፤ የአፍኣ ። ወይም ፡ የውስጥ ፡ መገላለጥ ።

**አጕልሐ** ፤ አጕላ ፤ አገዘፈ ፡ አስገለጠ ፤ አስረዳ ።

**ገልይ ፤ ዮት ፤ (ገለየ ፡ አው ፡ ገልየ ፡ ይገሊ ፡ ይግለይ ። ዕብ ፡ ጋላህ ፤ ገለጠ)** ፤ መቍረጥ ፡ መቈጥቈጥ ፡ መለየት ፤ መግለጥ ፡ መግፈፍ ፡ ማሳየት ፤ ራቍቱን ፡ ግንዱን ፡ መለመላውን ፡ መተው ፤ የዛፍ ፡ የሰው ። ይገልይዎ ፡ (ዮሐ፲፭ ፡ ፮) ።

**አግለየ** ፤ አስቈረጠ ፡ አስገለጠ ፤ አስለየ ፡ አስታወቀ ፤ እገሌ ፡ አሰኘ ፤ ራሱን ፡ ወይም ፡ ሌላውን ።

**እገሌ ፤ (ሊት ። ዕብ ፡ ፍሎኒ ። ሱር ፡ ፍላን ። ዐረ ፡ ፉላን)** ፤ የስም ፡ ለውጥና ፡ ምትክ ፤ ሀየንተ ፡ ስም ፤ በስም ፡ ፈንታ ፡ የሚነገር ፡ ቃል ። እከሌ ፤ እንቶ(ተ)ኔ ፤ እንትትን ፤ ያ ፡ ርሱ ፤ አንድ ፡ ሰው ፤ አንተ ፤ ሰውዬ ፤ ሰዌ ። አካሉ ፡ ታውቆ ፡ ስሙ ፡ ላልታወቀ ፡ ለተደበቀ ፡ ዐጸፋና ፡ በቂ ፡ እየኾነ ፡ ለሩቅም ፡ ለቅርብም ፡ ይነገራል ፤ አከለ ፡ በቃ ፡ ይላልና ፤ እከሌ ፡ ቅሉ ፡ አካሉን ፡ አካላዊነቱን ፡ ያሳያል ። ሰውዮውን ፡ ዐውቆ ፡ ስሙን ፡ ባለማወቅ ፡ ወይም ፡ በመደበቅ ፡ ስሙን ፡ ሳይጠሩ ፡ ግብሩን ፡ ለመግለጥ ፤ ሰውዮው ፡ ሴትዮይቱ ፤ አንድ ፡ ሰውዬ ፡ አንዲት ፡ ሴትዮ ፡ እንደ ፡ ማለት ፡ ነው ። ሑሩ ፡ ኀበ ፡ እገሌ ፡፡ እገሌ ፡ እምቤተ ፡ እገሌ ፡ ውእቱ ፡፡ አይቴ ፡ ሀለዉ ፡ እገሌ ፡ ወእገሊት ፡፡ ሤጥኩ ፡ በሤጠ ፡ እገሌ ፡፡ ረሳዕነ ፡ ግብረ ፡ እገሌ ፡ (ማቴ፳፮ ፡ ፲፰ ። አፈ ፡ ድጓ ። ግንዘ ። ፍ ፡ ነ ፡ ፴፫ ፡ ፫ ። ገድ ፡ አዳ) ። ሰማዕክኑ ፡ አ ፡ እገሌ ፡፡ ኢትትአመን ፡ አ ፡ እገሌ ፡ ትሕትናሁ ፡፡ አንተ ፡ ሆይ ፤ ሰውዬ ፡ ሆይ ፤ እንትኔ ፡ ማለት ፡ ነው ፡ (ዮሴፍ) ። ጸውዑ ፡ ሊተ ፡ እገሌሀ ፡ ወእገሊተ ፡ ቢል ፤ ያንንም ፡ ያችንም ፤ ርሱንም ፡ ርሷንም ፤ ወንዱንም ፡ ሴቲቱንም ፡ ሴቲቱንም ፤ ወይም ፡ ባልና ፡ ሚስቱን ፡ ያሰኛል ፡ (ሱቱ ፡ ዕዝ፮ ፡ ፶፩) ። አንዳንድ ፡ ጊዜም ፡ ቅጽል ፡ ይኾናል ። አንተ ፡ እገሌ ፡፡ ፈለጥከኒ ፡ እምአመትየ ፡ እገሊት ፡፡ ሑር ፡ ኀበ ፡ እገሊት ፡ ሀገር ፡ (ኪዳ ። ዮሴፍ ። ፊልክ ፡ ፫) ። ለሥራና ፡ ለመማሪያ ፡ ሲኾን ፤ እንትን ፤ አንዳች ፡ አንድ ፡ ነገር ፡ ያሰኛል ።

**እገሌያዊ ፤ (ዐረ ፡ ፉላኒ)** ፤ የእከሌ ፤ የእንቶ ፤ የርሱ ፡ የዚያ ፤ ያንድ ፡ ሰው ። አዘዘ ፡ ከመ ፡ ኢያንብራ ፡ ውስተ ፡ መካን ፡ እገሌያዊ ፡ (ፍ ፡ ነ ፡ ፳፱) ።

**ተገልየ** ፤ ተቈረጠ ፤ ተገለጠ ።

**ግሉይ ፤ (ያን ፡ ያት ፡ ሊት ። ዕብ ፡ ጋሉይ)** ፤ የተገለጠ ፡ ግልጥ ፤ ቍርጥ ።

**ግልየት** ፤ መግለጥ ፤ መገለጥ ፤ አገላለጥ ፡ ገለጣ ፡ ቈረጣ ። የመጽሐፍ ፡ ገጽ ፤ ሉሕ ፡ ፊት ፡ ለፊት ፡ ተገልጦ ፡ የሚታየው ፡ የሚነበበው ። በተለየ ፡ ግን ፡ ግልየት ፡ የሚባል ፤ ወንዙን ፡ ጥራዙን ፡ ማጠፊያውን ፡ ወስን ፡ አድ

ርት ፡ በጥፊትና ፡ በዕጥፋት ፡ ማኸል ፡ ወዲያ ፡ ማደና ፡ ወዲህ ፡ ማደ ፡ ያለው ፡ ባደ ፡ ስፍራ ፡ ነው ።

**ግልያ** ፤ ዝኒ ፡ ከማሁ ፡ ገጽ ፤ ግልየት ፤ ሢራክ ፡ ስንጠረዥ ። ሐሳበ ፡ እግርስ ፡ ነዋ ፡ ውስተ ፡ ግልያሁ ፤ ስፍረ ፡ ሰዓት ፡ (አዋል) ።

**ገሊል ፤ ሎት ፤ (ገለ ፡ አው ፡ ገለለ ፡ ይገልል ፡ ይግልል ። ዕብ ፡ ጋላል)** ፤ መምረጥ ፡ ማንጓለል ፤ መለየት ፡ ማስገለል ። ማንጋለል ፡ በዠርባ ፡ ማስተኛት ። ገልገለ ፡ የዚህ ፡ ዲቃላ ፡ ነው ።

**ተገለ** ፤ ተለየ ፡ ተገለለ ፡ ተንጓለለ ፤ ተንጋለለ ። (ተረት) ፤ ተንጋሎ ፡ ቢተፉ ፡ ተመልሶ ፡ ታፉ ።

**ግሉል ፤ (ላን ፡ ላት ፡ ልልት)** ፤ የተለየ ፡ የተገለለ ፤ የተንጓለለ ፡ የተንጋለለ ።

**ግላል** ፤ እንጉላይ ፡ ንፋሽ ፤ ሐሠር ፡ ምራጭ ፤ እንግሊላ ፡ የኂሊት ።

**ገሊላ ፤ (ዕብ ፡ ግሊላ ፤ ጋሊል)** ፤ ስመ ፡ ሀገር ፤ የምድረ ፡ እስራኤል ፡ ስሜን ፤ በዮርዳኖስና ፡ በጥብርያደስ ፡ በዐቢይ ፡ ባሕር ፡ መካከል ፡ ያለ ፤ የይሳኮርና ፡ የዛብሎን ፡ ክፍል ፤ ታችኛው ፤ ላይኛውም ፡ የአሕዛብ ፡ ክፍል ፡ ሳይቀር ። ገለልተኛ ፡ ገጠር ፡ ዐልፎ ፡ ዐልፎ ፡ ሀገርና ፡ መንደር ፡ ያለበት ፤ ዐውድ ፡ ዘውር ፡ ማለት ፡ ነው ፡ (ኢያ፳ ፡ ፯ ። ፩ነገ ፡ ፱ ፡ ፲፩) ። ናዝሬት ፡ ዘገሊላ ። ቃና ፡ ዘገሊላ ። ወገሊላ ፡ ዘአሕዛብ ፡ (ሉቃ፩ ፡ ፳፮ ። ዮሐ፪ ፡ ፩ ። ማቴ፬ ፡ ፲፭) ።

(ጥላ) **ጋላ** ፤ በቁሙ ፤ ልዩነት ፡ ያለው ፡ ባለመለዮ ፤ ሕዝብ ፡ ጭፍራ ። ስመ ፡ ነገድ ፡ ጋሎስ ፡ ከሚባል ፡ ሕዝብ ፡ የወጣ ፤ ወይም ፡ ከማኸል ፡ አፍሪቃ ፡ የመጣ ፤ ያማራ ፡ ጠላት ፡ ደመኛ ። (ተረት) ፤ በግና ፡ ተዥላ ፤ ዐማራና ፡ ጋላ ። ጋላን ፡ ገድሎ ፡ ምነው ፡ ጋሌ ፡ በማለት ፡ ፈንታ ፡ ምነው ፡ ገለሌ ፡ ማለት ፡ ከዚሁ ፡ ከስሙ ፡ የወጣ ፡ ነው ።

**ጋላት** ፤ ጋሎች ፡ ጭፍሮች ፡ ወታደሮች ፤ ክልካዮች ፡ አጋፋሮች ። (ግጥም) ፤ ሐዋርያት ፡ ጋሎች ፡ ጥልውት ፡ ቢሸሹ ፡ ታስሮ ፡ ተሰቀለ ፡ ዐማኑኤል ፡ ጕሹ ። ቦኡ ፡ ጋላት ፡ ሤመነ ። ዘመጠወ ፡ ርእሶ ፡ ለጋላት ። ተፈነዉ ፡ ጠርባናት ፡ ሜትራይቀይ ፡ ዘውእቶሙ ፡ ጋላት ፡ በትእዛዘ ፡ ዲዮቅልጥያኖስ ፡ ከሓዲ ፡ ከመ ፡ ይምትሩ ፡ ርእሶ ፡ (፪ነገ ፡ ፲፱ ፡ ፴፪ ። ድጓ ። መጽ ፡ ምስ) ።

**ጐልሎ ፤ ሎት ፤ (ጐለለ ፡ ይጔልል ፡ ይጐልል)** ፤ መጕለል ፤ በቤት ፡ ራስና ፡ በጕልቻ ፡ ላይ ፡ ማስቀመጥ ፡ ማኖር ፤ መጣድ ፡ ማስረር ።

**ጕላ ፤ አው ፡ ጕሌ ፤ (ብ ፡ ጐላል ። ዐረ ፡ ወዕብ ፡ ጉሎት ። ጽር ፡ ጉላት)** ፤ አፍላል ፤ መንቀል ፤ የሸክላ ፡ ቅል ፤ ጕልላት ፡ የመንቀል ፡ ዐይነት ። ወገብረ ፡ ክልኤተ ፡ አዕማደ ፡ ወመልዕልቴሆሙ ፡ ጕላት ፡ (፪ዜና ፡ ፬ ፡ ፲፪) ። አንዳንድ ፡ መጣፍ ፡ ኀላት ፡ ብሎ ፡ በሳብዕ ፡ ይጥፋል ።

**ጕልማ ፤ (ዐማርኛ)** ፤ በቁሙ ፤ አባት ፡ ለልጁ ፡ ጌታ ፡ ሳሸክሩ ፡ የሚሰጠው ፡ መሬት ፡ ግዛት ። (ግጥም ፤ ተጠማኝ ፡ ወይም ፡ ተጋዥ) ፤ አይኾንም ፡ እንጂ ፡ ከኾነማ ፤ ከመጋዝ ፡ ይሻላል ፡ ጕልማ ።

**ጐሊም ፤ ሞት ፤ (ጐለመ ፡ ይጐልም ፡ ይጕልም ። ዕብ ፡ ጎሌም)** ፤ መጕለም ፤ ጕልማ ፡ መስጠት ። መጕልመስ ፡ ማደግ ፤ መጐላመም ፡ ጕልማማ ፡ ባለጕልማ ፡ መኾን ። ጕለም ፡ እንዲሉ ፡ ጕልማሜ ፡ ሲሉ ።

**ገላሚዎስ ፤ -ኅሥሥት ፤ -ከሚሌዎን ።**

**ጋልሙት ፤ (ዕብ ፡ ጋልሙድ)** ፤ ዘዘኝ ፡ ሴስኛ ፡ አውሬ ፤ የድመት ፡ የሙጭሙጭላ ፡ ዐይነት ። በቁሙ ፤ ጋለሞታ ፡ ባለመሸታ ።

**ገለሠ ፤—ተቀመጠ ፤ ሸነኀ ፤—ገሊስ ፡ ገለሰ ።**

**ገሊዕ ፤ ዖት ፤ (ገልዐ ፡ ይገልዕ ፡ ይግላዕ ። ዕብ ፡ ጋሎዕ)** ፤ መንቃት ፡ መሠንጠቅ ፤ መሰበር ፡ መድቀቅ ፤ መንከት ፡ መንካት ፤ መጕዳት ፤ የሸክላ ፡ ያጥንት ።

**ገልዕ ፤ (ዕብ ፡ ሔሬሽ)** ፤ ገል ፤ የሸክላ ፡ ስባሪ ፡ እንክትክች ፡ የሳት ፡ መጫሪያ ። እሳት ፡ በገል ፡ ውሃ ፡ በቅል ፡ እንዲሉ ። ብሩር ፡ ዘይትወሀብ ፡ ምስለ ፡ ሕብል ፡ ከመ ፡ ገልዕ ፡ ውእቱ ። የብስ ፡ ሥጋሁ ፡ ከመ ፡ ገልዕ ። ትጽሕፍ ፡ ኅሊናሃ ፡ ውስተ ፡ ገልዕ ፡ (ምሳ፳፮ ፡ ፳፫ ። ገድ ፡ ተክ ። ስንክ ፡ ጥር፳፯ ። ኢዮ፪ ፡ ፰ ። መዝ ፳፩ ፡ ፲፭) ።

**ገልዓት ፤ አግልዕት** ፤ ገሎች ፤ ገላልት ። አሰሩ ፡ ውስተ ፡ ከማዱ ፡ ሐብለ ፡ ወደቤሁ ፡ ስቀሉ ፡ ገልዓተ ፡ ዘአጽለምዎሙ ፡ በፍሕም ። ከመ ፡ ዘያስተጣግዕ ፡ አግልዕተ ፡ (ስንክ ፡ መጋ፳፯ ። ሢራ፳፪ ፡ ፯) ።

**ገለዓድ ፤ (ዕብ ፡ ጊልዓድ)** ፤ ስመ ፡ ሀገር ፤ ተራራ ፤ ከዮርዳኖስ ፡ ማዶ ፡ ያለ ፡ (ዘኍ፴፪ ፡ ፩) ።

**ገሊፍ ፤ ፎት ፤ (ገለፈ ፡ ይገልፍ ፡ ይግልፍ ። ሱር ፡ ግላፍ ። ዕብ ፡ ጋላፍ)** ፤ መቅረጥ ፡ ማነጥ ፡ ማንጠጥ ፤ ጣያት ፡ መሥራት ፤ በንጨት ፡ በደንጊያ ፤ በልብስ ፡ ላይ ፡ መሣል ፡ መመሰል ፡ መፈደል ፡ መጠረዝ ፡ መጥለፍ ። እለ ፡ ይገልፍዎ ፡ ለዕፅ ። ይክል ፡ ገሊፈ ፡ አምሳል ። ገለፈ ፡ ላዕሌሁ ፡ በቀልተ ፡ ወአክሊላተ ። ይግልፍዎ ፡ ውስተ ፡ ኩኵሕ ። እለ ፡ ይገልፉ ፡ ወየኀርዉ ፡ ዐይነ ፡ ማኅተም ። ግልፍ ፡ ላዕሌሆሙ ፡ አስማተ ። ቀጠንት ፡ ዘያሰረግውዎሙ ፡ በሕብራት ፡ ዘገለፉ ፡ በሙ ፡ (ኢሳ፵፩ ፡ ፯ ። ፪ዜና ፡ ፪ ፡ ፲፬ ። ፫ ፡ ፭ ፡ ፯ ። ኢዮ፲፱ ፡ ፳፬ ። ሢራ፴፰ ፡ ፳፯ ። ዘፀ፳፰ ፡ ፱ ። ፍ ፡ ነ ፡ ፳፫) ።

**ገላፊ ፤ (ፊት ፡ ፍያን ፡ ያት ፤ ለፍት)** ፤ የሚቀርጽ ፡ አንጣጭ ፡ ምስል ፡ አፍሳሽ ።

**አግለፈ** ፤ አስቀረጸ ፤ ምስል ፡ አሠራ ፡ አስፈሰሰ ፡ (፫ነገ ፡ ፯ ፡ ፳፱) ።

**ተገልፈ** ፤ ተቀረጸ ፤ ተሣለ ፡ ተመሰለ ። ይትገለፉ ፡ አናቅጽኪ ። ዘተገልፈ ፡ በሰሌዳ ። ውስተ ፡ ከርሠ ፡ እምየ ፡ ተገለፍኩ ፡ ሥጋ ፡ (ኢሳ፷ ፡ ፲፰ ። ስንክ ፡ መስ፳፯ ። ጥበ፯ ፡ ፩) ።

**ግሉፍ ፤ (ፉን ፡ ፉት ፡ ልፍት) ፤** የተቀረጸ ፤ የተጣፈ ፡ የተሣለ ። (ግልፍተኛ ፡ ቍጡ) ። እብነ ፡ ባሕርይ ፡ ግሉፍ ። ግሉፍ ፡ ውስተ ፡ ጽሌ ፡ ልቦሙ ። ጽላት ፡ ጽሑፍ ፡ ወግሉፍ ። ወግሉፋን ፡ ኪሩቤል ፡ ወፀበራት ፡ (ጥበ፲፰ ፡ ፳፱ ። ኤር፲፯ ፡ ፩ ። ስንክ ፡ ነሐ፰ ። ሕዝ፵፩ ፡ ፲፰) ።

**ግልፈት ፤** መቅረጽ ፤ መቀረጽ ፡ አቀራረጽ ። ቅርጽ ፡ ንጥ ፡ ፍልፍል ፤ ያበጠ ፡ የስመጠ ። ግልፈተ ፡ ዐይኑ ፡ ማኅተም ። ወግልፈት ፡ ላዕሌሃ ። አልባስ ፡ እለ ፡ አልቦሙ ፡ ግልፈት ፡ (ዘፀ፳፰ ፡ ፳፩ ። ፪ዜና ፡ ፬ ፡ ፳ ። አፈ ፡ ተ፳፰) ።

**ግልፎ ፤ (ብ ፡ ግልፍ(ፈ)ዋት) ፤** ቅርጽ ፡ ንጥ ፤ የተቀረጸ ፡ ጣዖት ፤ የሰው ፡ ምስል ። አርእስተ ፡ አዕማድ ፡ ዘግልፎ ። ዙሉ ፡ ግልፎሃ ። ወአቅንእዎ ፡ በግልፎሆሙ ። ግልፍዋተ ፡ ኢትግበሩ ። ግልፈዋተ ፡ ጣዖት ፡ (፫ነገ ፡ ፯ ፡ ፳፯ ። ሚክ፩ ፡ ፯ ። መዝ ፡ ፸፯ ። ኩፋ ፡ ፰ ። አርጋ ፡ ፬) ። ግንፋልን ፡ እይ ።

**ግልፈፈ ፤ (ተቀ ፡ ግ) ፤** ገፈፈ ፡ ገለፈፈ ፤ የቈርበት ፡ የከንፈር ። (ዐማርኛ) ።

**ገሊጽ ፤ ጾት ፤ (ገለጸ ፡ ይገልጽ ፡ ይግልጽ) ፤** መግለጥ ፡ መግፈፍ ፡ ማሳየት ፤ መንገር ፡ መተርጐም ፡ ማስረዳት ።

**ተገልጸ ፤** ተገለጠ ፡ ግልጥ ፡ ኾነ ፤ ታየ ፡ ተረዳ ። (ሙሴ) ፡ ሶበ ፡ ይትገለበብ ፡ ይትረአይ ፡ ወሶበ ፡ ይትገለጽ ፡ ይሴወር ፡ ወኢይትዐወቅ ፡ (አዋል) ።

**ግሉጽ ፤ (ጻን ፡ ጻት ፡ ልጽት) ፤** የተገለጠ ፡ ግልጥ ።

**ገሊስ ፤ ሶት ፤ (ገለሰ ፡ ይገልስ ፡ ይግልስ ። ትግ ፡ ገልሰ ። ዕብ ፡ ጋላስ ። ዐረ ፡ ጀለሰ ፤ ተቀመጠ) ፤** መለበድ ፡ ልብድ ፡ መስፋት ፤ ቈርበት ፡ ማልበስ ፡ መደጐስ ፤ መደልደል ፡ ማመቻቸት ፤ መሸብለል ፡ መጠቅለል ፤ የኮርቻና ፡ የጭንት ።

**ግላስ ፤** በቁሙ ፤ የኮርቻ ፡ ልብስ ፤ ምንጣፉ ፡ ምቹው ፡ መቀመጫው ፡ (ዐማርኛ) ።

**ጐልቶ ፤ ቶት ፤ (ጐለተ ፡ ይጌልት ፡ ይጐልት) ፤** መጐለት ፡ መትከል ፤ የጕልቻ ። ማውረስ ፡ መስጠት ፤ የገንዘብ ፡ የርስት ። ይጐልቶሙ ፡ ለአብያተ ፡ ክርስቲያናት ። በጊዜ ፡ ጐልቶቱ ። ወለእመ ፡ ጐለተ ፡ ላቲ ፡ ኢትስድ ፡ (ስንክ ፡ ጥር፳፫ ። ፍ ፡ ነ ፡ ፲፰ ። ፳፱ ፡ ፩) ።

**ጐላቲ ፤ (ቲት ፡ ትያን ፡ ያት) ፤** የሚጐልት ፡ ጐላች ፤ ሰጭ ፡ አውራሽ ። ወለእመ ፡ ፈቀደ ፡ ጐላቲ ፡ ከመ ፡ ይሠየም ፡ ዲበ ፡ ዘጐለተ ፡ (ፍ ፡ ነ ፡ ፲፰) ።

**ተጐለተ ፤** በቁሙ ፤ ጕልት ፡ ኾነ ፡ ተሰጠ ፡ ተወረሰ ። ዘተጐለተ ፡ ሎቱ ፡ (ፍ ፡ ነ ፡ ፲፰) ።

**ጕልት ፤ (ታት) ፤** ጕልቻ ። በቁሙ ፡ ዐዲስ ፡ ርስት ፤ ሰው ፡ በፈቃዱ ፡ ለዘመድ ፡ ለባዕድ ፡ ወይም ፡ ለገዳም ፡ የሚያወርሰው ፤ ገንዘብ ፡ ጥሪት ፤ ቦታ ፡ መሬት ። ንሕነ ፡ ጐለትነ ፡ ጕልተ ፡ ለገበዘ ፡ አዙስም ። ብፅዓታት ፡ ወጕልታት ፡ (ክብ ፡ ነገ ። ፍ ፡ ነ ፡ ፲፰) ።

—፤ የማይፈልስ ፡ ቀለም ፡ ገቢር ፡ ተገብሮ ፡ የሚከት ፡ የማይለወጥ ። ስሉ ፡ ስብሉ ፤ ዮም ፡ ትማልም ፡ አፉሁ ፤ እደ፡ሁ ፤ የመሰለው ፡ ኹሉ ።

**ጎላት ፤—መንቀሎች ፤—ጐልሎ ፡ ጐለለ ።**

**ጉማ ፤—ድምፅ ፡ ዜማ ፤—የነፍስ ፡ ዋጋ ፤—ገዱም ፡ ጌመ ።**

**ጊሜ ፤—ጉም ፤—ገዱም ፡ ጌመ ።**

(ጥ) **ጋማ ፤ (ጽርእ ፡ ወቅብጥ) ፤** ስመ ፡ ፊደል ፡ ማልስ ፡ ገ ። አልፋ ፡ ወቤጣ ፡ ወጋማ ፡ (ሥር ፡ ጻዙ) ።

**ጋማ ፤ (ዐማርኛ) ፤** በቁሙ ፤ የፈረስ ፡ የበቅሎ ፡ ያህያ ፡ ጠጕር ፤ ያንገት ፡ የማዥራት ፡ ጭራ ። የጋማ ፡ ከብት ፡ እንዲሉ ። ያንበሳ ፡ ጐፈር ፡ አንፋሮ ፡ በራስ ፡ የሚታሰር ። ጋሜ ፡ የሰው ፡ ራስ ፡ ጠጕር ፤ ማኽሉ ፡ ተላጭቶ ፡ በዙሪያው ፡ የሚቀር ፤ ዐብሮ ፡ በቀል ፡ ጐፈር ።

**ጋሜ ፤** የደጋን ፡ ዕንጨት ፡ ቀጥታ ፡ ዘለግታ ፡ ያለው ፡ ለብልቦ ፡ ሲያርቁት ፡ እንደ ፡ ቅን ፡ አሽከር ፡ የሚታዘዝ ፤ (ግጥም ፤ ሽበታም ፡ ወይዘሮ ፡ የ፰ ፡ ዓመት ፡ ልጅ) ፤ ራሴ ፡ ጥጥ ፡ ኹኖ ፡ ፈታይ ፡ ስለምን ፡ ልቤ ፡ ተነደፈ ፡ በጋሜ ፡ ደጋን ።

**ጐሜእ ፤ (ዕብራ) ፤** ስመ ፡ ዕፅ ፡ በግብጽ ፡ ወንዝ ፡ ዳር ፡ የሚበቅል ፤ ውስጠ ፡ ክፍት ፡ የሸንበቆ ፡ የቀርከሓ ፡ ዐይነት ፡ ታንኳ ፡ ፍልኳ ፡ የሚኾን ። ንዋየ ፡ ጐሜእ ፡ (ኢሳ፲፰ ፡ ፪) ።



ጐሜእ ፡

**ገሚእ ፤ አት ፤ (ገምአ ፡ ይገምእ ፡ ይግማእ ። ዕብ ፡ ጋሜእ ፡ ማገ ፤ ጠጣ ፤ አሸተተ) ፤** መግማት ፡ መበሽቀጥ ፤ ጽዩእ ፡ መኾን ።

**ግሙእ ፤ (ኣን ፡ ኣት ፡ ምእት) ፤** የገማ ፡ ግም ፡ በሽቃጣ ። (ተረት) ፤ ግም ፡ ለግም ፡ ቢተቃቀፍ ፡ አይነቃቀፍ ።

**ግምአት፤** መግማት፤ አገማም፡ ግማት፡ ክፉ፡ ሽታ።

**ግምኤ፤—ማሰሮ፤—ገምዖ፡ ገምዐ፤ ግምዔ።**

**ገመገም፤** በቁሙ፤ (ዐማርኛ)።

**ገሚድ፤ ዶት፤ (ገመደ፡ ይገምድ፡ ይግምድ፤ አው፡ ገምዶ፡ ዶት፤ ገመደ፡ ይጌምድ፡ ይገምድ። ዕብ፡ ጋማድ፡ ዐረ፡ ጀመደ)፤** መጕመድ፡ መጕማመድ፤ መቍረጥ፡ ማጨድ፡ መጨርገድ፤ መገዝገዝ፡ ማረድ። መቍረስ፡ መገምደል። መግመድ፡ መፍተል፤ ማክረር። ጊዜ፡ ገሚድ፡ በጽሐ። ዘእንበለ፡ ይግምድዎ። ይገምዱ፡ አስካለ። እስከ፡ ማእዜኑ፡ ትገምዲ፡ መጥባሕት። ገመዱ፡ መሌሊቶሙ፡ ከመ፡ ሥጋ፡ ውስተ፡ ጽህርት። ይጌምድ፡ ሥጋሁ፡ በእብን፡ (ማሕ፩፡ ፲፪። ኢዮ፰፡ ፲፪። ኢሳ፲፰፡ ፭። ኤር፳፱፡ ፯። ማር፭፡ ፭)። መላላቱና፡ መጥበቁ፡ ቱሱሕ፡ ስለ፡ ኾነ፡ ነው፤ የቱሱሕን፡ ፍች፡ ተመልከት።

**ገማዲ፤ (ዲት፡ ድያን፡ ያት)፤** የሚጕምድ፤ ቈራጭ፡ ዐጫጅ፤ ገማጅ።

**አግመደ፤ አገመደ፤** አስጕመደ፡ (አስገመደ)፤ አስቈረጠ፡ አሳጨደ።

**ተገምደ፤ ተገመደ።** ታረደ፡ ተጕመደ፤ ተጕማመደ፤ ታጨደ፡ ተቈረጠ። በሰይፍ፡ ተገምዱ፡ ሕፃናት፡ ንጹሓን። ዘተገምደ፡ በመጥባሕት። ሐረገ፡ ወይን፡ እንተ፡ ትትገመድ፡ ወትትአረር። ስሒብዎ፡ ወከነ፡ ሥጋሁ፡ ይትጌመድ፡ (ስንክ፡ ታኅ፴። መጋ፲፭። ድጓ። አቡሻ፡ ፶)።

**ግሙድ፤ (ዳን፡ ዳት፡ ምድ)፤** የተቈረጠ፡ ቍርጥ፤ ጕምድ፡ ጕማዳ። ቶማስ፡ ዘአባላቲሁ፡ ግሙድ። ያዕቆብ፡ ግሙድ፡ (ስንክ፡ ነሐ፳፱። ኅዳ፳፯)።

**ግምደት፤ ግማዴ፤** መቍረጥ፡ መቈረጥ፤ አቈራረጥ፡ ቈረጣ፡ ዐጨዳ፤ ጕማድነት።

**ግምድ፤ ግማድ፤ (ዳት)፤** ቍራጭ፤ ጕመድ፡ ጕማጅ፤ ጕራጅ፡ ዕራፊ፤ ቅናሽ፡ ሙዳ፡ ጕማ። (ግጥም)፤ ኢየሩሳሌምን፡ ይመኛል፡ ሰው፡ ኹሉ፤ ግሸን፡ አይደለም፡ ወይ፡ ግማደ፡ መስቀሉ። ግማድ፡ ዘተርፈ፡ እምዕፀ። ግምደ፡ ደርግሕ፡ ልብስ። በግማደ፡ ልብሱ። ግማደ፡ ሥጋ። ግማዳት፡ ዘዙሉ፡ አባል። ግማዳተ፡ እብድ፡ (ጥበ፲፫፡ ፲፫። ማር፪፡ ፳፩። ፊልክ፡ ፲። ፪፻፵፫። ሕዝ፳፬፡ ፬። ኢዮ፲፯፡ ፯። ቅኔ)።

**ትግምድ፤** መቈረጥ፡ ቈራጥነት፤ ቈራጣ፡ መኾን። ትግምደ፡ አልባሲሆሙ፡ (ግንዘ)።

**ገመድ፤** በቁሙ፤ ሐብል። ሐቢልን፡ ተመልከት።

**ገማዲም፤** ስመ፡ ነገድ፤ ስመ፡ ትውልድ፡ ያፌታውያን፤ የጎሜር፡ ቍራጮች፡ (ሕዝ፳፯፡ ፲፩)።

**ገመል፤ ገምል፤ (ዕብ፡ ጋማል። ሱር፡ ጋምላ። ዐረ፡ ጀመል)፤** በቁሙ፤ ግመል፡ የቤት፡ እንስሳ፡ የጭነት፡ የኮርቻ፡ ከብት፤ በረሓ፡ ቈላ፡ የሚደፍር፡ ውሃ፡ ጥም፡ የሚችል፡ ዐንገተ፡ ረዥም፡ ነዊኀ፡ ቅልጥም፤ ክህያ፡ ክጋሰስ፡ አብልጦ፡ የሚይዝ፡ የሚሸከም። ቀጭኔ፡ የበዳ፡ ግመል፤ ነብርማ፡ ዝንጕርጕር፡ የበዳ፡ አህያ፡ የሚመስል፤ ዐዳኞች፡ እንዳውሬ፡ የሚገድሉት።



ገመል፡

**ገመላት፤ አግማል፤ (ላት)፤** ገመሎች፤ ግመሎች፤ ቀጭኔዎች። ጸጕረ፡ ገመል። ነሥአ፡ ዐሠርተ፡ አግማለ፡ እምአግማለ፡ እግዚኡ። አግማላቲሆሙ፡ (ማቴ፫፡ ፬። ዘፍ፳፬፡ ፲። መሳ፯፡ ፭)።

**ገመላዊ፤** ግመልማ፤ የግመል፡ ዐይነት፤ ግመል፡ ሳቢ፡ ጠባቂ፤ የግመል፡ እረኛ፡ ባለግመል። ቄሬል፡ ገመላዊ፡ (ስንክ፡ ታኅ፳፱)።

**ገምል፤** ስመ፡ ፊደል፡ ማለስ፡ ገ፤ በአበገደ። ዐረቦች፡ ጂም፡ ጀ፡ ይሉታል።

**ጋሜል፤ (ዕብ፡ ጊሜል)፤** ዝኒ፡ ከማሁ፤ ስመ፡ ፊደል፡ ገ። ፍችው፡ ፍጹም፡ ዐስብ፡ ዕሴት፡ ፍዳ። ጋሜል፡ ዕስየ፡ ለገብርከ፡ (መዝ፡ ፻፲፰፡ ፲፯)።

**ገመመ፤ (ይጌምም፡ ይገምም፤ ገምሞ)፤** ያዘ፡ ጨበጠ፤ ላጨ፡ ቈረጠ፤ ከረከመ፤ የለጓሚና፡ የላጭታ። ጋማ፡ ጋሜ፡ ማለት፡ ከዚህ፡ ወጥቷል። ኹለተኛም፡ ገሚም፡ ገመ፡ ይገምም፡ ይግምም፡ ብሎ፡ ዲቃላውን፡ ገምገመ፡ ሲሉት፡ ገመገም፡ ከዚህ፡ ይወጣል። ጌመንና፡ ጉማን፡ ተመልከት፤ ፍችው፡ ከዚህ፡ ጋራ፡ አንድ፡ ነው።

**ገምኖ፤ ኖት፤ (ገመነ፡ ይጌምን፡ ይገምን)፤** ማግመን፡ ማሳረር፤ መጥበስ። ማሳደፍ፡ ማቈለፍለፍ፤ ማርከስ፡ ማስነወር፤ መለወጥ፡ መቀየር፤ የቃል፡ የነገር። ኅፀብኩ፡ እገርየ፡ እፎኑ፡ እጌምኖን። እለ፡ ኢገመኑ፡ አልባሲሆሙ። ገመነ፡ ይሁዳ፡ መቅደስየ። እለ፡ ይጌምኑ፡ ስመ፡ ቅዱስ፤ እስመ፡ ገመንዋ፡ ለዲና፡ እኅቶሙ። ኢይገምን፡ ቃሎ፡ (ማሕ፭፡ ፫። ራእ፫፡ ፬። ሚል፪፡ ፲፩። ኩፋ፡ ፴። ዘኍ፴፡ ፫)። አንዳንድ፡ መጣፍ፡ በገመነ፡ ፈንታ፡ አግመነ፡ አገመነ፡ ይላል፤ አያሰኝም። አገመኑ፡ መሥዋዕተ። ያጌምንዎ፡ ለሥጋሆሙ፡ (አዋል። ፪ጴጥ፡ ፪፡ ፲። ይሁ፡ ፰። ራእ

**ድብ ፤—በቁሙ ፤—ደቢው ፡ ደበወ ።**

**ደቢብ ፤ በት ፤ (ደበ ፤ ደበበ ፡ ይደብብ ፡ ይድብብ ። ዕብ ፡ ዳብብ ፤ ኀለየ ፡ ነበበ)** ፤ መደበብ ፡ መዘርጋት ፤ መወጠር ፡ መገተር ፤ የጥላ ፡ ያጐበር ። መድበብ ፤ መጥቈር ፤ ደባባ ፡ መኾን ፤ የመልክ ፡ የሕብር ፤ ድባ ፤ መዳብ ፡ እንዲሉ ። ወደ ፡ ደቡብ ፡ መኼድ ፤ ደቡብ ፡ ደቡብ ፡ ማየት ፤ ደቡባዊ ፡ መኾን ። ደብደበን ፡ እይ ፤ የዚህ ፡ ዲቃላ ፡ ነው ።

**ድባብ** ፤ በቁሙ ፤ ጃን ፡ ጥላ ፤ የሚደበብ ፡ የሚዘረጋ ፡ የሚታጠፍ ፡ የሚጠቀለል ፤ ጌጥና ፡ ሽልማት ፡ መረሻት ፡ ያለው ፤ ወይም ፡ ሌጣ ። ጸዋሬ ፡ ድባብ ፡ (ታሪ ፡ አክ) ።

**ደቡብ** ፤ የማእዝን ፡ ስም ፤ ፀቢይ ፡ ማእዝን ፡ የሰሜን ፡ ትይዩና ፡ አንጻር ፡ ፊት ፡ ለፊት ፡ በሊባና ፡ በአዜብ ፡ መካከል ፡ ያለ ፤ የምዕራብ ፡ ቀኝ ፡ የምሥራቅ ፡ ግራ ። ሰሜንን ፡ ተመልከት ። ሖሩ ፡ ገጸ ፡ እምደቡብ ፡ እስከ ፡ ሰሜን ፡ (ሕዝ፳ ፡ ፵፰) ። ደቡብ ፡ የምሥራቅ ፡ ግራ ፡ እንደ ፡ ኾነ ፡ ሰሜንም ፡ የምዕራብ ፡ ግራ ፡ ነውና ፤ በዚህ ፡ ምክንያት ፡ ተሳስቶ ፤ በደቡብ ፡ ፈንታ ፡ ሰሜን ፤ በሰሜን ፡ ፈንታ ፡ ደቡብ ፡ እያለ ፡ በብዙ ፡ ቦታ ፡ ተጥፎ ፡ ይገኛል ፡ (ኢሳ፲፱ ፡ ፲፫ ፡ ፴፩ ። ፵፭ ፡ ፳፩ ። ፵፱ ፡ ፲፪) ።

**ተደበ** ፤ ተደበበ ፤ ተዘረጋ ፤ ተዋቀረ ።

**ድቡብ ፤ (ባን ፡ ባት ፡ ብብት)** ፤ የተደበበ ፡ የተዘረጋ ፤ ዝርግ ። ደባባ ፤ መዳብማ ።

**ተድባብ ፤ (ባት)** ፤ ጣራ ፡ ባጥ ፤ ጠፈር ፡ መዋቅር ፤ መክደኛ ፡ ክዳን ፤ ጥላ ፡ ከለላ ፡ ዳስ ፡ ጐጆ ። ተሞቅሖ ፡ መትሕተ ፡ ተድባበ ፡ ቤት ። ወትገብር ፡ ላቲ ፡ መልዕልቴሃ ፡ ተድባበ ፡ ዘወርቅ ። ይትዔገሥ ፡ ቍረ ፡ ክረምት ፡ ወሐሩረ ፡ ሐጋይ ፡ ታሕተ ፡ ሰማይ ፡ ዘእንበለ ፡ ተድባብ ፡ (ጥበ፲፯ ፡ ፪ ። ዘፀ፳፭ ፡ ፲፯—፳፪ ። ስንክ ፡ ሐም፳፭) ። የማእዝን ፡ ራስ ፡ ጫፍ ፤ የቤት ፡ የቅጽር ፡ መሰኮት ፡ ቅስት ፤ ዝንቦ ፡ ቀጸላ ፤ ደርብ ፡ ዕንቍላል ፡ ግንብ ፤ ሰገነት ፤ ዘውድ ፡ አክሊል ፡ ጕልላት ፤ የመርከብ ፡ ዕንጨት ፡ በኋላና ፡ በፊት ፡ በማእዝኑ ፡ ራስ ፡ የሚኾን ። በስተላይ ፡ ለሚኾን ፡ ኹሉ ፡ ይነገራል ። አውረድዎ ፡ እንተ ፡ ተድባበ ፡ ቅጽር ። ተድባበ ፡ ቤተ ፡ መቅደስ ። ወይደንን ፡ እንተ ፡ ተድባብ ። ወለእመ ፡ ሐነጽከ ፡ ቤተ ፡ ሐዲሰ ፡ ትገብር ፡ ሎቱ ፡ ተድባበ ፡ ለናሕስከ ። ለእመ ፡ አረፍት ፡ ይእቲ ፡ ንሕንጽ ፡ ዲቤሃ ፡ ተድባበ ፡ ዘብሩር ። ተምህሩ ፡ ይግበሩ ፡ ተድባበ ፡ አሕማር ። ወከኑ ፡ ይገብሩ ፡ ተድባባተ ፡ አሕማራት ፡ (ግብ፱ ፡ ፳፭ ። ማቴ፬ ፡ ፭ ። ማሕ፪ ፡ ፱ ። ዘዳ፳፪ ፡ ፰ ። ማሕ፰ ፡ ፱ ። ስንክ ፡ ጥር ፲፯ ። የካ፪) ።

**ዲባግ ፤ (ጋት ። ዐረ ፡ ዲባጅ)** ፤ ልብስ ፡ ሐር ፤ ዝንጕርጕር ፡ ባለብዙ ፡ ሕብር ፤ ወርቀ ፡ ዘቦ ፡ ግምጃ ። ሚራያት ፡ ወዲባጋት ። አልባሰ ፡ ዲባጋት ። ቀጠንት ፡ ወኢዲባጋት ። ጸውዖ ፡ ብእሲ ፡ ባዕል ፡ ለዲዮጋንስ ፡ ጠቢብ ፡ ውስተ ፡ ቤቱ ፡ ወከነ ፡ ስርግወ ፡ በዲባጋት ፤ ወብእሲሁሰ ፡ ኢኮነ ፡ ግሡጸ ፡ (መቃ ። ስንክ ፡ መስ፲፮ ። አፈ ፡ ተ፳፰ ። ፈላስ) ።

**ደብደበ ፤ (ደበ ። ዐረ ፡ ዘበ ፤ ዘብዘበ)** ፤ ፈራ ፡ ፀሰበ ፡ ተጨነቀ ፤ የሚመጣበትን ፡ ስላወቀ ። የሐዝን ፡ ወይደበድብ ፡ (ፊልክ ፡ ፻፳፩ ። ቀሌ) ።

—፤ ፈዘዘ ፤ ተንፋ ፡ ዱባ ፡ መሰለ ፤ የሆድ ፡ የሰውነት ፡ አብዝቶ ፡ ከመብላት ፡ የተነሣ ። ወሶበ ፡ ይነቅህ ፡ ኢይደበድብ ፡ ነፍስቱ ፡ (ሢራ፴፬ ፡ ፳) ።

—፤ በቁሙ ፤ ደበደበ ፡ መላልሶ ፡ መታ ፡ ቀጠቀጠ ፤ ደብዳቢ ፡ እንዲሉ ። አረገዘ ፡ ድብድብ ፡ ኾነ ፤ የሰብል ፤ ምስጢሩ ፡ ማበጥ ፡ መንዘርጠጥ ፡ ነውና ፡ ተንፋ ፡ ካለው ፡ ይገባል ።

—፤ ጣፈ ፡ ለጠፈ ፤ ሰፋ ፡ ጠቀመ ፡ ደረተ ። ደብዳቤ ፡ ድብዳብ ፡ ደባደቦ ፡ እንዲሉ ፤ ድብድባ ፡ ዳቦ ፡ ዱባ ፡ ማለትም ፡ የዚህ ፡ ዘር ፡ ነው ። (ግጥም ፤ ድኻ ፡ ተማሪ) ፤ ጋቢዬ ፡ አትለቂ ፡ ተዪ ፡ ይሻልሻል ፤ መርፌኙ ፡ ተሰብስበው ፡ ይደበድቡሻል ።

**አደብደበ** ፤ አስደበደበ ። አስጨነቀ ፤ አፈዘዘ ፡ አደከመ ። ለእመ ፡ አደብደበታ ፡ ኀጢአት ፡ ለነፍስ ፡ (ፊልክ ፡ ፺፭) ።

**አንደብደበ** ፤ አንደበደበ ፤ ተንደበደበ ፤ ደባደቦ ፡ ኾነ ፡ መሰለ ፤ የገላ ፡ (ዐማርኛ) ።

**ዲብዲቆን ፤ (ጽር ፡ ዲፕቲኮን)** ፤ ሰሌዳ ፤ መጽሐፈ ፡ ተዝካር ፤ የሙታን ፡ ወይም ፡ የሕያዋን ፤ የማኅበርና ፡ የመምህራን ፡ የጳጳሳትና ፡ የቅዱሳን ፡ ስም ፡ በተራ ፡ የሚጣፍበት ፤ የባስልዮስን ፡ ቅዳሴና ፡ ወዕቀቦሙን ፡ በእንተ ፡ ብፁዕን ፡ የመሰለ ፡ መዝገበ ፡ አስማት ። መጽሐፈ ፡ ዲብዲቆን ፡ ዘቅዱሳን ። ኀበ ፡ ተለክአ ፡ ዲብዲቆን ፡ ዘማኅበረ ፡ ነቢያት ፡ (መጽ ፡ ምስ ። አርጋ ፡ ፬) ።

**ደቢው ፤ ዎት ፤ (ደበወ ፤ ይደቡ ፡ ይድቡ ። ደበየ ፤ ዴፐ)** ፤ ማድባት ፡ መሸመቅ ፤ ቀስ ፡ ዝግ ፡ ማለት ፤ መደበት ፡ መጣን ፡ መጨቈን ፡ መደቋቈስ ፤ ያውሬ ፡ የጠላት ፡ የንቅልፍ ።

**ድቡት** ፤ ሽመቃ ፤ ቀስታ ፡ ዝግታ ፤ ድብታ ፡ አደባበት ። ርቱዕ ፡ በድቡት ፡ ንግበሮ ፡ ለዝ ። ከመ ፡ ዘበድቡት ፡ ወበቀሲል ፡ ያሐምመከ ፡ (ግብ፲፱ ፡ ፴፮ ። ሄርማ ። ፪ጢሞ ፡ ፬ ፡ ፪) ።

**ድቡተ** ፤ ቀስ ፡ ብሎ ፡ በቀስታ ፤ በሹልክታ ፤ ሳይታይ ፡ ሳይሰማ ። ዐርገ ፡ ድቡተ ፡ እንተ ፡ ካልእ ፡ ገጽ ። ወፀአ ፡ ድቡተ ። ወሶበ ፡ ስእነ ፡ ሠጊረ ፡ ድቡተ ፡ ሖረ ፡ (ገድ ፡ ተክ ። ድጓ) ።

**ድብ ፤ (ባት ። ዕብ ፡ ዶብ ። ሱር ፡ ዴባ ። ዐረ ፡ ዱብ ፤ ዱበት)** ፤ በቁሙ ፤ አውሬ ፡ የዥብ ፡ ወገን ፤ የሚያደባና ፡ የሚያሸምቅ ፤ አድብቶ ፡ የሚይዝ ፡ የሚነጥቅ ፤ ጥላው ፡ የሚያፈዝ ፡ የሚደብት ፤ ጠጕራም ፡ ዐመድማ ፤ (ወና ፡ ሴ) ። ድብ ፡ ኅራስ ። ድብ ፡ ርኁብ ። ድብ ፡ እንተ ፡ ትነሁ ። ቤተ ፡ አናብስት ፡ ወድባት ። ከመ ፡ ትፈኑ ፡ ድባተ ፡ ብዙኀ ፡ (፪ነገ ፡ ፲፯ ፡ ፰ ። ሆሴ ፲፫ ፡ ፰ ። ሰቈ፫ ፡ ፲ ። ስንክ ፡ መስ፳፯ ። ጥበ፲፭ ፡ ፲፰) ።

—፤ ስመ ፡ ከዋክብት ፡ እንሰባቱ ፤ ከመንፈቀ ፡ ሰማይ ፡ ወዲያ ፡ ወደ ፡ ሰሜን ፡ ወገን ፡ ጅብ ፡ ብለው ፡ ታፍገ ውና ፡ ተመስገው ፡ ድርገት ፡ ኹነው ፡ የሚታዩ ፤ ባለመር ከቦች ፡ የሚመሩባቸው ። ኖትያዊ ፡ ይኤጽር ፡ ንበ ፡ ከዋ ክብት ፡ እመ ፡ የሐውር ፡ ውስተ ፡ ባሕር ፡ ዘከመ ፡ ይ መርሖ ፡ ወያከይዶ ፡ ለሐመሩ ፡ (ማር ፡ ይሥ፳፰) ።



ድብ ፡

**ደብይ ፤ዮት ፤(ደበየ ፡ ይደቢ ፡ ይድቢ ። ደበወ)** ፤ ማደባየት ፤ ከፈር ፡ ከመሬት ፡ ከድቤ ፡ ላይ ፡ መጣል ፡ ማንከባለል ፤ ደባ ፡ መሥራት ፤ ሳይታሰቡ ፡ ወደ ፡ ሰው ፡ ቤት ፡ መግባት ፡ ዘው ፡ ጥልቅ ፡ ዠቅ ፡ ማለት ፤ መውረር ፡ መዝረፍ ፤ መቀማት ፡ መመንተፍ ። ደበዩኒ ፡ እለ ፡ አልቦሙ ፡ ምሕረት ። ሮዱኒ ፡ ወደበዩኒ ። ይ ደቢ ፡ አብያተ ፡ ሰብእ ። ከመ ፡ ኢይድብያ ፡ ለቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ (ኢዮ፴ ፡ ፳፩ ። መዝ ፡ ፴፯ ። ግብ፰ ፡ ፫ ። መጽ ፡ ምስ) ።

**ደባዪ ፤(ዪት ፡ ይያን ፡ ያት ፤ በይት)** ፤ ወራሪ ፡ ዘራፊ ፤ ቀማኛ ። ደባዩ ፡ አባግዐ ፡ (አዋል) ።

**ድቤ ፤(ዐማርኛ)** ፤ ዐፈር ፡ መሬት ፤ ትቢያ ፡ ዐቧራ ። ደባ ፡ ደቦ ፡ ደባይ ፡ ደባያት ፡ ማለት ፡ የዚህ ፡ ዘር ፡ ነው ።

**ደቢል ፤ ሎት ፤(ደበለ ፡ ይደብል ፡ ይ ድብል)** ፤ መደበል ፡ ማዳበል ፤ መሸረብ ፡ መደረብ ፤ የሐብል ፡ የፈደል ። መስካት ፡ ማሳካት ፤ በፈትል ፡ ወይም ፡ ርስ ፡ በርሱ ፤ የድባ ፡ የበለስ ፡ የዋንጫ ።

—፤ ማከብ ፡ መሰብሰብ ፡ ማከማቸት ፤ የሸንጎ ። መጽ ሐፍ ፡ ግን ፡ በደበለና ፡ በተደብለ ፡ ፈንታ ፡ አመድበለ ፡ መድበለ ፡ ይላል ፤ የተሳሳተ ፡ ነው ። ሰላም ፡ ሰላም ፡ ለእንድራኒቆስ ፡ እብሎ ፡ ውሒዘ ፡ መንፈስ ፡ ዘሰትየ ፡ ምስለ ፡ ሐዋርያት ፡ በአመድብሎ ። በቍስጥንጥ ንያ ፡ ዘመድበሉ ፡ (ስንክ ፡ ግንቦ፰ ። ጥር፲፩) ።

**መድበል** ፤ ማከማቻ ፡ መከማቻ ፤ መሰብሰ ቢያ ፡ መደለቻ ፤ ሸንጎ ፡ ጉባኤ ፡ የሰው ፡ መንጋ ። መድ በለ ፡ ማኅበር ። መድበለ ፡ ቅዱሳን ፡ አንተ ። አዘዘ ፡ ይግበሩ ፡ መድበለ ። ለእለ ፡ ምስሌሁ ፡ መድበል ፡ (ማሕ፯ ፡ ፩ ። ስንክ ፡ ሠኔ፲፯ ። ሚያ፲፯ ። መስ፱) ። የቅ ጽል ፡ ስም ፡ ወንዶችና ፡ ሴቶች ፡ የሚያስተባብር ፤ ቀደ ምት ፤ ደኅርት ፤ ገበርት ፤ ቀተልት ፤ ይህን ፡ የመሰለ ።

**ተዳበለ** ፤ በቁሙ ፤ ተባበረ ፡ ተጨፋፈረ ፤ ተሸ ረበ ፡ ተደራረበ ። ተዳበለ ፡ ፀራዊ ፡ ወተመዊአ ፡ ጕየ ፡ (ተረ ፡ ቄር፲) ።

**ዱብል ፤(ላቲን)** ፤ ደባል ፤ ዕጥፍ ፡ ድርብ ፡ መንታ ፡ ፊደል ፤ ደጊመ ፡ ቃል ። የበበ ፡ ነበበ ፤ ደለለ ፡ ከለለ ፤ ሐተተ ፡ ፈተተ ፤ ይህን ፡ የመሰለ ። ደበሎ ፡ ዐጕዛ ፡ ለምድ ፡ በላይ ፡ የሚደረብ ። (ተረት) ፤ ሀብታም ፡ ይኺ ዳል ፡ በበቅሎ ፤ ድኻ ፡ ይለብሳል ፡ ደበሎ ።

**ድብል ፤(ትግሬ)** ፤ ልብስ ፡ ጌሲ ፤ የደንጊ ያና ፡ የቀንድ ፡ ያጥንት ፡ ዐይነት ፡ ከራራ ፡ ጠንካራ ። ጥጉ ፡ ከባድ ፡ ሸክም ፤ ጭነት ፤ ውድን ፡ ወዲላ ። በቁሙ ፤ ድ በላ ፡ ያበባ ፡ እኽል ፡ ሲከኩት ፡ ፀጉት ፡ ያለው ፡ (ዐማርኛ) ።

**ዳቤላ ፤(ላት)** ፤ ደበል ፤ ታላቅ ፡ የፍየል ፡ አ ውራ ፤ የሚደረብና ፡ የሚታዘል ፡ የሚንጠላጠል ፤ የላም ፡ አውራ ፡ ኰርማ ፡ ወይፈን ። ዳቤላ ፡ ዘጠሊ ። ሰብዐቱ ፡ ዳቤላት ። ንስሐቦ ፡ ለዳቤላ ፡ ዘላሕም ፡ (ዳን፰ ፡ ፭ ። ኩፋ ፡ ፲፯ ። መጽ ፡ ምስ) ።

**ዳቤላም ፤(ዕብ ፡ ድቤሊም)** ፤ የበለስ ፡ ቋን ጦች ፡ ቍጥራቶች ፤ እንደ ፡ መቍጠሪያ ፡ የተሰኩ ። አን ዱን ፡ ስክ ፡ ድቤላ ፡ ይሉዋል ፤ እጌላን ፡ ተመልከት ፤ ከ ዚህ ፡ ጋራ ፡ አንድ ፡ ነው ። ባለብሉዮች ፡ ግን ፡ ዕፅዐ ፡ ጕ ርደ ፡ የወጣለት ፡ ደቄት ፡ ይሉታል ፡ (፩ዜና ፡ ፲፪ ፡ ፵) ።

(ጥ) **ድባን ፤(ዐረ)** ፤ ዝንብ ፤ ደበን ፤ አደበን ፡ ድ ብን ፡ አለ ፡ ማለት ፡ ከዚህ ፡ ወጥቷል ።

**ድብዕንቍል ፤ድንብዕቍል ፤(ላት)** ፤ ያን በሳ ፡ ወጥመድ ፡ እንደ ፡ ቀፎ ፡ ያለ ፡ (ሕዝ፲፱ ። ገድ ፡ ተክ) ።

**ደቢቅ ፤ቆት ፤(ደበቀ ፡ ይደብቅ ፡ ይድ ብቅ ። ዕብ ፡ ዳበቅ ፤ለጠቀ ፡ ተጠጋ)** ፤ መደበቅ ፡ መደባበቅ ፤ መሸጐጥ ፡ ማስጠጋት ፡ (ዐማርኛ) ።

**ደቢር ፤ ሮት ፤(ደበረ ፡ ይደብር ፡ ይድ ብር)** ፤ መደበር ፡ መገደም ፤ ደብር ፡ ገዳም ፡ መሥራት ፡ ማዘጋጀት ፤ ለንግድ ፡ ዕቃም ፡ ሳይቀር ፡ ለታሪክ ፡ ለመጽ ሐፍ ፡ ይኾናል ።

**ደባሪ ፤ መደብር** ፤ ሠራዒ ፡ መጋቢ ፤ ባለቤት ። ዮሐንስ ፡ መደብር ፡ ዘውእቱ ፡ ሠራዒ ፡ ብሂል ።

**ደብር ፤(ብ ፡ አድባር ፤ ራት)** ፤ ተራራ ፤ ጋራ ፡ ገመገም ፤ የምድር ፡ ዕንብርት ፡ ጕብር ፡ ታላቅ ፡ ረዥም ፤ ከወግር ፡ የሚበልጥ ። ደብረ ፡ ሲና ። ደብረ ፡ ዘይት ። ደብረ ፡ ታቦር ። አድባረ ፡ እስራኤል ፡ (ሕዝ፯ ፡ ፱) ። የተራራ ፡ ተራራ ፤ ከተራራ ፡ ኹሉ ፡ የሚበልጥ ፤ በረዶ ፡ የሚፈላበት ፡ ሰው ፡ የማይደርስበት ፤ እንደ ፡ ዳሸን ፡ እ ንደ ፡ ሄርሞን ፡ ያለ ፡ የሰማይ ፡ ጎረ ፡ ቤት ። አድባረ ፡ አራ ራት ። አድባር ፡ ነዋኀት ፡ ዘመትሕተ ፡ ሰማይ ፡ (ኩፋ ፡ ፰ ። ዘፍ፯ ፡ ፲፱ ። ፰ ፡ ፬) ።



ደብር ፡

—፤ ወሰን ፡ ደንበር ፤ መዲና ፡ ከተማ ፡ ታላቅ ፡ አገር ። ወኮነ ፡ አድባሪሆሙ ፡ ለከነዓን ፡ እምነ ፡ ሲዶን ፡ እስከ ፡ ጌራራ ። ደብረ ፡ አህጉር ። ዴበ ፡ ሖሉ ፡ አድባሪከ ። አድባረ ፡ ግብጽ ፡ (ዘፍ፲ ፡ ፲፱ ። ኢያ፲፱ ፡ ፲፩ ። ዘፀ፲ ፡ ፱ ፡ ፲፱ ። ኢሳ፭ ፡ ፳፯) ።

—፤ ገዳም ፡ ቤት ፡ ክሊያን ፤ ታላቁም ፡ ታናሹም ። ደብረ ፡ ሊባኖስ ። ደብረ ፡ ዐስቦ ። አድባራት ፡ ወገዳማት ። አበ ፡ መቃርስ ፡ ዘደብረ ፡ አስቄጥስ ፤ መዳልወ ፡ አልባብ ፡ ተሰምየት ፡ እስከ ፡ ዮም ፡ ደብሩ ፡ (ገድ ፡ ተክ ። ስንክ ፡ መጋ፳፯) ። ደብር ፡ ማለት ፡ በተራራ ፡ ላይ ፡ የሚሠራ ፤ ተራራ ፡ የሚያኽል ፡ ታላቅ ፡ ማለት ፡ ነው ፤ የምኵራብን ፡ ፍች ፡ ተመልከት ። (ሙሾ ፡ ስለ ፡ ድምፀ ፡ መልክም ፡ ደብተራ) ፤ ክህን ፡ ሞተ ፡ ብሎ ፡ አይነግሩም ፡ ዐዋጅ ፤ እንዲያው ፡ በየደብሩ ፡ መላክ ፡ ነበረ ፡ እንጅ ።

**ዳባር፤(ዕብራ)**፤ ነገር ፡ ቃል ፤ ባህል ፡ ብሂል ፤ አንዳች ፡ ጕዳይ ፡ መፍቅድ ።

**ዳቤር፤(ጽር ፡ ዳቢር ። ዕብ ፡ ድቢር)**፤ መቅደስ ፤ ቅድስተ ፡ ቅዱሳን ፤ ባርባው ፡ ክንድ ፡ ፊት ፡ ያለ ፡ ኻያው ፡ ክንድ ፤ መካነ ፡ ታቦት ፤ ቃለ ፡ እግዚ ፡ የሚሰማበት ፤ የሚነገርበት ፡ (፫ነገ ፡ ፮ ፡ ፲፮ ፡ ፲፱—፳፫ ። ፰ ፡ ፮ ፡ ፰ ። ዘፀ፳፭ ፡ ፳፪) ።

—፤ ስመ ፡ ሀገር ፡ ታናሽ ፡ ከተማ ፤ በይሁዳ ፡ ክፍል ፡ ያለች ፤ ካሌብ ፡ የወረሳት ። እለ ፡ ይነብሩ ፡ ውስተ ፡ ዳቤር ፤ ወስማ ፡ ለዳቤር ፡ ሀገረ ፡ መጽሐፍ ፡ (ኢያ፲፩ ፡ ፲፩) ። ዳቤር ፡ ያለውን ፡ ነገር ፡ እንደ ፡ ማለት ፡ መጽሐፍ ፡ ብሎ ፡ ፈታው ፤ መጽሐፍን ፡ ዳቤር ፡ ድቢር ፡ ማለት ፡ በፋርስ ፡ ቋንቋ ፡ ነው ፡ ይላሉ ፡ (ረበናት) ።

**ደበርቢር፤(ዐረ ፡ ዱብር፤ዘበን ፡ ድጎር)**፤ ታናሽ ፡ ድንኳን ፡ አጐበር ፤ ማረፊያ ፡ መጠጊያ ፤ ወይም ፡ እንደ ፡ ወንበርና ፡ እንዳትሮንስ ፡ ያለ ፤ ሲጠጉት ፡ ዠርባ ፡ የሚጐንጥ ፤ የሚጐረብጥ ፤ መንኮሳት ፡ በርሱ ፡ ላይ ፡ ዐርፈው ፡ ርሱን ፡ ተደግፈው ፡ እንቅልፋቸውን ፡ የሚያሳልፉበት ። ይኑሙ ፡ እንዘ ፡ ኢይሰክቡ ፡ አላ ፡ ከመ ፡ እንተ ፡ አትራኖስ ፡ ዘንድቅ ፡ ይግበሩ ፡ ደበርቢረ ፡ ወቦቱ ፡ ይንጽፉ ፡ አልባሲሆሙ ፡ ወይስክቡ ፡ ንቡረ ፡ (ሥር ፡ ጳኵ) ።

**ደብረወ፤(ተቀ ፡ ግ)**፤ ዳበረ ፡ አደገ ፡ ላቀ ፤ ባለቀ ፤ ለዘር ፡ በቃ ፤ ባለገ ፡ ማገጠ ።

**ደበራ**፤ የብልግና ፡ ሥራ ፤ ዝሙት ፡ ሴሰኘ ፤ ቅንዝር ፡ ምንዝር ።

**እንደበራ ፤ እንደባራ ፤ (ርው)**፤ ዲቃላ ፤ በዝሙት ፡ የተወለደ ፡ ያመንዝራ ፡ ልጅ ፤ ያልተሠራ ፡ ያልተቀጣ ፤ ሕገ ፡ ወጥ ፤ መረን ፡ አግድም ፡ አደግ ፤ ደፋር ፡ ዳንዴ ፤ ጣፎርዴ ። ወእመሰ ፡ ኢገሠጹክሙ ፡ እንደበራ ፡ አንትሙ ። ወልድ ፡ ዘኢተገሠጸ ፤ ፈረስ ፡ ዘኢተረየፀ ፡ እንደባራ ፡ (ዕብ፲፪ ፡ ፰ ። አዋል) ።

**መድበራ ፤ (ዕብ ፡ ሚድባር)**፤ ዱር ፡ የከብት ፡ መሰምሪያ ፤ ብዙ ፡ ሣር ፡ ቅጠል ፡ ውሃ ፡ ያለበት ። ወይም ፡ በጭራሽ ፡ ምናምን ፡ የሌለው ፡ ደረቅ ፡ በረሓ ፤ ምድረ ፡ በዳ ። ገዳም ፡ ዘመድበራ ። ማእከላ ፡ ለደብረ ፡ መድበራ ፡ (ኢያ፩ ፡ ፮ ። ሔኖ፳፱ ፡ ፩) ።

—፤ መድበል ፡ ማኅበር ፤ ጉባኤ ፡ አንድነት ። ይገብሩ ፡ መድበራ ፡ (ሔኖ፹፯ ፡ ፯) ።

**መድብራይጥስ፤(ጽር ፡ ማብዳሪቲስ ። ዕብ ፡ ሚድባራ)**፤ ጠፍ ፡ ባድ ፡ ባድማ ፤ የዱሮ ፡ ከተማ ፤ የተፈታ ፡ አገር ፤ ዱር ፡ ጣሻ ፤ በረሓ ፡ የኾነ ። መድብራይጥስ ፡ ዘቤቶን ፡ (ኢያ፲፰ ፡ ፲፪) ።

**ደብራን ፤ (ዐረ ፡ እደበራን ። ዕብ ፡ ክሲል)**፤ ጕቡኣን ፡ ከዋክብት ፡ ባንድነት ፡ የተደበሩ ፤ በጕሽ ፡ ስም ፡ የሚጠሩ ፤ ፈላስፎች ፡ ጕሽ ፡ የሚሏቸው ፡ እንንምስቶ ፤ ወይም ፡ ከምስቱ ፡ አንዱ ፡ ታላቁ ፡ በጣም ፡ የሚያበራው ። ባለብሉዮች ፡ ዳተኛ ፡ ይሉታል ። ወአስተጋብኦሙ ፡ ለደብራን ። ርኢከኑ ፡ ፍኖቶ ፡ ለደብራን ፡ ወሙፃአ ፡ (ኢዮ፱ ፡ ፱ ። ፴፰ ፡ ፴፩) ።

**ድቡስ ፤ ድንቡስ ፤(ሳት ። ዐረ ፡ ደቡስ፤ ብ ፡ ደባቢስ)**፤ ራሳም ፡ ቾንካር ። የብረት ፡ በሎታ ፤ ወይም ፡ ዘንግ ፡ ወፍራም ፡ ሽቦ ፡ ቋራም ፡ ስለታም ። አዘዘ ፡ ይዝብጥዎ ፡ በድቡሳት ፡ ዘኀጺን ፡ (ስንክ ፡ ታኅ፰ ። ጥር፩ ። ሐም፰ ። ሠኔ፳፯) ። ቀሠፍዎ ፡ በድንቡሳት ፡ በሊኃት ፡ እስከ ፡ ተሰብሩ ፡ ገበዋቲሁ ፡ ወቦኡ ፡ ውስተ ፡ ከርሡ ። ድንቡስ ፡ ክቡድ ፤ ድንቡሳት ፡ ዘብርት ፡ (ስንክ ፡ ሚያ፲፪ ። ፳፯) ።

(ጥ) **ድቡት ፤—ሸመቃ ፡ ቀስታ ፤—ደቢው ፡ ደበወ** ።

**ደብተር፤ ፤(ዕብ ፡ ዲፍታር ። ዐረ ፡ ደፍተር)**፤ በቁሙ ፤ መጣፊያ ፡ መክተቢያ ፤ የብራና ፡ የወረቀት ፡ መዝገብ ፤ ነጋዶች ፡ ጠርዘው ፡ አፍፈው ፡ መጣፍ ፡ አስመስለው ፡ ለየጸሓፊው ፡ የሚሼጡት ። የገንዘብ ፡ ቍጥር ፡ ዘወፅአ ፡ ዘገብአ ፡ የሚጣፍበት ። ደብተር ፡ ማለት ፡ ቃሉ ፡ የፋርስ ፡ ቋንቋ ፡ ነው ፡ ይባላል ።

**ደብተራ ፤(ጽር ፡ ዲፍቴራ)**፤ የምሂዕ ፡ የሠረገላ ፡ ተድባብ ፤ የመንበረ ፡ ታቦት ፡ አጐበር ፤ በስተ ላይ ፡ እንደ ፡ ድባብ ፡ እንደ ፡ ጃን ፡ ጥላ ፤ እንደ ፡ ባጥና ፡ እንደ ፡ ጣራ ፡ ኹኖ ፡ የሚሠራ ። ድንኳን ፡ መላጃን ፡ በዲፍቴራ ፡ አምሳል ፡ የተሠራ ፤ እንደ ፡ ብራና ፡ የሚወጠርና ፡ የሚገተር ፤ ቤተ ፡ መቅደስ ። ጸሓፊ ፤ ባለደብተር ፡ ባለብራና ። (ተረት) ፤ አይጥፍ ፡ ደብተራ ፤ ክንፍ ፡ የለው ፡ አሞራ ። ተከለ ፡ አብራም ፡ ደብተራሁ ። መትሕተ ፡ ደብተራ ፡ ሠቅ ። በውስተ ፡ ደብተራሁ ፡ ቅዱስ ። ከመ ፡


ደብተራ ፡

ትትሐነጽ ፡ ደብተራሁ ፡ (ኩፋ ፡ ፲፫ ። ፩ዜና ፡ ፲፯ ፡ ፩ ። ሚራጅ፱ ፡ ፲ ። ጦቢ፲፫ ፡ ፲) ።

**ደብተራት ፤ ደባትር ፤** ደብተሮች ፡ መዝገቦች ፤ የሚጣፍባቸው ፤ ወይም ፡ የሚጥፉ ፡ ጣፎች ፡ ባለ ደቁተሮች ። ድንኳኖች ፡ አጐበሮች ። ኖኅተ ፡ ደባትሪ ሆሙ ፡፡ ደባትር ፡ ዘነደ ፡ እሳት ፡፡ ደብተራት ፡ (ዘፀ፴፫ ፡ ፲ ። ቅዳ ፡ ሕር ። መቃ ፡ ገ፩) ።

**ደብተራዊ ፤** ድንኳን ፡ ተካይ ፡ የድንኳን ፡ አገልጋይ ፤ ባለድንኳን ፤ ሌዋዊ ፡ (አፈ ፡ ተ፲፯) ። መዘምርን ፡ ደብተራ ፡ ማለት ፡ ከሌዋውያን ፡ ስም ፡ የመጣ ፡ ነው ።



ደብተራ ፡

**ደብተረ ፤** ደበተረ ፤ ዘረጋ ፡ ነጠለ ፤ ወጠረ ፡ ገተረ ፤ በደብተረ ፡ ፈንታ ፡ አደብተረ ፡ ይላል ፡ (ገድ ፡ አዳ) ።

**ተደብተረ ፤** ተደበተረ ፤ ተተከለ ፡ ተዘረጋ ፡ ተወጠረ ፡ እንደ ፡ ድንኳን ፡ ኾነ ። ወተደብተረት ፡ ሎሙ ፡ ይእቲ ፡ እብን ፡ (ገድ ፡ አዳ ። መጽ ፡ ምስ) ።

**ድብቱር ፤** የተዘረጋ ፤ የተተከለ ። ኅበ ፡ ድብቱር ፡ ደባትረ ፡ እሳት ፡ (መጽ ፡ ምስ) ።

**ድብታሬ ፤** መተከል ፡ መዘርጋት ፤ ድብትርና ፡ ደብተርነት ።

**ድጓ ፤—የዜማ ፡ መጽሐፍ ፤—ደጊግ ፡ ደገ ፡ ደግደገ ።**

**ደጐብያ ፤ (ዕብ ፡ ኅባይ ። ዐረ ፡ ጃቢእ) ፤** ደጐብ ፤ አንበጣ ፤ ያንበጣ ፡ ወገን ፡ ኰብኰባ ፡ ፌንጣ ፤ ሌላውም ፡ ኹሉ ፤ አናኰዕን ፡ እይ ። ለሰው ፡ ሲኾን ፡ ጐበዝ ፡ ወጣት ፡ ሦታ ፡ ደበል ፡ ረድ ፡ ማለት ፡ ነው ፤ መሐዝን ፡ ተመ ፡ (ዮኤ፩ ፡ ፬ ። ፪ ፡ ፳፭ ። ናሖ፫ ፡ ፲፭ ፡ ፲፯) ። እመ ፡ በ ፡ ዘበልዐ ፡ አንበጣ ፡ ወደጐብያ ፡ አው ፡ ገመለ ፡ (ቀሌ) ።

**ደጊግ ፤ ጎት ፤ (ደገ ፡ ይደግግ ፡ ይድግግ ። ዕብ ፡ ዳጋህ ፤ በዘ ፡ ረበ) ፤** መደገግ ፡ መኸራት ፤ ማደግ ፡ መመንደግ ፤ ደግ ፡ ደገኛ ፤ ታላቅ ፡ ምጡቅ ፡ መኾን ። ደጋ ፡ (ማድጋ) ፡ ደደከ ፡ ማለት ፡ ከዚህ ፡ ወጥቷል ፤ አዳጋ ፡ ቍሊልታ ፡ ተራራ ፡ ኰረብታ ፡ ከፍ ፡ ያለ ፡ በታ ፡ ማለት ፡ ነው ፤ ልዕልናውን ፡ መደብ ፡ አድርጎ ፡ ደግነቱን ፡ ጤናማነቱን ፡ ያሳያል ። ደንገገን ፡ ተመልከት ፤ የዚህ ፡ ስሯጽ ፡ ነው ። በጋልኛም ፡ ዝኖንን ፡ ደጋጋ ፡ ማለት ፡ ከዚህ ፡ የወጣ ፡ ነው ፤ ነጌን ፡ እይ ።

**ደግደገ ፤ (ዲቃ ፡ ግ ። ዕብ ፡ ዳግዴግ ፤ ነካ ፡ ዳሰሰ) ፤** ከሳ ፡ ቀጠነ ፤ ደቀቀ ፡ ረቀቀ ፡ ሟሟ ። ማለደ ፡ ገሠገሠ ፤ ማለዳ ፡ ተነሣ ፤ ታጠቀ ፡ ተጣጠቀ ፤ ለበሰ ፡ ተላበሰ ፡ አደገደገ ።

**ድግዱግ ፤ (ጋን ፡ ጋት ፡ ድግት) ፤** የከሳ ፡ የቀጠነ ፤ ቀጭን ፡ ደግዳጋ ፤ ኩሳሳ ፡ ከሻዋ ። ድግዱግ ፡ ሥጋሆሙ ፡፡ ድግዱጋኒከሙ ፡፡ እስክንድር ፡ ድግዱግ ፡ መልክኡ ፡፡ ኮነ ፡ አበ ፡ ብሰይ ፡ ድግዱገ ፡ (ዘፍ፵፩ ፡ ፫ ። ዳን፩ ፡ ፲ ። ዮሴፍ ። ስንክ ፡ ሐም፳) ።

**ድግዳጌ ፤** መክሳት ፡ መቅጠን ፤ አክሳስ ፤ ክሳት ፡ ደግዳግነት ፡ (ስንክ ፡ የካ፳፭) ። መታጠቅ ፡ መልበስ ፤ አለባበስ ፡ አስተጣጠቅ ፤ ትጥቅ ፡ ድግድጋት ። ዱግ ፡ ደግ ፡ ማለት ፡ ከዚህ ፡ ወጥቷል ።

(ጥ) **ድግ ፤** በቁሙ ፤ መቀነት ፤ የሆድ ፡ ካሳ ፡ የወገብ ፡ ምሳ ፤ ወገብ ፡ የሚያጠና ፡ የሚደግፍ ።

**ድግደግ ፤ ድግዲግ ፤** ኀሕ ፡ ነግህ ፡ ጧት ፡ ማለዳ ፤ ነገታ ፡ ሳኒታ ፡ ማግስት ። እፎ ፡ ወድቀ ፡ እምሰማይ ፡ ኮከበ ፡ ጽባሕ ፡ ዘበደግደግ ፡ ይሠርቅ ፡፡ ወኢታትርፉ ፡ እምኔሁ ፡ ለደግደግ ፡ (ተረ ፡ ቁር፯ ። ዘፀ ፲፪ ፡ ፲) ።

**አደግደገ ፤** አከሳ ፡ አቀጠነ ፡ አጐሰቈለ ። አማለደ ፡ አስማለደ ፤ አስገሠገሠ ። አስታጠቀ ፤ አስደገደገ ። ደዌ ፡ አደግደገ ፡ ሥጋሁ ፡፡ ወያደገድጉ ፡ ከመ ፡ ላሕም ፡፡ አርባዕቱ ፡ ግብራት ፡ ያደገድጉ ፡ አባለ ፤ ሐዊረ ፡ ፍኖት ፡ ወትጋህ ፡ ዘልፈ ፡ ወጾዊም ፡ ወጽምእ ፡ በሐኑር ፤ አከሳ ፡ (ዮሴፍ ። መዝ ፡ ጽ፳ ። ፈላስ) ። ምንት ፡ ከመ ፡ ዝ ፡ ያደገድገከ ፤ አማለደ ፡ (፪ነገ ፡ ፲፫ ፡ ፬) ።

**አንደግደገ ፤ (ዲቃ ፡ ግ) ፤** በቁሙ ፤ አንደገደገ ፤ ተንደገደገ ፡ (ዐማርኛ) ።

**ድጓ ፤** የዜማ ፡ መጽሐፍ ፡ ስም ፤ ቅዱስ ፡ ያሬድ ፡ ባዩ ፡ ገብረ ፡ መስቀል ፡ ዘመን ፡ ያዜመውና ፡ የገጠመው ። የኋላም ፡ ሰዎች ፡ በየጊዜው ፡ ጨምረውበታል ፤ ፬፻ው ፡ መዝሙር ፡ የዳዊት ፡ ብቻ ፡ እንዳይደለ ፤ ድጓም ፡ የያሬድ ፡ ብቻ ፡ አይደለም ። ድግዱግ ፡ ድግዱገ ፡ ጽሕፈት ፤ ጥፈቱ ፡ የከሳ ፡ የቀጠነ ፡ ደቂቅ ፡ ረቂቅ ፡ የኾነ ፤ አሸዋ ፡ ኔብቅ ፤ ወይም ፡ ዜማ ፡ ቍዘማ ፤ ግጥምና ፡ ዜማ ፡ ማለት ፡ ነው ። ድጕዓን ፡ ተመልከት ። በደገ ፡ ዘይቤ ፡ ሲፈቱት ፡ ግን ፤ ደግ ፡ ደገኛ ፡ አስኻቶ ፡ የመጽሐፉን ፡ መጠን ፡ ታላቅነቱን ፡ ያሳያል ፤ በርቀቱ ፡ ላይ ፡ የመንፈቅ ፡ ስንክሳር ፡ ያኽላልና ። ፪ኛም ፤ ምእላድ ፡ መድብል ፡ እስትጉቡእ ፡ ብለው ፡ ይፈቱታል ፤ ቃሉ ፡ ከገድል ፡ ከታምር ፡ ከአዋልድ ፡ ሳይቀር ፤ ከብሉይ ፡ ከሐዲስ ፡ ከሊቃውንት ፡ ተለቅሞ ፡ ተቀሥሞ ፡ የወጣ ፡ ድርሳን ፡ ኀዉሥ ፡ መዝሙር ፡ ሐዲስ ፡ ማለት ፡ ነው ። ፫ኛም ፤ በፊደል ፡ ቍጥር ፡ ሲፈቱት ፡ ደ ፡ ፬ ፡ ገ ፡ ፫ ፤ ድጓ ፡ ፯ ፡ ይኾናል ፤ እስመ ፡ ጐልቊ ፡ ሰብዐ ፡ ፍጹም ፡ ውእቱ ፡ ይላልና ፡ (ሃይ ፡ አበ) ፤ ፯ ፡ ፍጹም ፡ ቍጥር ፡ ነው ። ድጓ ፡ ማለትም ፡ እንደ ፡ ስንክሳር ፡ ከመት ፡ እስከመት ፡ የተሠራ ፡ በየሱባዔው ፡

ክሑድ፡ እስከ፡ ቀዳም፡ ዕለት፡ ዕለት፡ ጧት፡ ማታ፡ የሚቀርብ፡ ፍጹም፡ ድርሰት፡ መሟዕተ፡ ስብሐት፡ መኾኑን፡ ያሳያል፤ ዋዜማ፡ ዘሠርክ፡ ዐዝል፡ ዘነግህ፡ ስብሐተ፡ነግህ፡ ይላልና። እየብቻውም፡ ነጥሎ፡ ቢፈቱት፤ ድ፡ የክፍሉን፡ ትርብዕት፤ እንደ፡ ወንጌል፡ ባ፬፡ ዐቢይ፡ ክፍል፡ ተክፍሎ፤ ዮሐንስ፤ አስተምሕሮ፤ ጾም፤ ፋሲካ፡ መባሉን፤ ጓ፡ ምዕራፍን፡ ዝማሬንና፡ መዋሥዕትን፡ ሦስቱን፡ ያሳያል። ዳግመኛም፡ ዋይ፡ ዜማ፡ ዘሰማዕኩ፡ በሰማይ፡ እመላእክት፡ ይላልና፤ ሰዓትነትን፡ ለዜማው፡ ብቻ፡ ቢሰጡት፤ ድ፡ የስልቱን፡ ትርብዕት፡ ቁምን፡ ዝማሜን፡ መረግድን፡ ጽፋትን፡ ያሳያል፤ እሊህ፡ አራቱ፡ የኪሩቤል፡ አምሳል፡ ናቸውና። ቁም፡ ከመ፡ ኪደተ፡ ብእሲ፤ ዝማሜ፡ ከመ፡ ኪደተ፡ አንበሳ፤ መረግድ፡ ከመ፡ ኪደተ፡ ላሕም፤ ጽፍዐት፡ ከመ፡ ኪደተ፡ ንስር፤ ወእሉ፡ ይትሜሰሉ፡ በአርባዕቱ፡ እንስሳ፡ (ገድለ፡ አብርሀ፡ ወአጽብሐ)። ጓ፡ የዜማውን፡ ትሥልስት፡ ዜማው፡ ግእዝና፡ ዕዝል፡ አራራይ፡ መኾኑን፡ ያሳያል። ዜማ፡ ጠቅላይ፡ ስም፡ ነው፡ ያንድነት፤ ስሙ፡ የሦስትነት። ምልክቱ፡ ግን፡ የኋላ፡ ሰዎች፡ ያበጁት፡ ነው፤ የያሬድ፡ አይደለም። ወበመዋዕሊሁ፡ ለዝንቱ፡ ንጉሥ፡ ገላውዴዎስ፡ ተንሥኡ፡ አዛዥ፡ ጌራ፡ ወአዛዥ፡ ራጉኤል፡ ካህናት፡ ማእምራነ፡ ዜማ፡ ወወጠኑ፡ አውፅኦ፡ ምልክት፡ ዘድጓ፡ (ታሪ፡ ነገ)። ከዚህ፡ የቀረውን፡ የድጓን፡ ዘይቤ፡ ምስጢርና፡ አፈታት፡ ከድጓ፡ መምህራን፡ ይጠይቋል።

**ደጊም፤ሞት፤(ደገመ፡ይደግም፡ይድግም)፤** መድገም፡ መደጋገም፤ ቀድሞ፡ የሠሩትን፡ ፪ኛ፡ መሥራት። ገሥጾ፡ ለዐርክከ፡ ዮጊ፡ ኢገብረ፡ ወእመኒ፡ ገብረ፡ ከመ፡ ኢይድግም። ለእመ፡ ቦ፡ ዘአበስከ፡ ኢትድግም። ደገሙ፡ ዓዲ፡ ወአበሱ። ኢይደግሙ፡ አበሳ፡ (ሢራ፲፱፡ ፲፫። ፳፩፡ ፩። መዝ፡ ፸፯። ሔኖ፩፡ ፰)።

—፤ ማንበብ፤ ማነብነብ፤ መጸለይ፡ መድገም፤ መናገር፡ መለፍለፍ። ነሥአ፡ መጻሕፍተ፡ አበዊሁ፡ ወደገሞን። ወትደግም፡ ምእተ፡ ወኀምሳ፡ መዝሙረ፡ ዳዊት። ኢይደግሙ፡ ነገረ፡ በዲበ፡ ነገርየ፡ (ኩፋ፡ ፲፱። ግንዘ። ኢዮ፳፱፡ ፳፪)።

**ደጋሚ፤(ሚት፡ምያን፡ያት)፤** በቁሙ፤ የሚደግም፤ የሚያነብ፡ አንባቢ። ዳዊት፡ ደጋሚ፡ እንዲሉ።

**ምድጋም፤(ማት)፤** መድገሚያ፤ ቦታ፡ መጣፍ፡ ጊዜ። ድጋም፡ ንባብ፤ ዜማ፡ የሌለው፡ ቃል።

**አድገመ፤** አስደገመ፤ አስነበበ፤ ድጋም፡ አስተማረ።

**ተደግመ፤** ተደገመ፤ መጣፉ። ፪ኛ፡ ጊዜ፡ ተደረገ፤ ሥራው። ዘኢኮነ፡ከማሁ፡እምፍጥረተ፡ዓለም፡ ወኢይደገም፡ እንከ፡ እምድኅሬሁ፡ (ዮኤ፪፡ ፪)።

**ድጉም፤(ማን፡ ማት፡ ግምት)፤** የተደገመ፤ የተደጋገመ፤ ዕጥፍ፡ ድርብ። የተደገመበት።

**ዳግም፤(ምት፡ ማን፡ ማት)፤** ድጋሚ፡ ዳግሞሽ፤ ዳግመኛ፡ ኹለተኛ። ዳግም፡ ልደት። ዳግም፡ ሞት። ዳግም፡ አፅት። ዳግም፡ ብእሲ። አዕቀጸኒ፡ ወናሁ፡ ዳግሙ፡ ዮም። ሰላም፡ ለክልስት፡ ያኖስ፡ ለዮናክንዲስ፡ ዳግሙ፡ (ማቴ፲፱፡ ፳፰። ራእ፪፡ ፲፩። ዘዳ ፲፯፡ ፲፰። ፩ቆሮ፡ ፲፭፡ ፵፯። ዘፍ፳፯፡ ፴፱። ስንክ፡ ሐምሮ)።

**ዳግመ፤** ደግሞ፡ መልሶ፤ ተመልሶ፤ ዳግመኛ። እንከ፡ ዳግመ። ዓዲ፡ ዳግመ። ወካዕበ፡ የሐውር፡ የአብስ፡ ዳግመ። ዳግመ፡ ይመጽእ፡ (ኤር፫፡ ፩። መሳ፲፫፡ ፱። ሢራ፴፩፡ ፴፩። ቅዳ)።

**ዳግማዊ፤(ዊት፡ ውያን፡ ያት)፤ ዳግማይ፤(ዪት፡ ሚት፤ ይያን፡ ያት)፤** በቁሙ፤ ኹለተኛ፡ ታናሽ፤ ተከታይ፡ ምክትል። አባ፡ ማርቆስ፡ ዳግማዊ። ወልደ፡ ዳግማዊት፡ ብእሲት። ዳግማይ፡ አዳም። በማይ፡ ዳግሚት፡ (ስንክ፡ ጥቅ፳፫። መስ፬። ውዳ፡ ፬። ቅዳ። ድጓ)።

**ድጋም፤** በቁሙ፤ መድገም፤ መደገም፡ አደጋገም፡ ደገማ፤ ድግሚያ፡ ጸሎት።

**ደጋን፤—በቁሙ፤—ዴግኖ፡ ዴገነ።**

**ዳጎን፤(ዕብራ)፤** ስመ፡ ጣዖት፤ የባሕር፡ ዳር፡ ሰዎች፡ ኢሎፍላውያን፡ የሚያመልኩት፤ ፊቱና፡ ራሱ፡ የሰው፤ ግንዱና፡ ገላው፡ መለመላው፡ የደራጎን፡ ያሣ፤ ዐይነቱ፡ ሦርዞና፡ ጕርዞ፡ ወይም፡ አንባዛና፡ ዐዞ፡ የሚመስል። ዳግ፡ ዓሣ፤ ዳጎን፡ ዓሣዊ፡ ዓሥማ፡ ዓሦ፡ ማለት፡ ነው፡ ኽርቦ፤ ነብሮ፡ እንደ፡ ማለት፡ (፩ነገ፡ ፭፡ ፪)።

**ድጕዓ፤(ሐማሴን)፤** አልቃሽ፡ አሿሿ፡ ገጣሚ። ቍዘማ፡ የልቅሶ፡ ዜማ፤ ሙሾ፡ ግጥም። ድጓን፡ ተመልከት፤ የዚህ፡ ዘር፡ ነው። ድጕዓ፡ ደግሞ፡ ከጕድዐ፡ ወጥቷል።

**ደጕዓሌ፤ደጓዕሌ፤(ዕብ፡ዴቄል። ሱር፡ ዴቅላ። ዐረ፡ደቀል)፤** የሰሌን፡ ዐይነት፡ ዛፍ፡ ተምር፤ ግንዱ፡ ቁመቱ፡ የበቀልት፤ ቅጠሉ፡ ሌላ፡ ዐይነት፤ እንደ፡ ውስጥ፡ እጅና፡ እንደ፡ ጣት፡ ያለ፤ ዲቃላ፡ ማለት፡ ከዚህ፡ ወጥቷል።

ደጕዓሌ፡

—፤ ሰሌን፡ የሰሌን፡ ቅጠል፡ ዘንባባውና፡ ዝንጣፊው፤ ፀመርቱ፡ ሙሽራው፤ የተሠራ፡ ወይም፡ ያልተሠራ። ወአኀበረ፡ በውሳጤታ፡ ታቦተ፡ አንጦኪያ፡ ደጕዓሌ። ነጸፈ፡ ውስተ፡ ግብ፡ ቈጽለ፡ ደጕዓሌ። ነሥአ፡ ኅዳጠ፡ ደጓዕሌ፡ ወሠጠቆ፡ ወበዕበት፡ ካልእ፡ አር

ሐሰ ። ፀፍረት ፡ ዘደኀዐሌ ። ፀፊረ ፡ ደኀዐሌ ፡ (ገድ ፡ ተክ ። ገድ ፡ ዮሐ ። ፊልክ ፡ ፵፰ ። ፻ር ። ስንክ ፡ ኅዳ፲፯) ።

**ደጊፍ ፡ ፎት ፤ (ደገፈ ፡ ይደግፍ ፡ ይድግፍ ። ትግ ፡ ደግፈ)** ፤ መደገፍ ፡ መደጋገፍ ፤ ማጽናት ፡ ማበርታት ፤ እንዳይወድቅ ፡ ማድረግ ፤ አይዞኽ ፡ ማለት ። ገደፈ ፡ ማለት ፡ ከዚህ ፡ ወጥቷል ፤ የዚህ ፡ ግልባጭ ፡ ነው ። ሶቀንና ፡ በመደን ፡ ተመልከት ፤ ደገፈ ፡ ያማርኛና ፡ የትግሬ ፡ ነው ። አንዳንድ ፡ ሰዎች ፡ ግን ፡ ብርዕ ፡ ሲሉ ፡ ብዕር ፡ እንደሚሉት ፤ ደገፈ ፡ ሲሉ ፡ ገደፈ ፡ ይላሉ ፤ ኹሉም ፡ ስሕተት ፡ ነው ።

**ደጐጽ ፤ ጾት ፤ (ደጐጸ ፡ ይደጕጽ ፡ ይድጕጽ ። ዕብ ፡ ዳጋሽ ፤ አጠበቀ ፤ የማጥበቅ ፡ ምልክት ፡ አደረገ ፤ የፊደል)** ፤ መውጋት ፡ መጠቈም ፡ ጠቅ ፡ ማድረግ ፤ መኳኰጥ ፡ መንካት ፡ መኰነጥ ፤ መኰሰም ፡ መደሰቅ ፤ መምታት ። መኰጸን ፡ እይ ፡ የዚህ ፡ መንቲያ ፡ ነው ። አሜከላ ፡ ለእመ ፡ አኀዝኮ ፡ በእዴከ ፡ ይደጕጽ ። አሕጻከ ፡ ደጐጻኒ ። ዘደጐጸ ፡ ዐይኖ ፡ ያወርድ ፡ አንብዐ ። ዘይደጕጸኒ ፡ ሥጋየ ። ደጐጸ ፡ እንግድዓሁ ። ወገረ ፡ አሐዱ ፡ እምኔሆሙ ፡ አሐደ ፡ ዐጽቀ ፡ ወደጐጸ ፡ ገጸ ፡ ንጉሥ ፡ (አፈ ፡ ድ፲ ። መገ ፡ ፴፯ ። ሢራጅ፪ ፡ ፲፱ ። ፪ቆሮ ፡ ፲፪ ፡ ፯ ። ገድ ፡ ተክ ። ዮሴፍ) ።

—፤ መደጐስ ፤ መደገስ ፡ ማስናዳት ፤ ማሥመር ፡ ማሳመር ፤ ማሰንበር ፤ ማስመጥ ፡ ማሳበጥ ፤ መሸለም ፡ ማስጌጥ ፤ መልክ ፡ ማውጣት ፤ ያንቀልባ ፡ የብራና ፤ ገለደን ፡ እይ ።

—፤ መዳጐስ ፤ ደኅሳ ፡ መኾን ፤ ወይም ፡ ማድረግ ። ምስጢሩ ፡ ማሳበጥ ፡ ከለው ፡ ይገባል ። ደንገፀን ፡ ተመልከት ፤ የዚህ ፡ ዲቃላ ፡ ነው ።

**ደኀጺ ፤ (ጺት ፡ ጽያን ፡ ያት)** ፤ የሚወጋ ፡ የሚኰንጥ ፤ ደኅሽ ፡ አሥማሪ ።

**መድጐጽ ፤ (ብ ፡ መዳጕጽ)** ፤ መውጊያ ፡ መኳኰጫ ፡ አርቃሾ ፡ ቿንካር ፤ የእንስሶች ፡ መንኪያ ፡ መጠቈሚያ ። ነገረ ፡ ጠቢባን ፡ ከመ ፡ መድጐጽ ፡ ላሕም ፡ (መክ፲፪ ፡ ፲፩) ።

—፤ በቁሙ ፤ ማሥመሪያ ፤ ማሰንበሪያ ፡ አፈ ፡ ዱልዱም ፡ ወስፌ ፤ መድጐስ ፡ የድጕስ ፡ መሣሪያ ፡ በየስሙና ፡ በያይነቱ ። መግለድን ፡ ተመልከት ።

**ተደጕጸ** ፤ ተወጋ ፡ ተነካ ፡ ተኰነጠ ፤ ተደጐሰ ፡ ተሠመረ ።

**ድጉጽ ፤ (ጻን ፡ ጻት ፡ ጕጽት)** ፤ የተወጋ ፡ የተነካ ፤ የተደጐሰ ፡ (ስንክ ፡ ሠኔ፲፯) ።

**ድጕጸት** ፤ መውጋት ፤ መወጋት ፡ መነካት ፤ ንኪት ፡ ሰንበር ፡ ዕበጥ ፤ ድጕስ ፡ ድጐሰት ። እንበለ ፡ ሕማም ፡ ወእንበለ ፡ ድጕጸት ፡ (መጽ ፡ ምስ) ።

**ተዳጐጸ** ፤ ተጣለ ፡ ተኳነጠ ፤ ተጐናነጠ ።

**አስተዳጐጸ** ፤ አጣላ ፡ አንካካ ፤ አኳነጠ ። ያስተዳጕጽ ፡ ማእከለ ፡ አዕርክት ። ልሳን ፡ ዐማፂ ፡ ዘያስተዳጕጽ ፡ ኀበ ፡ ንጉሥ ። እለ ፡ ኢያስተዳጕጻ ፡ (ሢራ ፳፰ ፡ ፱ ። ፶፩ ፡ ፮ ። ፩ጢሞ ፡ ፫ ፡ ፲፩) ።

**መስተዳጕጽ** ፤ የሚያጣላ ፡ አጣይ ፤ አሳባቂ ፡ ነገረ ፡ ሠሪ ። ልሳን ፡ መስተዳጕጽ ፡ ሆከሙ ፡ ለብዙኃን ። ኢይኩና ፡ መስተዳጕጻተ ፡ (ሢራ፳፰ ፡ ፲፬ ። ፍ ፡ ነ ፡ ፰ ፡ ፩) ።

**ደጕር ፤ ሮት ፤ (ደጐረ ፡ ይደጕር ፡ ይድጕር ። ዕብ ፡ ዳጋር)** ፤ ማሞቅ ፡ መታቀፍ ፤ ማመስ ፡ መቀፍቀፍ ፤ የንቍላል ። መዘርጋት ፡ ማርገብገብ ፤ የክንፍ ፤ ለመብረር ። ኹሉም ፡ የወፍ ፡ ሥራ ፡ ነው ። መስከት ፡ ክልክ ፡ ማግባት ፤ መስፈር ፡ መመዘን ፡ ማስተካከል ።

**ደጕር ፤ ድጕር ፤ (ዐረ ፡ ደጅር)** ፤ ድግር ፤ የሞፈር ፡ ክንፍ ፡ በግራና ፡ በቀኝ ፡ የሚቀጠል ፤ ሰረረን ፡ እይ ። በአንጻረ ፡ ድጕር ፡ ዕርፈ ፡ ወበአንጻረ ፡ ዕርፍ ፡ ድጕረ ። አርዑተ ፡ ብዕራ ፡ ወጸሪበ ፡ ድጕር ፡ (ኩፋ ፡ ፲፩ ። አዋል) ። ደንጐራ ፡ አዳጕራ ፡ ማለት ፡ ከዚህ ፡ ወጥቷል ።

**ዴግሬ ፤ (ላቲን ፡ ግራዱስ)** ፤ ደረጃ ፡ ዕርከን ፤ ልክ ፡ ሚዛን ፡ እንደ ፡ ድግር ፡ የተካከለ ።

**ደጕስ ፤ (ትግሬ)** ፤ ዳጕሳ ፤ የድግስ ፡ እኽል ፤ የጤፍ ፡ ዐይነት ፤ ዐረቄና ፡ ጠላ ፡ እንጀራ ፡ የሚኾን ።

**ዱድ ፤—ስመ ፡ ነገድ ፤—ደዊድ ፡ ዶደ ፤ ዶድ ።**

**ዴዴ ፤—ደጅ ፤—ደይደየ ፤ ዴደየ ።**

**ድድ ፤—መሠረት ፤—ወዲድ ፡ ወደ ።**

**ደደክ ፤ (ደገ ፤ ደግደገ)** ፤ ደጋ ፡ ብቄ ፤ ጉማም ፡ ብርዳም ፤ ውርጫም ፤ ነፋሳም ። ወምድረ ፡ ሴምስ ፡ ኢመርቄ ፡ ወኢደደክ ። ይባርክዎ ፡ ደደክ ፡ ወመርቄ ። ገነት ፡ ዘኢያየብሳ ፡ ነፋስ ፡ መርቄ ፡ ወደደክ ፡ (ኩፋ ፡ ፰ ። ዳንሮ ፡ ፵፰ ። ስንክ ፡ ጥቅ፳፩) ።

—፤ ቀቅ ፤ ቈፈር ፡ ነፋስ ፤ በደጋ ፡ የሚወርድ ፡ የብርድ ፡ ዐይነት ፡ ኹሉ ። አስሐትያ ፡ ወቍር ፡ ወሐመዳ ፡ ወደደክ ። ዘየዐርግ ፡ እምኔሁ ፡ ከመ ፡ ጢስ ፡ ውእቱ ፤ ወስሙ ፡ ደደክ ፡ (ሔኖ፷፯ ፡ ፲፪ ። ፰ ፡ ፲፰) ።

**ዲዲሞስ ፤—መንቲያ ፤—ዴደየ ።**

**ዴዳን ፤—ስመ ፡ ነገድ ፤—ደይዳን ።**

**ደዲቅ ፤ ቆት ፤ (ደደቀ ፡ ይደድቅ ፡ ይደድቅ ። ወድቀ ፤ ወገበ)** ፤ መደንገት ፤ ድንገት ፡ መኾን ፡ መደረግ ፤ የሥራ ። ሳይታሰቡ ፡ መድረስ ፡ መምጣት ፤ ከተፍ ፡ ማለት ፤ በድንገት ፡ ማግኘት ፡ መገኘት ፤ ግጭት ፡ መግጠም ። ደደቀ ፡ በውእቱ ፡ አዝማን ፡ ባእስ ፡ ማእከለ ፡ አይሁድ ፡ ወማእከለ ፡ አርማንያ ። እመ ፡ ደደቀ ፡ ብጽሐተ ፡ ነግድ ። እመ ፡ ቦ ፡ ካህን ፡ ዘደደቆ ፡ በንዋም ፡ ዝንየት ። ጽኑዐ ፡ ልብ ፡ ኢይደድቅ ፡ ሠናየ ። ወደደቆ ፡ ለአብ ፡ መምህረ ፡ (ዮሴፍ ። ፊልክ ፡ ፸፱ ። ቄድር ። ምሳ፲፯ ። ተረ ፡ ቄር) ።

—፤ መደደቅ ፥ መውጋት ፤ መደንጐር ፤ መፈንቀል ፥ መገልበጥ ፤ መቈፈር ፥ መመንቀር ፥ (ዐማርኛ) ። አንዳንድ ፥ መጽሐፍ ፥ ግን ፥ በደደቀ ፥ ፈንታ ፥ ተዳደቀ ፥ ይላል ፤ አያሰኝም ። እንተ ፡ ኢንሰይኩ ፡ ተዳደቀተኒ ፡፡ በከመ ፡ ይዳደቅ ፡ ለአብድ ፡ ከማሁ ፡ ሊተኒ ፡ ይዳደቀኒ ፡፡ ለአብዳን ፡ ይዳደቀሙ ፡ ሞት ፡፡ አልቦ ፡ ዘይዳደቃ ፡፡ ወተዳደቀ ፡ አሐዱ ፡ ካህን ፡፡ ከመ ፡ ይዳደቅዋ ፡ ለሀገር ፡ (ኢዮ፫ ፥ ፳፭ ። መክ፪ ፥ ፲፭ ። ምሳ፳፬ ፥ ፳ ። ጥበ፯ ፥ ፳፭ ። ሉቃ፲ ፥ ፴፭ ። ዮሴፍ) ።

**ተዳደቀ** ፤ ተገናኘ ፥ ተገኛኘ ፤ ተጋጠመ ። ተዳደቀ ፡ ዙሎሙ ፡ ውስተ ፡ ጸብእ ፡፡ ኢይደሉ ፡ ንዳደቃ ፡ ለጸብእ ፡ ዘእንበለ ፡ በትእዛዘ ፡ እግዚ ፤ አላ ፡ በተዳድቆ ፡ ግብት ፡ (ዮሴፍ ። ፊ ፥ መ ፥ ፱ ፥ ፲፪) ።

**ድድቅ ፤ (ቃት)** ፤ ድንገት ፤ ድንገተኛ ፥ ያልታሰበ ፤ አደጋ ፥ ሞት ፥ ጥፋት ፤ ክፉ ፥ ነገር ፥ ኹሉ ። አሐዱ ፡ ድድቅ ፡ ይዳደቆሙ ፡ ለክልኤሆሙ ፡፡ ተዳደቀ ፡ ድድቅ ፡ ለውእቱ ፡ ንዋይ ፡፡ ምንዳቤያት ፡ ወድድቃት ፡፡ እምዙሉ ፡ ድድቅ ፡ ዘይጸንሖ ፡ ለዐጓለ ፡ መሕያው ፡፡ እምድድቅ ፡ ዘውስተ ፡ ማያት ፡ (መክ፱ ፥ ፲፱ ። ፍ ፥ ነ ፥ ፵፩ ፥ ፩ ። መቃ ፥ ገ፳፱ ። አርጋ ፥ ፫ ። ደራሲ ። መዝ ፥ ፺) ።

**ዲድርክም ፤—የገንዘብ ፡ ስም ፤—ደይደር ።**

**ዲድስቅልያ ፤—የመጣፍ ፡ ስም ፤—ደይደስ ።**

**ደሀለ ፤—ሸሸ ፤—ደሐለ ።**

**ዳህምሞ ፤ ሞት ፤ (ዳህመመ ፥ ይዳሀምም ፥ ይዳህምም ። ዕብ ፥ ዳህም ፤ ብህመ)** ፤ መቈፈር ፥ መኰትኰት ፤ ዐፈር ፥ ማስታቀፍ ። መቈለል ፥ መደመም ፤ መመደብ ፤ መደብ ፥ መሥራት ፤ ላታክልት ። ደመመን ፥ እይ ፤ የዚህ ፥ ጎር ፥ ነው ።

**ዶድ ፤ (ዕብራ ። ሱር ፥ ዶዳ)** ፤ አጐት ፤ ያባት ፥ የናት ፥ ወንድም ፤ ያክሥት ፥ ባል ። ወዳጅ ፥ ዘመድ ፥ ባልንጀራ ፤ እኩያ ፥ አምሳያ ፤ ዐብሮ ፥ አደግ ፥ ወንድም ፥ አክል ።

**ዶዲ** ፤ የሰው ፥ ስም ፤ ወዳጄ ፥ ዘመዴ ፥ ማለት ፥ ነው ፥ (፪ነገ ፥ ፳፫ ፥ ፱ ፥ ፳፬) ። አንዳንድ ፥ መጣፍ ፥ ግን ፥ ዱድ ፥ ደዳኢ ፥ ይላል ፤ ስሕተት ፥ ነው ። ዱድ ፥ ታላቅ ፥ ድስት ፥ ቅርጫት ፤ ዱዳኢም ፥ የሽቱ ፥ ቅጠል ፥ ነው ፤ ዕንጐትን ፥ ተመልከት ።

**ጀውዛ ፤—ስመ ፡ ከከብ ፤—ገውዛ ።**

**ዶሐን ፤ (ዕብ ፥ ወሱር ። ዐረ ፥ ዱኅን)** ፤ ስመ ፥ እክል ፤ አንድ ፥ ዐይነት ፥ እኽል ፤ አገዳው ፥ ላንፋው ፥ የማሽላ ፤ ዐጫጭር ፥ ቀጫጭን ፥ ፍሬው ፥ የዳጉሳ ፥ ዐይነት ፥ (ሕዝ፬ ፥ ፱) ።

**ደውይ ፤ ዮት ፤ (ደወየ ፥ ይደዊ ፥ ይድወይ ። ዐረ ፥ ደዊየ ። ዕብ ፥ ዳዋህ ። ሱር ፥ ድዊይ)** ፤ መደወይ ፥ መታመም ፥ መበሸት ፤ ድውይ ፥ መኾን ፥ ጤና ፥ ማጣት ፤ በደዌ ፥ ዳኛ ፥ ባልጋ ፥ ቍራኛ ፥ መያዝ ። እመሂ ፡ ደወየ ፡ ኢይሴዩ ፡ ሐዩወ ፡፡ ደወዩ ፡ ከመ ፡ አባግዕ ፡፡ ደወየ ፡ ልብነ ፡፡ ደወይኩ ፡ ወሐወጽከሙኒ ፡ (ኢዮ፳፬ ፥ ፳፫ ። ዘካ፲ ፥ ፪ ። ሰቈ፭ ፥ ፲፯ ። ማቴ ፳፭ ፥ ፴፯) ።

**ድዉይ ፤ (ያን ፥ ያት ፤ ዱያን ፤ ድውይት ፥ ዊት)** ፤ በቁሙ ፤ የተደወየ ፤ ደዌ ፥ ያደረበት ፤ ታማሚ ፥ በሽተኛ ። ኢትትሀከይ ፡ ሐውጾ ፡ ድዉይ ፡፡ ዘድዉይ ፡ ሥጋሁ ፡፡ በእንተ ፡ ድዉያን ፡፡ መጋቤ ፡ ዱያን ፡፡ ነፍስ ፡ ድውይት ፡ (ሢራ፯ ፥ ፴፭ ። ፴ ፥ ፲፱ ። ፍ ፥ ነ ፥ ፳፭ ። ሲኖዶ) ።

**ደዋ ፤ (ትግ ፥ ወዐረ)** ፤ መድኀኒት ፤ የሚያም ፥ የሚገድል ፥ ደዌ ፥ የሚኾን ፤ ወይም ፥ የሚያድን ።

**ደዌ ፤ (ያት)** ፤ በቁሙ ፤ በሽታ ፥ ሕማም ፥ የቈየ ፥ የዘገየ ፥ ዐብሮ ፥ የሚኖር ፤ ወይም ፥ ዐልፎ ፥ ኻያጅ ፤ ኀጢአት ፥ ፍትወት ፤ ደዌ ፥ ነፍስ ። ደዌ ፡ መሪር ፡ ወእኩይ ፡ ደዌ ፡ ከርሥ ፡፡ ለእመ ፡ አሐዩ ፡ እምዛቲ ፡ ደዌ ፡፡ ሐይወ ፡ እምደዌሁ ፡፡ ደዌ ፡ ሲሕ ፡፡ ነበረት ፡ ይእቲ ፡ ደዌ ፡ ውስተ ፡ ልብ ፡ (፪ዜና ፥ ፳፮ ፥ ፲፭ ። ፬ነገ ፥ ፩ ፥ ፪ ። ኢሳ፴፰ ፥ ፱ ። ሢራ፴ ፥ ፲፯ ። ሱቱ ፥ ዕዝ፩ ፥ ፳፪) ።

**አድወየ** ፤ አደወየ ፥ ድውይ ፥ አደረገ ፤ ደዌ ፥ አሳደረ ። መጽአ ፡ ላዕለ ፡ ርእሱ ፡ ሐሩር ፡ ወአድወዮ ፡ ወሞተ ፡፡ ለእሉ ፡ አድወዮሙ ፡ ፍርሀት ፡፡ እንተ ፡ አድወያ ፡ ጋኔን ፡፡ መከራት ፡ እለ ፡ ያደውያ ፡፡ ምርዓይ ፡ ማየ ፡ ዘያደዊ ፡ (ዮዲ፰ ፥ ፫ ። ጥበ፲፯ ፥ ፰ ። ሉቃ ፲፫ ፥ ፲፭ ። ማር ፥ ይሥ፪ ፥ ፲፭ ። ፍ ፥ ነ ፥ ፴፯) ።

**ደዊል ፤ ሎት ፤ (ዶለ ፤ ደወለ ፥ ይደውል ፥ ይዱል ። ዕብ ፥ ዳዌል ፤ አከበ ፥ ደወረ ፥ ጠመጠመ ፤ የፈትል)** ፤ መወሰን ፥ መከለል ፤ የቦታ ። መደወል ፤ ማቃጨል ። መደል ፥ ማግባት ፤ መክተት ። ዱላ ፥ ዳውላ ፥ ደልዷላ ፥ ዱለት ፥ ማለት ፥ የዚህ ፥ ዘር ፥ ነው ።

**ደወል ፤ (ብ ፥ አድዋል)** ፤ ዙሪያ ፥ ዳርቻ ፥ ጫፍ ፤ ወሰን ፥ ደንበር ፤ ቀበሌ ፥ አውራጃ ። ኢታፍልስ ፡ ደወለ ፡ ገራህት ፡ ዘእንበሩ ፡ አበው ፡፡ ዙሉ ፡ ደወሉ ፡ ዘዐውዱ ፡፡ ደወለ ፡ ጤሮስ ፡፡ ደወለ ፡ ፋርስ ፡፡ ተጋብኡ ፡ እምአድዋለ ፡ ብሔርሙ ፡ (ምሳ፳፫ ፥ ፲ ። ሕዝ፵፭ ፥ ፩ ። ዘካ፱ ፥ ፪ ። ኢሳ፯ ፥ ፲፰ ። ኅሐ፲፪ ፥ ፳፰) ።

**ደወል ፤ (ላት)** ፤ በቁሙ ፤ መጥቅ ፥ መረዋ ፥ ቃጭል ፤ የደንጊያ ፥ የንጨት ፥ የብረት ፤ ሲደወል ፥ በዙሪያው ፥ ባውራጃው ፥ የሚሰማ ። ከመ ፡ ድምፀ ፡ ብርት ፡ ዘይነቅ ፡ ባለው ፥ ደወል ፥ እንዲል ፥ (፩ቆሮ ፥ ፲፫ ፥ ፩) ።

**ተዳወለ** ፤ ተዋሰነ ፤ ተወሳሰነ ፥ ተዳካ ። እለ ፡ ይዳወልዎ ፡ እለ ፡ ዐውዱ ፡ (፫ነገ ፥ ፴ ፥ ፲፯) ።

**ደዊር ፤ ሮት ፤ (ዶረ ፥ ይደውር ፥ ይዱር ። ዕብ ፥ ዳር)** ፤ መማገድ ፥ መረብረብ ፤ ማንደድ ፥ መቈስቈስ ፤ እሳት ፥ መለኰስ ።

**ዱር ፤** በቁሙ ፤ ደን ፡ ጫካ ፤ ምማ ፡ ብዙ ፡ ዛፍና ፡ ዕንጨት ፡ ያለበት ። ታሕተ ፡ ዱር ፡ ተኀባእኩ ፡ (አዋል) ።

**ዶር ፤(ዐረ ፡ ዱር ፤ ዶረ ፡ ጠራ ፡ በራ) ፤** ጥሩ ፡ ወርቅ ፤ ዕንቍ ፡ ፈርጥ ፤ በወርቅ ፡ ኀርወት ፡ የሚሰካ ። ወማእከሌሆሙ ፡ ታቦተ ፡ ዶር ፡ ዘስርጉት ፡ በሡራኄ ፡ ጺዳል ። ታቦት ፡ ዘዶር ፡ (መጽ ፡ ምስ ። ቅዳ ፡ ሕር) ።

**ዶር ፤(ዕብራ) ፤** ትውልድ ፤ ዘመን ፤ የትውልድን ፡ ፍች ፡ ተመልከት ። በዶሮሙ ፡ (ዘፀ፴ ፡ ፲) ። በዐረብ ፡ ግን ፤ ደር ፡ ተራ ፤ ዱራ ፡ ዑደት ፡ ይኾናል ።

**ደውርሀ ፤(ይደወርሀ ፡ ይደውርሀ ፥ ደውርሆ ፤ አው ፡ ዶርሀወ ፡ ይዶርሁ ፥ ዶርሀዎ ፤ ተቀ ፡ ግ) ፤** በዛ ፡ ተባዛ ፤ ረባ ፡ ተንሻሻ ።

**ዶርሆ ፤(ብ ፡ ደዋርህ) ፤** ደሮ ፤ ብዙ ፡ የሚወልድ ፡ የሚዋለድ ፡ ለማዳ ፡ የቤት ፡ ወፍ ። ምስጢሩ ፡ መርባት ፡ ነው ፤ ወንድና ፡ ሴት ፡ ያስተባብራል ። በድምፀ ፡ ክነፊሆሙ ፡ ለሱራፌል ፡ ይነቁ ፡ ዶርሆ ። ዶርሆ ፡ ተባዕት ። ከመ ፡ ዶርሆ ፡ እንተ ፡ ታስተጋብእ ፡ ዕጐሊሃ ፡ ታሕተ ፡ ክነፊሃ ። መጋዝእ ፡ ደዋርህ ። ክልኤተ ፡ እልፈ ፡ ደዋርሀ ፡ (ቀሌ ። ምሳ፳፱ ፡ ፳፯ ። ማቴ፳፫ ፡ ፴፯ ። ፫ነገ ፡ ፬ ፤ ፳፫ ። ገድ ፡ ተክ) ።



ደዋርህ ፡

**ዳዊት ፤(ዕብ ፡ ዳዊድ) ፤** የሰው ፡ ስም ፤ የእስራኤል ፡ ንጉሥ ፤ ፍቁር ፡ መፍቀሬ ፡ (፩ነገ ፡ ፲፯ ፡ ፲፫) ።

**ዳዊት ፤(ዕብ ፡ ትሂሊም) ፤** የመጽሐፍ ፡ ስም ፤ መጽሐፈ ፡ መዝሙር ፤ ዳዊትና ፡ እንደ ፡ ዳዊት ፡ ያሉ ፤ እንአሳፍን ፡ የመሰሉ ፡ የግዜር ፡ መዘምራን ፡ የደረሱት ። ብዙው ፡ የዳዊት ፡ ስለ ፡ ኾነ ፡ በዳዊት ፡ ስም ፡ ተጠርቷል ፡ እንጂ ፡ ፻፶ው ፡ ኹሉ ፡ የርሱ ፡ አይደለም ፤ ይኸውም ፡ በያርእስቱ ፡ ይታወቃል ፤ ከምርኮም ፡ በኋላ ፡ የተደረሰ ፡ አለ ። ይልቁንም ፡ እግዚአ ፡ ጸወነ ፡ ኮንከነ ፡ ካለው ፡ ዠምሮ ፡ ምሕረተ ፡ ወፍትሐ ፡ እስከሚለው ፡ ድረስ ፡ ፲፩ዱ ፡ መዝሙር ፡ የሙሴ ፡ ይባላል ። ምእት ፡ ወኀምሳ ፡ ዳዊት ። ጸሎት ፡ ዘእምዳዊት ፡ በዜማ ፡ (ግንዘ) ።

**ዶታይም ፤ ን ፤** ስመ ፡ ሀገር ፤ የኢይዝራኤል ፡ ቅርብ ፡ አጠገብ ፡ (ዘፍ፴፯ ፡ ፲፯) ።

**ድሕይ ፤ ዮት ፤(ደሐየ ፡ ይድሒ ፡ ይድሐይ ። ዐረ ፡ ደሐ ። ሱር ፡ ዳሒሐ) ፤** መፍጨት ፡ ማድቀቅ ፤ መገርደፍ ፡ መሰለቅ ፤ ማዘር ፡ ማሽክርከር ፤ መግፋት ፡ መመለስ ፡ የመጅ ።

**ደሓዪ ፤ መድሐዪ ፤ ሕይ ፤** የሚፈጭ ፡ ፈጭታ ፤ ባለወፍጮ ።

**መድሔ ፤(ብ ፡ መዳሕይ) ፤** መፍጫ ፤ መጅ ፤ የወፍጮ ፡ ልጅ ፤ ወይም ፡ ግልገል ። መድሔ ፡ ማሕረጽ ። እመ ፡ ኮነ ፡ በማይ ፡ መድሔ ፡ ወምድርኒ ፡ ማሕረጸ ፡ (ዘዳ፳፬ ፡ ፮ ። አርጋ ፡ ፫) ።

**ድሐየ ፤—ቈፈረ ፤—ደኀየ ፤ ደኀነ ።**

**ድሒክ ፤ ከት ፤(ድሕከ ፤ ደሐከ ፡ ይድሕክ ፡ ይድሐክ) ፤** መዳኽ ፤ አጕንብሶ ፡ በእጅና ፡ በእግር ፡ መኼድ ፤ ወይም ፡ እጅን ፡ ተይዞ ፡ በእግር ፡ ብቻ ፡ መወናከር ፤ አካኼድና ፡ አረማመድ ፡ መማር ፤ ለፊደልም ፡ ይኾናል ። በድሒክ ፡ ውስተ ፡ መርሕብ ። ሐንካስ ፡ ድሕክ ፡ እስከ ፡ ይበጽሕ ፡ ኀበ ፡ አባ ፡ ሳሙኤል ፤ ይድሕክ ፡ ወይስእል ። ወድሕከ ፡ ዲበ ፡ ምድር ። ይድሕክ ፡ በነቢበ ፡ ፊደላት ፡ (መጽ ፡ ምስ ። ገድ ፡ ሳሙ ። ስንክ ፡ ሐም፲ ። አፈ ፡ ተ፳፯) ። ድኪ ፡ ዳክዬ ፤ ድኽ ፡ ድኵት ፡ ማለት ፡ ከዚህ ፡ ወጥቷል ።

**ድሑክ ፤** የዳኸ ፡ የሚድኽ ፤ ታናሽ ፡ እግረ ፡ ኰንትሽ ፡ ደካማ ፤ እንዳሽኮኮና ፡ እንደ ፡ ላጽቂት ፡ ያለ ፤ ማናቸውም ፡ ፍጥረት ።

**አድሐከ ፤** አዳኸ ፡ አስዳኸ ፡ መዳኽ ፡ አስተማረ ። በበ ፡ ንስቲት ፡ ያድሕኮ ፡ (አፈ ፡ ድ፮) ።

**ምድሓክ ፤** መዳኺያ ፤ ደጄ ፡ ወልወል ፡ መርሕብ ።

**ድሒል ፤ ሎት ፤(ድሕለ ፡ ይድሕል ፡ ይድሐል ። ዐረ ፡ ደሐለ) ፤** ድል ፡ መኾን ፤ መሸሽ ፡ መኰብለል ፤ ማምለጥ ፡ መራቅ ፤ መደበቅ ። መጽሐፍ ፡ ግን ፡ በድሕለ ፡ ፈንታ ፡ ተድሕለ ፡ ይላል ። አመ ፡ ተድሕሉ ፡ ወጕዩ ። እምገጸ ፡ ሄሮድስ ፡ ዘተድሕለ ። እመንግሥተ ፡ ዓለም ፡ ዘተድሕለ ፡ (አዋል ። ስንክ ፡ ሚያ፳ ። መስ፱) ።

**ዳሕል ፤** ድል ፡ ሽሽት ፡ ኰብለላ ።

**ዳሕመመ ፤—ቈፈረ ፤—ዳህምሞ ፡ ዳሀመመ ።**

**ድሕነ ፤—ዳነ ፤—ድኂን ፡ ድኀነ ።**

**ድሕንጻ ፤(ድ ፡ ሕንጻ) ፤** በቁሙ ፤ እደ ፡ ሕንጻ ፤ የከራርና ፡ የበገና ፡ የመሰንቆ ፡ መምቻ ፤ እድ ፥ ልጁ ፤ ሕንጻ ፥ እናቱ ። ንባቡ ፡ ሐንጸን ፤ ምስጢሩ ፡ ደጕጸንና ፡ ደነጸን ፡ ይመስላል ፤ ጥሬነቱ ፡ ግን ፡ የሐነጸ ፡ ነው ። እድ ፡ ውእድ ፡ ተብሎ ፡ ወደ ፡ ወ ፡ እንደ ፡ ኼደ ፤ ሕንጻም ፡ ድሕንጻ ፡ ተብሎ ፡ ወደ ፡ ደ ፡ መጥቷል ። በድሕንጻ ፡ መንፈስ ፡ ዝብጢ ፡ አውታረ ፡ መሰንቆሁ ፡ ለልብየ ። እብል ፡ በሳመ ፡ በልሳንየ ፡ ድሕንጻ ። አ ፡ ፎጢኖስ ፡ ክንክ ፡ እንዚራሁ ፡ ለመንፈስ ፡ ስይጣን ፡ ወመሰንቆሁ ፡ ለመንፈስ ፡ ሐሰት ፤ ወደጕጻክ ፡ በድሕንጻሁ ፡ (ባታት ። ስንክ ፡ ጥቅ፳፯ ። መጽ ፡ ምስ) ።

**ድሒፍ ፡ ፎት ፡ (ደሐፈ ፡ ይድሕፍ ፡ ይድሐፍ ። ዐብ ፡ ዳሐፍ)** ፡ መግፋት ፡ ማዳፋት ፡ መገፍተር ፡ ማጣደፍ ፡ ማባረር ።

**ዳሕፍ** ፡ ዳፋ ፡ ግፍ ፡ ግፊ ፡ ድቀት ፡ ፍዳ ፡ ጡር ፡ የክፉ ፡ ብድር ። (ትረት) ፡ የኃጥኡ ፡ ዳፋ ፡ ዳድቁን ፡ አዳፋ ። ኢያመሥጥ ፡ ኃጥእ ፡ እምነ ፡ ዳሕፍ ፡ (ሢራ ፲፮ ፡ ፲፫) ።

**ድሕጸ ፡—ዳጠ ፡—ድኂፅ ፡ ድኅፀ ።**

**ድሒር ፡ ሮት ፡ (ደሐረ ፡ ይድሕር ፡ ይድሐር ። ዐረ ፡ ደሐረ)** ፡ ማባረር ፡ መስደድ ፡ መፍታት ፡ መልቀቅ ፡ ከቤት ፡ ማሶጣት ፡ ማሰናበት ፡ (ማቴ ፲፱ ፡ ፱ ። ማር ፲ ፡ ፩ ፡ ፲፩ ። ሉቃ ፲፮ ፡ ፲፰) ዘይድሕር ፡ ብእሲቶ ፡ ዘእንበለ ፡ ትዘሙ ። ኢይድሕር ፡ ብእሲ ፡ ብእሲቶ ፡ (ቀሌ ። ዲድ ፡ ፴፫) ።

— ፡ መዳር ፡ ማጋባት ፡ ሴት ፡ ልጅን ፡ በሕግ ፡ በሥርዐት ፡ ለምኛዋ ፡ መስጠት ፡ ምስጢሩ ፡ ያው ፡ ማሶጣት ፡ ነው ። ለወንድ ፡ ልጅም ፡ ይነገራል ። (ግጥም ፡ ልጃገረድ ፡ ስላባቷ ፡ ስርግ) ፡ እንዲህ ፡ ያለ ፡ ዘመን ፡ የተበላልጨ ፡ አባቴ ፡ ተዳሩ ፡ እኔ ፡ ተቀምጬ ።

— ፡ ማዘዝ ፡ መፍቀድ ፡ አድርግ ፡ ማለት ፡ ምስጢሩ ፡ ከማሰናበት ፡ ይገባል ፡ ሙሴሰ ፡ በከመ ፡ እከየ ፡ ልብክሙ ፡ ደሐረክሙ ፡ ትኅድጉ ፡ አንስቲያክሙ ፡ (ማቴ ፲፱ ፡ ፰) ።

**ደሓሪ ፡ (ሪት ፡ ርያን ፡ ያት ፡ ሐርት)** ፡ የሚድር ፡ የሚፈታ ፡ የሚሰድ ፡ የሚያባርር ።

**ተድሕረ** ፡ ተዳረ ፡ ተፈታ ፡ ተለቀቀ ።

**ድሑር ፡ (ራን ፡ ራት ፡ ሐርት)** ፡ የተዳረ ፡ የተፈታ ፡ ገለሞታ ። ዘአውሰበ ፡ ድሕርተ ፡ አርኰሰ ፡ ሥጋሁ ፡ (ዲድ ፡ ፴፫) ።

**ደሐረ ፡—መረቀ ፡—ድኂር ፡ ደኀረ ።**

**ድሕር ፡—ኋላ ፡—ድኅር ።**

**ደሐሰ ፡—ዳሰ ፡ ፈጨ ፡ ረገጠ ፡—ፀሒስ ፡ ፀሐሰ ።**

**ድኂኅ ፡ ኆት ፡ (ደኀኀ ፡ ይድኅኅ ፡ ይድኅኅ)** ፡ መፋር ፡ መፈርፈር ፡ መጥረብ ፡ መውቀር ፡ የዋሻ ፡ የጕሬ ።

**ድኁኅ ፡ (ኃን ፡ ኃት ፡ ኅኃት ፡)** የተፋረ ፡ የተጠረበ ፡ የተወቀረ ፡ ጥርብ ፡ ውቅር ። አድባር ፡ ድኁኃን ፡ (ድጓ ። ማሕ፱ ፡ ፲፯ ። ፰ ፡ ፲፱) ። ዋሻ ፡ ፍርኵታ ፡ አንባነት ፡ ዕርድነት ፡ ያላቸው ፡ ደንጊያ ፡ የመላባቸው ፡ ማለት ፡ ነው ። ባለብሉዮች ፡ ግን ፡ ጽኑዓን ፡ ይሉታል ፡ ባለቅኔዎችም ፡ ደኅን ፡ ጸና ፡ ይላሉ ።

**ደኀየ ፡ (ደኅን)** ፡ ቈፈረ ፡ ማሰ ፡ አጠለቀ ፡ የጕድጓድ ። ግበ ፡ ከረየ ፡ ወደኀየ ። ጸናሒ ፡ ግበ ፡ ዘይድኂ ። ወይድኅይዎሙ ፡ (መዝ ፡ ፯ ። ደራሲ ። ዲድ ፡ ፲፯) ።

**ተድኅየ** ፡ ተቈፈረ ፡ ተማሰ ፡ ጠለቀ ፡ ጕደጐደ ።

**ድኁይ** ፡ የተቈፈረ ፡ የተማሰ ፡ ጥልቅ ። ተገድፈ ፡ ሥጋከ ፡ ውስተ ፡ ከርየተ ፡ ግብ ፡ ድኁይ ፡ (ደራሲ) ።

**ድኂን ፡ ኖት ፡ (ድኅነ ፡ ይድኅን ፡ ይድኅን ። ዐብ ፡ ያሸዕ ፡ ሂዋሼዕ)** ፡ መዳን ፡ ማምለጥ ፡ መውጣት ፡ ከተያዙ ፡ በኋላ ፡ ወይም ፡ ሳይያዙ ፡ መቅረት ፡ መትረፍ ፡ እንዳይያዙ ፡ መኾን ፡ መጠንቀቅ ፡ መጠበቅ ፡ በሕይወት ፡ መኖር ፡ መታደስ ፡ መለምለም ። (ዐጋዥ ፡ ረዳት ፡ ጠበቃ ፡ ወባት ፡ ዋስና ፡ መድን ፡ ተያዥ ፡ ማግኘት) ፡ እንደ ፡ አዳም ። ሕይወን ፡ ተመ ፡ የዚህ ፡ መንቲያ ፡ ነው ፡ ሐይወ ፡ የግእዝ ፡ ድኅነ ፡ ያማርኛ ። አልቦ ፡ ድኂን ። መዋዕለ ፡ ድኂን ። ድኂኖ ፡ እምባሕር ። ወድኅነ ፡ ጢጦስ ፡ በይእቲ ፡ ዕለት ፡ እምቀትል ፡ ሠለስተ ፡ ጊዜያተ ። ወልደተ ፡ ዓለም ፡ ለድኂን ። ይእቲ ፡ ዕፀ ፡ ድኅነት ፡ (ኩፋ ፡ ፴፱ ። አስቴ ፱ ፡ ፳፱ ። ግብ ፳፰ ፡ ፱ ። ዮሴፍ ። ጥበ ፭ ፡ ፲፱ ። ሄርማ) ።

**ዳኅን ፡ (ንት ፡ ናን ፡ ናት)** ፡ የዳነ ፡ የሚድን ፡ ደኅና ፡ ባለጤና ፡ ንጹሕ ፡ ጽሩይ ። ዳኅንኑ ፡ አቡ ፡ እወ ፡ ዳኅን ። ዳኅንኑ ፡ ማኅተም ። ርኢ ፡ ለእመ ፡ ዳኅናንኑ ፡ አኀዊከ ፡ ወአባግዒሆሙኒ ፡ (ገድ ፡ ተክ ። ዳን ፲፫ ፡ ፲፯ ። ዘፍ ፴፯ ፡ ፲፬ ። ዓ፫ ፡ ፳፯ ። ማቴ ፳፫ ፡ ፲፯ ፡ ፲፰) ። በዳኅና ፡ ፈንታ ፡ ዳኅን ፡ ይላል ። ወከነ ፡ ሰላም ፡ ወዳኅን ፡ ላዕለ ፡ ኵሉ ፡ በሓውርት ። ዳኅን ፡ ወሰላም ፡ (ገድ ፡ ተክ ። ፩ተሰ ፡ ፩ ፡ ፫ ። ቀሌ) ።

**ድኁን ፡ (ናን ፡ ናት ፡ ኅንት)** ፡ የዳነ ፡ ያመለጠ ፡ ደኅና ፡ የኾነ ፡ የተፈወሰ ፡ ጥዑይ ፡ ንጹሕ ፡ ጽሩይ ፡ ያልተነካ ። ኢድኁን ፡ አንተ ፡ በሞተ ፡ ኢየሱስ ። ይረስዮ ፡ ምስለ ፡ ድኁናን ። ድኁነ ፡ ምስማዕ ፡ ወንጻሬ ፡ ድኁን ፡ እምነውር ። ድኁን ፡ እነ ፡ እምሐሜት ። ክርስቶስ ፡ ድኁን ፡ ውእቱ ፡ እምኅጣውእ ። ነፍስ ፡ ድኅንት ፡ (መጽ ፡ ምስ ። ግንዘ ። ፍ ፡ ነ ፡ ፵፫ ፡ ፩ ። አፈ ፡ ድ፱ ። ፲፭ ። ድጓ) ።

**ዳኅነ ፡ ድኁነ** ፡ ደኅና ፡ በደኅና ፡ ወደ ፡ ደኅና ፡ ድኖ ፡ ደኅና ፡ ኹኖ ። ዳኅነ ፡ ሀሉ ። ዳኅነ ፡ ይትናገሩ ፡ ለቢጾሙ ። ትነብር ፡ ዳኅነ ። ለእመ ፡ ዳኅነ ፡ አቶክሙ ። ይሬኢ ፡ ዳኅነ ። ወርእየ ፡ ዳኅነ ። መጽአ ፡ ድኁነ ፡ (ግብ ፳፫ ፡ ፴ ። ኤር ፱ ፡ ፰ ። ኢዮ ፲፩ ፡ ፲፰ ። ጦቢ ፭ ፡ ፲፯ ፡ ፲፩ ፡ ፯ ። ማር ፰ ፡ ፳፭ ። ዘረፋ) ።

**ድኅነት** ፡ መዳን ፡ መፈወስ ፡ ደኅንነት ፡ ጤና ። ወአንከሩ ፡ እምድኅነቱ ። እምአይቴ ፡ ተሰፈዉ ፡ እሉ ፡ ድኅነተ ፡ ሕፃን ። ድኅነተ ፡ ልብ ፡ ወአባል ። ድኅነት ፡ እምደዌያት ። ጾመ ፡ ድኅነት ፡ ምሕላ ፡ ድኅነት ፡ (ስንክ ፡ ሐምሌ ፱ ። አፈ ፡ ድጽ፯ ። ፍ ፡ ነ ፡ ፱ ። መር ፡ ዕዉ ። ድጓ) ።

**ዳኅና** ፡ ደኅንነት ፡ ጤና ፡ ሰላም ፡ ትንሣኤ ፡ ሕይወት ። አልቦ ፡ ዘይስእል ፡ ዳኅናኪ ። ተስእሎ ፡ በእንተ ፡ ዳኅናሁ ። ይዜንዉከ ፡ ዳኅና ፡ ብሔር ። እነግር ፡ ጽድቀከ ፡ በዳኅናየ ። በእንተ ፡ መንክር ፡ ዳኅናሁ ፡ (ኤር ፲፭ ፡ ፭ ። ፪ነገ ፡ ፲፩ ፡ ፯ ። ፩ነገ ፡ ፲ ፡ ፱ ። ኢሳ ፴፰ ፡

፳ ። ጥበ፳ ፡ ፪) ። በዳኅን ፡ ፈንታ ፡ ዳኅና ፡ ይባል ፤ ስሕተት ፡ ነው ። ነበረት ፡ ሀገር ፡ ዳኅና ፡ (፪ነገ ፡ ፲፩ ፡ ፳) ።

**አድኀነ** ፤ አዳነ ፤ አስዳነ ፤ ታደገ ፡ አወጣ ፤ ረዳ ፡ ዐገዘ ። ያድኅን ፡ በዕለተ ፡ ምንዳቤ ። ስእኑ ፡ አድኅኖ ። አድኅኑ ፡ ግፉዐ ። አድኅን ፡ ርእሰከ ፡ (ሚራ፪ ፡ ፲፩ ። ኢዮ፪ ፡ ፳ ። ኢሳ፩ ፡ ፲፯ ። ማቴ፳፯ ፡ ፵) ።

**አድኅኖ ፡ ት** ፤ ማዳን ፤ መታደግ ፡ መቤዠት ፤ ነጻ ፡ ማውጣት ፤ ትድግና ። በእንተ ፡ ሕቢት ፡ ወአድኅኖ ፤ አድኅኖሰ ፡ ዘነፍስ ፡ ውእቱ ፡ ወተሐብዮ ፡ ዘንዋይ ። ዘእግዚ ፡ አድኅኖ ። ወንትፌሣሕ ፡ በአድኅኖትከ ፡ (ፍ ፡ ነ ፡ ፳፯ ። መዝ ፡ ፫ ። ፱) ።

**አድኃኒ ፤ መድኅኒ ፤ (ኒት ፡ ንያን ፡ ያት)** ፤ የሚያድን ፡ የሚቤዥ ፡ የሚታደግ ፤ ታዳጊ ። የሰው ፡ ስም ። መድኅኔ ፡ ኵሉ ። መድኅንየ ። መድኅኒነ ፡ ኢየሱስ ፡ ክርስቶስ ። መድኃኔ ፡ ዓለም ። መድኅኒት ፡ መቤዠዊት ። አባ ፡ አድኃኒ ፡ (ጥበ፲፮ ፡ ፯ ። መዝ ፡ ፲፯ ። ፊልጵ፫ ፡ ፳ ። ቀሌ ። ድጓ ። ስንክ ፡ ጥር፫) ።

**መድኅን** ፤ ዝኒ ፡ ከማሁ ፤ የሚያድን ፡ አዳኝ ፤ በቁሙ ፡ መድን ፡ ዋስ ፡ ተያዥ ፡ ቤዛ ፡ ነጻ ፡ አውጭ ። እምጽዮን ፡ ይወፅእ ፡ መድኅን ። መድኅነ ፡ ዓለም ። ተወልደ ፡ ለክሙ ፡ ዮም ፡ መድኅን ። ውስተ ፡ ዘመድኅን ፡ መርሶ ። ወልቃሕስ ፡ ይደሉ ፡ ከመ ፡ ይኩን ፡ በአኅዝ ፡ አው ፡ በትሕቢት ፡ አው ፡ በመድኅን ፤ አው ፡ በመጽሐፍ ፡ እንተ ፡ ውስቴታ ፡ ሰማዕት ። መድኅነ ፡ ኮነ ፡ ሎቱ ። ወለብእሲት ፡ ኢይትወከፉ ፡ እምኔሃ ፡ መድኅነ ፡ ወኢተሐብዮ ፡ (ሮሜ፲፩ ፡ ፳፯ ። ዮሐ፬ ፡ ፵፪ ። ሉቃ፪ ፡ ፲፩ ። ስንክ ፡ ጳግ፩ ። ፍ ፡ ነ ፡ ፳፯) ።

**መድኅኒት ፤ (ታት)** ፤ በቁሙ ፤ መዳኛ ፡ ማዳኛ ፡ መዳኒት ፡ ፈውስ ፤ የሚያድን ። መድኅኒት ፡ በዘ ይትፌወስ ፡ ቍስል ። ጸሎትሰ ፡ መድኅኒት ፡ ይእቲ ። መድኅኒተ ፡ ዓለም ፡ ኮነ ፡ ደመ ፡ ጽጌኪ ፡ ክርስቶስ ። ጌራ ፡ መድኅኒት ። መድኅኒታት ፡ (አርጋ ። አፈ ፡ ተ ፳፯ ። ደራሲ ። ኢሳ፶፱ ፡ ፲፯ ። ግንዘ) ። ድኂን ፡ ድኅንት ፡ በማለት ፡ ፈንታ ፡ መድኅኒት ፡ ይባላል ፡ (፩ነገ ፡ ፲፩ ፡ ፱ ። ፩ጴጥ ፡ ፩ ፡ ፱) ። መሥዋዕተ ፡ መድኅኒት ። ዘይፈቅድ ፡ መድኅኒተ ፡ እምንጣውኢሁ ፡ (ዓሞ፭ ፡ ፳፪ ። ፈ ፡ መ ፡ ፪ ፡ ፩) ።

**ተድኅነ** ፤ ተዳነ ፡ ተዋሰ ፤ መድን ፡ ተያዥ ፡ ኾነ ፤ አዳናለኹ ፡ አለ ። ወመድኅነ ፡ ነፍስኒ ፡ ይደልዎ ፡ ከመ ፡ ያምጽእ ፡ ዘተድኅነ ፤ ወይኩን ፡ ቃለ ፡ ዘቲ ፡ ተድኅኖ ፡ ከመ ፡ ይበል ፡ ተድኅንኩ ፡ ለአብጽሖተ ፡ እገሌ ፡ ለእገሌ ፤ አው ፡ ተድኅንኩ ፡ ለእገሌ ፡ ገጸ ፡ እገሌ ፤ አው ፡ ተድኅኖተ ፡ እገሌ ፡ ላዕሌየ ። ኢይደሉ ፡ ተድኅኖቱ ፡ ለዘይደሉ ፡ ላዕሌሁ ፡ ቀትል ፡ (ፍ ፡ ነ ፡ ፳፯) ።

**ድኅንጻ ፤—በቁሙ ፤—ድሕንጻ ።**

**ድኂፅ ፤ ፆት ፤ (ድኅፀ ፡ ይድኅፅ ፡ ይድኅፅ ። ዐረ ፡ ደሐፀ)** ፤ መዳጥ ፡ መሰናከል ፤ መውደቅ ፤ የእግር ፡ የቃል ። ከመ ፡ ኢይድኅፀ ፡ በኵናተ ። ይኄይስ ፡ ትድኅፀ ፡ ወትደቅ ፡ ውስተ ፡ ምድር ፡ እምትድኅፀ ፡ በአፉከ ። ትድኅፀ ፡ ምክሩ ። ኢንድኅፀ ፡ በኀጢአት ። ከመ ፡ ኢንድኅፀ ፡ እምርትዕት ፡ ሃይማኖት ፡ (መዝ ፲፮ ። ሚራ፳ ፡ ፲፰ ። ኢዮ፲፰ ፡ ፯ ። ዲድ ፡ ፬ ። ፳፭) ። (ጥጨ) መጨንገፍ ፡ መውረድ ፤ ጭንጋፍ ፡ መኾን ፤ የፅንስ ፡ የሽል ። መዳጥ ፡ መደፍጠጥ ፤ መርገጥ ፡ መዠለጥ ፡ (ዐማርኛ) ።

**ድኁፅ ፤ ድኍፅ ፤ (ፃን ፡ ፃት ፡ ኅፅት)** ፤ የዳጠ ፤ የተሰናከለ ። የተዳጠ ፡ የተደፈጠጠ ። የሚድጥ ፡ ዳጭ ፡ (ገቢር) ።

**ድኅፀት** ፤ መዳጥ ፡ (ጥዳ) መዳጥ ፡ አዳዳጥ ፡ ድጦሽ ፤ መሰናከል ፡ (ፊልክ ፡ ፻፹፩ ። ፈላስ) ።

**ዳኅፅ ፤ (ፃት)** ፤ ዳጥ ፡ ድጥ ፤ መሰናከል ፡ ዕንቅፋት ፤ ኀጢአት ፤ ሕገ ፡ ወጥ ፡ ሥራ ። ጭንጋፍ ፡ ውርጃ ፡ ሽል ። ዳኅፀ ፡ ወጽልመት ። ያመጽኡ ፡ ዳኅፀ ፡ ለሕዝብ ። አበሳነ ፡ ስረይ ፡ ወዳኅፃቲነ ፡ እምሕግ ። ይኄይስ ፡ እምኔሁ ፡ ዳኅፀ ፡ (መዝ ፡ ፴፬ ። ዳን፲፩ ፡ ፴፪ ። መክ፮ ፡ ፫) ።

**አድኀፀ** ፤ አዳጠ ፤ አስዳጠ ፤ ዐንቀፈ ፡ አሰናከለ ፤ ሰረ፱ ፡ ዘረጠጠ ፤ ለመጣል ። አድኅፆ ፡ ለላእክ ። ኢይደግም ፡ አድኅፆተ ፡ እግሮሙ ። ተዐቀባ ፡ ኢታድኅፀከ ፡ ልሳንከ ። ኵሎሙ ፡ ዘያድኅፀ ። አድኅፀክዎ ፡ ለዲያብሎስ ፡ ወነሣትክዎ ፡ እመንበሩ ፡ (ዮሴፍ ። ፪ነገ ፡ ፳፩ ፡ ፳ ። ሚራ፳፫ ፡ ፳፯ ። ኢሳ፳ ፡ ፲፱ ። ቀሌ) ።

—፤ ጨነገፈ ፡ አስጨነገፈ ፡ አሶረደ ፤ ከመ ፡ ፃእፃእ ፡ ዘአድኅፀቶ ፡ ማሕፀነ ፡ እሙ ። ብእሲት ፡ ዘትሰቲ ፡ ፈውሰ ፡ ከመ ፡ ታድኅፅ ፡ ፃእፃአ ፡ እማሕፀና ፡ (ኢዮ፫ ፡ ፲፯ ። ፈ ፡ መ ፡ ፱ ፡ ፱ ። ዘፀ፳፩ ፡ ፳፪ ፡ ፳፫ ። ፍ ፡ ነ ፡ ፵፫) ። በአድኅፀ ፡ ፈንታ ፡ ድኅፀ ፡ ይባላል ፤ አያስኬድም ፡ (ኢዮ ፳፩ ፡ ፲) ።

**መድኅፂ ፤ ኅፅ** ፤ የሚያድጥ ፡ የሚያሰናክል ፡ አሰናካይ ። እሬኢ ፡ መድኅፂነ ፡ (ሱቱ ፡ ዕዝ፳ ፡ ፳፪) ።

**ምድኃፅ ፤ (ፃት)** ፤ (ጥዳ) መዳጫ ፡ መሰናከያ ፤ ቦታ ፡ ምክንያት ።

**ድኂር ፤ ሮት ፤ (ደኅረ ፡ ይድኅር ፡ ይድኅር ። አኀረ ። ዐረ ፡ ደኅረ ፤ ንእሰ)** ፤ መቈየት ፡ መዘግየት ፤ ማፈግፈግ ፡ ወደ ፡ ኋላ ፡ ማለት ፡ በኋላ ፡ መቅረት ፤ ኋለኛ ፡ መጨረሻ ፡ መኾን ፤ በግብር ፡ በነገር ፡ በማናቸውም ። ከመ ፡ ይትመየጥ ፡ ወኢይድኅር ። ለእመ ፡ ነበረ ፡ ሕዝባዊ ፡ ሠለስተ ፡ ሰንበተ ፡ ድኂሮ ፡ እምቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ይክልእዎ ፡ ትድምርተ ፡ (ዮሴፍ ። ቀኖና ፡ ግንር) ። ብዙ ፡ መጽሐፍ ፡ በደኀረ ፡ ፈንታ ፡ ተድኅረ ፡ ይባላል ፤ ስሕተት ፡ ነው ። ተድኂሮ ፡ መጽአ ። ኢይበድሩ ፡ ወኢይዴኀሩ ፡ አሐደ ፡ ዕለተ ። በእንተ ፡ እለ ፡ ተድኅሩ ። እመሂ ፡ ኢጲስቆጶስ ፡ ተድኅረ ፡ እምስብሐተ ፡ ነግህ ። ወኢተድኅረ ፡ አሐዱ ፡ እምኔሆሙ ፡ ለገቢረ ፡ ዝንቱ ። እንበለ ፡ ተድኅሮ ፡ (ኪዳ ። ሔኖ፹፱ ፡ ፲፪ ። ቅዳ ። ቀሌ ። ዮሴፍ ። ስንክ ፡ ኅዳ፲) ።

—፤ መመረቅ ፤ መባረክ ፤ ማመስገን ። ሶበ ፡ አሐዱ ፡ ይድኅር ፡ ወካልኡ ፡ ይረግም ። ለጸጋዊ ፡ ይድኅርዎ ፡ በሥነ ፡ ምግባሩ ። ድኅረኒ ፡ ዘይመውት ። ይድኅሩኒ ፡ ስእናን ። ይድኅሩኒ ፡ አራዊተ ፡ ገዳም ። ይረግሙነ ፡ ወንሕነ ፡ ንድኅሮሙ ። በአፉሆሙ ፡ ይድኅሩ ፡ ወበልቦሙ ፡ ይረግሙ ፡ (ሚራ፴፩ ፡ ፳፱ ። ፴፱ ፡ ፳፫ ። ኢዮ፳፱ ፡ ፲፫ ። ፴፩ ፡ ፲፱ ። ኢሳ፵፫ ፡ ፳ ። ፩ቆሮ ፡ ፬ ፡ ፲፪ ። መዝ ፡ ፷፩ ። ፸፩) ።

**ደኃሪ ፤(ሪት ፡ ርያን ፡ ያት ፤ ኀርት)** ፤ ኋለኛ ፡ የኋላ ፡ መጨረሻ ፤ ታናሽ ፡ ተከታይ ። አግሪጳስ ፡ ውእቱ ፡ ደኃሪ ፡ እምእለ ፡ ነግሡ ፡ በይሁዳ ። ደኃሪ ፡ ጸላኢ ። ደኃሪተ ፡ ገመስ ። እሙንቱ ፡ ደኃርያን ። ቀደምት ፡ ወደኀርት ፡ (ዮሴፍ ። ፩ቆሮ ፡ ፲፭ ፡ ፳፮ ። ማቴ፳ ፡ ፳፮ ። ዘኍ፪ ፡ ፴፭ ። ፪ዜና ፡ ፳፮ ፡ ፳፪) ።

**ደኃራዊ ፤ ይ ፤** ዝኒ ፡ ከማሁ ፤ ሀርቃኖስ ፡ ደኃራዊ ። ከመ ፡ ያቅም ፡ ደኃራየ ፡ (ዮሴፍ ። ዕብ፲ ፡ ፱) ።

**ድኅር ፤(ራት)** ፤ ኋላ ፡ ዠርባ ፤ ከማኸራት ፡ እስከ ፡ ተረከዝ ። በዠርባ ፡ አንጻር ፡ ያለ ፡ ቦታ ፤ የኋላ ፡ ኋላ ፤ ጓሮ ። ድኅሬሆሙ ፡ ለእልክቱ ፡ አልሕምት ፡ ይኔጽር ፡ ውስጠ ። ገቦሃ ፡ ዘድኅር ። ዘባነ ፡ እንተ ፡ ድኅር ፡ (፪ዜና ፡ ፬ ፡ ፬ ። ግብ፳፯ ፡ ፵፩ ። ቅዳ ፡ ሕር) ።

**ድኅረ ፤(ዐቢይና ፡ ደቂቅ ፡ አገባብ)** ፤ ኋላ ፡ በኋላ ፤ ወደ ፡ ኋላ ። ምስጢሩ ፡ ጊዜ ፡ ነው ፤ እም ፡ በ ፡ እንተ ፡ ይስማሙታል ። ዐቢይ ፡ ሲኾን ፤ እምድኅረ ፡ ተደሩ ፤ ወእምድኅረ ፡ መስሑ ፡ እያለ ፡ በቀዳማይ ፡ ይገባል ። ደቂቅ ፡ ሲኾን ፡ በቦታ ፡ በጊዜ ፡ ይገባል ። በማዕኩ ፡ ዐድኅሬየ ። ቀመት ፡ እንተ ፡ ድኅሬሁ ። ድኅረ ፡ ማዕጾ ። ፈረሱ ፡ ለፈርያን ፡ ይቤ ፡ ድኅረ ፡ ድኅረ ፤ እስመ ፡ እግሩ ፡ ኢለመደ ፡ ባሕረ ፤ ቦታ ፡ (ሕዝ፫ ፡ ፲፪ ። ሉቃ፳ ፡ ፵፱ ። ኢሳ፶፯ ፡ ፰ ። ቅኔ) ። እምድኅረ ፡ ሐቅ ። እምድኅረ ፡ ፍልሰተ ፡ ባቢሎን ። ወድኅረ ፡ ሖሎሙ ፡ አስተርአየኒ ፡ ሊተ ። ቅድመ ፡ ጠይቅ ፡ ወድኅረ ፡ ትጌሥጽ ፤ ጊዜ ፡ (ማር፲፱ ፡ ፯ ። ማቴ፩ ፡ ፲፪ ። ፩ቆሮ ፡ ፲፭ ፡ ፰ ። ሢራ፲፩ ፡ ፯) ። (ዕር፲፱ ፡ ቍ፫፱) ።

**ድኅሪት ፤** ኋሊት ፤ የኋሊት ፤ ኋላ ፤ እንግሊላ ። የሐርስ ፡ ድኅሪት ። እቡራን ፡ ድኅሪት ። ኢገብኡ ፡ ድኅሪተ ። ከመ ፡ ይደቀ ፡ ድኅሪት ፡ (ሉቃ፱ ፡ ፷፪ ። መዋሥ ። ስንክ ፡ ሐም፳፩ ። ኢሳ፳፰ ፡ ፲፫) ።

**ድኅርና ፤** ደኃራዊነት ፤ ኋለኛ ፡ መጨረሻ ፡ መኾን ። ለቅድምናከ ፡ ወለድኅርናከ ፡ (ፍ ፡ ነ ፡ መቅ) ።

**አድኅረ ፤**(አስመረቀ ፡ አስመሰገነ) ፡ አቈየ ፤ አስቈየ ፤ አዘገየ ። አስከተለ ፤ በኋላ ፡ አደረገ ። አድኅሩ ፡ ፍትሐ ፡ ላዕሌሁ ። እመ ፡ አድኅርከኒ ። አድኅርከዋ ፡ እምተበዞሮ ፤ አቈየ ፡ (ዮሴፍ ። አዋል) ። ሞተ ፡ በሃይማኖት ፡ ወአድኅረ ፡ ሰብአ ፡ ድኅሬሁ ። አድኅረ ፡ መብዝኀተ ፡ ሰብኡ ፡ ምስለ ፡ እኍሁ ። አ ፡ አብዳን ፡ እፎ ፡ አድኅርክምዎ ፡ ለመለኮተ ፡ አምላክነ ፡ ጰራቅሊጦስ ፡ እምጥንተ ፡ ህላዌሆሙ ፡ ለፍጡራን ፡ (ዮሴፍ ። መጽምስ) ። በአድኅረ ፡ ፈንታ ፡ አስተደ(ድ)ኅረ ፡ ይላል ፤ ፍችው ፡ አድራጊና ፡ አስደራጊ ፡ ነው ፤ ዳ ፡ ካዓስ ፡ አደራራጊነት ፡ የለውም ። ለእመ ፡ አንተ ፡ አስተደኀርከ ፡ ቀቲሎታ ። አስተድኅረ ፡ ወልዶ ፡ ጢጦስ ፡ ይዕግታ ፡ ለሀገር ። ኢታስተድኅሮ ፡ እስከ ፡ ጌሠም ። ወያስተድኅሩ ፡ መብልዖሙ ፡ እስከ ፡ ይመሲ ፡ (ዮሴፍ ። ፍ ፡ ነ ፡ ፫ ። አቡሻ ፡ ፲፪ ። ዮሐ፪ ፡ ፲) ።

**አስተዳኅረ ፤** አከታተለ ፤ አራደፈ ። አስተዳኅረ ፡ መጻዝኒሃ ፡ (ቅዳ ፡ ኤጲ) ።

**ተድኅረ ፤** ተመረቀ ፤ ተባረከ ፤ ተመሰገነ ።

**ድኁር ፤(ራን ፡ ራት ፡ ኅርት)** ፤ የተመረቀ ፡ ምሩቅ ። የቈየ ፡ የዘገየ ።

**ድኁር ፤(ዐማርኛ)** ፤ ዐሜር ፡ ግሜር ፤ ድንክ ፡ ጐባጣ ፤ ሕጹጽ ፡ ታናሽ ። ግናይን ፡ ተመልከት ።

**መድኅር ፤(ርት ፡ ራን ፡ ራት)** ፤ ቅጽልና ፡ ጥሬ ። የሚመርቅ ፡ መራቂ ፤ የሚያቈይ ፡ የሚያዘገይ ፤ ቅጽል ። ምርቃት ፡ በረከት ፡ ምስጋና ፡ ብፅዓን ፤ ጥሬ ። መድኅረ ፡ አብ ። መርገም ፡ ወመድኅር ። አቅረብነ ፡ ለክሙ ፡ መርገመ ፡ ወመድኅረ ፡ (ሚራ፫ ፡ ፱ ። ፪ቆሮ ፡ ፮ ፡ ፰ ። ቀሌ) ።

**ደይበ ፤ በት ፤(ደየበ ፡ ይዴይብ ፡ ይደይብ ። ትግሬ)** ፤ ማረግ ፡ ወደ ፡ ላይ ፡ መውጣት ፤ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ማለት ፤ በላይ ፡ መኾን ። መመደብ ፤ መደብ ፡ ዕርከን ፡ መሥራት ። ዐርገንና ፡ ለዐለን ፡ እይ ፤ የዚህ ፡ አግዋር ፡ ናቸው ።

**ዲብ ፤ ዲበ ፤(ደቂቅ ፡ አገባብ)** ፤ ላይ ፡ በላይ ፤ ወደ ፡ ስለ ፡ ይኾናል ፤ ሳይናበብ ፡ ሳይዘረዘር ፡ እንደ ፡ ላዕለ ፡ ብቻውን ፡ አይነገርም ። ዘሐነጸ ፡ ቤቶ ፡ ዲበ ፡ ኰዅሕ ። ኢይትኀደግ ፡ እብን ፡ ዲበ ፡ እብን ። ሀሎ ፡ ዲቤሁ ፡ ልብስ ፡ ጥቁብ ። ከልብ ፡ ይገብእ ፡ ዲበ ፡ ቅያኡ ። ዲበ ፡ ሀጕሉ ፡ ውሉዶሙ ፡ ይግዕሩ ፡ (ማቴ፯ ፡ ፳፬ ። ፳፬ ፡ ፪ ። ፊልክ ፡ ፻፴፮ ። ምሳ፳፮ ፡ ፲፩ ። ሔኖ፲፪ ፡ ፮) ። ኀበና ፡ ዲበ ፡ ይወራረሳሉ ፤ ስለዚህ ፡ በኀበ ፡ ፈንታ ፡ ዲበ ፡ ይላል ። ነበረ ፡ ዲበ ፡ ዐዘቅት ፡ (ዘፀ፪ ፡ ፲፭) ። የወዲያኛው ፡ ትግሬም ፡ ወደ ፡ ሲል ፡ ዲብ ፡ ይላል ። ባማርኛ ፡ ግን ፡ ጕባ ፡ ጕባታ ፡ ታናሽ ፡ ቊሊልታ ፡ አዳጋ ፡ ቦታ ፤ እንዳርባጫ ፡ ያለ ፡ ማለት ፡ ነው ። (ተረት) ፤ የወዳጅ ፡ ኽርብ ፤ ልጁን ፡ ከዲብ ። ድብኝትም ፡ የዚሁ ፡ ዘር ፡ ነው ።

**መደብ ፤(ዕብ ፡ ዐሩጋ ፤ ዐዛራ)** ፤ በቁሙ ፤ ዕርከን ፡ ምዕራግ ፤ መውጫ ፡ መወጣጫ ፡ ስፋትና ፡ ከፍታ ፡ ያለው ፤ ላታክልትም ፡ ይነገራል ፡ (ሕዝ፲፯ ፡ ፲ ። ፵፫ ፡ ፲፱ ፡ ፲፯ ፡ ፳) ። ደመ ፡ ቅሥፈቱ ፡ ያርሕስ ፡ መደበ ። ተፈትሑ ፡ ሖሩ ፡ አራዊት ፡ ወበልዑ ፡ ስጕርንደ ፡ ሰማንያ ፡ መደበ ፡ (ስንክ ፡ ጳግ፱ ። ገድ ፡ ተክ) ።

—፤ የርባታ ፡ ክፍል ፡ ዐሥሩ ፡ ስራዊት ፡ ወይም ፡ መራሕያን ።

**መደባዊ ፤ ይ ፤** መደበኛ ፤ መደባም ፡ ባለመደብ ፤ የመደብ ። ባላባት ፡ ዋና ፡ ደቀ ፡ መደባይ ፡ (ገድ ተክ) ።

**መደቤና ፤(ዕብ ፡ ማድሜና)** ፤ ስመ ፡ ሀገር ፡ የብንያም ፡ ክፍል ፡ (ኢሳ፲ ፡ ፴፩) ።

**ጀይብ ፤(ዐረብ)** ፤ የቀሚስ ፡ ሕፅን ፡ ስላጤ ፤ በስላጤው ፡ ላይ ፡ የሚሰፋ ፡ ኪስ ፡ ከረጢት ፤ ውስጠ ፡ ክፍት ፡ ኹኖ ፡ ማረሚያ ፡ ገንዘብ ፡ የሚከት ፡ (ፈ ፡ መ ፡ ፴፩ ፡ ፩) ። ምስጢሩ ፡ የዲብና ፡ የድብኝት ፡ ነው ።

**ዲያብሎስ ፤(ጽር ፡ ዲያቦሎስ ። ዐረ ፡ ኢብሊስ)** ፤ በቁሙ ፤ ሰይጣን ፡ ጋኔን ፡ ክፉ ፡ መልአክ ፤ የሰይጣንን ፡ ፍች ፡ ተመልከት ፤ ከዚህ ፡ ጋራ ፡ አንድ ፡ ነው ። ባስመጣፎች ፡ ግን ፤ ዐማዊ ፡ ገፋዊ ፡ ጸናኒ ፡ ፈታዊ ፤ ኀማሚ ፡ አምላክና ፤ ነድ ፡ ውዑይ ፡ ያፍ ፡ ሰራሪ ፡ ይሉታል ፤ ዘይቤው ፡ ከደየበና ፡ ከደበወ ፤ ምስጢሩ ፡ ከሰይጣን ፡ ይስማማል ፡ (ጥበ፪ ፡ ፳፬ ። ማቴ፬ ፡ ፩ ። ፲፫ ፡ ፴፱) ።

**ዴግኖ ፤ ኖት ፤(ዴገነ ፡ ይዴግን ፡ ይዴግን ። ትግ ፡ ዳገነ ። ዕብ ፡ ዳዮግ ፤ አሥግሮ ፡ ዓሣ)** ፤ መከተል ፡ ማባረር ፤ መሸት ፡ ማደን ፤ ማጥመድ ፡ ማስብ ፡ መደገን ፤ ስመያዝ ፡ ስመግደል ፡ ስመማረክ ። ዴግንየ ፡ እእኅዞሙ ። ዴግንዎ ፡ ወትእኅዝዎ ። ይዴግንዋ ፡ ለአሪትሙ ። ለእመ ፡ ዴገንካ ፡ ለጽድቅ ፡ ትረክብ ። ይዴግን ፡ ኅበ ፡ ሐመልማል ፡ (ዘፀ፲፭ ፡ ፱ ። መዝ ፡ ፸ ። ሮሜ፱ ፡ ፴፩ ። ሢራ፳፯ ፡ ፰ ። ኢዮ፴፱ ፡ ፰) ።

**ዴጋኒ ፤(ኒት ፡ ንያን ፡ ያት ፤ ዴገንት)** ፤ ደጋኝ ፡ አጥማጅ ፤ ዐዳኝ ። የሚከተል ፡ ተከታይ ፤ ፈላጊ ፡ አባራሪ ፡ ዠግና ፤ ጐቤ ፡ ገሥጋሽ ። ኤዎስጣቴዎስ ፡ አሠረ ፡ ቶማስ ፡ ዴጋኒ ። ዴጋኔ ፡ ፀሩ ፡ (ድጓ ። ስንክ ፡ ሚያ፳፰) ።

**ዴጋን ፤ ደጋን ፤(ናት)** ፤ በቁሙ ፤ ቀስት ፡ የንጨት ፡ የብረት ፤ ጉባባ ፡ ጉባጣ ፤ ጠማማ ። ደጋን ፡ ያማርኛ ፡ ቀስት ፡ የግእዝ ፡ ነው ። እስ ፡ ፍናዊሆሙ ፡ መብእስ ፡ ወደጋን ፡ መንኩራኵሮሙ ፡ (ምሳ፪ ፡ ፲፭) ።



ደጋን ፡

**አዴገነ** ፤ አስደገነ ፤ አስከተለ ፡ ተከታይ ፡ ላከ ። ወአዴገንዎ ፡ ውስተ ፡ ለኪስ ፡ ወቀተልዎ ፡ (፬ነገ ፡ ፲፬ ፡ ፲፱) ።

**ዴድዮ ፤ ዮት ፤(ዴደየ ፡ ይዴዲ ፡ ይዴዲ ። ዕብ ፡ ዳዴህ ፤ ሂዳዴ)** ፤ መዝለል ፡ መፈንጠት ፤ እንጥር ፡ ፍንጥር ፡ ድቅ ፡ ድቅ ፡ ማለት ፡ የግልገል ፡ የጥጃ ። አካኼድ ፡ አረማመድ ፡ መማር ፤ ማስተማር ፤ ዳዲ ፡ ዳዲ ፡ ወይም ፡ እቴ ፡ ሥማሬ ፤ ታቴ ፡ ሥማሬ ፡ ማለት ፡ የሕፃን ፡ የሞግዚት ።

**ዴዴ ፤(ብ ፡ ዴዴያት ፤ ዴዳያት ፤ ዴድያት)** ፤ ደጃፍ ፡ በረንዳ ፡ ወልወል ፤ የቤት ፡ መዠመሪያ ፡ ክፍል ፤ ከበር ፡ ከቅጥር ፡ በውስጥ ፡ ያለ ፡ ቦታ ፤ ወይም ፡ ታላቅ ፡ የውጭ ፡ በር ፤ ደጀ ፡ ሰላም ። ዴዴሁ ፡ ለባዕል ። እስ ፡ ውስተ ፡ ዴዴ ፡ ቤት ፡ ክር ። በዴዴያተ ፡ አብያት ። ዴድያተ ፡ አንቀጽ ። ወዴዳያቲሃ ፡ (ሉቃ፲፮ ፡ ፳ ። ቀሌ ። ሕዝ፴፫ ፡ ፴ ። ኤር፩ ፡ ፲፭ ። ራእ፳፩ ፡ ፳፩) ።

**ዲዲሞስ ፤(ጽርእ ። ዕብ ፡ ቶማእ)** ፤ መንታዊ ፤ መንቲያ ፡ ማለት ፡ ነው ፤ ቶማስን ፡ እይ ፡ (ዮሐ፲፩ ፡ ፲፮) ።

**ዴዳን ፤(ዕብ ፡ ድዳን)** ፤ ስመ ፡ ነገድ ፤ የኵሽ ፡ የልጅ ፡ ልጅ ፤ የሸባእ ፡ ወንድም ፤ ዐደንን ፡ ያቀና ፡ ያረበች ፡ አባት ፡ (ዘፍ፲ ፡ ፯ ። ሕዝ፳፯ ፡ ፲፭) ። የአብርሃም ፡ ልጅ ፡ ከኬጡራ ፡ የተወለደ ፡ (ዘፍ፳፭ ፡ ፫) ።

**ዲድርክም ፡ ሚ ፤(ጽር ፡ ዲድራኽሞን)** ፤ የገንዘብ ፡ ስም ፡ እንደ ፡ ሩብና ፡ እንደ ፡ ፈረንክ ፡ ያለ ፤ አንዱ ፡ ዲድርክም ፡ ኻያ ፡ አቦሊ ፡ ነው ። የአቦሊን ፡ ፍች ፡ ተመልከት ፡ (ዘሌ፳፯ ፡ ፫—፯) ።

**ዲድስቅልያ ፤(ጽር ፡ ዲዳስከሊያ)** ፤ የመጽሐፍ ፡ ስም ፤ ፫ኛው ፡ የሐዋርያት ፡ መጽሐፍ ፤ ትምርት ፡ ማለት ፡ ነው ። ወሣልስ ፡ መጽሐፍ ፡ ዲድስቅልያ ፡ ዘውእቱ ፡ ትምህርት ፤ ወኍላቄሁ ፡ አርብዓ ፡ ወሠለስቱ ፡ አንቀጽ ፡ (ፍ ፡ ነ ፡ መቅ) ።

**ደይኖ ፤ ኖት ፤(ደየነ ፡ ይዴይን ፡ ይደይን ፤ ዳነየ ። ዕብ ፡ ወሱር ፡ ዳን ። ዐረ ፡ ዳነ)** ፤ መዳኘት ፤ መፍረድ ፡ መቅጣት ፤ መገሠጽ ፡ መቈጣት ። ወይዴይኖሙ ፡ በዐቢይ ፡ (ሉቃ ፡ ዕዝ፲፱ ፡ ፵፩) ።

**ደያኒ ፤ መደይን** ፤ የሚዳኝ ፡ ዳኛ ፤ ፈራጅ ፡ ቀጭ ። ደያኔ ፡ ጽድቅ ፡ (ፊልክ ፡ ፻፳፱) ።

**ተደየነ** ፤ ተዳኘ ፡ ተቀጣ ፤ ተፈረደበት ፤ ፍርድ ፡ ለበሰ ፤ ቅጣት ፡ ተቀበለ ። ወዘሰ ፡ ኢአምነ ፡ ይደየን ። ከመ ፡ ይደየኑ ፡ መዓልተ ፡ ወሌሊተ ። ዘከመ ፡ ይደየኑ ፡ ኃጥአን ፡ በዘነኔ ፡ እሳት ፡ (ማር፲፮ ፡ ፲፮ ። ራእ፳ ፡ ፲ ። ቀሌ) ።

**ድዩን ፤(ናን ፡ ናት ፡ ይንት)** ፤ የተዳኘ ፡ የተቀጣ ፤ ፍርድ ፡ የለበሰ ፤ የተፈረደበት ።

**ደይን ፤(ናት)** ፤ ቍርጥ ፡ ፍርድ ፤ የማይላጥ ፡ የማይለወጥ ፤ የማይመለስ ፡ ቃል ፤ ንዑ ፡ ኀቤየ ፡ ሑሩ ፡ እምኔየ ፤ ይህን ፡ የመሰለ ። ኢትግበር ፡ ዘንተ ፡ ደይነ ። ትንግሡ ፡ ዘለደይን ፡ ዕለተ ፡ ደይን ፡ (ዘፍ፲፰ ፡ ፳፭ ። ዮሐ፭ ፡ ፳፱ ። ማቴ፲ ፡ ፲፭) ።

—፤ ፍጻም ፡ ቅጣት ፤ መከራ ፡ ሥቃይ ፤ የሥቃይ ፡ ቦታ ። መካነ ፡ ደይን ። ጠቢሰ ፡ ደይኖሙ ። ዐዘቅተ ፡ ደይን ። ይጼዐኑ ፡ ውስተ ፡ ደይን ። አንቀጸ ፡ ደይን ፡ (ኩፋ ፡ ፯ ። ራእ፲፱ ፡ ፲፩ ። ሉቃ ፡ ዕዝ፯ ፡ ፩ ፡ ፱ ። አርጋ ፡ ፬) ። ዲን ፡ ድኝ ፡ ማለት ፡ ደይን ፡ ከማለት ፡ ወጥቷል ፤ ከብሪትን ፡ እይ ።

**መዲና ፤(ናት)** ፤ በቁሙ ፤ ታላቅ ፡ ከተማ ፡ መናገሻ ፤ ፍርድ ፡ የሚቈረጥበት ፤ በይግባኝ ፡ የሚኬድበት ። ቀሮንቶስ ፡ ልህቀተ ፡ አኪይያ ፡ እንተ ፡ ይእቲ ፡ መዲና ።

ወገብረ ፡ መዲናሁ ፡ በጐንደር ። ወኢወፅአ ፡ እመዲ ናሁ ፡ (አዋል ። ታሪ ፡ ነገ) ።

**ዲና ፤ (ዕብራ) ፤** ስመ ፡ ብእሲት ፤ ወለተ ፡ ያዕቆብ ፤ ፍርዲ ፡ ፍርዲቱ ፡ ማለት ፡ ነው ። ወንድሞቿ ፡ ስምዖንና ፡ ሌዊ ፡ በርሷ ፡ ምክንያት ፡ የሴኬምን ፡ ሰዎች ፡ ስለ ፡ ዘረፉና ፡ ስለ ፡ ፈጁ ፤ ሽፍታ ፡ ኹሉ ፡ በነዚህ ፡ አምሳል ፡ ዲና ፡ ይባላል ፤ የዲና ፡ ወንድም ፡ ማለት ፡ ነው ። ሴኬም ፡ ህየ ፡ በዲና ፡ ተሀጕለ ፤ ወበሳራ ፡ አቤሜሌክ ፡ ቈስለ ፡ (ቅኔ ። ዘፍ፴፬ ፡ ፳፩ ። ፴፬ ፡ ፩—፯ ፡ ፳፬—፴) ።

**ዲኖ ፤ (ትግሬ) ፤** ዐጕዝ ፡ ሌጦ ፤ ደበሎ ። ፍርድ ፡ ልበስ ፡ ማለት ፡ ከዚህ ፡ ወጥቷል ፤ ዐድልን ፡ ተመልከት ። ባማርኛ ፡ ግን ፡ ጅን ፡ ጅናም ፡ የባሕር ፡ ጐሽ ፡ የጋኔን ፡ በሬ ፡ ማለት ፡ ነው ። ይኸውም ፡ ከባሕር ፡ እየወጣ ፡ ሣር ፡ ይበላል ፤ ከየብስ ፡ እንስሳትም ፡ ይወልዳል ፤ ከርሱ ፡ የሚወለድ ፡ ላም ፡ ኹሉ ፡ በጣም ፡ ብርቱ ፡ ነው ፤ በገር ፡ አይያዝም ፡ አይጠመድም ፤ ብሂሞትን ፡ እይ ።

**ዳን ፤** የዲና ፡ ወንድም ፤ ስመ ፡ ነገድ ፡ ስመ ፡ ሀገር ፤ ፈረደ ፡ ማለት ፡ ነው ። ሰመየቶ ፡ ስሞ ፡ ዳን ። ተለዎሙ ፡ እስከ ፡ ዳን ። እምዳን ፡ እስከ ፡ ቤርሳቤሕ ፡ (ዘፍ፴ ፡ ፮ ። ፲፬ ፡ ፲፬ ። ፪ነገ ፡ ፲፯ ፡ ፲፩) ።

**ዳይቅ ፤ (ዕብ ፡ ዳየቅ) ፤** መታኰሻ ፡ ግንብ ፤ የውጭ ፡ ጠላት ፡ በቅጥር ፡ ዠርባ ፡ የሚሠራው ፤ ወይም ፡ በዚያ ፡ ላይ ፡ ኾኖ ፡ እንዳንደርቢ ፡ ወደ ፡ ከተማ ፡ የሚሰደው ፡ የሚወረውረው ፡ ደንጊያ ። ከመ ፡ ይሕንጽ ፡ ዳይቀ ፡ (ሕዝ፳፩ ፡ ፳፪) ።

**ዲያቆን ፤ (ናት ። ጽር ፡ ዲያክኖስ) ፤** በቁሙ ፤ አገልጋይ ፡ የቄስ ፡ ተወራጅ ፡ በአንብሮተ ፡ እድ ፡ የሚሾም ። ሶበ ፡ ትሰይሞ ፡ ለዲያቆን ፡ አንብር ፡ እዴከ ፡ ላዕሌሁ ። ሊቀ ፡ ዲያቆናት ። ንፍቀ ፡ ዲያቆን ፤ የዲያቆን ፡ ተወራጅ ፡ ምክትል ፡ (ፍ ፡ ነ ፡ ፯ ። ፰) ።

**ዲያቆናይ ፤ ዊ ፤ (ይያን ፡ ውያን) ፤** ዝኒ ፡ ከማሁ ። እስጢፋኖስ ፡ ዲያቆናይ ፡ ምእመን ፡ በሰማይ ፡ (ድጓ) ።

**ዲያቆናይት ፤ (ዊት ፤ ይያት ፡ ውያት) ፤** ሴት ፡ ዲያቆን ፤ የ፳ ፡ ዓመት ፡ ባልቴት ፤ በሴቶች ፡ ወገን ፡ እንደ ፡ ዲያቆን ፡ ኹና ፡ የምትላክ ፡ የምታገለግል ። ወዲያቆናዊት ፡ ትገሥጾን ፡ ለአንስት ፡ ወታዐርፎን ፡ ወትር ድኦን ። እለ ፡ ያወስቡ ፡ መነከሳይያት ፡ ወዲያቆናይያት ፡ (፩ጢሞ ፡ ፭ ፡ ፱ ። ፍ ፡ ነ ፡ ፯ ። ፵፰) ።

**ዲቁና ፤** በቁሙ ፤ ዲያቆንነት ፡ ዲያቆን ፡ መኾን ፤ የዲያቆን ፡ ሹመት ፡ ማዕርግ ። ሢመተ ፡ ዲቁና ። መልእክተ ፡ ዲቁና ። ግብረ ፡ ዲቁና ፡ (ፈ ፡ መ ፡ ፯ ፡ ፭ ። ፍ ፡ ነ ፡ ፯ ። ስንክ ፡ ጥቅ፱) ።

**ዴቆን ፤ (ይዴቁን ፡ ይዴቁን) ፤** ዲያቆን ፤ ዘቆን ፤ ዲያቆን ፡ ኾነ ። ዜቆነን ፡ ተመልከት ፤ የዚህ ፡ ምክሼና ፡ መንቲያ ፡ ነው ።

**ዴር ፤ (ሱር ፡ ዳይራ ። ዐረ ፡ ደይር) ፤** ገዳም ፡ ዱር ፤ የመነኮሳት ፡ በታ ፡ ሰፈር ። ዘሩ ፡ ደዌር ፡ ነው ፤ ወና ፡ የ ፡ ተወራራሾች ፡ ስለ ፡ ኾኑ ፡ በየ ፡ ምክንያት ፡ ወደዚህ ፡ መጥቷል ፤ ዱርና ፡ ዴር ፡ ፩ ፡ ስም ፡ ናቸው ። ኀበ ፡ ተሐንጸ ፡ ተዝኪር ፡ ወኀበ ፡ ተሣረረ ፡ ዴር ፡ (ስንክ ፡ የካ፱) ።

**ዳየር ፤** አንባ ፡ ኰረብታ ፤ ዙሪያው ፡ ገደል ፤ የግሼና ፡ የግሸን ፡ ተራራ ፤ ምስጢሩ ፡ ገዳምነት ፡ ነው ።

**ድያስ ፤ ድዮስ ፤ ድያ ፤ (ጽር ፡ ዲዎስ) ፤** ወፍራም ፡ ረዥም ፡ ጣዖት ፤ አምላክ ፡ ዐቢይ ፡ ማለት ፡ ነው ። ዜዉስን ፡ እይ ፡ (ግብ፲፬ ፡ ፲፪ ፡ ፲፫ ። ስንክ ፡ ኅዳ፲፱) ።



ድያ ፡

**ዲዮስቆሬዶስ ፤ (ጽር ፡ ዲዎስኩሮን) ፤** መንታ ፡ ጣዖት ፡ ወንድማማች ፤ የድያስ ፡ ልጆች ፡ የሚባሉ ። ባለሐዲሶች ፡ ግን ፡ መስቀል ፡ ይሉታል ፡ (ግብ፳፰ ፡ ፲፩) ።

**ዲዮስቆሮስ ፤ (ጽር ፡ ወቅብጥ) ፤** የሰው ፡ ስም ፤ በዳኬዎስና ፡ በመርቅያን ፡ ዘመን ፡ የነበረ ፡ ስማዕት ፤ ያምላክ ፡ ወገን ፡ ቤተ ፡ ሰብ ፤ ልደ ፡ ቤት ፡ አገልጋይ ፡ (ቅዳ ። ሃይ ፡ አበ) ።

**ዲዮስጶራ ፤ (ጽር ፡ ዲያስፖራ) ፤** ዝርዋን ፡ ዘበዝርወት ፡ ዘበስደት ፡ ዘበፍልሰት ፡ (ያዕ፩ ፡ ፩) ።

**ዴፐ ፤ ደየፐ ፤ (ደበወ ፤ ደበየ) ፤** ሸመቀ ፡ አሸመቀ ፤ አደባ ፡ ደፈጠ ፡ ተደበቀ ፤ ለመግደል ፡ አደጋ ፡ ለመጣል ። ዘዴፐ ፡ ለከ ፡ ይቅትልከ ። ዴፑ ፡ በፍኖት ፡ (ዮሴፍ) ።

**—፤** ጦር ፡ ወጥመድ ፤ አኖረ ፤ ደበቀ ፡ ሸሸገ ። ዴፐ ፡ ሎቱ ፡ ዐይወ ፡ ከመ ፡ የኀይል ፡ ቦቱ ፡ (ዮሴፍ) ።

**ዲፓ ፤ (ዲባ) ፤** ሸመቃ ፡ ሽመቃ ፤ ደበቅ ፡ ጦር ፡ ደባ ፡ ተንኰል ። ነበረ ፡ ዲፓ ። ቀመ ፡ ዲፓ ። ጸንሐቶ ፡ ዲፓ ፡ ለንጉሥ ። ወይጸንሕዎ ፡ ሎቱ ፡ በዲፓ ፡ (፩ነገ ፡ ፲፭ ፡ ፭ ። መሳ፱ ፡ ፴፱ ። ዮሴፍ) ።

**ደኪም ፤ ሞት ፤ (ደከመ ፡ ይደክም ፡ ይድክም) ፤** መድከም ፡ መታከት ፤ መዛል ፡ መስነፍ ፡ መላም ፡ መለስለስ ፤ ማነስ ፡ መኰሰስ ። እገሪከ ፡ ይረውጻ ፡ ወይደክማከ ። ወደኪሞ ፡ በሐዊረ ፡ ፍኖት ፡ ነበረ ። ደክመት ፡ ነፍስየ ፡ (ኤር፲፪ ፡ ፭ ። ዮሐ፬ ፡ ፮ ። ሉቃ ፡ ዕዝ፲፪ ፡ ፳) ።

**—፤** መፍዘዝ ፤ መስለል ፤ የዐይን ፡ የቃል ፤ ማርጀት ፡ መታመም ፤ ምስጢሩ ፡ ያው ፡ ድካም ፡ ነው ። ደክማ ፡ አዕ

ይንትየ ፡ በአንብዐ ። ቃለ ፡ ወለተ ፡ ጽዮን ፡ ደክመ ። ኢደክመት ፡ እምንይላ ። ደክመ ፡ አቡከ ። ዘእንበለ ፡ ት ድክም ፡ (ሰቈ ፩ ፡ ፲፭ ። ኤር ፴ ፡ ፴፭ ። ኩፋ ፡ ፴፭ ። ዘፍ ፵፰ ፡ ፭ ። ሚራ ፲፰ ፡ ፳፭) ። ደክተሙን ፡ እይ ፤ የዚህ ፡ ስ ሯጽ ፡ ነው ።

**ድኩም** ፤ (ማን ፡ ማት ፡ ክምት) ፤ የደከመ ፡ ደካማ ፡ ኩሳሳ ፤ ታናሽ ፡ ወራዳ ፤ አሮጌ ፡ በሽተኛ ፤ ልም ፡ ልምሉም ፤ ርጥብ ፡ ለጋ ፡ ጩቅላ ። ድኩም ፡ ወጽኑስ ። መንግሥት ፡ ድኩም ። ልደትኪ ፡ እማሕፀነ ፡ ድክ ምት ፡ ሥጋ ። አዕይንቲሃ ፡ ድኩም ። ልሳን ፡ ድክ ምት ። ድኩማን ፡ ደቂቅ ፡ (ገላ ፬ ፡ ፱ ። ሕዝ ፲፯ ፡ ፲፬ ። ስንክ ፡ ግን ፭ ። ኩፋ ፡ ፳፰ ። ምሳ ፳፭ ፡ ፲፭ ። ዘፍ ፴፫ ፡ ፲፫) ።

**ድክመት** ፤ መድክም ፤ አደክከም ፤ ድካም ፡ ደካምነት ። እም ድኅረ ፡ ርሥኣኑ ፡ ወድክመቱ ፡ (ፊ ልክ ፡ ፶፪) ።

**ድክምና** ፤ ደካምነት ፤ ድካም ። እንዘ ፡ ሀለው ክኒ ፡ አንቲ ፡ ለድክምና ፡ መጽንዒ ፡ (አዋል) ።

**ድካም** ፤ (ማት) ፤ በቁሙ ፤ ስንፍና ፡ ሀኬት ፤ ልፋት ፡ ጥረት ፡ አገልግሎት ። እንበለ ፡ ድካም ። ከመ ፡ ያእምር ፡ ድካሞ ። ድካመ ፡ ፍጥረቱ ፡ ወአእምሮቱ ። ሑዳዴ ፡ ወድካም ። ዕሴተ ፡ ገድላቲሆሙ ፡ ወድካ ማቲሆሙ ፡ (ስንክ ፡ ጳግ ፪ ። ኢዮ ፴፯ ፡ ፯ ። ፊልክ ፡ ፶፰ ። ዮሴፍ ። ፈ ፡ መ ፡ ፭ ፡ ፪) ።

**አድከመ** ፤ አደከመ ፤ አለፋ ፡ አቃከተ ፡ አስለቸ ፤ አስነፈ ። ያደክም ፡ ቃሎ ፡ ወይዬውህከ ። ያደክም ፡ ኀይሎ ፡ እንዘ ፡ ይትቀነይ ። ስካር ፡ ያደክም ፡ ኅሊና ፡ (ሚራ ፳፬ ፡ ፭ ። ፴፰ ፡ ፴ ። ቀሌ) ።

**መድክም** ፤ (ምት ፡ ማን ፡ ማት) ፤ የሚያደ ክም ፤ አድካሚ ። ዛቲ ፡ ግብር ፡ መድክምት ፡ ጥቀ ፡ (ፊልክ ፡ ፳፫) ።

**ደኰዐ** ፤ (ይደኵዕ ፡ ይድኳዕ ፤ ደኲዕ) ፤ ወደቀ ፡ ተጣለ ፡ ተረሳ ።

**ድኩዕ** ፤ (ዕብ ፡ ዳከአ ፡ ዐፈር ፡ ትቢያ) ። ፍግ ፡ ፋንድያ ፡ በጠጥ ፤ ዐዘባ ። ይከይድዎሙ ፡ ከመ ፡ ድዙዕ ። እከው ፡ ድዙዐ ። ተግሣጽ ፡ ለሕፃን ፡ ያሜንዮ ፡ በከመ ፡ ያሜንዮ ፡ ድዙዕ ፡ ለምድር ፡ (ኤር ፳ ፡ ፪ ። ሉ ቃ ፲፫ ፡ ፳ ። ፊላስ ፡ ገ፳) ።

**ደኰስበተሬ** ፤ (ጽር ፡ ዶክሳ ፡ ፓቴሬ) ፤ ስብሐት ፡ ለአብ ፡ ማለት ፡ ነው ። አርቶደክስን ፡ እይ ። ወ ትብል ፡ ደዙስበተሬ ፡ አርባዕተ ፡ ጊዜ ፡ (ግንዘ) ።

**ደክተመ** ፤ (ደከመ ፤ ተ ፡ ስሯጽ ። ዕብ ፡ ያቴም) ፤ ደኸየ ፤ የሙት ፡ ልጅ ፡ ኾነ ። አባት ፡ እናት ፡ ዐጣ ። ድኻ ፡ ማለት ፡ ቅሉ ፡ ከዚህ ፡ ወጥቷል ፤ ዕብራይስ ጥም ፡ ድኻ ፡ ሲል ፡ ዳኽ ፡ ይላል ። ደክተመት ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ። ለእለ ፡ ተርፉ ፡ ድኅሬሁ ፡ ርድአሙ ፤ ወለእለሂ ፡ ደክተሙ ፡ ሐፅኖሙ ፡ (አቡሻ ፡ ፶ ። ግንዘ) ።

**ድክቱም** ፤ (ማን ፡ ማት ፡ ትምት) ፤ የደኸየ ፡ የተጣለ ፤ አባት ፡ እናቱ ፡ የሞቱበት ። ድክት ምት ፡ ይእቲ ፡ እምአቡሃ ፡ ወእማ ። ድክቱማን ፡ (አ ዋል ። ፍ ፡ ነ ፡ ፳፬ ፡ ፫) ።

**ደክታም** ፤ (ብ ፡ ደካትም) ፤ ድኻ ፡ አደግ ፤ ድኻ ፡ የሙት ፡ ልጅ ። እፎ ፡ ኢይፌድፍድ ፡ ሐዘንየ ፡ እንዘ ፡ እኤጽር ፡ አንስቲያሆሙ ፡ ከዊኖን ፡ ደክታመ ፡ ወውሉዶሙ ፡ ዕጓለ ፡ ማውታ ። ደክታም ፡ ነፍስየ ፡ እምእማ ፡ ወአባ ። ንዋየ ፡ ደካትም ፡ (ዮሴፍ ። ስንክ ፡ ታኅ ፳፬ ። ፍ ፡ ነ ፡ ፴፫ ፡ ፬) ።

**ድክታሜ** ፤ **ድክትምና** ፤ ድኽነት ፡ አይቶ ፡ ዐጣነት ፤ የሙት ፡ ልጅነት ። በእንተ ፡ ዕጓለ ፡ ማውትና ሆሙ ፡ ወድክትምናሆሙ ፡ (ዮሴፍ ። ፍ ፡ ነ ፡ ፲፯) ።

**አደክተመ** ፤ አደኸየ ፡ ድኻ ፡ አደረገ ፤ አባት ፡ እናት ፡ አሳጣ ። አደክተመኒ ፡ እምአቡየ ፡ ወእምየ ፡ (ዮሴፍ) ።

**ደልጎ** ፤ ጎት ፤ (ደለገ ፡ ይዴልግ ፡ ይደ ልግ ። ዕብ ፡ ዳላግ ፤ ዳላቅ) ፤ መዝለል ፡ (ጥወ) መ ወርወር ፤ ዘሎ ፡ ተራምዶ ፡ ማለፍ ፤ መፍጠን ፡ መቀል ጠፍ ፤ መናር ፡ መጓን ፤ ላም ፡ እንዳየ ፡ አንበሳ ፡ መኾን ፤ ያርበኛ ። ማዘለል ፡ መወርወር ፡ አርቆ ፡ መጣል ፤ የፍላጻ ፡ የጦር ። ንኅረይ ፡ ለርእስነ ፡ ኅሩያነ ፡ ስብአ ፡ እለ ፡ ይ ዴልጉ ፡ ውስተ ፡ ቀትል ፡ ወንሑር ፡ ላዕሌሁ ፡ ወንት ቃተል ፡ ምስሌሁ ፡ (ኩፋ ፡ ፴፯) ።

**ተዳለገ** ፤ ተወራወረ ፤ ተመካከተ ። ዕደው ፡ ን ያላን ፡ ወእለሂ ፡ ይዳለጉ ፡ ጠፍኡ ፡ (ኩፋ ፡ ፵፰) ።

**ድላግ** ፤ ዝላይ ፡ ውርወራ ፡ መከታ ፤ የሰልፍ ፡ ሥራ ። ከመ ፡ ያእትት ፡ እምላዕሌየ ፡ ዘቀትለ ፡ ፀራዊ ፡ ድላገ ፡ ውሒዘ ፡ ረድኤትከ ፡ ይኩን ፡ በዐውድየ ፡ ዐ ይገ ፡ (ደራሲ) ።

**ዳልጋ** ፤ (ዐማርኛ) ፤ የባሕር ፡ በሬ ፤ ጅን ። የ በሬ ፡ ዐንገት ፡ ትርፉ ፡ እንጥልጥሉ ፡ ቈርበት ፤ ደላጎ ፤ የ ጤፍ ፡ ዛላ ። ማናቸውም ፡ ትርፍ ፡ ነገር ፡ ኹሉ ።

**ድልጉማ** ፤ (ዐረ ፡ ዱምሉጅ) ፤ የእጅ ፡ የ ጣት ፡ ጌጥ ፡ ጥምዝ ፡ የወርቅ ፡ አንባር ፤ ጎቲም ፡ ቀለበት ፡ ወይም ፡ ባለዕንቊ ፡ ፈርጥ ። ወከመ ፡ ድልጉማ ፡ ው ስተ ፡ እደ ፡ የማን ። ሕልቀትየ ፡ ዘአጽባዕትየ ፡ ወድ ልጉማየ ፤ አንባር ፡ (ሚራ ፳፭ ፡ ፳፭ ። ኩፋ ፡ ፵፭) ። ከመ ፡ ባዝግና ፡ ወርቅ ፡ ውስተ ፡ ክሣድ ፡ ወከመ ፡ ድልጉማ ፡ ዘውስተ ፡ አጻብዕ ፡ (ፊላስ ፡ ገ፲፰ ። ደልገን ፡ ማለት ፡ ከ ዚህ ፡ ይስማማል ።

**ደሊው** ፤ ዎት ፤ (ደለወ ፡ ይደሉ ፡ ይ ድሉ ። ዐረ ፡ ደላ ። ሱር ፡ ድላ ። ዕብ ፡ ዳላህ ፤ ሔበ) ፤ መጥለቅ ፡ መቅዳት ፤ መሳብ ፡ መጉተት ፤ ከጕድ ጓድ ፡ ከጥልቅ ፡ ከዐዘቅት ፡ ማውጣት ። ማንሣት ፡ መስ ቀል ፡ ማንጠልጠል ፤ መመዘን ፡ መለካት ፡ ማስተካከል ። (ማዘጋጀት ፤ ማስናዳት) ። ወደለዉ ፡ ዐስብየ ። ደለ ውኩ ፡ ሎቱ ፡ ወርቀ ። ወደለውኩ ፡ ሎሙ ፡ ወርቀ ፡ ወብሩረ ። እመ ፡ ደለውከ ፡ ቃለከ ፡ በመዳልው ። ወ ትደልዎ ፡ (ዘካ ፲፩ ፡ ፲፪ ። ኤር ፴፱ ፡ ፲ ። ዕዝ ፳ ፡ ፳፭ ።

ሚራ፳፰፡ ፳፩። ሕዝ፵፡ ፮)። ዳግመኛም፡ በቀደስ፡ ቤት፡ ደልዎ፤ ደለወ፡ ይደሎ፡ እያለ፡ በ፪፡ መንገድ፡ ይኼዳል። ተደለወና፡ መደልው፡ የዚህ፡ አንጻር፡ ናቸው።

**ደላዊ** ፤ (ዊት፡ ውያን፡ ያት) ፤ የሚመዝን፡ መዛኝ፤ ውሃ፡ ቀጂ፡ ባለማሕየብ።

**ደለው** ፤ (በሬ፡ እደለው) ፤ ስመ፡ ኮከብ፤ ደላዌ፡ ማይ፤ ሐያቢ፡ በዓለ፡ ማሕየብ፡ ማለት፡ ነው። መልኩ፡ በሥዕል፡ ሲያዩት፡ ውሃ፡ ቀጂ፡ ይመስላል፤ ኮከብነቱም፡ የጥር፡ ነው፤ ከፀሓይ፡ ጋራ፡ ፳፱፡ ዕለት፡ ዓ፩፡ ኬክሮስ፡ ይመግባል፡ (አቡሻ፡ ፬)።

**መድለው** ፤ (ብ፡ መዳልው) ፤ **አው፡ መድሎት** ፤ (ታት) ፤ መመዘኛ፡ ማስተካከያ፤ ሚዛን፡ ደንጊያ፡ ልክ፤ ብዙ፡ ስምና፡ ክፍል፡ ያለው። መድሎት፡ ሰቅል። መድሎት፡ ልጥር። ወተረክበ፡ መድሎት፡ ውእቱ፡ አክሊል፡ መክሊተ። መዳልው፡ ዐቢይ፡ ወንኡስ። መዳልወ፡ አልባብ። መዳልወ፡ ፀሓይ፡ (ዘፀ፴፱፡ ፪። ስንክ፡ ሚያ፫። ፩ዜና፡ ፳፡ ፪። ምሳ፳፡ ፫። ስንክ፡ ጥቅ፩። ክብ፡ ነገ)።


መድሎት፡

**ደለወ** ፡ (ዐጉል) ፤ ኾነ፡ ተገባ፤ ደላ፡ ተመቸ፡ ተስማማ። (ገበዘ፡ ተገበዘ፡ ግብዝ፡ ኾነ)። ዘይደሉ፡ ለመልእክተ፡ ሖሉ። ለከ፡ ይደሉ፡ ስብሐት። ወደለዎ፡ ብሔር፡ (ጥበ፲፭፡ ፯። መዝ፡ ፷፬። ሉቃ፲፪፡ ፲፯)።

**አድለወ** ፤ አስመዘነ። አደላ፤ አስደላ፤ አስመቸ፡ ደስ፡ አሰኘ፤ ግቡ፡ አደረገ፡ አበቃ። ታደሉ፡ ሊተ፡ መክሊተ፡ ብሩር። ኢታድሉ፡ ለሰብእ፡ እንበይነ፡ ላሕዩ። ለእግዚ፡ አድልዎ፡ ኢይክሉ። ዘንተ፡ ሕዝበ፡ አድሉ፡ ለነሚአ፡ ምስጢርከ፡ (፫ነገ፡ ፳፡ ፴፱። ሚራ፲፭፡ ፪። ሮሜ፳፡ ፳። ቅዳ፡ ሕር)።

**አድላዊ** ፤ **መድልው** ፤ **መደልው** ፤ (ዋን) ፤ የሚያስመዝን፤ አስመዛኝ። በቁሙ፤ የሚያደላ፤ የሚያስመች። ግብዝ፡ ሰነፍ፤ ሞኝ፡ ዋሾ። ብእሲ፡ መደልው። አ፡ መደልው። ፈሪሳውያን፡ መደልዋን። ረበናት፡ መደልዋን፡ (ኢዮ፴፬፡ ፴። ማቴ፯፡ ፭። ፳፫፡ ፲፫። ዳንኤ፡ ፭)። ባለቅኔዎች፡ ግን፡ አመድለወ፡ ብለው፡ ይገሉና፤ መደልውን፡ ከዚህ፡ ያወጣሉ።

**አስተደለወ** ፤ (ያስተዴሉ፡ ያስተደሉ፤ **አው፡ አስተዳለወ፡ ያስተዳሉ፡ ያስተዳሉ**) ፤ የደለወና፡ የአድለወ፡ ድርብ፤ አድራጊና፡ አስደራጊ። አዘጋጀ፡ አሰናዳ። አደላደለ፡ አስመቸ፡ አመቻቸ። ያስተዴሉ፡ ለዓለም፡ መፍቅዶ። ወያስተዴሉ፡ ክረምተ፡ ለምድር። አስተዳለወ፡ መንበሮ። አስተዳለወ፡ ሀገረ፡ (ሚራ፴፱፡ ፴፩። መዝ፡ ፺፬። ፺፪። ዕብ፲፩፡ ፲፮)።

**ተደልወ** ፤ ተመዘነ፤ ተካከለ፡ (ሔኖ፵፩፡ ፩። ፵፫፡ ፪)። እስመ፡ በመዳልው፡ ተደልወ፡ ዓለም። ሶበ፡ ተደልወት፡ ምስለ፡ ብርሃን፡ (ሉቱ፡ ዕዝ፪፡ ፵፯። ጥበ፯፡ ፳፱)።

**ተደለወ** ፤ ተዘጋጀ፡ ተደራጀ፤ ተሰናዳ። ተደላደለ፡ ተቀማጠለ፤ ተድላ፡ አደረገ፡ በተድላ፡ ኖረ፤ ተደሰተ። ተደለዉ፡ አሕዛብ፡ ለጹብእ። ተደለው፡ ከመ፡ ትሑር። ወመጽአ፡ ሳኦል፡ ተደሊዎ። ባዕድ፡ ይዴሎ፡ በንዋየ፡ ዚአሁ። ከመ፡ ትደሎ፡ አመ፡ ተድላሁ። እምትደለው፡ ወትትፌጋዕ፡ በንዋየ፡ ነኪር፡ (አስቴ፩፡ ፯። ጦቢ፩፡ ፲፯። ፩ነገ፡ ፳፯፡ ፬። ኢዮ፲፰፡ ፳። ሚራ፡ ፳፱፡ ፪፡ ፳፪)።

(፩) **ድልው** ፤ (ዋን፡ ዋት፡ ሉት) ፤ የተመዘነ፡ የተካከለ፡ ልከኛ፤ አነሰ፡ በዛ፡ የማይባል። ቃሎሙ፡ ለጠቢባን፡ ድልው፡ በመዳልው። ድልወ፡ ዕርየት፡ (ሚራ፳፩፡ ፲፭። ፊልክ፡ ፫)።

(፪) **ድልው** ፤ የተገባ፤ የተዘጋጀ፡ የተሰናዳ፡ ዝግጁ። ዘድልው፡ ለክብር። ድልው፡ መንበርከ። በዓልየ፡ ድልው። ድልዋኒከሙ፡ ሀልዉ። እልኩ፡ እለ፡ ድልዋት። ወድሉት፡ ይእቲ፡ (ሚራ፵፱፡ ፲፪። መዝ፡ ፺፪። ማቴ፳፪፡ ፰። ፳፬፡ ፵፬። ፳፭፡ ፲። ራእ፳፩፡ ፪)። ድልኽ፡ ማለት፡ ከዚህ፡ ወጥቷል።

**ድልወት** ፤ (ታት) ፤ መመዘን፡ (ጥመ) መመዘን፤ መዛኝና፡ ተመዛኝ፡ መኾን፤ አመዛዘን፡ ምዘና፡ ሚዛን፤ ልክ፡ መጠን፡ (ዘፍ፳፬፡ ፳፪። ዘፀ፴፡ ፴፬። መሳ፰፡ ፳፯)። ወድልወቱ፡ ለዙሉ፡ ብርት፡ ወኀጺን፡ ዘላዕሌሁ፡ ኀምሳ፡ ምእት፡ ሰቅሎን፡ (፩ነገ፡ ፲፯፡ ፭። ፪ነገ፡ ፲፬፡ ፳፯)።

—፤ አገባብ፡ ርትዕ፤ እውነት፤ የተገባ፡ የሚገባ። በጽድቅ፡ ተኰነኑ፡ ዘከመ፡ ድልወተ፡ እከዮሙ። እንዘ፡ አኮ፡ ድልወት፡ ሊተ፡ አድኀንከኒ፤ አኮ፡ ድልወት፡ ሊተ፡ ኣንቃዕዱ። በበ፡ ድልወታት። ነበብከ፡ ድልወተ፡ (ጥበ፲፱፡ ፲፪። ዲድ፡ ፯። ፍ፡ ነ፡ ፱፡ ፪። ቄር፡ ጸላ)።

**ተድላ** ፤ በቁሙ፤ ደስታ፡ ድሎት፡ ምቾት፤ ምቹ፡ ፍራሽ፡ ፈርሽ፡ የዙፋን፡ የኮር። ኢያፍቱከ፡ ተድላሆሙ፡ ለረሲዓን። ገነተ፡ ተድላ። ተድላ፡ ርእስየ። ፍትሕ፡ ወርትዕ፡ ተድላ፡ መንበሩ፡ (ሚራ፱፡ ፲፪። ዘፍ፫፡ ፳፫። ፩ቆሮ፡ ፲፡ ፴፫። መዝ፡ ፺፯)።

—፤ አገባብ፤ ክብር፤ ገንዘብ። እስመ፡ ከመ፡ ዝ፡ ተድላ፡ ለነ። ተድላ፡ መለኮት። መዘግብቲሆሙ፡ ከመ፡ እምላእ፡ ተድላ፡ (ማቴ፫፡ ፲፭። ቄር። ምሳ፰፡ ፳፩)።

**ተዳለወ** ፤ (ይዳለው) ፤ ተደራራገ፤ ተዘገጃጀ፡ ተሰነዳዳ፡ ተመቻቸ።

**ዳሌጥ ፤(ዕብ፡ ዳሌት ። ጽር ፡ ዴልታ ። ግእ፡ ድልት)** ፤ ስመ ፡ ፊደል ፡ ራብዕ ፡ ደ ፤ መዝገቢያ ፡ ሳንቃ ፡ ማለት ፡ ነው ፡ (መዝ ፡ ፻፲፰ ፡ ፳፭—፴፪ ። ሰቈ፩ ፡ ፬ ። ፪ ፡ ፬ ። ፫ ፡ ፬ ። ፬ ፡ ፬) ።

**ደልሎ ፤ ሎት ፤(ደለለ ፡ ይዴልል ፡ ይደልል ። ዕብ ፡ ዳላል ፤ ታላል)** ፤ መመየድ ፤ መከፍከፍ ፤ ጠጕርን ፡ በሚደ ፡ ማበጠር ፡ ማጕፈር ፤ መበተን ፡ ማጕተን ፤ መንቀስ ፡ መከናከን ፤ ለቤት ፡ ከዳንም ፡ ይኾናል ። ወይም ፡ መሥራት ፡ መጣስ ፤ መሸረብ ፡ መጕንጕን ፤ መፍተል ፡ መቈንደል ። በቁሙ ፡ መደለል ፡ ማታለል ፤ መሸንገል ። (ተረት) ፤ ደሮን ፡ ሲደልሏት ፡ በመጫኛ ፡ ጣሏት ። ደላል ፡ ደላላ ፤ ድላል ፡ ደለል ፡ ማለት ፡ ከዚህ ፡ ወጥቷል ።

**ተደለ ፤ ተደለለ** ፤ በቁሙ ፤ ተከፈከፈ ፡ ተበጠረ ፤ ተቈንደለ ።

**ድሉል ፤(ላን ፡ ላት ፡ ልልት)** ፤ የተመየደ ፡ የተከፈከፈ ፡ ክፍክፍ ፤ ወይም ፡ ወደ ፡ ታች ፡ የተጣሰ ፡ የተዝረፈረፈ ፤ ግልበልስ ፡ ያለ ፤ የተቈናዘለ ፤ የተጋመደ ፡ የተመሳቀለ ። ድምድማሁ ፡ ድሉል ። ሥዕርተ ፡ ርእስኪ ፡ ድሉላት ። ላሕይት ፡ ይእቲ ፡ ብእሲት ፤ ድምድማሃ ፡ ድሉል ፡ (ማሕ፭ ፡ ፲፩ ። አርጋ ፡ ፮ ። ገድ ፡ ተክ) ።

**ድላሌ** ፤ (ላ ፡ ጥ ፡ ክ) መከፍከፍ ፤ አከፋከፍ ፤ ክፍክፋ ፤ ክፍክፋት ፤ የጠጕር ፡ ሥራ ፤ ዐይነቱ ፡ መልኩ ፤ ጠባዩ ፡ አኳኋኑ ። ርእሱ ፡ ወርቀ ፡ ቄፋዝ ፡ ወድላሌሁ ፡ ጸሊም ፡ ከመ ፡ ቋዕ ። ለሥዕርትኪ ፡ ሰላም ፡ ዘድላሌሁ ፡ ጸሊም ፡ (መጽ ፡ ምስ ። ደራሲ) ።

**ደሊላ ፤(ዕብ ፡ ድሊላ)** ፤ ቀጭን ፡ ክር ፤ ገመድ ፡ ፈትል ፤ ወይም ፡ ሥም ፡ ረቂቅ ፡ መንዲል ፤ የጠጕር ፡ ማስሪያ ፡ መሸፈኛ ። የሶምሶን ፡ ሚስት ፡ (መሳ፲፮ ፡ ፬) ። ስሟ ፡ እንደ ፡ ትንቢት ፡ ኹኖ ፡ ተነግሯል ።

**ድልማኑታ** ፤ ስመ ፡ ሀገር ፤ የገሊላ ፡ ምዕራብ ፡ (ማር ፡ ፰ ፡ ፲) ።

**ደሊቅ ፤ ቆት ፤(ደለቀ ፡ ይደልቅ ፡ ይድልቅ ። ዐረ ፡ ደሊቀ ። ዕብ ፡ ዳላቅ ፤ ነደ)** ፤ መታወክ ፡ መናወጥ ፤ መጋለብ ፡ መውለብለብ ፤ የባሕር ፡ የእሳት ። በቁሙ ፤ መደለቅ ፡ መምታት ፤ የከበሮና ፡ የርግጫ ።

**አድለቀ** ፤ አወከ ፡ አናወጠ ፤ አስመታ ፡ አስደለቀ ። መጽሐፍ ፡ ግን ፡ በደለቀና ፡ በአድለቀ ፡ ፈንታ ፡ ኹለቱን ፡ አዕማድ ፡ ደርቦ ፡ አድለቅለቀ ፡ ይላል ።

**አድለቅለቀ** ፤ አንዋወጠ ፤ ተንዋወጠ ፡ (መዝ ፡ ፳፰ ። ፶፱ ። ፺፰) ። አነ ፡ ኣድለቀልቃ ፡ ለምድር ። ወኣድለቀልቀን ፡ ለአህጉር ። ዘያድለቀልቃ ፡ እመሠረታ ፤ ገቢር ፡ (ዕብ፲፪ ፡ ፳፮ ። ኢሳ፲ ፡ ፲፬ ። ኢዮ፱ ፡ ፮) ። ያድለቀልቅ ፡ ሰማየ ፡ ወምድረ ። አድለቅለቁ ፡ አድባር ፡ እምኔሁ ። ርዕደት ፡ ወአድለቅለቀት ፡ ምድር ፤ ተገብሮ ፡ (ዮኤ፬ ፡ ፲፮ ። ናሖ፩ ፡ ፭ ። መዝ ፡ ፲፯) ።

**ድልቅልቅ ፤(ቃት)** ፤ ሁከት ፡ ንውጽውጽታ ፤ ሽብር ፡ ድብልቅልቅ ። አድለቅለቀ ፡ ዐቢይ ፡ ድልቅልቅ ። ወናሁ ፡ ኮነ ፡ ዐቢይ ፡ ድልቅልቅ ። ወይከውን ፡ ዐቢይ ፡ ድልቅልቅ ፡ ወረኀብ ፡ በበ ፡ ብሔሩ ፡ (ግብ፲፮ ፡ ፳፮ ። ማቴ፳፰ ፡ ፪ ። ሉቃ፳፩ ፡ ፲፩) ።

**ዲሎሳን ፤(ጽር ፡ ዲሎሲስ ። ዕብ ፡ ኡሪም)** ፤ የበዓል ፡ መብራቶች ፤ ለደስታና ፡ ለክብር ፡ የሚበሩ ። ቃላት ፡ ነገራት ፡ ከሊቀ ፡ ካህናት ፡ ልብስ ፡ የሚስሙ ። አልባስ ፡ ትክህና ፡ ሊቀ ፡ ካህናት ፡ ቃለ ፡ እግዚ ፡ ሲጠይቅ ፡ የሚለብሳቸው ። ካህን ፡ ዘይለብስ ፡ ዲሎሳነ ። ልብሰ ፡ ዲሎሳን ፡ (ዕዝ፪ ፡ ፷ ። ፭ ፡ ፵) ።

**ድልት ፤ (ድንት)** ፤ ስመ ፡ ፊደል ፡ ራብዕ ፤ የግእዝ ፡ አራተኛ ፡ ፊደል ፡ ደ ። ፍችውን ፡ በዳሌጥና ፡ በድንት ፡ ተመልከት ።

**ደምዎ ፤ ዎት ፤ (ደመወ ፡ ይዴሙ ፡ ይደሙ)** ፤ መድማት ፤ ደም ፡ መኾን ፤ ደም ፡ መልበስ ፤ መምሰል ።

**አድመወ** ፤ አደማ ፡ አስደማ ፤ ደም ፡ አደረገ ፤ በደም ፡ በከለ ። አ ፡ ሔዋን ፡ ናሁ ፡ ይበኪያ ፡ ሖሎን ፡ አዋልድኪ ፤ ወይዴምዋ ፡ በከመ ፡ አድመውኪያ ፡ አንቲ ፡ ለእንትኩ ፡ ዕፀ ፡ (ቅዳ ፡ አት) ።

**ደም ፤(ማት ፡ ዕብ ፡ ዳም ። ሱር ፡ ድማ ። ዐረ ፡ ደም)** ፤ በቁሙ ፤ ቀይ ፡ ፈሳሽ ፡ ከሕያው ፡ ከሥጋው ፡ የሚገኝ ፡ (ዘፍ፱ ፡ ፬—፮) ። ሥጋ ፡ ወደም ። እምነ ፡ ዘደም ። ደማቲሆሙ ፡ ወደምየ ። በእንተ ፡ ክዒወ ፡ ደማቲሆሙ ። ርቱዕ ፡ ንክዐው ፡ ደማቲነ ፡ በእንተ ፡ ክርስቶስ ፡ እምሳለ ፡ ማይ ፡ (ሚራ፲፬ ፡ ፲፰ ። ዮሐ፮ ፡ ፲፫ ። ዮሴፍ ። ፊልክ ፡ ፻፴ ። አፈ ፡ ተ፭) ። ዘር ፤ ወገን ። ተደምሮ ፡ በደም ። ዘተርፈ ፡ እምነ ፡ ደሞሙ ፡ ለእለ ፡ ያርብሕ ፡ (ፈ ፡ መ ፡ ፭ ፡ ፩ ። ኢያ፲፫ ፡ ፲፪) ።

**ደማዊ ፤(ዊት ፡ ውያን ፡ ያት)** ፤ የደም ፤ ደማም ፡ ደመ ፡ ነፍስ ፡ ያለው ፡ ደም ፡ የሚወጣው ፤ ደሙ ፡ ሲያልቅና ፡ ሲደርቅ ፡ የሚሞት ፤ በባሕርና ፡ በየብስ ፡ የሚኖር ፡ ሕያው ፡ ሥጋው ፤ ተላዋሽ ፡ ተንቀሳቃሽ ፡ ያሙስና ፡ ያርብ ፡ ፍጥረት ፤ ለማግሰኞም ፡ ፍጥረት ፡ ይነገራል ። ደመ ፡ አስካል ። ደሙ ፡ በለስ ። ደመ ፡ ዕጕሥታር ፡ (ዘፍ፵፱ ፡ ፲፩ ። መጽ ፡ ምስ) ።

**ደመ ፡ ኪዳን** ፤ የግዝረት ፡ የመሥዋዕት ፡ ደም ፤ ኪዳን ፡ ስለ ፡ ማጥናት ፡ የሚፈስ ።

**ደመ ፡ ነፍስ** ፤ የሰው ፡ የንስሳ ፡ ደም ፤ ከዕፀዋት ፡ ደም ፡ የተለየ ። በደም ፡ የሚሣል ፡ እንስሳዊ ፡ አእምሮ ።

**ደመ ፡ ሰማዕት** ፤ ስለ ፡ ሃይማኖት ፡ በግፈኞች ፡ እጅ ፡ የሚፈስ ፡ የምእመናን ፡ ደም ።

**ደመ ፡ ትክቶ** ፤ የሴቶች ፡ ግዳጅ ፤ ባሕርያዊ ምንጭ ፡ አበባ ፤ በየወሩ ፡ ፯ ፡ ፯ ፡ ቀን ፡ የሚታይ ።

አትከ ፡ ኢይኩን ፡ ሁከት ፡ (ዮሐ፩ ፡ ፫ ። ሔኖ፰ ፡ ፩ ። ጥበ፲፯ ፡ ፰ ። አስቴ ፡ ፩ ። ቀሌ ። ኪዳ) ።

**ሀወለ ፤—ቀላቀለ ፤—ሐወለ ።**

**ሀውል ፤(ዕብ ፡ ሄቤል)** ፤ ኣበት ፡ እንፉለት ፡ ከሞቀ ፡ ገላ ፡ ከፍ ፡ የሚወጣ ። ከንቱ ፡ ነገር ፡ ዕብለት ፤ ዋዛ ፡ ፈዛዛ ፡ ማቅ ፡ ሥላቅ ፤ ስድብ ፡ ነቀፋ ።

**ሀውለየ ፤(ተቀ ፡ ግ)** ፤ አፌዘ ፡ ሣቀ ፡ ተሣለቀ ፤ ነቀፈ ፡ ሰደበ ፡ አረከሰ ፤ ከንቱ ፡ አደረገ ። ከመ ፡ ዝ ፡ የሀወልይዎ ፡ ለእግዚ ፤ ወእለ ፡ ጸጋ ፡ ትስብእቱ ፡ ይመይጡ ፡ ውስተ ፡ ሀውልዮ ። ተሀወልዮኑ ፡ ለእግዚ ፡ ቃል ፡ በዘሐመ ። ኢተሀውልዮ ፡ ለዐቃቤ ፡ ሥራይ ፡ እመ ፡ በትሕትና ፡ አሕየወ ። ኢየሀውልይዎኬ ፡ ለክርስቶስ ፡ ኃጥኣን ። ኢተሀውሊኬ ፡ ሕማማቶ ። እመ ፡ አረሚ ፡ ሀውሊይዎ ፡ ለምስጢር ፡ (ተረ ፡ ቄር፩ ። ፭ ። ፲ ። ፲፰) ።

**ሀየ ፤—በዚያ ፡ ክዚያ ፤—ሀይይ ፡ ሀየ ፤ ሀየየ ።**

**ሀይብ ፤—በቁሙ ፡ ዐይብ ፤—ሔበ ፡ ሐይብ ።**

**ሀዪድ ፤ ዶት ፤(ሄደ ፤ ሀየደ ፡ የሀይድ ፡ ይሂድ)** ፤ መቀማት ፡ መንጠቅ ፤ በምክንያት ፡ መውሰድ ። እነሥአከ ፡ ወአሀይደከ ። ወየሀይደከሙ ፡ ገራህተከሙ ። ኢትትዐገሉ ፡ ወኢትሂዱ ፡ መነሂ ፡ (፩ነገ ፡ ፪ ፡ ፲፪ ። ፰ ፡ ፲፬ ። ሉቃ፫ ፡ ፲፬) ።

—፤ ማንጸብረቅ ፤ መሳብ ፡ መበዝበዝ ። ሰብሰ ፡ ዳዊት ፡ ዘየሀይድ ፡ ዐይነ ። አሣእኒሃ ፡ ሀየደ ፡ አዕይንቲሁ ። ዐበየ ፡ ብርሃኑ ፡ የሀይድ ፡ አዕይንተ ፡ (፪ነገ ፡ ፯ ፡ ፲፬ ። ዮዲ፲፮ ፡ ፱ ። ቀሌ) ።

—፤ መሄድ ፡ መራመድ ፤ እግርን ፡ ማንሣት ፡ መንጠቅ ። ምስጢሩ ፡ ያው ፡ መውሰድ ፡ ነው ፤ ኬደ ፡ መርገጥ ፡ መደፍጠጥን ፡ ሄደ ፡ አንሣሥን ፡ ያሳያል ፤ ኬደ ፡ ሖረ ፡ የግእዝ ፤ ሄደ ፡ ያማርኛ ። ነጠቅ ፡ ነጠቅ ፡ አርግ ፡ እንዲሉ ፡ ቶሎ ፡ ቶሎ ፡ ሂድ ፡ ሲሉ ።

**ሀያዲ ፤(ዲት ፡ ድያን ፡ ያት)** ፤ የሚቀማ ፡ ቀማኛ ፤ ነጣቂ ፡ ወሳጅ ፡ (ሉቃ፲፰ ፡ ፲፩ ። ፩ቆሮ ፡ ፭ ፡ ፲ ፡ ፲፩ ። ፮ ፡ ፲) ። እምእደ ፡ ሀያዲሁ ። ሀያዴ ፡ ንዋየ ፡ ባዕድ ። ሰራቂ ፡ ወዐማፂ ፡ ወሀያዲ ፡ ወመማጢ ። ሀያድያን ፡ (ኤር፳፪ ፡ ፫ ። ቀሌ ። ፈ ፡ መ ፡ ፲፯ ፡ ፪ ። ፍ ፡ ነ ፡ ፵፩) ።

**ሀይድ** ፤ ቅሚያ ፤ ንጥቂያ ፤ ምክንያት ፡ ያለው ፡ አወሳሰድ ፡ (መዝ ፡ ፷፩ ። ኢሳ፷፩ ፡ ፰) ።

**ተሀይደ** ፤ ተቀማ ፡ ተነጠቀ ፤ ተማረከ ፤ ገንዘቡ ፡ ወይም ፡ ርሱ ፡ ራሱ ። ዘያስተጋብእ ፡ ብዕለ ፡ በዐመፃ ፡ ይትሀየድ ፡ ብዕሉ ፡ እምኔሁ ። ዘእንበለ ፡ ትትሀየድ ፡ ብእሲቱ ፡ እምኔሁ ። ሰማይ ፡ ይትሀየድ ። ተሀይዱ ፡ ደቂቅነ ፡ (ዲድ ፡ ፲፱ ። ኩፋ ፡ ፲፫ ። ሔኖ፹፫ ፡ ፫ ። ሱቱ ፡ ዕዝ፲ ፡ ፵፩) ።

**ሀዪድ ፤ (ዳን ፡ ዳት ፡ ይድ)** ፤ የተቀማ ፡ የተነጠቀ ፤ ገንዘብ ፡ ሰው ።

**ሂደት** ፤ መቀማት ፡ (ጥቀ) መቀማት ፡ አቀማም ፡ አወሳሰድ ፤ ቅሚያ ፡ ንጥቂያ ፡ (አርጋ) ። መሄድ ፡ መራመድ ፤ አካሄድ ፡ አረማመድ ፤ እግር ፡ አንሣሥ ።

**ተሃየደ** ፤ ተቃማ ፡ ተሻማ ፤ ተናጣጠቀ ፤ ርስ ፡ በርሱ ።

**ሀይወ ፤—ዳነ ፤—ሐዩው ፡ ሐይወ ።**

**ሄጠ ፤—ሸነገለ ፤—ኀዩጥ ፡ ኄጠ ።**

**ሀይይ ፤ዮት ፤(ሀየ ፤ ሀየየ ፡ የሀይይ ፡ ይሀየይ ። ሀከየ)** ፤ ቻል ፡ ማለት ፤ መናቅ ፡ ማቅለል ፤ መተው ፡ መጣል ። መጽሐፍ ፡ ግን ፡ በሀየየ ፡ ፈንታ ፡ ተሀየየ ፡ ይላል ፤ አያስኝም ። ኢትትሀየይ ፡ ትእዛዘ ፡ እምከ ። ተሀየዩ ፡ ሥርዐቶ ። እሙንቱ ፡ ተሀየዩ ፡ ወንለፉ ። ትትሄየይ ፡ ኀጣይአ ፡ ሰብእ ። ለዕቡያን ፡ ይትሄየዮሙ ፡ እግዚ ፡ (ምሳ፩ ፡ ፯ ። ቀሌ ። ማቴ፳፪ ፡ ፭ ። ጥበ፲፩ ፡ ፳፱ ። ያዕ፬ ፡ ፮ ።

**ሀያዪ ፤(ተሀያዪ)** ፤ ቻል ፡ ባይ ፡ ቻልተኛ ፤ ታጋሽ ። ጳውሎስ ፡ ሐዋርያ ፡ ከነ ፡ ተሀያዩ ፡ ስብሐተ ፤ ኀሳረ ፡ ወጽዕለተ ፡ (ፊልክ ፡ ፵፯ ። ፶፱ ። ፻፩) ።

**አሀየየ** ፤ ቻል ፡ አሰኘ ፤ አስነፈ ፡ አስተወ ፤ አስጣለ ። ኢፈቀደ ፡ አምላክ ፡ ያርኢከ ፡ ሙስናሃ ፡ ለሀገር ፡ ወአምጽአ ፡ ኑዛዜ ፡ ላዕሌከ ፡ ወአህየየከ ፡ (ራእ ፡ ባሮ) ።

**ተሀየ ፤ ተሀየየ** ፤ ቻል ፡ ተባለ ፤ ተተወ ፡ ተጣለ ። ብእሲ ፡ ዐማፂ ፡ ይትሄየይ ፡ (ምሳ፲፪ ፡ ፪) ።

**ሀዩይ ፤(ያን ፡ ያት ፡ ይይት)** ፤ ቻል ፡ የተባለ ፤ የተናቀ ። ቻል ፡ ያለ ፡ ቻልተኛ ፤ ሰነፍ ። መንዘህልልሰ ፡ ወህዩይ ። ፍናዊሆሙ ፡ ለህዩያን ፡ (ፊልክ ፡ ፶፱ ። ምሳ፲፫ ፡ ፲፩) ።

(ጥ) **ሀየት** ፤ ቻል ፡ ማለት ፤ ቻልታ ፡ ስንፍና ። እምህየት ፡ ወእምፀርዐት ፡ (ሊጦን) ።

**ሀየ** ፤ የቦታ ፡ ዐጸፋ ፤ በዚያ ፡ ከዚያ ፡ ወደዚያ ፤ ሩቅን ፡ ያሳያል ፤ እንደ ፡ ከሃ ፡ ነው ። ተከለ ፡ ገነተ ፡ ወሤሞ ፡ ህየ ። ህየ ፡ ይሠየማ ፡ ወህየ ፡ ይትዐቀባ ፡ ነፍሳቲሆሙ ፡ ለጻድቃን ። ቦ ፡ ዘይወፅእ ፡ እምሥራቅ ፡ ወየሐውር ፡ ለምዕራብ ፡ ከመ ፡ ይስቂ ፡ በህየ ። ተንሥእ ፡ ወፃእ ፡ ሐቅለ ፡ ወበህየ ፡ እነግረከ ፡ (ዘፍ፪ ፡ ፰ ። ቅዳ ፡ ግሩ ። አት ። ሕዝ፫ ፡ ፲፱) ።

**ህየንተ ፤(ህየ ፡ እንተ)** ፤ ዐቢይና ፡ ደቂቅ ፡ አገባብ ። ህየና ፡ እንተ ፡ ተጋጥሞ ፡ አንድ ፡ ኅርመት ፡ ኹኗል ፤ እ ፡ ስለ ፡ ተጐረደ ፡ መጋጠሚያው ፡ አያስታውቅም ፤ ይህን ፡ የመሰለ ፡ ብዙ ፡ አለ ። ስለ ፡ በ ፡ ፈንታ ፡ እንደ ፡ ይኾናል ፤ በለና ፡ በ ፡ ፈንታ ፡ አንድ ፡ ወገን ፡ ናቸው ፤ ምስጢሩ ፡ እንደ ፡ ፍዳ ፡ ነው ፤ ለውጥ ፡ ሤጥ ፡ ቤዛ ፡ ካሳ ፡ ዕዳ ፡ ብድር ፡ ያሳያል ። በአንቀጽ ፡ ሲገባ ፡ ዘን ፡ በር ፡ ከፋች ፡ ያደርጋል ፤ አንዳንድ ፡ ጊዜም ፡ ብቻውን ፡ ይገባል ። ምንት ፡ ተዐስዮሙ ፡ ህየንተ ፡ ዘገብሩ ። ህየንተ ፡ ዘትረድኦ ፡ አቅበጽካሁ ። ህየንተ ፡ ተቀንዩ ። ህየንተ ፡ ዳመወ ፡ (ሚራ፯ ፡ ፳፰ ። ቀሌ ። ኩፋ ፡ ፵፰ ። ስንክ ፡ ጥቅ፱) ። በዘርና ፡ በስም ፡ ሲገባ ፤ ፈደዩኒ ፡ እኪተ ፡ ህየ

ንተ ፡ ሠናይት ። ህየንተ ፡ አበውኪ ፡ ተወልዱ ፡ ለኪ ፡ ደቂቅ ። ተቀንየ ፡ ያዕቆብ ፡ ህየንተ ፡ ራሔል ፡ ይላል ። እንደ ፡ ቢኾን ፤ ህየንተ ፡ ቈፀለ ፡ ዕፀ ፡ ከማሁ ፡ አነ ። አሕመልምል ፡ ሊተ ፡ ነፍስየ ፡ ህየንተ ፡ ዕፀ ፡ ትክልት ፡ ማእከለ ፡ ገነት ፡ ይላል ፡ (አርጋ) ። ህየንቴሁ ፡ ሃ ፡ ብሎ ፡ ሲዘረዝር ፤ ስለ ፡ ርሱ ፡ ፈንታ ፤ በርሱ ፡ ፈንታ ፤ እንደ ፡ ርሱ ፡ ያሰኛል ። ህቦሙ ፡ ህየንቴየ ፡ ወህየንቴከ ፡ (ማቴ ፲፯ ፡ ፳፯) ። (ዕር ፲፱ ፡ ቍ ፳፱) ።

**ሄከ ፤—አላመጠ ፤—ሐዬከ ፡ ሔከ ።**

**ሀይከል ፤ (ዕብ ፡ ሄከል ፡ ሱር ፡ ሄከላ ። ዐረ ፡ ሀይከል)** ፤ ታላቅ ፡ ቤት ፡ አዳራሽ ፡ ሰቀላ ፤ ቤተ ፡ መቅደስ ፤ ከዚያውም ፡ ዃው ፡ ክንድ ፡ መካከለኛው ፡ ክፍል ፤ ጽርሕ ። ሀይከለ ፡ ቍድስ ፡ (ዮሴፍ) ።

—፤ መቅደስ ፡ ምሥዋዕ ፡ መንበረ ፡ ታቦት ፤ በተገናኝ ፡ ማደሪያ ፡ ማለት ፡ ነው ። ሲያበዛ ፡ ሀይከላት ፤ ሀያክል ፡ ይላል ።

**ሀየለ ፤—በረታ ፤—ኀይሎ ፡ ኀየለ ።**

**ሀየል ፤ (ላት ። ዕብ ፡ አያል ። ሱር ፡ አያላ ። ዐረ ፡ ኢየል)** ፤ ዋሊያ ፡ ዋላ ፤ ቀንዳም ፡ ቀንደ ፡ ገላላ ፤ ባለብዙ ፡ ዐጽቅ ፡ ባለተቀጥላ ፤ ነዊን ፡ ዐፅም ፡ እግረ ፡ ሽመላ ፤ የሬቆ ፡ ወገን ፡ የበረሓ ፡ እንስሳ ። ዘይረትዖን ፡ ከመ ፡ ሀየል ፡ ለእገርየ ። ወከመ ፡ ወሬዛ ፡ ሀየል ። ህየ ፡ ተጋብኡ ፡ ሀየላት ፡ እስመ ፡ ሀየል ፡ ቀታሊሁ ፡ ለከይሲ ። ሀየላት ፡ ወለዱ ፡ በውስተ ፡ ገዳም ፡ (መዝ ፲፯ ። ማሕ፪ ፡ ፱ ። ተረ ፡ ቁ፳፰ ። ኤር፲፱ ፡ ፩) ።

ሀየል ፡

**ሄላ** ፤ የወይን ፡ ዘለላ ፤ የበሰለ ፡ ደሙ ፡ የመላ ። አጥባትኪ ፡ ከመ ፡ ሄላ ፡ ዘእምኔሆን ፡ ይውሕዝ ፡ ሐሊብ ፡ (አርጋ ። ማሕ፯ ፡ ፰) ። እኄላን ፡ ተመ ፤ የዚህ ፡ መንቲያ ፡ ነው ፤ ባለብሎዮች ፡ ግን ፡ ምንጭ ፡ የበለስ ፡ ቋንጣ ፡ የስሌን ፡ ፍሬ ፡ ይሉታል ። ንባቡ ፡ ሀየላዊ ፤ ምስጢሩ ፡ መስተፍሥሒ ፡ ከመ ፡ ሀየል ። እስከል ፡ ሄላ ፡ መባሉ ፡ በምሳሌ ፡ እንጂ ፡ ቃል ፡ በቃል ፡ አይደለም ።

**ሄላንሳን ፤—ክቡር ፡ ልብስ ፤—ቂላኖስ ።**

**ሀይመነ ፤ (ሱር ፡ ሃይሜን ። ዐረ ፡ ሀይመነ)** ፤ አመነ ፡ ታመነ ። ንባቡ ፡ ከየማን ፡ ፍችው ፡ ከአሚን ፡ የወጣ ፡ ነው ፤ የመነነና ፡ አይመነን ፡ ተመልከት ።

**ሀይማኒ ፤ (ኒት ፡ ንያን ፡ ያት)** ፤ ያመነ ፡ የሚያምን ፤ የሚታመን ፤ አማኒ ፡ ተአማኒ ።

**መሀይምን ፤ (ንት ፡ ናን ፡ ናት)** ፤ ዝኒ ፡ ከማሁ ፤ ምእመን ፤ ያመነ ፡ የታመነ ፤ አማኒ ፡ እሙን ፡ የማይጠረጠር ። መሀይምን ፡ ውእቱ ፡ በዙሉ ። ስምዕ ፡ መሀይምን ። ክርስቲያናዊት ፡ መሀይምንት ። ማሕየዊ ፡ ለዙሉ ፡ ሰብእ ፡ ወፈድፋደሰ ፡ ለመሀይምናን ፡ (ኵፋ ፲፯ ። ራእ፩ ፡ ፭ ። ኪዳ ። ፩ጢሞ ፡ ፬ ፡ ፲) ። በቊሙ ፡ ማይምን ፤ ያልተማረ ፡ ያልተካነ ፡ ሕዝባዊ ፡ ጨዋ ። (ተረት) ፤ ከማይምን ፡ ባለጌ ፡ የተማሪ ፡ አሮጌ ።

**ሃይማኖት ፤ (ሱር ፡ ሃይማኑታ)** ፤ የዑደት ፡ የምሕላ ፡ ጸሎት ፡ ከቤተ ፡ ክሲያን ፡ ውጭ ፡ በዙሪያው ፡ በገረገራው ፡ የሚባል ፤ እንደ ፡ ጥምቀት ፡ እንደ ፡ ጕዞ ፡ ፍታት ፡ ያለ ፤ ወረብ ፡ ለዘብ ፤ የታቦት ፡ ዘፈን ። ሀይመና ፡ ሀይመን ፡ እንዲል ፡ (ያሬርጌ ፡ ጨፋሪ) ።

—፤ በቊሙ ፤ ማመን ፡ መታመን ፤ እምነት ፡ ጽኑ ፡ ተስፋ ፤ የአምልኮት ፡ ባህል ፤ በልብ ፡ በረቂቅ ፡ ሐሳብ ፡ የሚሟል ። ሃይማኖተ ፡ ዕቀብ ፡ ምስለ ፡ ቤጽከ ። ብእሲ ፡ ዘተእምር ፡ ከመ ፡ ቦ ፡ ሃይማኖት ። እለ ፡ አዕረፉ ፡ በሃይማኖተ ፡ ክርስቶስ ፡ (ሚራ፳፱ ፡ ፳፫ ። ፳፯ ፡ ፲፱ ። ዲድ ፡ ፴፱) ።

**ሃይማኖት ፡ ቅድስት** ፤ ምስጢረ ፡ ሥላሴ ፤ ምስጢረ ፡ ሥጋዌ ፡ (ይሁ ፡ ፫) ።

**ሃይማኖት ፡ ርትዕት** ፤ ኦርቶዶክሳዊት ፤ የኦርቶዶክስ ፡ ባህል ፡ (ቅዳ) ።

**ሃይማኖተ ፡ አበው** ፤ የሊቃውንት ፡ መጽሐፍ ፤ ድርሳን ፡ መልእክት ፤ የኋላ ፡ ሰዎች ፡ ከየመጣፉና ፡ ከየቋንቋው ፡ ለቅመው ፡ ተርጕመው ፡ እንደ ፡ ፍትሐ ፡ ነገሥት ፡ ሰብቻው ፡ አንድ ፡ ክፍል ፡ መጣፍ ፡ ያደረጉት ፡ ታላቅ ፡ ምእላድ ፤ በቅዳሴ ፡ ጊዜ ፡ የሚነበብ ።

**ሃይማኖተ ፡ እስላም** ፤ እስላማዊ ፡ ባህል ፤ ስው ፡ ሠራሽ ፡ ትምርት ፡ ከኦሪት ፡ ከወንጌል ፡ የማይገጥም ፡ (አቡሻ ፡ ፶) ።

**ሃይማኖተ ፡ ንስጡር** ፤ ንስጥሮሳዊ ፡ ባህል ፡ እንደ ፡ አይሁድ ፡ እንደ ፡ ሙሐመድ ፤ ቃል ፡ ሥጋ ፡ ኮነን ፡ የሚነቅፍና ፡ የሚያጸይፍ ፤ ቃል ፡ በሰው ፡ ዐደረ ፡ እንጂ ፡ ሰው ፡ አልኾነም ፤ ሰው ፡ ኹኖ ፡ አልተቀባም ፡ ብሎ ፡ የቃልን ፡ ሰው ፡ መኾን ፡ መሲሕነቱን ፡ የሚክድ ፡ (ቄር) ።

**ሀየንተ ፤—ስለ ፡ ፈንታ ፤—ሀየየ ፡ ሀየ ።**

**ሀዪጽ ፤ ጾት ፤ (ሄጾ ፡ የሀይጽ ፡ ይሂጽ ። ዐረ ፡ ሀበ ፤ ሀፈ)** ፤ መነቅነቅ ፡ መበበቅ ፤ የሾተል ፡ የጦር ። መሳብ ፡ መንደፍ ፤ መወርወር ፡ ማወንጨፍ ፤ መውጋት ፡ መግመስ ፡ መፈንከት ። ሀይጾተ ፡ ቀስት ፡ ወደርብየ ፡ ዙያንው ። ነደፈ ፡ ወሄጾ ፡ ለንጉሥ ፡ ማእከለ ፡ በንብው ። ፈነወ ፡ ሐጸ ፡ ወሄጾ ፡ ጥቦ ። የሀይጹ ፡ ሥዕርተ ፡ ወኢይስሕቱ ። ወፀፎ ፡ ለእብን ፡ ወሄጾ ፡ ውስተ ፡ ፍጽሙ ፡ (መቃ ፡ ፯፲፱ ። ፪ዜና ፡ ፲፰ ፡ ፴፫ ። ኵፋ ፡ ፴፰ ። መሳ፳ ፡ ፲፯ ። ሚራ፵፯ ፡ ፬) ።

**ተሀይጸ** ፤ ተነደፈ ፡ ተወረወረ ፤ ተወጋ ፡ ተገመሰ ። ከመ ፡ ሀየል ፡ ዘተነድፈ ፡ ወተሀይጸ ፡ ከብዶ ።

ኢተሀይጾ፡ውስተ፡ሕማም። ተሀይጾ፡በሐጸ፡ቃሉ፡ ለጳውሎስ፡(ምሳ፡፯፡፳፫። ተረ፡ቄርጀ፮። ገድ፡ ተክ)።

**ሂጾት፤** መንደፍ፡መነደፍ፤አንዳደፍ፡ነደፉ፡ ውርወራ፤ ንድፊያ፡ ውጊያ፤ውግታት፡ግምሳት። አከ፡ በዘቀስት፡ሂጾት፡(ቄር፡ ገ፯)።

**ሀከይ፤ዮት፤(ሀከየ፡ የሀኪ፡ ይሀኪ። ሀየየ፤ አከየ)፤** መስነፍ፡መታከት፡መድከም፡መሰ ልቸት፤ ሥራ፡ መተው፡ መጥላት፤ መለገም፡ ቸል፡ ማ ለት። መጽሐፍ፡ግን፡በሀየየ፡ፈንታ፡ተሀየየ፡እንዲል፤ በሀከየም፡ ፈንታ፡ ተሀከየ፡ ይላል። ዘይዴሙ፡ በሥ ጋሁ፡ወይትሀከይ፡በነፍሱ። ኢናፀርዐ፡ቅኔ፡እደ ዊነ፡ወኢንትሀከይ። ኢትትሀከዩ፡ለንስሓ። ኢትት ሀከይ፡ገቢረ፡ሠናይ። ኢይትሀከይ፡መዊተ፡(አ ርጋ። ዲድ፡፲፫። ቀሌ። ምሳ፫፡፳፯። ግብ፳፭፡፲፭)።

(ጥ) **ሀካይ፤(ያን፡ያት)፤** የታከየ፤ሀኬተኛ፤ሰ ነፍ፡ ታካታ፤ ሥራ፡ ፈት፡ (ምሳ፮፡፮። ፲፡፬። ማቴ ፳፭፡፳፮)። በሀካይ፡ ፈንታ፡ ተሀካዪ፡ ይላል። ኢት ኩን፡ተሀካዩ፡(ምሳ፮፡፱)።

**ሀኬት፤** በቁሙ፤ ስንፍና፡ ቸልታ፤ ንዝህላል ነት፤ ተንኰል፡ ክፋት። በሀኬት፡ወበፀርዐተ፡ዕደው፡ ይወድቅ፡ናሕስ። እመ፡ ዘረከባ፡እምሕሠማት፡ ክነ፡በሀኬት፡ዚኣሁ። ሶበ፡ተሀጕለ፡ንዋየ፡አመጋቢ፡ በእደ፡ መጋቢ፡ ዘእንበለ፡ ጽልሑት፡ ወኢሀኬት፡ (መክ፲፡፲፰። ፍ፡ነ፡፳፰፡፴)።

**አሀከየ፤** አሰነፈ፡ አታከተ፤ አሰለቸ። እስመ፡ በአኀጽሮ፡ ይኄይስ፡ ድርሳን፤ ከመ፡እምብዝኁ፡ ኢያሀኪክሙ፡(ተረ፡ቄር፳፬)። በአሀከየ፡ፈንታ፡አስተ ሀከየ፤አስተሀከየ፡ይላል፤ፍችው፡አንድ፡ነው። ዛቲ፡ መጽሐፍ፡መዜንው፡ ሠናይ፤ ኢያዐቅፋ፡ ትጋሀ፡ ሌሊት፡ወኢያደክማ፡ ወኢያስተሀኪያ፡ ብዝኀ፡ ነ ጽሮ፡(ፈላስ)።

**አሀካዪ፤ መሀክይ፤** የሚያሰንፍ፡ አስናፊ። ጽሒፍ፡ ሊተሰ፡ ኢመሀክይ፡ ወለክሙሰ፡ ጽኑዕ፡ (መጽ፡ ምስ)።

**ተሃከየ፤(ይትሃከይ)፤** ተሳነፈ፤ ተሰናነፈ፤ ተደራረገ።

**አስተሃከየ፤** አሳነፈ፤ አሰናነፈ፤ አደራረገ።

**መስተሃክይ፤** የሚያሳንፍ፡አሳናፊ፤ አሰናናፊ።

**ሀከከ፤(ሆከ)፤** አወከ፤ አሸበረ። ሆከንና፡ ዐከ ወን፡ ተመልከት።

**ሀከክ፤** ሁከት፡ ሽብር፤ ጠብ፡ ክርክር፤ ቱማታ፡ ፍጅት። ዕለተ፡ሀከክ። ማየ፡ሀከክ። አኮ፡ በሀከክ፡ ወበትዝልፍት። እለ፡ ይገብሩ፡ሀከክ። እስመ፡ በሀ ከክ፡ ኀደርክሙ፡ ወበሀከክ፡ ይወድቅ፡ ደቂቅከ፡ (ኢሳ፳፱፡፩። መዝ፡ ፻፳፫። ግብ፲፱፡፴፯። ሮሜ፲፫፡ ፲፯። ኩፋ፡ ፲)።

**ተሀከከ፤(ተሀውከ)፤** ታወከ፡ ተሸበረ፤ ዐ ዘነ፡ ተቈረቈረ። እስመ፡ አኀው፡ ሶበ፡ ዘርከይዎ፡ ለ አባ፡ ሙሴ፡ ተብሀለ፡ ሎቱ፡ ኢተሀከከኑ፡ ልብከ፤ ወ ይቤ፡ ተሀከኩ፡ ወባሕቱ፡ ኢተናገርኩ፡(ፊልክ፡፶፱)።

**ሀኩክ፤(ካን፡ ካት፡ ክክት)፤** ሀዉክ፤ ወጪ፡ ወራጅ፤ ወላዋይ። ኀሊና፡ሀክክት፡(ፊልክ፡፶፩)።

**ሀከከ፤—ዐከከ፤ፎከተ፤—ሐኪክ፡ ሐ ከክ።**

**ሁል፤—ርኩስ፤—ሐዊል፡ ሖለ፡ ሐ ወለ፤ ሑል።**

**ሀላ፡ ሀሊብ፤—ድንኳን፤—አሆላ፡ አ ሆሊብ።**

**ሀለደ፤—ጨረሰ፤—ኀልዶ፡ ኀለደ።**

(ጥ) **ሀልዎ፤ዎት፤(ሀለወ፤ሀሎ፤ይሄሉ፡ የ ሀሉ። ዕብ፡ ሀያሀ)፤** መኖር፡ መገኘት፤ መኾን፡ መ ፈጠር። ኮነንና፡ መጽአን፡ ተመ፤ የዚህ፡ አግዋር፡ ናቸው። እግዚአብሔር፡ አምጻኤ፡ ኵሉ፡ ዓለም፡ እምኀበ፡ ኢሀልዎ፡ ኀበ፡ ሀልዎ። ሀለወ፡ ወኢሀለወ። ዘሀሎ፡ ወይሄሉ። ወሀሎ፡ አሐዱ፡ ብእሲ፤ አለ፡ ኖረ፡ ነበረ፡ (ፈላስ። ራእ፲፯፡፰። ፩፡፬። ዮሐ፫፡፩)።

**ሀላዊ፤(ዊት፡ ውያን፡ ያት)፤** የሚኖር፤ ኗ ዋሪ፤ ኗኝ። ነፍስሰ፡ሀላዊት፡ይእቲ፡ወኢትትዌለጥ፡ (ፈላስ)።

**ሀልው፤(ዋን፡ ዋት፡ ሉት)፤** ያለ፡ የኖረ፡ የነበረ፤ የሚኖር፡ ነባር፤ ቀዋሚ፡ እውነት። ፈጠረ፡ ፍጥረተ፡ ይኩን፡ ህልወ። መ ድኀኒነ፡ ዘህልው፡ እ ምቅድመ፡ ዓለም። ብዕል፡ ህልው። ንርአይ፡ ሊ እመ፡ ነገሩ፡ ህልው። ህልወ፡ ቃለ። አማን፡ ህልወ፡ እብለክሙ፡(ጥበ፪፡፲፯። ዲድ፡፴፯። ዮሴፍ። ምሳ ፳፪፡፳፭። ዮሐ፲፯፡፯)።

**ህላዌ፤(ውያት)፤** መኖር፡ መኾን፤ አኗዎር፤ ኑሮ። ንዜኑ፡ ህላዌሁ፡ ለአብ፡ ምስለ፡ ወልዱ፤ ወህ ላዌሁ፡ ለወልድ፡ ምስለ፡ አቡሁ። ሠለስቱ፡ ህላዌ፡ በአካላት፡ ወአሐዱ፡ ህላዌ፡ በመለኮት፡(ቅዳ፡ ግሩ። ሃይ፡ አበ፡ ባስ)። ይህ፡ ቃል፡ ለሦስቱ፡ ኹሉ፡ የተለየ፡ የአካል፡ ህላዌና፡ ግብር፡ እንዳላቸው፡ ያሳያል፤ ትርጓ ሜውም፡ ይህ፡ ነው። ወላዲ፡ የአብ፡ አካል፤ መውለድ፡ ማሥረጽ፡ ግብሩ፤ ከዊነ፡ ወላዲ፡ ወይም፡ ወላዲነት፡ ህላዌው፤ ባማርኛ፡ ባሕርይ፡ ይባላል፤ ልዩነት፡ ያለው፡ ገጽ፡ ቁመት፡ አቋቋም፡ መልክ፡ ማለት፡ ነው። ተወላዲ፡ የወልድ፡ አካል፤ መወለድ፡ ግብሩ፤ ተወላዲነት፡ ህላ ዌው። ሠራጺ፡ የመንፈስ፡ ቅዱስ፡ አካል፤ መሥረጽ፡ ግብሩ፤ ሠራጺነት፡ ህላዌው፤ ሠለስቱ፡ ህላዌ፡ ይህ፡ ነው። ወአሐዱ፡ ህላዌ፡ ያለውም፤ መውለድና፡ ማሥ ረጽ፡ መወለድ፡ መሥረጽ፡ በዚያው፡ ባንዱ፡ ባሕርይ፡ ባንዱ፡ መለኮት፡ ነውና፤ ባሕርይ፡ የሦስቱ፡ መሟሪያ፡ መኾኑንና፡ አንድነቱን፡ መደብ፡ አድርጎ፡ እንደ፡ አካ ላት፡ ወላዲ፡ ተወላዲ፡ ሠራጺ፡ አለመባሉን፡ ያሳያል። ምስጢሩ፤ ባሕርይ፡ ሳይከፋፈል፤ አካል፡ ሳይቀላቀል፤ ስምና፡ ግብር፡ ሳይፋለስ፡ የአካል፡ ህላዌ፡ ሳይፈርስ፤ ባን

ድንትና ፡ በሦስትንት ፡ ጸንቶ ፡ መኖር ፡ ነው ። ፫ ፡ መለኮት ፡ የሚሉ ፡ ግን ፤ ወላዲ ፡ ባሕርይ ፡ ተወላዲ ፡ ባሕርይ ፡ ሠራጺ ፡ ባሕርይ ፡ እያሉ ፤ የአካላትን ፡ ስምና ፡ ግብር ፡ ለባሕርይ ፡ ሰጥተው ፡ ይፈታሉ ።

**ህላዌ**፤ አካል ፡ ገጽ ፤ አቋቋም ፡ ቁመት ፤ አኳኋን ፡ ኹነታ ። አካል ፡ ማለት ፡ ባሕርይና ፡ ግብርን ፡ መልክንና ፡ ስምን ፡ ኹሉን ፡ ሰብስቦ ፡ የሚይዝ ፤ ሰብሳቢ ፡ ገዥ ፡ አዛዥ ፡ ባለቤት ፡ ማለት ፡ ነው ፤ የአካልን ፡ ፍች ፡ ተመልከት ። እግዚአብሔር ፡ በዓለ ፡ ሠለስቱ ፡ ህላዌ ፡ አሐዱ ፡ በባሕርይሁ ፡ ወሥልጣኑ ፡ ወመለኮቱ ። እስመ ፡ አበዊነ ፡ ሰመይዎ ፡ በዝንቱ ፡ ገጸ ፡ መካን ፡ (በአንቀጸ ፡ ተዋሕደ) ፡ ለህላውያት ፡ አካላተ ፤ አትናቴዎስኒ ፡ ረሰየ ፡ ህላዌ ፡ አሐደ ፡ አካለ ፡ ዘእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ ዘተሠገወ ። እስመ ፡ ህላዌ ፡ ይትበሀል ፡ በእንተ ፡ ክዋኔ ፡ ወአካል ፤ ወክዋኔሂ ፡ ይትበሀል ፡ ከመ ፡ ውእቱ ፡ ህላዌ ፡ ዘያስተጋብእ ፡ ኵሎ ፤ ወአካልሰ ፡ ዘአሐዱ ፡ ህላዌ ፡ ውእቱ ። ተውሕደ ፡ አንድ ፡ የኾነ ፡ አካል ፡ ማለት ፡ ነው ፤ ገጽ ፡ አቋቋም ፡ ቁመት ፡ ያልነው ፡ የአካል ፡ ባሕርይ ፡ ይባላል ፤ አካል ፡ ያለገጽ ፡ ያላቋቋም ፡ አይገኝምና ። እስመ ፡ በዝየ ፡ ይሰመይ ፡ አካል ፡ ህላዌ ፡ አካሉ ፡ ለወልድ ፤ ወአከ ፡ ውእቱ ፡ ህላዌ ፡ ዘያስተጋብእሙ ፡ ለሥሉስ ፡ ቅዱስ ፤ ወበእንተ ፡ ዝ ፡ ተሠገወ ፡ እግዚ ፡ ቃል ፡ (አክሲ ። ሃይ ፡ አበ ፡ ብን ። ዲዮ ። መቃር) ። ህላዌን ፡ የአካል ፡ ባሕርይ ፡ ማለት ፡ አካልን ፡ አቋቋም ፡ ብሎ ፡ ነው ።

**ህላዌ**፤ ባሕርይ ፤ ጠባይ ። ብሕረንና ፡ ጠብዐን ፡ ተመልከት ። ኀቡረ ፡ ህላዌ ፡ ምስለ ፡ አብ ፡ በመለኮቱ ፤ ኀቡረ ፡ ህላዌ ፡ ምስሌነ ፡ በትስብእቱ ። ወኢተወለጠ ፡ ህላዌ ፡ ቃል ፡ ኀበ ፡ ህላዌ ፡ ሥጋ ፡ ወህላዌ ፡ ሥጋ ፡ ኀበ ፡ ህላዌ ፡ ቃል ፤ ዳእሙ ፡ ይሄልዉ ፡ ክልኤቱ ፡ ህላውያት ፡ በበ ፡ ህላዌሆሙ ፡ እንበለ ፡ ውላጤ ፡ (ተረ ፡ ቄር ። ሃይ ፡ አበ ፡ መጠሊ) ። ህላዌ ፡ በአንቀጸ ፡ ተዋሕዶ ፡ አካል ፡ ስለ ፡ ኾነ ፡ አሐዱ ፡ እንዲባል ፡ በአንቀጸ ፡ ተፀቅቦም ፡ ባሕርይ ፡ ስለ ፡ ኾነ ፡ ክልኤቱ ፡ ይባላል ፤ እውነተኛው ፡ የሊቃውንት ፡ ዐዋጅ ፡ ይህ ፡ ነው ። ወኢተዋሐደ ፡ በመንፈቀ ፡ ህላዌ ፡ ወኢኮነ ፡ ካልአ ፡ እንስሳ ፡ በአንትጎ ፤ አላ ፡ ምሉእ ፡ ወፍጹም ፤ በአሐዱ ፡ ህላዌ ፡ ይገብር ፡ ዘክልኤቱ ፡ ህላውያት ፡ (ሃይ ፡ አበ ፡ ኤፍ) ። አሐዱ ፡ ያለው ፡ አካል ፤ ክልኤቱ ፡ ያለው ፡ ባሕርይ ፡ እንደ ፡ ኾነ ፡ አስተውል ። ባሕርያት ፡ ፪ ፡ እንደ ፡ ሆኑ ፡ የባሕርያት ፡ ፍሬ ፡ ግብራትም ፡ ፪ ፡ ናቸው ፤ ተወላዲው ፡ ፩ ፡ አካል ፡ ሲኾን ፡ ልደቱ ፡ ፪ ፡ እንዲባል ፤ ግብሩም ፡ ሠሪው ፡ አንድ ፡ ሲኾን ፡ እንደ ፡ መሣሪያው ፡ እንደ ፡ ባሕርይ ፡ ፪ ፡ ይባላል ። ግብርን ፡ አሐዱ ፡ ማለት ፡ ልደትንም ፡ አሐዱ ፡ ያሰኛል ፤ ልደት ፡ ቅሉ ፡ ግብር ፡ ነውና ፡ ፪ ፡ መባሉ ፡ ስለዚህ ፡ ነው ፤ ግብር ፡ ባሕርይን ፤ ገቢር ፡ አካልን ፡ ይከተላል ። ቦቱ ፡ መንክራት ፡ ወዓዲ ፡ ቦቱ ፡ ሕማማት ፡ ወውእቱ ፡ አሐዱ ፡ ህላዌ ፤ በመለኮቱ ፡ ይገብር ፡ መንክራተ ፡ ወበትስብእቱ ፡ ይትዌከፍ ፡ ሕማማተ ። ርኢክኑ ፡ ዘከመ ፡ እፎ ፡ ሎቱ ፡ ክልኤቱ ፡ ግብራት ፡ ኅቡረ ። ወዐቀበ ፡ እሎንተ ፡ ክልኤተ ፡ ግብራተ ፡ በኵሉ ፡ ዘመን ። ወኢንበል ፡ ከመ ፡ መንክራት ፡ ለአሐዱ ፡ ወሕማማት ፡ ለካልኡ ፤ አላ ፡ እሙንቱ ፡ ለዝንቱ ፡ አሐዱ ፡ ባሕቲቱ ፤ ከመ ፡ አምላክነ ፡ ወእግዚእነ ፡ ኢየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ አሐዱ ፡ አካል ፡ ሥግው ፡ ወአሐዱ ፡ ህላዌ ፡ ዘንብረ ፡ ኵለንታሁ ፡ ለወልድ ፡ ዘውእቱ ፡ ቃል ፡ ወነፍስ ፡ ወሥጋ ፡ ወልቡና ፡ ወምግባር ። ህላዌ ፡ ዘንብረ ፡ ኵለንታሁ ፡ ያለውን ፡ ቃል ፡ ሥጋ ፡ ነፍስ ፡ ልቡና ፡ ምግባር ፡ ብሎ ፡ ቈጠረ ፤ ልቡና ፡ ምግባር ፡ የሌለው ፡ ሌላ ፡ ህላዌ ፡ ይኾናል ፡ እንጂ ፡ የሰው ፡ ህላዌ ፡ አይባልምና ፡ (ሃይ ፡ አበ ፡ ጎር ። ኤጲ ። መቃር) ።

**ህላዌ**፤ ጠቅላይ ፡ ስም ፤ ኵላዊ ፡ አስተጋባኢ ፤ ስምንቱ ፡ ካቶሊክ ፡ እንደ ፡ ማለት ፡ ነው ። ለፈጣሪ ፡ ሳይቀር ፡ በሰማይ ፡ በምድር ፡ ላለ ፡ ፍጥረት ፡ ኹሉ ፡ ይነገራል ። ወአእምሩ ፡ እስመ ፡ ስመ ፡ ህላዌ ፡ ይትበሀል ፡ በገጸ ፡ መካን ፡ ህየንተ ፡ ህላዌ ፡ ኵሉ ፡ ዘመድ ፡ (ሃይ ፡ አበ ፡ ዲዮ) ። አስተጋባኢ ፡ ስም ፡ ስለ ፡ ኾነ ፡ እንደ ፡ ጠባይዕ ፡ ለአካል ፡ በሚመችበት ፡ አካል ፤ ለባሕርይ ፡ በሚመችበት ፡ ባሕርይ ፡ ይባላል ። ባማርኛ ፡ ሌላ ፡ ስም ፡ ታጥቶለት ፡ እንጂ ፡ በአካልና ፡ በባሕርይ ፡ መካከል ፡ ሌላ ፡ የተለየ ፡ ማእከላዊ ፡ ስም ፡ ያስፈልገው ፡ ነበር ። በምድር ፡ ያለ ፡ የፍጥረት ፡ ኹሉ ፡ ሥር ፡ አራቱ ፡ ባሕርያት ፡ ናቸው ፤ ማይ ፡ መሬት ፡ ነፋስ ፡ እሳት ፤ እሊህ ፡ አራቱ ፡ እየተዋሐዱ ፡ ሌላ ፡ ዐይነት ፡ ባሕርይ ፤ ሥጋን ፡ ዕንጨትን ፡ ያስገኛሉ ። የተለየ ፡ የባሕርይ ፡ ስሙ ፡ ሥጋ ፡ ዕንጨት ፡ ነው ፤ አራቱ ፡ ባሕርያት ፡ ተውሕደ ፡ ሥጋ ፡ ኹኖ ፡ ዕንጨት ፡ ኹኖ ፡ የቆመበት ፡ ውሳጣዊ ፡ አስተጋባኢ ፡ ስሙ ፡ ህላዌ ፡ ተብሏል ። «ጽርኣውያን ፡ ህላዌን ፡ ወስያ ፤ ባሕርይን ፡ ፊሲስ ፡ ይሉታል ። ላቲናውያንም ፡ ህላዌን ፡ ሱብስታንስያ ፤ ባሕርይን ፡ ናቱራ ፡ ይሉታል» ። አካል ፡ ለባሕርይ ፡ አይነገርም ፤ ባሕርይም ፡ ለአካል ፡ አይነገርም ፤ ህላዌ ፡ ግን ፡ ኹለቱ ፡ አንድ ፡ ኹነው ፡ የቆሙበት ፡ አስተጋባኢ ፡ ስም ፡ ስለ ፡ ኾነ ፡ ለኹለቱ ፡ ኹሉ ፡ ይነገራል ። የወጣበት ፡ የስምንቱ ፡ ምስጢር ፡ ግን ፡ አጥብቆ ፡ አጥልቆ ፡ ሲመረመር ፡ አኳኋንንና ፡ አቋቋምን ፡ የተዋሕደውን ፡ ጽናትና ፡ አኗኗር ፡ ያሳያል ፡ እንጂ ፡ አካልን ፡ ብቻ ፡ ባሕርይንም ፡ ብቻ ፡ አያሳይም ። የንጨት ፡ ኹሉ ፡ ባሕርይ ፡ አንድ ፡ ሲኾን ፡ ህላዌው ፡ እየቅል ፡ ነው ፤ ብርቱ ፡ አለ ፡ ግብዝ ፡ አለ ፤ ካራቱ ፡ ባሕርያት ፡ የተፈጠረ ፡ ኹሉ ፡ እንዲህ ፡ ነው ። የመላእክትና ፡ የነፍስ ፡ ባሕርይ ፡ ግን ፡ መሠረት ፡ የሌውም ፡ እምኀበ ፡ አልቦ ፡ ነው ፤ መላእክትን ፡ ዘይሬስዮሙ ፡ መንፈሰ ፡ ወነደ ፡ እሳት ፡ ቢላቸው ፤ የሚራቀቁ ፡ የሚማወቁ ፡ ተለኣክያን ፡ ማለት ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ እኛ ፡ ከምናውቀው ፡ ነፋስና ፡ እሳት ፡ ማለት ፡ አይደለም ፤ ከዚህስ ፡ ቢኾን ፡ እንደ ፡ መጠኑ ፡ ባየናቸው ፡ በሰማናቸው ፡ ነበር ። አካላውያን ፡ ኹነው ፡ ተፈጥረዋል ፤ ባሕርያቸው ፡ ከአካላቸው ፡ አይቀድምም ፤ የአካላቸው ፡ አኳኋን ፡ ህላዌ ፡ ይባላል ፤ የነፍስም ፡ እንደ ፡ መላእክት ፡ ነው ። የነፍስ ፡ ባሕርይ ፡ ወደ ፡ ሥጋ ፡ ባሕርይ ፡ ወደ ፡ ግዘፍ ፡ ሱይሳብ ፤ የሥጋም ፡ ባሕርይ ፡ ወደ ፡ ነፍስ ፡ ባሕርይ ፡ ወደ ፡

ርቀት ፡ ሳይሳብ ፤ ነፍስና ፡ ሥጋ ፡ ተውሕደው ፡ ፩ ፡ አካል ፡ ፩ ፡ ህላዌ ፡ ፩ ፡ ሰው ፡ ይገኛል ። እስመ ፡ ከዋኔሁ ፡ ለሰ ብእ ፡ ውእቱ ፡ ግብር ፡ እለ ፡ ኢይትማሰሉ ፡ በበይና ቲሆሙ ፡ ወኢየኀብሩ ፤ ወቃልኒ ፡ ኢየኀብር ፡ ምስለ ፡ ሥጋ ፡ በከመ ፡ ኢትኀብር ፡ ነፍስ ፡ ምስለ ፡ ሥጋ ፡ እ ንዘ ፡ ብእሲሁ ፡ አሐዱ ፡ እምነፍስ ፡ ወሥጋ ፡ ወአሐዱ ፡ ገጽ ፡ እምዘኢየኀብሩ ፡ ግብራት ። ነፍስና ፡ ሥጋ ፡ ተው ሕደው ፡ አንድ ፡ ኹነው ፡ የቆሙበት ፡ አካል ፡ ህላዌ ፡ ይ ባላል ፤ ለቃልም ፡ በተለየ ፡ አካሉ ፡ የተለየ ፡ ህላዌ ፡ አለው ፤ አስቀድመን ፡ እንደ ፡ ተናገርን ።

**ህላዌ** ፤ መኖሪያ ፤ መኗሪያ ። ምስጢሩ ፡ አናምር ፡ ከለው ፡ ይገባል ። ኅበ ፡ ህላዌሁ ፡ ተመይጠ ፡ ልሳኑ ፡ ውቁይ ፤ ኅበ ፡ ህላዌሁ ፡ አግብእ ፡ (ስንክ ፡ ጥር፳) ፡ ዳግ መኛም ፡ ባሕርይ ፡ ያላካል ፤ አካል ፡ ያለባሕርይ ፡ ብቻ ፡ ብቻውን ፡ አይኖርምና ፡ አንዱ ፡ ላንዱ ፡ ቦታ ፡ መኾኑን ፡ ያሳያል ።

**ህላዌ** ፤ ሥራ ፤ ግብር ። ህላዌ ፡ ገፍዕ ፤ የግፍ ፡ ሥራ ፡ ግዙፍ ፡ ግፍ ፡ (ሔኖ፺፩ ፡ ፩) ። እንዲህ ፡ ከኾነ ፡ የህላዌንና ፡ የጠባይዕን ፡ ፍች ፡ በየስልቱ ፡ ማስተዋል ፡ ይ ገባል ፤ ኹለቱ ፡ ኹሉ ፡ ፩ ፡ ናቸውና ።

**ህሉና** ፤ **ህልውና** ፤ ነዋሪነት ፤ አነዋወር ፡ ኑሮ ። ህሉና ፡ ሥላሴ ። ህሉና ፡ መለኮት ፡ (ቅዳ) ።

**አህለወ** ፤ አኖረ ፤ አስኖረ ፤ አስቀመጠ ፤ ነዋሪ ፡ አ ደረገ ፤ አስደረገ ። ወምስለ ፡ ብዙኅ ፡ ምሕረት ፡ ታሃ ልወነ ፡ (ጥበ፲፪ ፡ ፲፰) ።

**ምህላው** ፤ መኖሪያ ፤ ቦታ ፡ ሀገር ። ነፍስ ፡ እመ ፡ ተፈልጠት ፡ እምሥጋ ፡ በሞት ፡ ገብአት ፡ ኅበ ፡ ብርሃን ፤ ዘውእቱ ፡ ማኅደሩ ፡ ወምህላዊ ፡ ወፍግ ዓሃ ፡ ወተድላሃ ። ነሥአ ፡ ለሀገረ ፡ ባቢሎን ፡ ወተወ ፈየ ፡ ምህላወ ፡ ብልጣሶር ፡ (ዮሴፍ) ።

**ሀለወ** ፤—**ጠበቀ** ፤—**ኀሊው ፡ ኀለወ** ።

**ሀለየ** ፤—**ዘፈነ** ፤—**ሐልይ ፡ ሐለየ** ።

**ሀሊል** ፤ (**ሀለ ፡ የሀልል ፡ ይሀልል ። ዕብ ፡ ሀሎል ፡ ሄል**) ፤ ማወደስ ፡ ማመስገን ፤ መየበብ ፡ መ ዝፈን ።

**ሃሌ** ፤ (**ሀሌ ። ዕብ ፡ ሀሌል**) ፤ ሃሌታ ፤ ስብ ሐት ፡ ውዳሴ ፤ መዝሙር ፡ ግናይ ፤ ቅኔ ፡ ሐዲስ ፡ ምስ ጋና ፤ መዘምራን ፡ ሃሌ ፡ ሃሌ ፡ ብለው ፡ የሚመሩት ፤ በ ሃሌታ ፡ የሚዘምሩት ። አንቀጽ ፡ ሃሌታ ፡ እንዲሉ ። (ተ ረት) ፤ መዝሙር ፡ በሃሌ ፤ ነገር ፡ በምሳሌ ፤ ጠጅ ፡ በብ ርሌ ። ሃሌታና ፡ እልልታ ፡ በምስጢር ፡ አንድ ፡ ነው ፤ አስለን ፡ ተመልከት ።

**ሃሌ ፡ ሉያ** ፤ (**ዕብ ፡ ሀልሉ ፡ ያህ**) ፤ ሰ ብሑ ፡ እግዚአ ፤ ሀልሉ ፡ ስብሑ ፤ ያህ ፡ እግዚእ ፡ አም ላክ ። ወርኀ ፡ ሃሌ ፡ ሉያ ፡ (ዘፀ፲፫ ፡ ፬) ። አቢብን ፡ ተመ ልከት ።

**ህላል** ፤ (**ዐረ ፡ ሂላል**) ፤ ሠርቀ ፡ ወርኅ ፤ ል ደት ፡ ወርኅ ፤ ሐዲስ ፡ ስጋ ፡ ጨረቃ ።

**ህላሊ** ፤ ሠርቃዊ ፡ ወርኃዊ ፤ የጨረቃ ፡ ወር ። አውራኅ ፡ ህላል ፤ ህላሊ ፡ (አቡሻ ፡ ፳፩) ።

**ሆሙ** ፤ (**ሁ**) ፤ የሩቅ ፡ ወንዶች ፡ ዝርዝር ፡ ጠ ቃሽ ። የሁን ፡ አፈታት ፡ እይ ።

**ሀሙዲዳ** ፤ (**ዕብ ፡ ሀሞዔድ**) ፤ ዕድሜ ፡ የ ተወሰነ ፡ ጊዜ ፡ ወራት ፤ የበዓል ፡ የቀጠሮ ፡ ቀን ። ሄጲ ኪር ፡ ሀሙዲዳ ፡ (ኤርሚ ፡ ፲፯) ። ባለብሉዮች ፡ ግን ፡ ሰባራ ፡ ምቱረ ፡ ሥርው ፡ ፈሪ ፡ ይሉታል ።

**ሆሚር** ፤—**መስፈሪያ** ፤—**ሐሜር** ።

**ሆን** ፤—(**ሁ ፡ ሆሙ**) ፤ የሩቅ ፡ ሴቶች ፡ ዝር ዝር ፡ ጠቃሽ ።

**ሀኖስ** ፤ (**ጽር ፡ አኖስ ፡ ያኖስ**) ፤ ክፉሉ ፡ ስም ፡ የውቅያኖስ ፡ ክፋይ ፤ ብጥብጥ ፡ ባሕር ፤ የሚታወክና ፡ የሚናወጽ ፤ የሚደምፅና ፡ የሚደረጽ ። ይኸውም ፡ ከጠ ፈር ፡ በላይ ፡ ያለው ፡ ሚሶው ፡ ውሃ ፡ ነው ፤ አንዱ ፡ እጅ ፡ ጠፈር ፡ አንዱ ፡ እጅ ፡ ውቅያኖስ ፡ እንዲባል ፤ ይህ ፡ ደ ግሞ ፡ ሀኖስ ፡ ይባላል ፡ (ዘፍ፯ ፡ ፲፩ ። ኩፉ ፡ ፩ ። ሱቱ ፡ ዕ ዝ፯ ፡ ፵፩) ። ወበውእቱ ፡ መዋዕል ፡ ይወፅእ ፡ መቅሠ ፍት ፡ ለእግዚእ ፡ መናፍስት ፤ ወይትረኀዉ ፡ ዙሉሙ ፡ መዛግብተ ፡ ማያት ፡ ዘመልዕልተ ፡ ሰማያት ፡ ወዲበ ፡ አንቅዕት ፡ እለ ፡ መትሕተ ፡ ሰማያት ። ወይደምሩ ፡ ዙሉሙ ፡ ማያት ፡ ዘምስለ ፡ ማያት ፡ ዘመልዕልተ ፡ ሰማያት ፤ ማይሰ ፡ ዘመልዕልተ ፡ ሰማይ ፡ ተባዕታይ ፡ ውእቱ ፤ ወማይ ፡ ዘመትሕተ ፡ ምድር ፡ አንስቲያ ዊት ፡ ይእቲ ፡ (ሔኖ ፡ ፵፩) ። ብዙዎች ፡ መተርጕማን ፡ ግን ፡ ፪ቱን ፡ እጅ ፡ ውሃ ፡ ጠፈር ፡ አደረገው ፡ ይላሉ ፡ እ ንጂ ፤ ከጠፈር ፡ በላይ ፡ ብጥብጥ ፡ ባሕር ፡ አለ ፡ አይሉም ።

**ሀውቢም** ፤ (**ዕብራ**) ፤ ወፍራሞች ፤ ደንዳ ኖች ። ወፍሮች ፡ ድንዳኔዎች ፡ (ሕዝ፴፩ ፡ ፳፯) ።

**ሄዔኪር** ፤ (**ዕብ ፡ ሄዔቢር**) ፤ አሳለፈ ፡ አሻ ገረ ፤ አስተላለፈ ፤ የጊዜ ፡ የወራት ። ሐተታውን ፡ በቢድን ፡ ፍች ፡ እይ ፤ ባለብሉዮች ፡ ግን ፡ ደክማ ፡ ዘበጽሐ ፡ ጊ ዜሁ ፡ ኅሱር ፡ ይሉታል ፡ (ኤርሚ ፡ ፲፯) ።

**ሀፈው** ፤ **ዎት** ፤ (**ሀፈወ ፡ የሀፉ ፡ ይሀፉ ። ዐረ ፡ ሀውፍ ፤ ሁፍ ፤ ውውይ ፡ ነፋስ**) ፤ መው ዛት ፡ መድከም ፤ መሞቅ ፡ በላበት ፡ መጠመቅ ። ፈት ወት ፡ ትትኀፀብ ፤ እስመ ፡ ሀፈወት ። እስከ ፡ የሀፍዉ ። ጾመ ፡ ወጸለየ ፡ ደከመ ፡ ወሀፈወ ። በጸዊረ ፡ መስ ቀሉ ፡ ሀፈወ ፤ እስመ ፡ ክቡድ ፡ ውእቱ ፡ (ዳንኤ ፡ ፲፩ ። ሥር ፡ ጸዘ ። ግንዘ ። ቅዳ ፡ ግሩ) ።

**ሀፍ** ፤ (**ዕብ ፡ ዚዓህ**) ፤ ወዝ ፡ ላበት ፤ ድካም ፡ (ዘፍ፫ ፡ ፲፱ ። ሉቃ፳፪ ፡ ፵፬) ። አብዝኅ ፡ ስግደተ ፡ እስከ ፡ ይውሕዝ ፡ ሀፉ ፡ ከመ ፡ ማይ ። ዘእንበለ ፡ ጻማ ፡ ወ ሀፍ ። ፈነዉ ፡ ሲሳዮሙ ፡ እምንዋይ ክሙ ፡ ወሀፈ ፡ ገጽክሙ ፡ (ገድ ፡ ተክ ። አፈ ፡ ተ፫ ። ዲድ ፡ ፳፩) ።

—፤ ሙቀት ፤ ሐሩር ። ቍር ፡ ወሀፍ ። ብሔረ ፡ ጽምእ ፡ ወሀፍ ። ሀፍ ፡ ወሞቅ ፡ (ዘፍ፰ ፡ ፳፪ ። ዘዳ፴፪ ፡ ፲ ። ሔኖ፷፪ ፡ ፲፮) ።

**ሀርበደ፤(አብደ። ዐረ ፡ ዐርበደ፤ ከፋ ፡ ክፉ ፡ ኾነ)፤** አረበደ፤ ቸኰለ። ተቈጣ ፡ አበደ ፡ እብድ ፡ አለ ። ደነገጠ ፡ ደነበረ ፤ ወገሸ ፡ አገረገረ ፤ ሸሸ ፡ ሮጠ ፡ ፈረጠጠ ፤ የከብት ። ከመ ፡ ዕጐልት ፡ እንተ ፡ ተሀረብድ ፡ ሀርበደ ፡ ኤፍሬም ፡ (ሆሴ፱ ፡ ፲፮) ።

—፤ ተቀናጣ ፤ ተቀማጠለ ፤ ሰው ፡ ልፍድ ፡ አለ ፤ የዘመናይ ። ወለእመ ፡ ቀተለ ፡ በሀርብዶ ፡ ኢይከውን ፡ ዙኑ ኔሁ ፡ ከመ ፡ ዙነኔ ፡ ሰብዳን ፡ (ፍ ፡ ነ ፡ ፵፯) ። አንዳንድ ፡ መጣፍ ፡ በተሀርብደ ፡ ይላል ፡ ስሕተት ፡ ነው ።

**ሀርብድና፤** መቀማጠል ፤ ቅምጥልነት ፤ የቅንጦት ፡ ሥራ ። ወለእመ ፡ ከንከ ፡ ዘመነንካሁ ፡ ለህርብድና ፡ ጕየይ ፡ እምእበ ፡ ይንዐውዎ ፡ (ማር ፡ ይሥ፪ ፡ ፲፪) ።

**ሄሮድያኖስ፤(ጽር ፡ ሄሮዲዎስ)፤** የሞራ ፡ ስም ፤ ሽመላ ፡ ሽመላዊ ፤ እግረ ፡ ሽመል ፡ ዐንገተ ፡ ግመል ፤ እግሩ ፡ ሽመል ፡ የሚያካክል ። (ተረት) ፤ ካህንና ፡ ሽመላ ፡ ያልዘራውን ፡ ይበላ ። ሄሮድያኖስ ፡ በሰማይ ፡ የአምር ፡ ዕድሜሁ ፡ (ኤር፰ ፡ ፯ ። ዘሌ፲፩ ፡ ፲፱ ። መዝ ፡ ፻፫ ። ዘዳ፲፬ ፡ ፲፰) ።

ሄሮድያኖስ ፤

**ሄሮድስ፤(ዕብ ፡ ሆርዶስ)፤** የሰው ፡ ስም ፤ ኤዶማዊ ፡ የእስራኤል ፡ ንጉሥ ፤ በዘመነ ፡ ልደት ፡ የነበረ ፡ (ማቴ፪ ፡ ፩) ።

**ሀረመ፤—ተወ፤—ሐሪም ፡ ሐረመ ።**

**ሄርማ፤** የመጽሐፍ ፡ ስም ፤ ሐዋርያው ፡ ቅዱስ ፡ ጳውሎስ ፡ የጠፈው ፤ እንደ ፡ ማልስ ፡ ቆሮንቶስ ፡ ያለ ፡ ከቀኖር ፡ ያልገባ ፡ ትርፍ ፤ ወሬድየ ፡ ብሔረ ፡ ሮሜ ፡ ብሎ ፡ የሚዠምር ። ስምነቱ ፡ ሄርሜን ፡ ከማለት ፡ የወጣ ፡ ነው ፤ ሄርሜናዊ ፡ ያሰኛል ፤ ጸሐፊው ፡ ሄርሜን ፡ ስለ ፡ ተባለ ፡ መጽሐፉም ፡ ሄርማ ፡ ተብሏል ።

**ሄርሜን፤(ጽር ፡ ሄርሜን)፤** ጣዖት ፡ ስመ ፡ ጣዖት ፤ በመንታ ፡ መንገድ ፡ ላይ ፡ የሚያቆሙት ። መሪ ፡ አስተማሪ ፤ ትርጁማን ፡ አፈ ፡ በሃማን ፡ ማለት ፡ ነው ፡ (ግብ፲፬ ፡ ፲፪) ።

**ሀሴቦን ፤ (ጽር ፡ ሄሴቦን) ፤** ውስጠ ፡ ዐውስጥ ፤ ውሳጣዊ ። ዙሉ ፡ ከብራ ፡ ለወለተ ፡ ንጉሥ ፡ ሀሴቦን ፡ (መዝ ፡ ፵፬) ።

**ሄሴፎት፤(ዕብ ፡ ሀአሲፎት)፤** የጥራጊ ፡ የጕድፍ ፡ መጣያ ፤ ያዘባ ፡ የፍግ ፡ መቈለያ ፤ ባለብሉዮች ፡ ግን ፡ ግናይ ፡ ይሉታል ። አንቀጸ ፡ ሄሴፎት ፡ (ነሐ፲፪ ፡ ፴፩) ።

**ሆሴዕ፤(ዕብ ፡ ሆሼዕ)፤** የሰው ፡ ስም ፤ ነቢይ ፡ ንጉሥ ። አድኅን ፡ ባልሐ ፤ ረድእ ፡ አውፅእ ፡ እመሥገርት ፡ ማለት ፡ ነው ፡ (ሆሴ፩ ፡ ፩ ። ፬ነገ ፡ ፲፭ ፡ ፴) ።

**ሆሳዕና ፤ (ዕብ ፡ ሆሺዓሀ—ናእ) ፤** አንቀጽና ፡ ጥሬ ፤ አድኅነነ ፤ አድነና ፤ አድነንዮ ፤ እባክኽ ፡ አድነን ፤ የአን ፡ ፍች ፡ ተመልከት ፡ (ማር፲፩ ፡ ፲ ። ዮሐ፲፪ ፡ ፲፫) ።

—፤ መድኀኒትነት ፤ መድኀኒት ፡ መኾን ፤ ወይም ፡ መባል ። ሆሳዕና ፡ ለወልደ ፡ ዳዊት ። እምሆሳዕናሁ ፡ ለ ርእየ ፡ ተኣምረ ፡ ወመንክረ ፡ (ማቴ፳፩ ፡ ፱ ። ቅዳ ፡ ጎር) ።

—፤ የበዓል ፡ ስም ፤ የሰሌን ፡ በዓል ፤ ሰሌን ፡ ይዘው ፡ እያመሰገኑ ፡ የሚያውዱበት ፤ ለብሉዩ ፡ የመጸለት ፡ ፯ኛ ፡ ቀን ፤ ለሐዲሱ ፡ ግን ፡ ከትንሣኤ ፡ በፊት ፡ ያለ ፡ እሑድ ። (የደሮች ፡ ዘፈን) ፡ በሆሳዕና ፡ ተሰበሰብና ፤ በሳምንቱ ፡ አለብን ፡ ሞቱ ። ዋዜማ ፡ ዘሆሳዕና ። በሳኒታ ፡ ሆሳዕና ፡ በሰኑይ ፡ ዕለት ፡ (ድጓ ። ዲድ ፡ ፳፱) ።

ሆሳዕና ፤

—፤ ሰሌን ፡ የሰሌን ፡ ቅጠል ፤ ቈጽለ ፡ ዘይት ፤ ባርሰነት ፡ ኵሐ ፤ የመሰለው ፡ ኹሉ ፤ የሆሳዕና ፡ ለት ፡ የሚያዝ ። ዘይትን ፡ ወሆሳዕና ። ልብሱ ፡ እምልሕጸ ፡ ሆሳዕና ፡ ወቈጽሉ ፤ ሰሌን ፡ (ስንክ ፡ መስ፫) ።

**ሁስጱ፤(ጽር ፡ ሒሶፖስ)፤** የቀንበጥ ፡ ችቦ ፤ ለባልግ ። አዛብን ፡ ተመልከት ፤ ከዚህ ፡ ጋራ ፡ ፩ ፡ ነው ፤ ባለብሉዮች ፡ ግን ፡ ለይተው ፡ ስምዛ ፡ አሸከት ፡ ይሉታል ። ቈጽለ ፡ ሁስጱ ። ሐምለ ፡ ሁስጱ ፡ (ዘሌ፲፬ ፡ ፬ ፡ ፯ ። ፫ ነገ ፡ ፬ ፡ ፴ ። ዮሐ፲፱ ፡ ፳፱ ። ዕብ፱ ፡ ፲፱) ።

**ሀትሒላ፤(ዕብራ)፤** መዝሙር ፡ ምስጋና ። መልእክ ፡ ሀትሒላ ፡ (ነሐ፲፩ ፡ ፲፯) ።

**ሄጳ፤—ወጋ ፡ ገመሰ፤—ሀቡጽ ።**

**ሄጳዴጤን፤(ጽር ፡ ሂፖዲቲስ ። ዕብ ፡ ምዒል)፤** ልብስ ፡ ተክህና ፤ የላይ ፡ ልብስ ፡ ታላቅ ፡ ቀሚስ ፡ እጀ ፡ ሰፊ ፡ መቋረፊያ ። ጳዴሬን ፡ እይ ፤ ከዚህ ፡ ጋራ ፡ ፩ ፡ ነው ፡ (ዘፀ፳፰ ፡ ፬ ። ዘሌ፰ ፡ ፯) ።

**ሄጳዲያቆን፤** (ጽር ፡ ሂፖዲያክኖስ)፤ የዲያቆን ፡ ተወራጅ ፤ ንፍቀ ፡ ዲያቆን ፡ (መጽ ፡ ምስ)።

**ሄጳጳ፤** (ጽር፡ሂፖፓ፤ሂፖፖስ)፤ ስሙ ፡ ያፍ ፡ ንኡስ ፤ መጠኑ ፡ የርግብ ፡ የዋኖስ ፤ ቍንጮዉም ፡



እፈ ፡ ረዥም ፡ የሾለቅ ፡ ዐይነት ፡ ዝንጕርጕር ፡ ኵሳኵስ ። ባለብሉዮች ፡ ግን ፡ ዐቢይ ፡ አሞራ ፡ ይሉታል ፡ (ዘሌ፲፩ ፡ ፲፱ ። ዘዳ፲፬ ፡ ፲፰)።

(ጥ) **ሀፐለ፤** (ዐረ ፡ አበለ ፤ ወበለ)፤ ዐጠበ ፤ መታ ፡ ደበደበ ። በመርገጥና ፡ በመጠቅጠቅ ፡ ፈንታ ፡ በ ዱላ ፡ እየመቱ ፡ የሚያጥቡት ፡ ዕጥበት ፡ አለና ፤ ዕጥበቱ ንም ፡ አመታቱንም ፡ ባንድነት ፡ ያሳያል ።

**ሀፓሊ፤ መሀፕል፤ መሀፒል፤** እየመታ ፡ የሚያጥብ ፡ ዐጣቢ ። ገራህት፡መሀፒል ። ዘኢይክል፡ መሀፒል፡አጻዕድዎ፡ከማሁ፡(ኢሳ፯ ፡ ፫ ። ፴፮ ፡ ፪ ። ማር፱ ፡ ፫)።




**ወ፤** ፳ኛ ፡ ፊደል ፤ በግእዝ ፡ አልፍ ፡ ቤት ፡ በአ በገደ ። ስሙ ፡ ዋዌ ፤ ቍጥሩ ፡ ስድስት ፤ አኀዝ ፡ ሲኾን ፡ ወ፡ስድስት፤ስድስት ፡ ቱ ፡ ይባላል ። ዕብራውያን ፡ ግን ፡ ስድስትን ፡ መደብ ፡ አድርገው ፡ በራሱ ፡ ላይ ፡ ነቍጣ ፡ እየጨመሩ ፡ ስድስት ፡ እልፍ ፡ ይሉታል ። ፳ኛ ፡ ማለት ፡ ምስጢሩ ፡ ዐርብንና ፡ የዐርብን ፡ ፍጥረት ፡ መደብ ፡ አድ ርጎ ፤ ዳግማይ ፡ አዳም ፡ ሥጋው ፡ ቃልን ፡ ምስጢረ ፡ መ ስቀልን ፡ ያሳያል ፤ የዋዌን ፡ ፍች ፡ ተመልከት ።

**ወ፤** (ሂ ፡ ኒ ፡ ዓዲ)፤ ንኡስ ፡ አገባብ ። አጫ ፋሪ ፤ ማስሪያ ፡ ከፋይ ፤ አኃናኝ ። ም ፤ ና ፤ ቻልታ ፡ ዘተ ረስዐ ፤ ውጥን ፡ ጨራሽ ፤ የአኃዝ ፡ ጠቅላይ ፡ ከ ፤ በ ፡ ጊዜ ፤ ስንኳ ፤ ግን ፤ ስ ፤ ፈጽሞ ፤ አዳማቂ ፤ ትች ፡ ይኾናል ። ም ፡ ሲኾን ፡ በኹሉ ፡ ይገባል ፤ በልዐ፡ወሰትየ፡ሰምዐ፡ወ ርእየ ። ና ፡ ሲኾን ፡ በስም ፡ ይገባል ፤ ጴጥሮስ፡ወጳው ሎስ ፤ ያዕቆብ፡ወዮሐንስ ። በሦስት ፡ ስሞች ፡ ሲገባ ፤ መዠመሪያው ፡ ና ፡ ኹለተኛው ፡ ም ፡ ይኾናል ፤ ጳው ሎስ፡ ወስልዋኖስ ፡ ወጢሞቴዎስ ። በብዙ ፡ ስሞች ፡ ሲገባ ፡ ጭራሽ ፡ ም ፡ ይኾናል ፤ ወይም ፡ ጠቅላይ ፡ ኹኖ ፡ በአብ ፡ በወልድ ፡ በመንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ስም ፡ ያሰኛል ። ተንሥአ፡ወኀደገ፡ልብሶ ፤ ተጠምቀ፡ወአድኀኑ፡ር እሶ ፤ ቻልታ ፤ ልብሱን ፡ ጥሎ ፡ ራሱን ፡ አድንኖ ። ዘተ ረስዐ ፡ ሲኾን ፡ የኋሊት ፡ ይፈታል ፤ ወ ፡ የወደቀበት ፡ ማ ሰሪያ ፤ ያልወደቀበት ፡ ቻልታ ፡ ይኾናል ፤ ይበሉ፡ወይ ርአይ ፤ ገብቶ ፤ ሐመ፡ወሞተ ፤ ታሞ ፤ ሖረ፡ወመጽአ ፤ ኺዶ ፡ መጣ ። ተሰቅለ፡ጴጥሮስ፡ወከማሁ፡እንድር ያስ ፤ ተውህበ፡ጳውሎስ፡ሙቁሐ፡ወካልኣንሂ፡ሙ ቁሓን ፤ ውጥን ፤ ይህ ፡ የፊቱን ፡ በኋላ ፡ ሲጨርስ ፡ ነው ። የኋላውን ፡ በፊት ፡ ሲጨርስ ፤ ሰማይ፡ወምድር፡የ ኀልፍ፡ይላል ፤ ሰማይም ፡ ያልፋል ፤ ምድርም ፡ ታልፋ ለች ፡ ያሰኛል ፤ ሰማይ ፡ ምድር ፡ ያልፋል ፡ ተብሎም ፡ በጠቅላይነት ፡ ሊፈታ ፡ ይቻላል ፤ ባላገባቦች ፡ ግን ፡ ጋራ ፡ ይሉታል ። ዐሠርቱ፡ወክልኤቱ ፤ ሰብዓ፡ወኀም ስቱ ፤ ሠለስቱ፡ ምእት፡ ዐሠርቱ፡ ወሰመንቱ ፤ ጠቅ ላይ ። እልፍ፡ወዕሥራ፡ምእት፡ከ ፡ ና ። ወተወሊዶ፡ ወጸቢሖ ፤ በ ፡ ጊዜ ። ኢወሀቦ፡ርስተ፡ ወኢመጠነ፡ ምከያደ፡ እግር ፤ ስንኳ ። ጸድቀ፡ ቄርሎስ፡ ወኢጸ ድቀ፡ንስጥሮስ ፤ ግን ። እንጂም ፡ ይኾናል ፤ ምስጢሩ ፡ ያው ፡ ነው ፤ በልዐ፡ወኢሰትየ ፡ ብሎ ፡ አልጠጣም ፡ እ ንጂ ፡ ያሰኛል ። ምንተ፡ ንበልዕ፡ ወምንተ፡ንሰቲ ስ ። ሖረ፡ወንሰፈ ፤ ከተበ፡ወጸሐፈ ፤ ፈጽሞ ። ፈጽሞ ፡ ያሰኘው ፡ ያናቅጽ ፡ ኅብረት ፡ የፍች ፡ አንድነት ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ ምስጢሩና ፡ ሙያው ፡ ከጫፋሪነት ፡ አይወጣም ። አዳማቂ ፡ ሲኾን ፡ እንደ ፡ ከመ ፡ በሣልሳይ ፡ አንቀጽ ፤ ስምዐኒ ፡ ወእንግርከ ፤ ቅረበኒ፡ ወእግሰስከ ፤ ኢትግ በራ ፡ ለእኪት፡ ወኢይርከብከ፡ እኩይ፡ እያለ ፡ ይገ ባል ። ትች ፡ ሲኾን ፤ ምንተ ፡ ትሁቡኒ ፡ ወአነ ፡ ኣገብኦ ፡ ለክሙ ፡ ይላል ። ወ ፡ እኹል ፡ ገብ ፡ ፊደል ፡ ስለ ፡ ኾነ ፡ ስልቱና ፡ አፈታቱ ፡ ብዙ ፡ ነውና ፤ የቀረውን ፡ በግስ ፡ ዐመ ልና ፡ በፊደል ፡ ታሪክ ፡ በንኡስ ፡ አገባብ ፡ ተመልከት ። ኹለተኛም ፡ የግስ ፡ ዐመል ፡ ኹኖ ፡ ፊደልን ፡ ኹሉ ፡ ዛ ዕብና ፡ ሳብዕ ፡ ያደርጋል ። የካዕብ ፡ የሳብዕ ፡ ሥረያቸው ፡ ወ ፡ ነው ፤ ሥረይነቱ ፡ እንዲት ፡ እንደ ፡ ኾነ ፡ በፊደል ፡ ታሪክ ፡ እይ ። በማርኛም ፡ እንደ ፡ መ ፡ ባዕድ ፡ ዘር ፡ ይኾናል ፤ ጠመደ ፤ ወጥመድ ። ነበረ ፤ ወንበር ። ሰፋ ፤ ወሰፌ ። ነፋ ፤ ወንፊት ። ዐገመ ፤ ዋገምት ፤ የመሰሰው ፡ ኹሉ ።

**ዊ፤** (ዊ—ዪ)፤ ወገን ፡ ቅጽል ፤ የ ። ምድራዊ ፡ ሰማያዊ ፡ እያለ ፡ እንደ ፡ ምእላድ ፡ በጫፍ ፡ በትራስ ፡ ይገ

ባል ። ፪ኛም ፡ ግብረ ፡ ሰብእ ፡ ያለውን ፡ ግብር ፡ ሰብ እዊ ፡ ይላልና ፡ በዚህ ፡ ምክንያት ፡ የሙሻዘር ፡ ውስጠ ፡ ዘ ፡ ይባላል ። ዊና ፡ ዩ ፡ አንድ ፡ ወገን ፡ ናቸው ።

**ዋ፤ (ዋ—ኣ)፤** የራብዕ ፡ ሥረይ ፡ (ዋየል) ፡ ላ ራቱ ፡ ዲቃሎች ፤ ኣ ፡ ኋ ፡ ኳ ፡ ቋ ፤ ጉዋ—ኋ ። በነዚህ ፡ አንጻር ፡ ለሚገኙም ፡ ለራብዖች ፡ ኹሉ ፡ ላማርኛ ፡ ፊ ደል ፡ ሥረይ ፡ ይኾናል ፤ ቡዋ—ቧ ። ባማርኛም ፡ የሐዘ ንና ፡ የንቀፌታ ፡ ቃል ፡ ይኾናል ።

**ው፤** አብኹ ፡ ምእላድ ። በግላ ፡ በጋልው ፤ በላ ድው ፡ ወላትው ፤ የመሰለው ፡ ኹሉ ። የወዲያኛው ፡ ትግ ሬም ፤ ቀርቡ ፡ መጽኡ ፡ ፈርሁ ፡ ደንገፁ ፡ ሲል ፡ ቀርበው ፡ መጽአው ፡ ፈርሀው ፡ ደንገፀው ፡ ይላል ።

**ው፤** ያማርኛና ፡ የጥንታዊ ፡ ግእዝ ፡ ዝርዝር ፤ ግእ ፡ ቀተለው ፡ ሎ ፤ ቀተልከው ፡ ኮ ። ዐማ ፡ ገደለው ፤ ገደልከው ። ውን ፡ ጐርደ ፡ ቀተሎ ፡ ልኮ ፡ ማለት ፡ የሐ ዲስ ፡ ግእዝ ፡ ነው ።

**ወእደ፤ ውእደ፤ (እድ ፡ ወእድ)፤** ዐቢ ይና ፡ ደቂቅ ፡ አገባብ ። ከ—ተ—ዘንድ ፤ የ ፤ ቅጽል ። ወ እደ ፡ አልቦ ፡ አልሕምት ፡ ምፅንጋዕ ፡ ንጹሕ ። ላሞች ፡ ከሌሉ ፤ ተሌሉ ፡ ዘንድ ፤ ወይም ፡ ከ ፡ ተሌሉበት ፡ ዘንድ ። ምኔት ፡ ውእደ ፡ ሰሲሁ ፡ ይነብር ፤ የሚኖርበት ። ወመ ጽአ ፡ ኀቤሃ ፡ አሐዱ ፡ ወሬዛ ፡ እምወእደ ፡ ይትኄ ባእ ፤ ከተደበቀበት ፡ (ምሳ ፲፱ ፡ ፪ ። ሥር ፡ ጻሆ ። ዳን ፩ ፡ ፴፯ ። (ዕር ፲፱ ፡ ቍ፭) ።

—፤ ደቂቅ ፡ ሲኾን ፡ ወደ ፤ አጠገብ ፡ ይኾናል ፤ ወደ ፡ ወ ዴት ፡ ማለት ፡ ዐማርኛው ፡ ከዚህ ፡ ወጥቷል ። እቱ ፡ ው እደ ፡ ሕዝብከ ፤ ወደ ። በውእደ ፡ ማየ ፡ ባሕር ፤ አጠ ገብ ፡ (ኩፋ ፡ ፰) ። ኀበና ፡ መንገለም ፡ እንደዚሁ ፡ ናቸው ፤ ዘሩ ፡ አደወ ፡ ነውና ፡ የእድን ፡ አፈታት ፡ ተመልከት ።

**ውእቱ፤ (ዕብ ፡ ወሑር ፡ ሁ ። ዐረ ፡ ሁወ)፤** ነባር ፡ ቅጽልና ፡ ነባር ፡ አንቀጽ ፡ ከሁ ፡ የወጣ ፤ ያ ፤ ያኛው ፤ ርሱ ፤ ቅጽልና ፡ ዐጸፋ ፡ ለሩቅ ፡ ወንድ ። ይ እቲ ፤ ውእቶሙ ፡ እሙንቱ ፤ ውእቶን ፡ እማንቱ ፤ አነ ፡ አንተ ፡ ንቲ ፡ ትሙ ፡ ትን ፤ ንሕነ ፡ እያለ ፡ እስከሥር ፡ ይረ ባል ፤ የሁን ፡ አፈታት ፡ እይ ። ውእቱ ፡ ብእሲ ፤ ይእቲ ፡ ብእሲት ። ለውእቶሙ ፡ አሕዛብ ፤ በውእቶን ፡ መዋ ዕል ፤ ቅጽል ። ውእቱ ፡ ይጸንዕ ፡ እምኔየ ፤ ዐጸፋ ። ዝ ኩንና ፡ ዝስኩን ፡ ዝክቱን ፡ ተመልከት ፤ የዚህ ፡ አንጻር ፡ ናቸው ። አንቀጽ ፡ ሲኾን ፡ ደግሞ ፤ ነው ፡ አለ ፤ ኖረ ፡ ነ በረ ፤ ኾነ ፤ እስከ ፡ ንሕነ ፡ ድረስ ፤ ኹሉ ፡ እንዲህ ፡ ነው ። ውእቱና ፡ በ ፡ ሎ ፡ ኮንና ፡ ሀሎ ፡ ሱቱፋን ፡ ናቸው ፡ ይወ ራረሳሉ ፤ ይኸውም ፡ ቀዳሚሁ ፡ ቃል ፡ ውእቱ ፡ ወው እቱ ፡ ቃል ፡ ኀበ ፡ እግዚእ ፡ ውእቱ ፡ ባለው ፡ ይታወ ቃል ። ውእቱ ፡ ባንድ ፡ ጊዜ ፡ ዐጸፋና ፡ አንቀጽ ፡ ይኾ ናል ፤ ዘወረደሂ ፡ ውእቱ ፡ ወዘዐርገሂ ፡ ውእቱ ። ፪ ኛም ፡ በግብር ፡ ለውጥ ፡ ሩቁን ፡ በቅርብ ፡ ቅርቡን ፡ በ ሩቅ ፤ አንዱን ፡ በብዙ ፤ ብዙውን ፡ ባንድ ፤ ወንዱን ፡ በሴት ፤ ሴቱን ፡ በወንድ ፡ ያናገራል ። አንተ ፡ ውእቱ ፡ ዘይገብር ፡ ዙሎ ፤ አምላክ ፡ ውእቱ ፡ ዘለብሰ ፡ ሥጋ ። ማርያም ፡ ይእቲ ፡ ኪሩቤል ፤ ወኪሩቤል ፡ እሙ ንቱ ፡ ማርያም ፡ ሰ ፡ በ ፡ እምጸዊረ ፡ አምላክ ። የፊተ ኛው ፡ ኹለቱ ፡ አካልን ፡ ያመጣል ፤ የኋለኛውም ፡ ኹ ለቱ ፡ ግብርን ፡ ይገልጣል ። በአካል ፡ ለውጥ ፡ ግን ፡ በየ ራሱ ፡ ያናግራል ፤ ወይም ፡ ተለዋጭ ፡ ይኾናል ። እመ ፡ አምላክ ፡ ማርያም ፡ ይእቲ ፤ ማርያም ፡ እመ ፡ አም ላክ ፡ ይእቲ ። ድንግል ፡ ዘተናገራ ፡ ኢሳይያስ ፡ ማር ያም ፡ ይእቲ ፤ ማርያም ፡ ዘተናገራ ፡ ኢሳይያስ ፡ ድ ንግል ፡ ይእቲ ፤ እብን ፡ ዘወሀቦ ፡ ሰይጣን ፡ ለእግዚ እነ ፡ ኅብስት ፡ ውእቱ ፤ ኅብስት ፡ ዘወሀቦ ፡ ሰይጣን ፡ ለእግዚእነ ፡ እብን ፡ ውእቱ ። ቅጽል ፡ ከባለቤት ፡ ሲ ርቅ ፡ ተለዋጭ ፡ ይባላል ፤ ተለዋጭ ፡ ደግሞ ፡ ግብር ፡ ነገር ፡ ባሕርይ ፡ ይተረጕማል ፡ አካል ፡ ያመጣል ፡ አስቀድመን ፡ እንደ ፡ ተናገርነ ፤ አካልም ፡ ኹኖ ፡ ቅጽልም ፡ ኹኖ ፡ ማስ ሪያ ፡ ከወደቀበት ፡ ተለዋጭ ፡ ይኾናል ። ፫ኛም ፡ በሰዋ ስው ፡ ኹሉ ፡ በጥሬ ፡ በቅጽል ፡ በሚስማማው ፡ ቃል ፤ ሳይጣፍና ፡ ሳይነገር ፡ ተደብቆ ፡ ያስራል ፤ ይልቁንም ፡ በ ቅኔ ፡ ንባብ ። ተሠግዎቱ ፡ ለቃል ፡ ወተጸልቦቱ ፡ በሥጋ ፡ ያድኅን ፡ ዓለመ ፡ ወይቤዙ ፡ ሰብአ ። ዘተሰቅለ ፡ በቀ ራንዮ ፡ ሥግው ፡ አምላክ ፡ ጽድቅ ፡ ወአኮ ፡ ብእሲ ፡ ዕሩቅ ፤ የውእቱ ፡ መመርመሪያ ፡ ያድኅንና ፡ ይቤዙ ፤ አም ላክ ፡ ጽድቅ ፡ ናቸው ።

**ወባ፤ (ዐረ ፡ ወባእ)፤** የበሽታ ፡ ስም ፤ ከክፉ ፡ ሽታ ፡ የሚመጣ ፤ በሽታ ፡ ምክንያት ፡ የሚጋባ ፡ እንደ ፡ ጕንፋን ፡ ያለ ። በቁሙ ፡ ወባ ፤ ንዳድ ። ሕማመ ፡ ወባ ፡ (ዮሴፍ) ።

**ወቦ፤** ስመ ፡ ኮከብ ፤ ስመ ፡ ጭፍራ ። ወቦና ፡ በቾ ፡ እንዲሉ ።

(ጥ) **ወበ፤ (ወቢብ ፡ ወበ ፤ ነጠቀ)፤** ያውሬ ፡ ስም ፤ የነብርና ፡ ያንበሳ ፡ ዲቃላ ። ወቦ ፡ ሸማኔ ፡ እንዲሉ ። ኹሉም ፡ ዐማርኛ ፡ ነው ።

**ዌበርከኤቦት፤ (ጽር ፡ ዌባርካቦት ። ዕብ ፡ ኢካቦድ)፤** የሰው ፡ ስም ፤ ኢስብሐት ፡ ወኢ ክብር ፤ ክብር ፡ የለውም ፡ ማለት ፡ ነው ። ባለብሉዮች ፡ ግን ፡ ትክብር ፡ ኹኖ ፡ ትሾም ፡ ኹኖ ፡ በስደት ፡ ይሉታል ። አባቱና ፡ አንቱ ፡ ሙተው ፡ እስራኤል ፡ ድል ፡ ኹነው ፡ ታቦተ ፡ ጽዮን ፡ ወደ ፡ ኢሎፍሊ ፡ የተማረከች ፡ ለት ፡ ስለ ፡ ተወለደ ፤ ኢካቦድ ፡ ተብሏል ፡ (፩ነገ ፡ ፬ ፡ ፳፩) ።

**ወጊእ፤ አት፤ (ወግአ ፡ ይወግእ ፡ ይ ጋእ፤ አው ፡ ይውጋእ ። ዕብ ፡ ናጋሕ ። ዐረ ፡ ወጀአ)፤** መውጋት ፡ መደደቅ ፡ መደንጐር ፤ መዘርከት ፡ መቸብለክ ፡ መቸክቸክ ። መውገጥ ። ለእመ ፡ ወግአ ፡ ላሕም ፡ ብእሴ ። ወጋእክሙ ፡ ከመ ፡ አስዋር ። በ ሐሡ ፡ ይወግእ ፡ በአቅርንቲሁ ። ወግአኒ ፡ በሡያንው ። ወግአኒ ፡ ሦክ ። እለ ፡ ወግእዎ ፡ (ዘፀ፳፩ ፡ ፳፰ ። ኤር፳፯ ፡ ፲፩ ። ዳን፰ ፡ ፬ ። ኢዮ፲፯ ፡ ፲፫ ። መዝ ፡ ፴፩ ። ራእ፩ ፡ ፯) ። ድል ፡ ማድረግ ፡ ማሸነፍ ፡ መግደል ፤ የሸሸውን ፡ ማሳ ደድ ፡ መከተል ። ብከ ፡ ንወግአሙ ፡ ለዙሎሙ ፡ ፀርነ ፡

(መዝ ፡ ፵፫ ። ኢያ፲ ፡ ፲ ። ፲፯ ፡ ፲ ። ዘዳ፩ ፡ ፵፬ ። ዮዲ፲፯ ፡ ፲፱) ። ዋግ ፡ ማለት ፡ ከዚህ ፡ ወጥቷል ።

**ወጋኢ ፤ (ኢት ፡ እያን ፡ ያት) ፤** የሚወጋ ፤ የሚወግጥ ፤ ወጊ ፡ ተዋጊ ፡ (ዘፀ፳፩ ፡ ፴፮ ። ፍ ፡ ነ ፡ ፵፭) ።

**ሞግአ ፡ መውግእ ፤ ሙጋእ ፤ (ብ ፡ መዋግእ) ፤** መውጊያ ፡ መውጊጫ ፤ ማፍረሻ ፤ ቀንድ ፡ ዘ ገር ፤ ሙገጫ ፡ የሙገጫ ፡ ግልገል ፤ ድጅኖ ፡ ደንጉራ ። ተወግአ ፡ በአሐዱ ፡ ሙጋእ ። ይጕድዕዎ ፡ ውስተ ፡ ሞግእ ። ከመ ፡ ይትክሉ ፡ ሞግአ ፡ ኀጺን ፡ ላዕለ ፡ ቅጽር ። ተከለ ፡ መዋግአ ፡ ዘነፍጥ ፡ (ሥር ፡ አኸ ። አዋል ። ዮሴፍ) ።



ሞግእ ፡

**ተወግአ ፤** ተወጋ ፤ ተወገጠ ። (ተረት) ፤ ያወቀ ፡ ተጠነቀቀ ፤ የዘነጋ ፡ ተወጋ ። ሰላም ፡ ለገበዋቲከ ፡ በቅትራተ ፡ ኀጺን ፡ እለ ፡ ተወግኡ ፡ (ደራሲ) ።

**ውጉእ ፤ (ኣን ፡ ኣት ፡ ግእት) ፤** የተወጋ ፡ ውግ ፤ የተወገጠ ፡ ውግጥ ። እለ ፡ ውጉኣን ፡ በኲናት ። ቅብዐ ፡ ዘይት ፡ ውጉእ ፡ (ዘፀ፳፯ ፡ ፳ ። ዘሌ፳፬ ፡ ፪) ።

**ውግአት ፤** መውጋት ፡ መወጋት ፡ አወጋግ ፤ ውጊ ፡ ውጊያ ፤ ውግታት ፤ በቁሙ ፡ ውጋት ። ውግአተ ፡ ሦክ ፡ (ስንክ ፡ ጥር፫) ።

**ተዋግአ ፤** ተዋጋ ፤ ተተማተመ ። ይትዋግኡ ፡ በኲናት ፡ (አዋል) ።

**ወግአ ፤—ጋተ ፡ አገነፋ ፤—ወጊዕ ፡ ወግዐ ።**

**ወጊብ ፤ ቦት ፤ (ወገበ ፡ ይወግብ ፡ ይገብ ፤ ይውግብ ። ዐረ ፡ ወጀበ) ፤** መወገብ ፤ ድንገት ፡ መምጣት ፡ መውደቅ ። ያደጋ ፡ አመጣጥ ፤ ደደቀን ፡ እይ ፤ የዚህ ፡ ጎር ፡ ነው ። ወገብ ፡ መያዝ ፤ እስከ ፡ ወገብ ፡ መድረስ ፤ የውሃ ።

**አውገበ ፤** አደነገተ ፤ ሥራውን ፡ በድንገት ፡ ሠራ ፤ አደጋ ፡ ጣለ ። አውገብዎሙ ፡ ወወረዱ ፡ ላዕሌሆሙ ። ያወግቦ ፡ ወይነፅኖ ። ዕለት ፡ እኪት ፡ አውገበተኒ ። ወታወግቦሙ ፡ ዕለት ፡ እኪት ፡ (ትበጽሖሙ ፡ ግብተ) ። እለ ፡ ይፈቅዱ ፡ ያውግቡ ፡ (ኢያ፲፩ ፡ ፯ ። ሉቃ፱ ፡ ፴፱ ። ሱቱ ፡ ዕዝ፲ ፡ ፴፱ ። ሚክ፪ ፡ ፫ ። ቄር) ። ባለብሉዮች ፡ ግን ፤ አፍርሀ ፡ አደንገፀ ፡ ይሉታል ፤ ባለቅኔዎችም ፡ አኩረፈ ፡ ይሉታል ።

**» ግብት ፤** ድንገት ፤ ግጭት ፤ አደጋ ፤ አስቀድሞ ። ሳይታሰብና ፡ ሳይታወቅ ፡ እንዲያው ፡ ደርሶ ፡ የሚኾን ። ነገር ፤ እጅግ ፡ ታናሽ ፡ ጊዜ ፡ እንደ ፡ ደቂቃና ፡ እንደ ፡ ሴኮንድ ፡ እንደ ፡ ቅጽበት ፡ ያለ ። እመሰ ፡ ግብት ፡ ውእቱ ። ኀጢአት ፡ ዘግብት ፡ (ዘኍ፴፭ ፡ ፳፪ ። ፈ ፡ መ ፡ ፪ ፡ ፲፩) ። ባዕድ ፡ ነገድ ፡ በማለት ፡ ፈንታ ፡ ዐርከ ፡ ግብት ፡ አምላከ ፡ ግብት ፡ ይላል ፤ ድንገት ፡ የተገኘ ፡ ማለት ፡ ነው ፤ (ሚሬ፱ ፡ ፲ ። መዝ ፡ ፹) ።

**» ግብተ ፤** ድንገት ፡ በድንገት ፤ ወዲያው ፡ ቶሎ ፡ በቅርብ ፤ ሳይቈይ ፡ ሳይዘገይ ። ግብተ ፡ መጽአ ። ግብተ ፡ በረቀ ። ግብተ ፡ ሀለዉ ። ሐደሰ ፡ ግብተ ፡ (ሉቃ፪ ፡ ፲፫ ። ግብ፱ ፡ ፫ ። ዮዲ፱ ፡ ፫ ። ዕብ፲ ፡ ፳) ።

**» ግብታዊ ፤** ድንገተኛ ፤ የድንገት ፤ በድንገት ፡ የኾነ ፡ ያልታሰበ ። ሞተት ፡ በሞት ፡ ግብታዊ ፡ (አዋል) ።

**ወገብ ፤ (ዐማርኛ) ፤** በቁሙ ፤ ሐቋ ፡ ገቦ ፡ ጕንድ ። (ተረት) ፤ በሰማይ ፡ ቢዞር ፡ ዘመዱ ፡ አንበጣ ፤ በምድር ፡ ወገቡን ፡ ይይዛል ፡ ፌንጣ ።

**ወጊግ ፤ ጎት ፤ (ወገ ፤ ወገገ ፡ ይወግግ ፡ ይገግ ፡ ይውግግ ፤** መውገግ ፤ ወገግ ፡ ማለት ፡ የንጋት ።

**ወገግ ፤** ስመ ፡ ሀገር ፤ ዐሰቦት ። ሳሙኤል ፡ ዘወገግ ፤ ደብረ ፡ ወገግ ፡ (ገድ ፡ ተክ) ።

**ውጋጋን ፤ (ዐማርኛ) ፤** በቁሙ ፤ ወገግታ ፡ የፀሐይ ፡ የእሳት ፡ ጸዳል ፤ ፈገገን ፤ ጎሕንና ፡ ንግሀን ፡ እይ ።

**ወጊድ ፤ ዶት ፤ (ወገደ ፡ ይወግድ ፡ ይገድ) ፤** መወገድ ፡ መራቅ ፤ መፍሰስ ፡ መጕረፍ ፤ ላይ ፡ ላዩን ፡ ማለፍ ።

**አውገደ ፤** አሶገደ ፤ ወግድ ፡ አለ ፤ አራቀ ። ወግዳ ፡ ውጋዴ ፡ ማለት ፡ ከዚህ ፡ የወጣ ፡ ስም ፡ ይመስላል ።

**ሞገድ ፤ (ዳት ፤ መዋግድ ፤ ዳት ። ዐረ ፡ መውጅ) ፤** በቁሙ ፤ ማዕበል ፡ የባሕር ፡ ጐርፍ ፡ የውሃ ፡ ተራራ ፡ ፈረሰኛ ፤ እንደ ፡ ገመገም ፡ እየኾነ ፡ ከማኸል ፡ ወደ ፡ ዳር ፤ ከዳር ፡ ወደ ፡ ማኸል ፡ የሚኼድ ፡ የሚነጕድ ፤ ነፋሳት ፡ የሚከቡትና ፡ የሚነዱት ፡ የሚያወጡትና ፡ የሚያወርዱት ። የእሳት ፡ ላንቃ ፡ ነበልባል ። ሞገደ ፡ ባሕር ፡ እንተ ፡ ይዘብጣ ፡ ነፋስ ፡ ወያነውኃ ። ወይትሀወክ ፡ እሞገዳት ። እምአፉሁ ፡ መዋግደ ፡ እሳት ፡ ወፅአ ። መዋግዳት ፡ (ያዕ፩ ፡ ፮ ። ማቴ፲፬ ፡ ፳፬ ። ሱቱ ፡ ዕዝ፲፫ ፡ ፲፩ ። ቀሌ) ። በሞገድ ፡ ፈንታ ፡ ሞገት ፡ ይላል ፤ ሙግት ፡ ማለት ፡ ከዚህ ፡ ወጥቷል ። ዐረቡ ፡ በመውጅ ፡ ፈንታ ፡ መውጀት ፡ ይላልና ፤ ይህም ፡ እንደዚያ ፡ ነው ፡ (አስቴ፫ ፡ ፪ ። ሱቱ ፡ ዕዝ፪ ፡ ፶) ።

—፤ ሞገድ ፡ ልክ ፡ ያለው ፡ የበጋ ፡ ሁከት ፤ ማዕበል ፡ ከልክ ፡ ያለፈ ፡ የክረምት ፤ ጐርፉ ፡ ወደብ ፡ የሚያፈርስ ፡ ወደ ፡ የብስ ፡ የሚፈስ ፡ (መዝ ፡ ፵፩) ።

**ሞገዳዊ ፤** ሞገደኛ ፡ ሞገዳም ፡ ባለሞገድ ። ሞጋች ፡ ተሟጋች ፤ ሸፋጭ ።

**ሞገደ፡(ይሞግድ)፤** በቁሙ፤ አወከ፡ ደረጠ፡ ብጠበጠ። ማገደ፡ ዠገደ፤ የዕንጨት።

**አሞገደ፤** አስሞገደ፤ ማዕበል፡ ሞገድ፡ አስነሣ። እለ፡ ያሞግዱ፡ ወየሀውኩ፡(አፈ፡ ተ፴፬)።

**ተሞገደ፤** ታወከ፤ ተማገደ።

**ተሻገደ፤(ይትሻገድ፤ አው፡ ተምዋ ገደ፤ ተመዋገደ)፤** ወቅሐን፡ ተመልከት።

**ሙጋድ፤(ዕብ፡ ሞቄድ፤ ሞቅዳ)፤** ማገደ፤ የመሥዋዕት፡ ዕንጨት፡ ጥሩ፡ ፍልጥ፤ መልካም፡ ሽታ፡ ያለው።

**ወጊዝ፤ዘት፤(ወገዘ፡ ይወግዝ፡ ይገዝ)፤** መውገዝ፡ መገዘት፡ መለየት፤ መካድ፡ መርገም። መጽሐፍ፡ ግን፡ በወገዘ፡ ፈንታ፡ አውገዘ፡ ይላል። ወኪያሁ፡ ያወግዝዎ፡ እምነ፡ ማኅበሩ። አውገዝዎሙ፡ እስከ፡ ዛቲ፡ ዕለት። ብእሲ፡ ዘአውገዘ፡ ሔጺስቆጶስ፤ ለየ፡(ዕዝ፲፡ ፰)። እለ፡ ታወግዙ፡ ግዘታተ፡ ከመ፡ ኢይፍትሑ። ዘይፈቅድ፡ ይጠመቅ፡ ይምሀርዎ፡ ያውግዝ፡ ሰይጣነ፡ ወይእመን፡ በክርስቶስ፤ ኣወግዘከ፡ ሰይጣን፡ ወኵሎ፡ ምግባራቲከ። አውገዘ፡ ለከይሲ፤ ካደ፡ ረገመ፡(ሔኖ፲፩፡ ፬። ዲድ፡ ፴፬፡ ስንክ፡ የካ፪)።

**ወገዝ፤(ብ፡ አውጋዝ)፤** በቁሙ፤ ያደገ፡ ጥጃ፡ ታናሽ፡ ወይፈን፡ ጊደር፤ በመብል፡ ጊዜ፡ ከበሬ፡ የሚለይ፡ ማለት፡ ነው፡(ዐማርኛ)።

**አውገዘ፤** አሶገዘ፡ አስገዘተ፤ አስለየ። ልማዱ፡ ግን፡ አወገዘ፡ ነው።

**ተወግዘ፤** ተወገዘ፡ ተገዘተ፤ በግዝት፡ ተለየ። ካህን፡ ዘተወግዘ፡(አብጥ፡ ፲)።

**ውጉዝ፤(ዛን፡ ዛት፡ ግዝት)፤** በቁሙ፡ የተወገዘ፡ የተለየ፤ ርጉም። ውጉዘ፡ ለይኩን። ኢትኩን፡ ውግዘተ፡(ገላ፩፡ ፰። ዘካ፲፬፡ ፲፩)።

—፤ ሕርም፡ የተባለ፡ የተከለከለ፤ ሕግ፡ የንቀፈው፡ ያጸየፈው፡ ሥራ፤ ማናቸውም፡ ኹሉ። ቀቲልሰ፡ እምኍልቁ፡ ዐበይት፡ ኀጣውእ፡ ክሉኣት፡ ወውጉዛት፡ በልብ፡ ወበሕግ፡(ፍ፡ ነ፡ ፵፯)።

**ውግዘት፤** መውገዝ፤ መወገዝ፡ አወጋገዝ፤ በቁሙ፡ ግዝት፤ ውጉዝነት። ዘከልእዎ፡ ቍርባነ፡ በእንተ፡ ውግዘት። ኢይፍትሑ፡ እምኔሁ፡ ግዘቶ፡(አብጥ፡ ፱። ቀኖ፡ ኒቅ፺)።

»**ግዝት፤(ታት)፤** ዝኒ፡ ከማሁ፤ መገዘት፡(ጥገ) መገዘት፡ አገዛዘት፤ በቁሙ፡ ግዝት፡ ርግማን። ግዝት፡ ዘነበበ፡ ባቲ፡ ዮሐንስ፡ ዘቡርልስ። አንቀጸ፡ ግዝት። ንባበ፡ ግዝት፡(ሃይ፡ አበ። ስንክ፡ ታኅ፺)።

**ወግዝ፤(ዛት)፤** ሕርም፡ ልዩ፡ ክልክል፤ የግዜር፡ ገንዘብ። ዘዐለወ፡ በወግዝ፡(፩ዜና፡ ፪፡ ፯)።

**ተዋገዘ፤** በቁሙ፤ ተገዛዘተ፡ ተማማለ፤ ተለያየ፤ ተከራከረ፡(ሔኖ፮፡ ፬)። ከመ፡ እትዋገዝ፡ ለልብየ፡ ወእፌስዮ፡ መልአከ፡ በማለት፡ ፈንታ፡ ግዘተ፡ እትዋገዝ፡ ይላል፡(ሮንገ፡ ፲፩፡ ፴፬)።

**ወገል፤(ዐረ፡ ሸንገል)፤** በቁሙ፤ ከርፈስ፡ ዕርፍን፡ ከሞፈር፡ ከድግር፡ የሚያያይዝ። ስዕሉን፡ እይ።



ወገል፡

**ወገን፤(ዐማርኛ)፤** በቁሙ፤ መንጋ፡ ዘመድ። ወገን፡ ጠባቂ፡ ባለወገን፡ እንዲሉ።

**ወግዐ፤—በቁሙ፡ ወጋ፤—ወጊእ፡ ወግአ።**

**ወግዐ፤(ገዐተ)፤** ጋተ፡ አስጐነጨ፤ አስጐረጐጨ፤ በጥርኝ፡(አወጋ፡ ተረከ)። ወትፈቅዱ፡ ሐሊበ፡ ይውግዑክሙ። ሐሊበ፡ ወጋዕኩክሙ፡(ዕብ፭፡ ፲፪። ፩ቆሮ፡ ፫፡ ፪)።

**ተወግዐ፤** ተጋተ፤ ገጨ፡ ጐርጐጨ፡ አደረገ። መጠጡንና፡ ወጉንም፡ ያሳያል። እለ፡ ክልእዎሙ፡ ኢይትወግዑ፡ ሐሊበ። እስመ፡ ኵሉ፡ ዘይትወጋዕ፡ ሐሊበ፡ ሕፃን፡ ውእቱ፡(ኢሳ፳፰፡ ፱። ዕብ፭፡ ፲፫)።

**ወግዕ፤** በቁሙ፤ ወግ፡ ታሪክ፡ አንቲካ፡ ወሬ፡ ከሽማግሎች፡ አፍ፡ የሚገኝ። ዜና፡ ወግዕ፡ ዘመንግሥት፡ ሺዋ፡ ዘሰማዕናሁ፡ እምእለ፡ ይዛውዑ፡ ዜና፡ ወግዕ፡(ታሪ፡ ነገ)። ልማድ፡ ደንብ፡ አበል፡ ለሹም፡ ወይም፡ ለሌላ፡ የሚገባ፡(ዐማርኛ)።

**ወግዓዊ፤** ወገኛ፡ ወጋም፤ ባለወግ።

**ወጊር፤ሮት፤(ወገረ፡ ይዌግር፡ ይውግር፤ አው፡ ይወግር፡ ይገር)፤** መወርወር፡ ማጓን፡ መጣል። ውርወራ፡ የወል፤ ጐናሽ፡ ወደ፡ ላይ፤ ጥሎሽ፡ ወደ፡ ታች፡ ወይም፡ ፊት፡ ለፊት። ዘገር፡ ማለት፡ ከዚህ፡ ወጥቷል፤ ዘይትወገር፡ ያሰኛል። ዘይወግር፡ እብነ፡ ላዕሌሁ፡ ትወርድ፡ ዲበ፡ ርእሱ። ንሣእ፡ እብነ፡ ወገር፡ ላዕለ፤ አጓን፡(ሢራ፳፯፡ ፳፭። ሄርማ)። ገርዎ፡ ውስተ፡ ተከዚ። ወገሩ፡ አብትሮሙ። ዘያስተሐይጻ፡ ለድንግል፡ ወይወግር፡ ዐይኖ፡ ከመ፡ ያርኵሳ፡ ጣለ፡(ዘፀ፩፡ ፳፪። ጊ፡ ፲፪)።

—፤ መውገር፡ በደንጊያ፡ መምታት፤ መግመስ፡ መፈንከት፤ መስበር፡ መቀጥቀጥ፤ ደንጊያን፡ መቈለል፡ መከመር። ወገረቶ፡ በስባረ፡ ማሕረጽ። ወገሮሙ፡ እግዚ፡ በእብነ፡ በረድ። ለይገሩ፡ በእብን። ወነሥኡ፡ እብነ፡ ከመ፡ ይውግርዎ፡(መሳ፱፡ ፶፫። ኢያ፲፡ ፲፩። ዮሐ፰፡ ፶፱። ፲፡ ፴፩)።

—፤ ማጠን፡ ማጤስ፡ ማቃጠል፤ የዕጣንን፡ ቍቀር፡ ከፍሕም፡ ላይ፡ መጣል። መኰንን፡ ኀሠሠ፡ ከመ፡ ይክሕዶ፡ ለክርስቶስ፡ ወይውግር፡ ዕጣነ፡ ለጣዖታት። ወእምዝ፡ ይውግር፡ ዕጣነ፡(ስንክ፡ መጋ፺። ቅዳ)።

የወገረ ፡ ምስጢር ፡ በትግርኛ ፤ አለሌው ፡ ባዝራይቱን ፡ መታት ፡ እንደ ፡ ማለት ፡ ነው ።

**ወጋሪ** ፤ (ሪት ፡ ርያን ፡ ያት ፤ ገርት) ፤ የሚወረውር ፡ የሚጥል ፡ ጣይ ። ወገርተ ፡ እብን ፡ (ገድ ፡ ኪሮ) ።

—፤ በቁሙ ፤ ዓሣ ፡ አጥማጅ ፤ መረቡን ፡ ወደ ፡ ባሕር ፡ ዓሣውን ፡ ወደ ፡ የብስ ፡ የሚጥል ። ዓሣ ፡ ወጋሪ ፡ እንዲሉ ።

**ዋግራ** ፤ የሬት ፡ ሽቱ ፤ ወይም ፡ ወገርት ። ማዐሮን ፡ ተመልከት ።

**ወግር** ፤ (ብ ፡ አውግር ፡ ራት ። ዕብ ፡ ይጋር ፤ ጋል ። ሱር ፡ ያግራ) ፤ የደንጊያ ፡ ክምር ፡ ቍልል ፤ እንደ ፡ ኰረብታ ፡ ያለ ። አሰዱ ፡ እብነ ፡ ወገብሩ ፡ ወግረ ። ወሰመያ ፡ ላባ ፡ ወግረ ፡ ስምዕ ፡ ወያዕቆብኒ ፡ ሰመያ ፡ ከማሁ ። ዛቲ ፡ ወግር ፡ ወዛቲ ፡ ሐውልት ፡ (ዘፍ፴፩ ፡ ፵፯ ፡ ፵፰ ፡ ፶፪) ።

—፤ በቁሙ ፤ ኰረብታ ፡ ቍሊልታ ፤ ተሬ ፡ ጕባ ፡ ጕባታ ፤ አዳጋ ፡ ከፍተኛ ፡ ቦታ ፤ ደፈር ፡ ሸንተረር ፡ ከተራራ ፡ የሚያንስ ። እቀውም ፡ ዲበ ፡ ርእሰ ፡ ወግር ፤ ዐርጉ ፡ ውስተ ፡ ርእሳ ፡ ለወግር ። ወኮነ ፡ ወግረ ፡ ዐቢየ ፡ ውእቱ ፡ ጕድፍ ። ወግረ ፡ ኃጥኣን ። አውግር ፡ ልዑላት ። ወባቲ ፡ አውግራትኒ ፡ ወአድባራት ፡ (ዘፀ፲፯ ፡ ፱ ፡ ፲ ። ስንክ ፡ መጋ፲ ። ኢሳ፳፰ ፡ ፴፩ ። ፴ ፡ ፳፩ ። አፈ ፡ ተ፴፱) ።

**አውገረ** ፤ አሶገረ ፡ አስመታ ፡ አስጣለ ።

**ተወግረ** ፤ በቁሙ ፤ በደንጊያ ፡ ተመታ ፤ ተደበደበ ፡ (ዘፀ፲፱ ፡ ፲፫ ። ፳፩ ፡ ፴፪) ። ለተወግሮቱ ፡ በእብን ። ወበሕግነሰ ፡ ሠርዐ ፡ ሙሴ ፡ ከመ ፡ ትትወገር ፡ በእብን ፡ (ኩፋ ፡ ፴፫ ። ዮሐ፰ ፡ ፭) ።

**ተዋገረ** ፤ ተማታ ፡ ተወራወረ ፤ ደንጊያ ፡ ተጣጣለ ፡ (ግብ ፡ ፲፱ ፡ ፭) ።

**ውጉር** ፤ (ራን ፡ ራት ፡ ግርት) ፤ የተወገረ ፡ የተደበደበ ፤ ደንጊያ ፡ የተጕራበት ፡ የተከመረበት ። ረከቦሙ ፡ ለጣዖታት ፡ ውጉራነ ፡ ወስቡራነ ፡ (ስንክ ፡ መጋ፲፯) ።

**ውግረት** ፤ መውገር ፡ መወገር ፡ አወጋገር ፤ ውግራት ፡ ውርወራ ፡ ደንጊያ ፡ አጣጣል ፡ አወራወር ፤ የደንጊያ ፡ ስልፍ ፡ ጦርነት ፤ እንዳንደርቢና ፡ እንደ ፡ በረድ ፡ ያለ ። ተኰነነ ፡ ምዕረ ፡ በውግረት ፡ ወምዕረ ፡ በንድፈተ ፡ አሕጻ ። ኮነ ፡ ጸብእ ፡ ማእከሌሆሙ ፡ በንዋየ ፡ ሐቅል ፡ ወበውግረተ ፡ አእባን ፡ ወበሞፀፍ ። ቀተሰ ፡ በውግረተ ፡ እብን ፡ ወበኀጺን ፡ (ስንክ ፡ ሐም፭ ። ዮሴፍ ። ቀሌ ። ፍ ፡ ነ ፡ ፶ ፡ ፫) ።

—፤ ማጠን ፡ መታጠን ፤ አስተጣጠን ። ኢተደመረ ፡ በውግረተ ፡ ዕጣን ፡ ለአማልክት ፡ (ስንክ ፡ ኅዳ፳፭) ።

**ሙጋር** ፤ መውገሪያ ፤ መወገሪያ ፤ መጣያ ፡ መወርወሪያ ፡ ቦታ ። ተአተተ ፡ ሕቀ ፡ እምኔሆሙ ፡ መጠነ ፡ ሙጋረ ፡ እብን ፡ (ሉቃ፳፪ ፡ ፵፩ ። ስንክ ፡ ነሐ፲፱) ።

**ሞገር** ፤ ጥና ፤ የዕጣን ፡ መውገሪያ ። ዕጣን ፡ ሞገር ፡ እንዲሉ ፤ ቅኔው ፡ በዕጣን ፡ ፈንታ ፡ ስለ ፡ ገባ ።

**ሞገርት** ፤ ውርወራ ፡ ጥሎሽ ፤ እንዝጥዝጣሽ ። ዘበሞገርተ ፡ እብን ፡ ወዕፀወ ፡ ገዳም ፡ (፩ነገ ፡ ፲፬ ፡ ፲፬) ።

**ወገሬ** ፤ የማሽላ ፡ ስም ፤ የይፋት ፡ ማሽላ ፡ ራሱ ፡ ምንቸት ፡ የሚያካክል ። ፍችው ፡ ደጎኔ ፡ መልካሜ ፡ ማለት ፡ ነው ። (ወገሬት) ፡ ወገር ፡ ዕደር ፡ እንዲል ፤ ደኅና ፡ ዕደር ፡ ሲል ፡ (ጕራጌና ፡ እስላም) ። ፪ኛም ፡ የወገራ ፡ ሰው ፡ ማለትን ፡ ያስማል ፤ ወገራ ፡ በጕንደርና ፡ በስሜን ፡ መካከል ፡ ያለ ፡ አገር ፡ ነው ። (ግጥም) ፤ ወገራ ፡ እግዚእ ፡ ዘኢፈጠራ ፤ ከቤት ፡ ቢገቡ ፡ ጢሱ ፤ ከደጅ ፡ ቢወጡ ፡ ነፋሱ ፤ እኽሉን ፡ ቢበሉት ፡ ፈሱ ።

**ወጊስ** ፤ ሰት ፤ (ወገሰ ፡ ይወግስ ፡ ይገስ ። ትግ ፡ ሐገሸ ፤ ፈሥሐ) ፤ መወግሸት ፤ መቈጣት ። ወጌሻ ፡ ሐኪም ፡ መኾን ፡ መፈወስ ፡ ማዳን ፤ ማፀን ፡ መጠገን ፤ ከዚህ ፡ የተነሣ ፡ መወደድ ፡ መክበር ። መዋብ ፡ ማማር ፤ ደስ ፡ ማሰኘት ፤ የመልክ ፡ የግብር ። መጽሐፍ ፡ ግን ፡ በወገሰ ፡ ፈንታ ፡ ሞገሰ ፡ ይላል ፤ ወገደንና ፡ ወቅሐን ፡ እይ ፤ የዚህ ፡ አምሳል ፡ ናቸው ። ለብፁዕ ፡ ቂርቆስ ፡ አልቦ ፡ ዘይሞግሶ ፤ በክብር ፡ የሚበልጠው ፡ (መዋሥ ። ድጓ) ።

**ሞገስ** ፤ በቁሙ ፤ ሞጋሳ ፡ ውድ ፡ ውዴታ ፤ ባለሟልነት ፤ ጸጋ ፡ ክብር ፡ ውዳሴ ፡ ብፅዓን ፤ ግርማ ፡ ውበት ፡ ደም ፡ ግባት ፡ ጣዕም ፡ ሥን ። ቦሙ ፡ ሞገስ ፡ በኀበ ፡ ኵሉ ፡ ሕዝብ ። እንተ ፡ ተፀቢ ፡ ሞገስ ፡ ይሁበነ ። ረከብኪ ፡ ሞገሰ ። ገጽከ ፡ ምሉእ ፡ ሞገሰ ። ሞገሳ ፡ ለብእሲት ፡ ያስተፌሥሖ ፡ ለምታ ፡ (ግብ፪ ፡ ፵፯ ። ያዕ፬ ፡ ፮ ። ሉቃ፩ ፡ ፴ ። አስቴ፭ ፡ ፪ ። ሢራ፳፮ ፡ ፲፫) ።

**አሞገሰ** ፤ ወደደ ፡ አከበረ ፤ ባለሟል ፡ አደረገ ፤ አወደሰ ፡ አመሰገነ ፤ በቅኔ ፡ በግጥም ። ኣሜንያ ፡ ወኣሞግሳ ፡ (ዘካ፱ ፡ ፯) ።

**መሞግስ** ፤ (ስት ፡ ሳን ፡ ሳት) ፤ የሚወድ ፡ የሚያከብር ፤ ወዳ ፡ የሚያሶድድ ፤ ባለሟል ፡ የሚያደርግ ፤ የሚያስደርግ ። መሞግስት ፡ (አርጋ) ።

**ተሞገሰ** ፤ ከበረ ፡ ተመሰገነ ፤ ብፁዕ ፡ ተባለ ፤ ባለሟል ፡ ኾነ ፤ ልጅነት ፡ አገኘ ። አባ ፡ ዮሐኒ ፡ ፈድፋደ ፡ ኅየሰ ፡ ተሞገሰ ። ዮሐንስ ፡ ተፈሥሐ ፡ ወተሞገሰ ። እመ ፡ በመንፈሱ ፡ ለኢየሱስ ፡ ንትሞገስ ፡ ወንጼውዖ ፡ ለእግዚ ፡ አቡነ ፡ (መዋሥ ። ቊር ፡ ስምዓት) ።

**ሞገት** ፤—**ሞገድ** ፤—**ወጊድ** ፡ **ወገደ** ።

**ወድአ** ፤ **አት** ፤ (ወድአ ፡ ይዌድእ ፡ ይወድእ ። ዐረ ፡ ወደዐ ፤ አደረገ ፤ ላከ) ፤ መጨረስ ፤ መፍጀት ፤ መፈጸም ፡ መከተት ፤ የግብር ፡ የነገር ። ትዌድእዎ ፡ ወኢታተርፉ ፡ እምኔሁ ። እሳት ፡ ዘይዌድእ ። ሕያው ፡ ነፍስከ ፡ ከመ ፡ ኢትወድእ ፡ አመትከ ፡ ዘሀለወ ፡ ምስሌሃ ። ነጸረ ፡ ንጉሥ ፡ በዘወድኡ ፡ ማእደ ፡ (ዘፀ፲፪ ፡ ፱ ፡ ፲ ። ዘዳ፱ ፡ ፫ ። ዮዲ፲፪ ፡ ፬ ። ዱን፲፫ ፡ ፲፰) ።

**ወዳኢ** ፤ **መወድእ** ፤ የሚጨርስ ፡ ጨራሽ ፤ ፈጻሚ ፡ ከታች ።

**ወድአ** ፤ **(ንኡስ ፡ አገባብ)** ፤ ቀድሞ ፡ አስቀድሞ ፤ አካቶ ፡ ፈጽሞ ፤ ጭራሽ ፡ በጭራሽ ። እስ ፡ ወድኡ ፡ ሞቱ ። ወድአ ፡ ተሠይመ ። ወዳእነ ፡ ግእዝናሆሙ ። ወዳእነ ፡ ሞትነ ። ወዳእነ ፡ ቀተርነ ፡ ኖኅተ ፡ (መክ፩ ፡ ፪ ። ማቴ፫ ፡ ፲ ። ሮሜ ፡ ፫ ፡ ፱ ። ፮ ፡ ፪ ። ሉቃ ፲፭ ፡ ፯) ።

**ተወድአ** ፤ ተጨረሰ ፤ ተፈጸመ ፤ ተፈጀ ፡ ዐለቀ ። ይትዌዳእ ፡ ኵሉ ፡ እኩይ ። መዛግብተ ፡ እክል ፡ ወሥርናይ ፡ ይትዌዳእ ፡ በፃፄ ፡ ወበነቀዝ ። ተወድአ ፡ ወርቅነ ። ፍሥሓ ፡ ዘኢይትዌዳእ ፡ (ሔኖ ። መቃ ። ዘፍ ፵፯ ፡ ፲፰ ። ኪዳ) ።

**ውዳኤ** ፤ መጨረስ ፤ (ጥጨ) መጨረስ ፡ አጨራረስ ፡ ጭረሳ ። ጭራሽ ፡ ከታች ፤ ፍጻሜ ፡ (ፊልክ) ።

**ወደብ** ፤ **(ዐማርኛ)** ፤ በቁሙ ፤ የባሕር ፡ ጠረፍ ፡ በር ፡ መግቢያ ፤ የመርከብ ፡ መቋሚያ ።

**ወዲድ** ፤ **ዶት** ፤ **(ወደ ፤ ወደደ ፡ ይወድድ ፡ ይደድ)** ፤ መውደድ ፡ ማፍቀር ። ማግባት ፡ መጨመር ፤ አንዱን ፡ ባንዱ ፡ ውስጥ ፡ ወይም ፡ በመካከል ፡ እንደ ፡ ሳጋ ፡ እንደ ፡ ሽብልቅ ፡ እንደ ፡ ስፌጽና ፡ እንደ ፡ ዚቅ ። ወደየን ፡ ተመልከት ፤ የዚህ ፡ መንቲያ ፡ ነው ።

**አውደደ** ፤ አዎደደ ። አዋደደ ፡ አስማማ ፤ ሰካ ፡ አሳካ ፤ ቸነከረ ፡ አንድ ፡ አደረገ ፤ የግብር ፡ የነገር ። አግበረ ፡ አርባዕተ ፡ ምእተ ፡ ጸናጽለ ፡ ወአውደዶን ፡ ዲበ ፡ መሣግር ። አውደድዎ ፡ ውስተ ፡ ወርቅ ። አውድድ ፡ ውስተ ፡ ሥጋየ ፡ ፈሪሆተከ ፡ (፪ዜና ፡ ፬ ፡ ፲፫ ። ዘፀ፴፯ ፡ ፲፫ ። መዝ፻፲፰ ፡ ፻፳) ።

—፤ ሽፈን ፡ ለበጠ ፤ በልባጥ ፡ አስጌጠ ፤ ምስጢሩ ፡ ያው ፡ ማዋደድ ፡ ነው ። ወለቤት ፡ ዐቢይ ፡ አውደዶ ፡ ወእጽንዖ ፡ በዕፀወ ፡ ዘግባት ፡ (፪ዜና ፡ ፫ ፡ ፭) ። በአውደደ ፡ ፈንታ ፡ አስተዋደደ ፡ ይላል ፤ ፍችው ፡ አንድ ፡ ነው ፤ ከድራጊንት ፡ በቀር ፡ አደራራጊንት ፡ የለውም ፡ (ዘኍ፬ ፡ ፮ ፡ ፰ ፡ ፲ ፡ ፲፩ ። ምሳ፰ ፡ ፴) ። ዘእንበለ ፡ ያስተዋድድ ፡ እግዚ ፡ ምቋመ ፡ አድባር ፡ ወአውግር ። አሠነየ ፡ ለነ ፡ ወአስተፍሥሐ ፡ መንግሥተነ ፡ ወአስተዋደደ ፡ አህጉሪነ ፡ ወሥልጣንነ ፡ ላዕለ ፡ ብዙኃን ፡ አሕዛብ ። አስተዋድዶ ፡ መዝሙረ ፡ ማሕሌት ። አስተዋደደ ፡ መዝሙራተ ። ወአዳብዕየ ፡ ያስተዋድዳ ፡ መዝሙረ ፡ (መቃ ፡ ገ፳፫ ። ዮሴፍ ። ስንክ ፡ የካ፳ ። ቀሌ ። መዝ ፡ ፻፵፩) ።

**ተወደ** ፤ ተወደደ ፡ ተፈቀረ ። ተሰካ ፤ ተጨመረ ፡ (ዘፀ፳፰ ፡ ፲፭) ።

**ተዋደደ** ፤ በቁሙ ፤ ተገባ ፡ ተመቸ ፡ ተስማማ ፤ ተሳካ ፡ ተዛመደ ፤ ጸና ፡ ተደላደለ ። (ምሳ፲፯ ፡ ፯ ። ፲፱ ፡ ፲፱) ። አላ ፡ ተዋደደ ፡ ወተደለወ ፡ ዝንቱ ፡ ስም ፡ ለዘበሥጋ ፡ ተወልደ ። ዘቦቱ ፡ የኀድር ፡ ኵሉ ፡ ሥጋ ፡ ወይትዋደድ ፡ በአሥራው ፡ ወመሌሊት ። ሠነየ ፡ ንብረቶሙ ፡ ወተዋደደ ፤ ሰበ ፡ ተዋደደ ፡ ትእዛዙ ። ተዋደደ ፡ ነገርነ ፡ ወረትዐ ፡ መንግሥትነ ፡ (ቄር ፡ ጸላ ። ቆላ፪ ፡ ፲፱ ። ዮሴፍ) ።

**ተዋድዶ** ፤ መዋደድ ፡ መስማማት ፤ በፍቅር ፡ በችንካር ፡ አንድ ፡ መኾን ።

**ውዱድ** ፤ **(ዳን ፡ ዳት ፡ ድድ)** ፤ የተወደደ ፡ ውድ ፤ የተዋደደ ፡ የተስማማ ፤ የማይወልቅ ፡ የማይነቃነቅ ። ውስተ ፡ ውጽቦ ፡ ወርቅ ፡ ዕንቈ ፡ ሰርድዮን ፡ ውዱድ ። አድባር ፡ እለ ፡ ውዱዳን ። እለ ፡ ውዱዳት ፡ እማንቱ ፡ (ምሳ፳፭ ፡ ፲፪ ። ዘፍ፵፱ ፡ ፳፮ ። ደራሲ) ።

**ውዱድ** ፤ የሰማይ ፡ ስምና ፡ ቅጽል ፤ መጨረሻ ፡ ሰማይ ፡ (ሕዝ፩ ፡ ፳፫ ፡ ፳፬) ። በቀዳሚ ፡ ገብረ ፡ እግዚ ፡ ሰማየ ፡ ወምድረ ፤ ወመልዕልተ ፡ ሰማይ ፡ ውዱድ ፡ አስተዳለወ ፡ መንበረ ፡ (ደራሲ) ።

**ሙዳድ** ፤ **ሞዳድ** ፤ **(ብ ፡ መዋድድ)** ፤ ማዋደጃ ፡ ማስማሚያ ፤ ዛቢያ ፡ ችንካር ፡ ቍልፍ ፤ የመሰለው ፡ ኹሉ ። ወመዋድዲሆን ፡ ዘብሩር ፡ (ዘፀ፴፯ ፡ ፲፯ ። ፴፰ ፡ ፲፯) ። የሰው ፡ ስም ፤ ሙሴ ፡ ከመረጣቸው ፡ ከሰባ ፡ ኹለቱ ፡ አንዱ ፡ (ዘኍ፲፩ ፡ ፳፮) ።

»**ድድ** ፤ **(ዳት)** ፤ በቁሙ ፤ ማውድ ፡ መሠረት ፤ ምዕማድ ፡ ስክተት ። ድደ ፡ መሠረት ። ዐምዳ ፡ ወድዳ ፡ ለጽድቅ ። ይጸውር ፡ ድደ ፡ ወይነብር ፡ ጠፈረ ፡ (ቆላ፩ ፡ ፳፫ ። ፩ጢሞ ፡ ፫ ፡ ፲፭ ። ቅዳ) ።

—፤ ድምድማት ፤ መደምደሚያ ፡ የሕንጻ ፡ ራስ ፤ የባጥ ፡ የመዋቅር ፡ መሠረት ፡ ወይም ፡ መጋጠሚያ ። ድደ ፡ ንጽሕ ፡ ወመሠረተ ፡ ቅድስና ። መስቀል ፡ ዐምዳ ፡ ወድዳ ፡ ለቤተ ፡ ክርስቲያን ። አነዳሁ ፡ ዘሐቁ ፡ ወሌለዩ ፡ እምነ ፡ ድዱ ፡ (አርጋ ፡ ፫ ። ድጓ ። ስንክ ፡ ግን፳) ።

**ወድይ** ፤ **ዮት** ፤ **(ወደየ ፡ ይወዲ ፡ ይደይ ። ወደደ)** ፤ መጨመር ፡ መደል ፡ ማግባት ፤ ማኖር ፡ ማድረግ ፤ መወርወር ፡ መጣል ። ወደዩ ፡ ሐሞተ ፡ ውስተ ፡ መብልዕየ ። ይወዲ ፡ እዴሁ ፡ ውስተ ፡ ግበ ፡ አርዌ ፡ ምድር ። ደይ ፡ ቃሎ ፡ ውስተ ፡ ልብከ ። እወዲ ፡ እዴየ ፡ ዲበ ፡ አፉየ ። ኢትደዩ ፡ ባሕርየክሙ ፡ ቅድመ ፡ አሕርው ። ወደይዎ ፡ ውስተ ፡ ግበ ፡ አናብስት ። ወደየት ፡ አዕይንቲሃ ፡ ላዕለ ፡ ዮሴፍ ። ዘወደየ ፡ እሳተ ፡ ውስተ ፡ አህጉር ፡ (መዝ ፡ ፷፰ ። ኢሳ፲፩ ፡ ፰ ። ኢዮ፴፪ ፡ ፴፪ ። ፴፱ ፡ ፴፬ ። ማቴ፯ ፡ ፮ ። ዳን፲፫ ፡ ፴፩ ። ዘፍ፴፱ ፡ ፯ ። ፍ ፡ ነ ፡ ፶ ፡ ፯) ።

**ወዳዪ** ፤ **(ዪት ፡ ይያን ፡ ያት ፤ ደይት)** ፤ ጨማሪ ፤ ነገሬ ፡ ሠሪ ፤ ክፉ ፡ አድራጊ ። ወዳዪ ፡ እከይ ፡ ወጽልእ ፡ ማእከለ ፡ ሰብእ ፡ (ሲኖዶ) ።

**ሙዳይ** ፤ **(ያት)** ፤ በቁሙ ፤ ማኖሪያ ፡ መጨመሪያ ፤ መክተቻ ፡ ዕቃ ። ዕፍረት ፡ ዘተሰውጠ ፡ እሙዳይ ፡ ውስተ ፡ ሙዳይ ፡ (ቀሌ) ። ለንዋያት ፡ ኹሉ ፡ ይነገራል ፤ ዋዲያት ፡ ማለት ፡ ከዚህ ፡ ወጥቷል ።

**ሙዳየ ፡ በለስ** ፤ የበለስ ፡ መልቀሚያ ፡ ታናሽ ፡ እንቅብ ፡ ቅርጫት ፡ (ተረ ፡ ባሮ) ።

**ሙዳየ፡ ዘቢብ፤** አገልግል፡ ቅንብቻ፤ ቢት፤ ኪስ፡ ከረጢት፡ (፩ነገ፡ ፳፭፡ ፲፰)።

**ሙዳየ፡ ማይ፤** የውሃ፡ ዕቃ፤ እንስራ፡ ፊቀን፤ ብርሚል፡ ጋን፤ ቀርበታ፡ (ዮዲ፯፡ ፳)።

**ሙዳየ፡ ምጽዋት፤** የገንዘብ፡ ማጥን፤ ምእመናን፡ አምኃቸውን፡ የሚያገቡበት፤ አፈ፡ ጠባብ፡ ሆደ፡ ሰፊ፤ ገንዘብ፡ የሚያስገባ፡ እጅ፡ የማያስገባ፤ ገንዘቡ፡ ሲመላ፡ ተከፍቶ፡ እንደ፡ ንፍሮ፡ የሚዘረገፍ፡ (፪ዜና፡ ፳፬፡ ፲፩። ማር፲፪፡ ፵፩)።

**ሙዳየ፡ ዕጣን፤** በቁሙ፤ ታናሽ፡ ስፌት፡ ወይም፡ ቢት፡ የዕጣን፡ ማቅረቢያ፡ (ቅዳ)።



ሙዳየ፡ ዕጣን፡

**ሙዳየ፡ ዕፍረት፤** የሽቱ፡ ዕቃ፤ ስፌት፡ ናርጅ፤ ቢልቃጥ።

**ሙዳየ፡ ዔረግ፤** የበጋ፡ እንቅብ፤ የመከር፡ ቅርጫት፡ ፍሬ፡ የተመላ፡ (ዓሞ፰፡ ፩)።

**ሙዳየ፡ ቀለም፤** የቀለም፡ ቀንድ፤ ወይም፡ ቢልቃጥ፡ (ሕዝ፱፡ ፪)።



ሙዳየ፡ ቀለም፡

**ሙዳየ፡ ቀርጠሎን፤** የወይን፡ እሸት፡ ቅርጫት፤ ዘለላውን፡ የሚሸከሙበት፡ (ዘዳ፳፮፡ ፬)።

**ተወድየ፤** ተጨመረ፡ ገባ፤ ተጣለ፡ ተጣነ። ይነሥእ፡ እምዘይትወደይ፡ ውስቴቱ። ተወድየ፡ ውስተ፡ ቤተ፡ ሞቅሕ። ገሪፍ፡ እንተ፡ ተወድየት፡ ውስተ፡ ባሕር። ኢትወድየ፡ ላዕሌሃ፡ አርዑት፡ (ዮሐ፲፪፡ ፯። ዕር፡ ኢሳ፪፡ ፲፫። ማቴ፲፫፡ ፵፯። ዘኍ፲፱፡ ፪)።

**ውዱይ፤** (ያን፡ ያት፡ ዲት) የተጨመረ፡ ጭምር፤ ቅልቅል።

**ውዳይ፤** (ትግሬ) ግብር፤ ሥራ። ውዳይ፡ ሐዋርያት፡ (ግብ፡ ፩)።

**ውድየት፤** መጨመር፡ (ጥጨ) መጨመር፤ አጨማመር፡ ጭመራ፤ ጭምርነት። ከመ፡ ውድየተ፡ ወይን፡ ሐዲስ፡ በሐዲስ፡ ዝቅ፡ (ስንክ፡ ኅዳ፲፯)።

**ውዴት፤** ዝኒ፡ ከማሁ። ነገር፡ መሥራት፡ ማሳበቅ፤ ያንዱን፡ ነውር፡ ለሌላው፡ መንገር፤ በጆሮው፡ ማግባት፡ በልቡ፡ መስንቀር። ሰብቅ፡ ክስ፡ ሐሜት። ውዴት፡ እኪት። ውዴት፡ ዘሐሰት። ኢይስማዕ፡ ውዴተ፡ ሐሰት፡ ላዕለ፡ ካልእ። መጽሐፈ፡ ውዴት። በዓለ፡ ውዴት። (ዘፍ፴፯፡ ፪። ዘፀ፳፫፡ ፩። ዲድ፡ ፱። ነሐ፱፡ ፳። ፍ፡ ነ፡ ፭)።

**ተዋደየ፤** ነገር፡ ተሣራ፤ ተማማ፡ ተካሰሰ፤ ተጣላ።

**አስተዋደየ፤** አሳበቀ፤ ነገር፡ ሠራ፤ ከሰሰ፡ አካሰሰ፡ አወናጀለ፤ አሳጣ። ሐሰተ፡ አስተዋደዩኒ። ኢኀደጉ፡ አስተዋድዮቶሙ። ዮጊ፡ በጽልእ፡ አስተዋደይዎ። አስተዋደዩኒ፡ ኀበ፡ ንጉሥ። አስተዋዲ፡ ርእስየ፡ ኀበ፡ እግዚ፡ (ዳን፩፡ ፵፫። ፫፡ ፳፪። ሚራ፲፱፡ ፲፭። ጦቢ፩፡ ፲፱። መዝ፡ ፴፩)።

**መስተዋድይ፤** አሳባቂ፡ ነገረ፡ ሠሪ፤ ከሳሽ፡ አሳጭ፤ ጠላት፡ ባለጋራ፤ ወድቀ፡ መስተዋድይ፡ ዘአስተዋደዮሙ፡ ለአኀዊነ። ጻድቅ፡ መስተዋድየ፡ ርእሱ። አዘዝክዎሙ፡ ለመስተዋድያንሂ፡ ይምጽኡ፡ ኀቤከ፡ (ራእ፲፪፡ ፩። ምሳ፲፰፡ ፲፯። ግብ፳፫፡ ፫)።

**ወደፈ፤** (ወፀፈ) ጣለ፡ ወረወረ፡ አሽቀንጠረ፤ የማይረባን፡ ነገር።

**ወዲፈት፤** (ብ፡ ወዲፋት) ዕላቂ፡ ውዳቂ፡ ጨርቅ፡ ቍረንጮ፡ ቅርንጥስ። ባለብሎዮች፡ ግን፡ ያልተከለለ፡ ማቅ፡ ዳሙዣ፡ ይሉታል። ወይጠበልልዎ፡ በወዲፈት። ዘእንበለ፡ ወዲፈት፡ ወአነዳ፡ ላሕም፡ (ኤር፳፪፡ ፲፱። ገድ፡ ተክ)።

**ወዲቅ፤ ቆት፤** (ወድቀ፡ ይወድቅ፡ ይደቅ። ዐረ፡ ወደቀ) መውደቅ፡ (ጥጣ) መጣል፤ ድንገት፡ ከላይ፡ ወደ፡ ታች፡ መውረድ፡ እንደ፡ ዝናም፤ ወይም፡ ከቁም፡ በምድር፡ ላይ፡ መደፋት፤ ፍግም፡ ማለት። ወዲቅ፡ እመካናት፡ ልዑላት። ወድቀ፡ እምሰማይ። ነዳይ፡ ለእመ፡ ወድቀ፡ ይከይድዎ፡ ቢጹ። ወድቁ፡ በገጾሙ፡ (ፊልክ፡ ፺፭፪። ኢሳ፲፬፡ ፲፪። ሚራ፲፫፡ ፳፩። ማቴ፲፯፡ ፯)።

—፤ መግባት፤ መያዝ። ይወድቁ፡ ውስተ፡ ግብ። ከመ፡ ኢትደቅ፡ ውስተ፡ መሥገርታ። እመ፡ በሕሉ፡ ወደቀ፡ ኢትደቅ፡ ውስተ፡ እደ፡ ጸላእትከ፡ (ማቴ፲፭፡ ፲፬። ሚራ፱፡ ፫። ፳፭፡ ፲፬)።

—፤ መፍረስ፡ መናድ፤ ድል፡ መኾን፡ በጦርነት፡ መሞት። ጥቅም፡ ወአረፍት፡ ዘወድቀ። ወወድቁ፡ እምደቂቀ፡ ብንያም፡ እልፍ፡ ወሰማንያ፡ ምእት። ሣልስትኪ፡ ይወድቁ፡ በኲናት፡ (ኵፋ፡ ፵፯። መሳ፳፡ ፵፬። ሕዝ፭፡ ፲፪)።

—፤ መተኛት፡ መጋደም፤ መጣመር፡ ወይም፡ መከመር፤ የዝሙት። እመ፡ ቦ፡ ዘወድቀ፡ ዐርከ፡ ምስለ፡ ዐርክቱ። ዘይወድቅ፡ ምስለ፡ ብእሲት። ብእሲ፡ ዘቦቱ፡ ብእሲት፡ ወወድቀ፡ ላዕለ፡ ብእሲ፡ ተባዕት። ዘወድቀ፡ በእንስሳ፡ (ቄድር። ሲኖዶ)።

—፤ መስገድ፡ መንበርከክ፤ በግንባር፡ መተከል፤ ምድርን፡ በአፍ፡ መሳም። ወድቀ፡ አብራም፡ በገጹ። ወ

ድቁ፡ ወሰገዱ፡ ሎቱ። ወድቀ፡ ወአስተብቍዖ፡ (ዘፍ ፲፰ ። ፱ ። ማቴ፪፣ ፲፩ ። ፲፰፣ ፳፯) ።

—፤ ማዘን፣ መፍራት፤ ማቀርቀር፣ ዐንገትን፣ መድፋት ። ለምንት፡ ይወድቅ፡ ገጽከ። ኢይደቅ፡ ልቡ፡ ለእግዚእየ፡ (ዘፍ፬፣ ፮ ። ፩ነገ፣ ፲፯፣ ፴፪) ።

—፤ መሻር፣ መዋረድ፤ ከሹመት፣ ከክብር፣ መውጣት፣ መለየት ። ይደቅ፡ እምሚመቱ። ይደቅ፡ እማዕርጊሁ። ወድቀት፡ እምክብራ። ወደቅሙ፡ እምጸጋሁ፡ (አብጥ፣ ፴፩ ። ፈ፣ መ፣ ፮፣ ፩ ። ቀሌ ። ገላ፭፣ ፬) ። በወድቀ፣ ፈንታ፣ ተወድቀ፣ ተዋደቀ፣ ይላል፤ ስሕተት፣ ነው ። ቈጽለ፡ ኖኅት፡ ኢይትወደቅ፡ ዘእንበለ፡ ፈቃድየ። ሶበ፡ ቀሠፍዎ፡ ሥጋሁ፡ ተበጽለ፤ እስከ፡ ተዋደቀ፡ በበ፡ ክፍል፡ ክፍለ፡ (ቀሌ ። ስንክ፣ ሐም፳፭) ።

**ውዱቅ**፤ (ቃን፣ ቃት፣ ድቅት)፤ የወደቀ፤ የፈረሰ፤ ውዳቂ፣ ውድቃን፤ ወዳቃ፣ ዘቅዛቃ፤ ውድቅ ። ናሁ፡ ሆሎፎርኒስ፡ ውዱቅ፡ ውስተ፡ ምድር፡ በድኑ። ረከብዎ፡ ውዱቀ፡ ወምዉተ። ያነሥእሙ፡ ለውዱቃን። አረፍት፡ ውድቅት። ውዱቅ፡ እማዕርግ፤ የተሻረ፣ ሽር፣ (ዮዲ፲፬፣ ፲፰ ። ተረ፣ ባሮ ። ሚራ፵፱፣ ፲፫ ። ቀሌ) ።

»**ድቀት**፤ (ታት)፤ መውደቅ፣ መሰናከል፤ አወዳደቅ፤ ውድቂያ፤ መከራ፣ ሞት፣ ኀጢአት ። እለ፡ ይትፌሥሑ፡ በድቀቱ፡ ለጻድቅ። ድቀት፡ ትጸንሖ። ይከውኑ፡ ለድቀት፡ ኅሱር። ታነሥእ፡ እምነ፡ ድቀቱ፡ ከመ፡ ኢይማስን። እስመ፡ መትረ፡ ግብራተ፡ ድቀታት፡ እለ፡ ያርሕቅዎ፡ እምእግዚ፡ (ሚራ፳፯፣ ፳፱ ። ኢዮ፲፭፣ ፳፫ ። ጥበ፬፣ ፲፱ ። ዲድ፣ ፮ ። ፊልክ፣ ፩) ። በድቀት፣ ፈንታ፣ ውድቀት፣ ይላል፤ ፍችው፣ አንድ፣ ነው ። በእንተ፣ ውድቀቱ፡ ለሳዶቅ፡ ካህን፡ (ክብ፣ ነገ) ። ፪ኛም፣ በፃእፃእ፣ ፈንታ፣ ድቀት፣ ይላል ። ለእመ፡ ድቀት፡ ይወርስ፡ አባሁ፡ (ፊልክ) ።

**ሙዳቅ**፤ (ቃት)፤ መውደቂያ፣ መዘቅዘቂያ፤ ማረፊያ፣ ቦታ፣ (ሔኖ፳፣ ፲፫ ። ፯፣ ፮) ።

**አውደቀ**፤ ጣለ፣ አወደቀ፤ አዋረደ፣ አሻረ ። አሳዘነ፤ መታ፣ ገደለ ። አውደቀት፡ በድኖ፡ እምነ፡ ምስካቡ። ወአውደቆ፡ ውስተ፡ ማዕምቅ። ለብዙኃን፡ አውደቆሙ፡ ትዕቢተ፡ ልቦሙ። በእንተ፡ ምክንያት፡ እንተ፡ ታወድቆ፡ ለቀሲስ፡ እማዕርጊሁ። ኢታውድቁ፡ ልበክሙ። ለምንት፡ አውደቀነ። አውደቅዎ፡ በሰይፍ፡ (ዮዲ፲፫፣ ፱ ። ራእ፳፣ ፫ ። ሚራ፫፣ ፳፬ ። ፍ፣ ነ፣ ፮፣ ፳ ። ነሐ፳፣ ፲ ። ኤር፲፬፣ ፲፱ ። ፪ዜና፣ ፵፪፣ ፳፩) ። ደደቀንና፣ ደነቀን፣ እይ፤ የወድቀ፣ አግዋር፣ ናቸው ።

**ወዲር**፤ (ወደረ፣ ይወድር፣ ይደር)፤ መወደር፤ መወዳደር፣ (ዐማርኛ) ።

**ወድሶ**፤ ሶት፤ (ወደሰ፣ ይዌድስ፣ ይወድስ ። ዕብ፣ ሆዳህ)፤ ማወደስ፣ ማሞገስ፤ ማመስገን፤ በምስጋና፣ ደስ፣ ማሰኘት ። ጥበብ፡ ትዌድስ፡ ርእሳ። ብዙኃን፡ ይዌድስዎ፡ እንበይነ፡ ጥበቢሁ። ንወድሶሙ፡ ለዕደው፡ ክቡራን። ይወድስከ፡ አፈ፡ ነኪር፡ (ሚራ፳፬፣ ፩ ። ፴፱፣ ፱ ። ፵፬፣ ፩ ። ምሳ፳፯፣ ፪) ።

**ወዳሲ**፤ **መወድስ**፤ የሚያወድስ፤ አወዳሽ፣ አመስጋኝ፤ ገጣሚ፣ ባለቅኔ ።

**መወድስ**፤ በቁሙ፤ ማወደሻ፣ ድርሰት፣ መዝሙር፣ ቅኔ፤ ግጥም ። ድርሰትየ፡ ዘውእቱ፡ መወድስ። ወመወድሱ፡ ዕዝል፡ (አዋል ። ግንዘ) ።

**አወደሰ**፤ አስወደሰ፣ አስመሰገነ፤ ብፁዕ፣ አሰኘ ።

**ተወደሰ**፤ በቁሙ፤ ተሞገሰ፤ ተመሰገነ፤ አበ፣ አበ፣ ተባለ ። አብደኑ፡ በኀበ፡ ሰብእ፡ ተወድሶ፤ ወአኮ፡ በኀበ፡ እግዚ። እስመ፡ ይትዌደስ፡ ኃጥእ፡ በፍትወተ፡ ነፍሱ፡ (ዲድ፣ ፳፭ ። መዝ፣ ፱) ።

**ውዱስ**፤ (ሳን፣ ሳት፣ ድስት)፤ የተወደሰ፤ የተመሰገነ፣ ምስጉን ። ንበር፡ ምስለ፡ ኄራን፡ ከመ፡ ትኩን፡ ውዱሰ፡ በኀበ፡ እግዚ። ኮነ፡ ነሃቤ፡ ወርቅ፡ ወብሩር፡ ወውዱስ፡ ውእቱ፡ በግብረ፡ እደዊሁ። ወዛ፡ እምግባሩ፡ ውድስት፡ ዘዘከርናሃ። ዛቲ፡ ይእቲ፡ መሥዋዕት፡ ውድስት፡ (ፈላስ፣ ገ፵፰ ። ስንክ፣ ሐም፲ ። ዮሴፍ ። አፈ፣ ተ፲፩) ።

**ውዳሴ**፤ (ስያት)፤ በቁሙ፤ ማወደስ፣ መወደስ፣ አወዳደስ፣ ውደሳ፣ ምስጋና ። ዘሰ፡ ዘነገርነ፡ ዝውዳሴ፡ ይውኅድ፡ እምክብርክን። ዝክረ፡ ጻድቃን፡ ምስለ፡ ውዳሴ። ፍቅረ፡ ውዳሴ፡ ከንቱ፤ ውዳስያት፡ (ቄር ። ምሳ፲፣ ፯ ። አፈ፣ ተ፳፯) ።

**ውዳሴ፡ አምላክ**፤ የመጽሐፍ፣ ስም፤ ከብዙ፣ ድርሳናት፣ የተለቀመ፣ የሊቃውንት፣ ቃል፤ ባለ፯፣ ክፍል፤ ከሰኞ፣ እስከ፣ እሑድ፣ የሚነበብ ።

**ውዳሴ፡ ማርያም**፤ ዝኒ፣ ከማሁ፤ ኤፍሬም፣ ስለ፣ ክብረ፣ ድንግል፣ የደረሰው፣ የ፯፣ ቀን፣ ድርሰት፤ በ፯ቱ፣ ዕለታት፣ የሚደገምና፣ የሚዜም፤ የዜማ፣ ትምርት፣ መዠመሪያ ።

**ተውዳስ**፤ (ሳት)፤ ውዳሴ፣ ምስጋና፤ የሚገባ፣ የማይገባ ።

**ምውዳስ**፤ ማወደሻ፣ መወደሻ፤ ቦታ፣ መማሪያ፣ ጊዜ፣ ምክንያት፣ (አዋል) ።

**ውሂብ**፤ ቦት፤ (ወሀበ፣ ይውህብ፣ የሀብ ። ዕብ፣ ያሀብ ። ሱር፣ ይሃብ ። ዐረ፣ ወሀበ)፤ በይውህብ፣ ፈንታ፣ ይሁብ፣ ይላል፣ የተሳሳተ፣ ነው፤ ሆበን፣ እይ ። መስጠት፣ መናኘት፤ ማደል፣ ማሳለፍ፤ የያዙትን፣ ከሌላ፣ እጅ፣ ማግባት፤ ማሲያዝ፣ ማስጨበጥ፣ ማስረከብ፤ ዕንክ፣ ተቀበል፣ ማለት፤ ማቅረብ፤ በእጅ፣ በቃል ። ቃል፡ ሠናይ፡ ይኄይስ፡ እምውሂብ። በእንተ፡ ሀብት፡ ወወሃቢ፡ ወዘይሁብዎ፡ ሎቱ፤ ወንዋይ፡ ዘይሁቡ፡ ኪያሁ። ሀቡ፡ አኰቴተ፡ ለእግዚ፡ (ሚራ፲፰፣ ፲፮ ። ፍ፣ ነ፣ ፳፮ ። መዝ፣ ፳፯) ።

—፤ ማዘዝ፣ ማስናበት፤ ምስጢሩ፣ ያው፣ መስጠት፣ ነው ። ለአዳም፡ ባሕቲቱ፡ ወሀቦ፡ ይክድን፡ ኀፍረቶ።

ወኢወሀቦ ፡ ከመ ፡ ይትመየጥ ፡ ቤተ ፡ አቡሁ ፡ (ኩፋ ፡ ፸ ። ፩ነገ ፡ ፲፰ ፡ ፱) ።

—፤ ማድረግ ፡ ማኖር ፡ ማሳደር ፤ ምስጢሩ ፡ የረሰየና ፡ የሤመ ፡ ነው ፤ ዕብራይስጥም ፡ ናታን ፡ ብሎ ፤ ወሀበ ፡ ረስየ ፡ ሤመ ፡ ይላል ፤ ረስየን ፡ እይ ። እሁብ ፡ ኪዳነ ፡ ምስሌክሙ ። ቀስቶ ፡ ወሀበ ፡ ውስተ ፡ ደመና ፤ ፍርሀተክሙ ፡ እሁብ ፡ ኀበ ፡ ኵሉ ፡ ዘውስተ ፡ ምድር ። ዘሕያው ፡ የሀብ ፡ ሠናየ ፡ ውስተ ፡ ልቡ ። ወእሁብ ፡ መንፈስየ ፡ ውስቴትክሙ ፡ (ዘፍ፱ ፡ ፱ ። ኩፋ ፡ ፯ ። መክ፯ ፡ ፸ ። ሕዝ፴፯ ፡ ፳፯) ። ማስዋብ ፡ ማሳመር ፡ ማስጌጥ ፤ ውብ ፡ ማድረግ ፡ (ዐማርኛ) ።

**ወሃቢ** ፤ (ቢት ፡ ብያን ፡ ያት) ፤ የሚሰጥ ፡ ሰጭ ፤ ዐዳይ ፡ አሳላፊ ፤ ለጋስ ፡ እጀ ፡ ሰፊ ። ወሃቢሃ ፡ ለሕግ ። ወሃቤ ፡ ሕይወት ። እግዚ ፡ ወሃቤ ፡ ዕሴት ፡ ወመክፈልት ፡ ለዘገብረ ፡ ፈቃዶ ። ብእሲ ፡ ፍሡሕ ፡ ወወሃቢ ፡ (ያዕ፩ ፡ ፲፱ ። ኪዳ ። ዮሴፍ ። ምሳ፳፱ ፡ ፰) ።

—፤ ዋቢ ፡ ዐላፊ ፤ በሰጠው ፡ ነገር ፡ የሚያልፍ ፡ የሚጣድ ፤ ምስጢሩ ፡ ያው ፡ ሰጭነት ፡ ነው ፤ (ተረት ፡ ዋቢ ፡ ያለው ፡ ይወጣል ፤ ዋቢ ፡ የሌለው ፡ ይሰምጣል ።

**ወሀብት** ፤ ወሃብያን ፡ ወሃብያት ።

**»ሀብ** ፤ (ቡ ፡ ቢ ፡ ባ) ፤ ንኡስ ፡ አገባብ) ፤ ትእዛዝ ፡ አንቀጽ ፤ (ወሀብከ ፡ ትውህብ) ፡ ስጥ ፡ ዐድል ፡ አሳልፍ ፤ አምጣ ። እስኪ ፤ና ፤ በል ። ሀቡ ፡ ንበል ። ሀቡ ፡ ንረድ ። ሀቡኬ ፡ ንግባእ ። ሀብኬ ፡ ንትኃሠሥ ፡ በአይ ፡ ፍኖት ፡ ተወልደ ። ሀባ ፡ ናመክሮን ፤ ሀባ ፡ ንፍትኖን ፡ (ዕዝ፫ ፡ ፭ ። ፩ነገ ፡ ፫ ፡ ፳፫ ። ክብ ፡ ነገ ። ቄር ፡ ጸሳ ። ሄርማ) ።

**አውሀበ** ፤ አሰጠ ፡ አስቀበለ ። ኢያውሀበከ ፡ እግዚ ፡ ክብረ ፡ (ዘኍ፳፬ ፡ ፲፩) ።

**ተውህበ** ፤ ተሰጠ ፡ ታደለ ፤ ዐለፈ ። ወልድ ፡ ተውህበ ፡ ለነ ። ዝናም ፡ አበየ ፡ ተውህቦ ፡ ለምድር ። ተውህበ ፡ መብልዐ ፡ ለአንስርት ። ተውህቦ ፡ ትትወሀብ ፡ ዛ ፡ ሀገር ፡ (ኢሳ፱ ፡ ፯ ። ኩፋ ፡ ፵፱ ። ኢዮ፲፭ ፡ ፲፫ ። ኤር፵፩ ፡ ፱) ።

—፤ ኾነ ፤ ተደረገ ። ተውህቡ ፡ ታሕተ ፡ እደዊሁ ፡ (ኩፋ ፡ ፲፩) ። ተዋበ ፡ አማረ ፡ ውበት ፡ አገኘ ።

**ውሁብ** ፤ (ባን ፡ ባት ፡ ህብት) ፤ የተሰጠ ፤ ተሰጭ ፡ የኾነ ። ውሁባን ፡ ሊተ ፡ (ዘኍ፫ ፡ ፱) ። የተሰጠው ፡ የታደለ ፤ ሀብታም ፡ ዕድላም ። ውብ ፡ መልከ ፡ መልካም ፤ ደመ ፡ ግቡ ፡ ደማም ፤ ውበት ፡ ደም ፡ ግባት ፡ የተሰጠው ፤ በተፈጥሮ ።

**»ሀብት** ፤ (ታት) ፤ በቁሙ ፤ አሰጣጥ ፡ ስጦታ ፤ ፅድል ፡ ፈንታ ፤ ጸጋ ፡ ብዕል ፤ ምጽዋት ፡ ዳረጎት ፤ ጕርሻ ፡ እጅ ፡ መንሻ ፤ በከንቱ ፡ የሚሰጥ ። ወሀቦሙ ፡ ሀብተ ፡ ወፈነዎሙ ። ሀብትከ ፡ ለከ ፡ ይኩንከ ። ኵሉ ፡ ሀብት ፡ ሠናይ ፡ እምላዕሉ ። ሀብታተ ፡ መንፈስ ፡ ቅዱስ ። በእንተ ፡ ሀብታት ፡ (ዘፍ፳፭ ፡ ፯ ። ዳን፭ ፡ ፲፯ ። ያዕ፩ ፡ ፲፯ ። ፊልክ ፡ ፻፸፱ ። ፍ ፡ ነ ፡ ፳፯) ። ውበት ፡ ውብነት ፤ መልክ ፡ ደም ፡ ግባት ፤ የተፈጥሮ ፡ ሀብት ።

**»ሀብሀብ** ፤ (ዕብ ፡ ሀብሃብ ፤ ጥብስ ፡ ሥጋ) ፤ የገዘሙት ፡ ዋጋ ፡ ለጋለሞታ ፡ የሚሰጥ ፡ (ሕዝ ፲፯ ፡ ፴፱ ። መጽ ፡ ምስ) ። ወይም ፡ ጋለሞታ ፡ ና ፡ ና ፡ ስጥ ፡ ስጥ ፡ አምጣ ፡ ጨምር ፡ የምትል ።

**ተዋሀበ** ፤ ተሰጣጠ ፤ ተቀባበለ ። ሕዝብ ፡ ይትዋሀቡ ፡ ሰላመ ፡ በበይናቲሆሙ ፤ ብእሲ ፡ ለብእሲ ፡ ወአንስት ፡ ለአንስት ፡ (ኪዳ) ።

**አስተዋሀበ** ፤ አሰጣጠ ፤ አቀባበለ ፡ አስተላለፈ ፡ (ዘፀ፳፩ ፡ ፴፩) ።

**ዋህድ** ፤—አንድ ፡ ብቻ ፤—ዋሕዶ ፡ ዋሐደ ፡ ዋሕድ ።

**ውሂህ** ፤ (ወህሀ ፡ ይወህህ ፡ የሀህ ። ምህወ ፤ መየ) ፤ መወህየት ፤ ውሃ ፡ ውህማ ፡ ውሃማ ፡ መኾን ፤ መቅለጥ ፤ የምህወንና ፡ የመየን ፡ አፈታት ፡ ተመልከት ።

**ወህውሀ** ፤ (ይወህውህ ፡ ይዋህውህ ፤ ወህውሆ ፤ ተቀ ፡ ግ) ፤ ውሃ ፡ ውሃ ፡ አለ ፡ የጣዕም ፡ የሕሙም ።

**ተወህውሀ** ፤ (ይትወሀዋህ ፡ ይትዋህዋህ) ፤ ጠራ ፡ በራ ፡ ጸደለ ፤ ውሃ ፡ መሰለ ፤ በረቀ ፡ አሸበረቀ ፤ አማረ ፡ ተዋበ ፤ የመልክ ፡ የኀብር ። ጸጋ ፡ ክብር ፡ አገኘ ፤ ተደሰተ ፡ በደስታ ፡ ኖረ ፤ ተመላለሰ ፤ ምስጢሩ ፡ ግን ፡ ጥምቀትና ፡ ሀብተ ፡ ልደት ፡ ነው ። ጻድቃንኒ ፡ ትፍሥሕተ ፡ ይትፌሥሑ ፡ ወይትወሀውሁ ፡ በአዝማን ፡ ዘአልቦ ፡ ኍልቍ ። ደቂቃ ፡ ለቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ይዐቀቡ ፡ ሥርዐታ ፡ ወይትዋህውሁ ፡ ውስቴታ ፡ ወያሠንዩ ፡ ግበሪሃ ። ይትወሀውሁ ፡ በኵሉ ፡ ክብር ፡ ወፍሥሓ ፡ ዘእንበለ ፡ ጻማ ፡ ወሕማም ፡ (ድጓ ። ቀሌ) ። እለ ፡ ቀደሙ ፡ የዐይሉ ፡ ገዳመ ፡ ወአድባረ ፡ ወድኀረ ፡ ይትወሀውሁ ፡ በአዕጻደ ፡ ነገሥት ። ይሰግዱ ፡ ላቲ ፡ ወይትወሀውሁ ፡ በቅድሜሃ ፡ (መጽ ፡ ምስ ። ስንክ ፡ ነሐ፳፩) ።

**ውህዋሄ** ፤ የመልክና ፡ የክብር ፡ ብርሃን ፤ ሥን ፡ ላሕይ ፤ ጸጋ ፡ ዕበይ ። ባለብሉዮች ፡ ግን ፡ የዋሐየ ፡ ዘር ፡ አድርገው ፡ (ውሕየት) ፡ መጕብኘት ፡ ይሉታል ። ዘረከበ ፡ ብእሲተ ፡ ኄርተ ፡ ረከበ ፡ ሞገሰ ፤ ወነሥአ ፡ እምኀበ ፡ እግዚ ፡ ውህዋሄ ፡ (ምሳ፲፰ ፡ ፳፪) ።

**ወም** ፤ (ዐማርኛ) ፤ ደጀን ፡ የኋላ ፡ ጦር ፤ የፊታውራሪ ፡ አንጻር ። ወምነት ፡ ተሾመ ፡ እንዲሉ ።

**ዋዌ** ፤ ስመ ፡ ፊደል ፡ ሳድስ ፤ ፮ኛው ፡ የግእዝ ፡ ፊደል ፡ ወ ፤ በአበገደ ። ወገል ፡ ሸንገል ፤ ሜንጦ ፡ ቈላፋ ፡ ብረት ፤ ቍልፍ ፡ ዘለበት ፡ ማለት ፡ ነው ፤ ሸንገል ፡ እንደ ፡ ሜንጦ ፡ ያለ ፡ የመስኮት ፡ ስናግ ፡ ነው ። ቍልፍ ፡ ማእከል ፡ ኹኖ ፡ ግራና ፡ ቀኙን ፡ እንዲያያይዝ ፤ አማፋሪነቱን ፡ ያሳያል ። ዘለበት ፡ ማለትም ፡ በግብሩ ፡ ላይ ፡ መልኩን ፡ ጨምሮ ፡ ያስረዳል ። ሆህያተ ፡ ቤት ፡ ወዋዌ ፡ (አፈ ፡ ድ፮) ።

**ዋው ፤ (ዕብ ፡ ወሱር ፡ ወዐረ)** ፤ ዝኒ ፡ ከማሁ ። ዋው ፡ ይምጻእ ፡ ምሕረትከ ፡ (መዝ ፡ ፻፲፰ ፡ ፺፩—፺፰ ። ሰቈ፩ ፡ ፮ ። ፪ ፡ ፮ ። ፫ ፡ ፲፭ ። ፬ ፡ ፯) ።

ዋዌ ፡

**ወውዖ ፤ ዖት ፤ (ወውዐ ፡ ይዌውዕ ፡ ይወውዕ ። ዐረ ፡ ወዕውዐ)** ፤ መጮኽ ፡ ማውካት ፤ መደንፋት ፤ እልል ፡ ማለት ። ወውዐ ፡ በዐቢይ ፡ ቃል ። ወውዑ ፡ ላዕሌሁ ። ይዌውዕ ፡ ዲበ ፡ ፀሩ ። ወውዑ ፡ ሎቱ ፡ አቢሳ ። ወውዑ ፡ ኵሉ ፡ ሕዝብ ፡ (ዳን፲፫ ፡ ፲፰ ። ኤር፪ ፡ ፲፭ ። ኢሳ፵፪ ፡ ፲፫ ። ፪ነገ ፡ ፳፩ ፡ ፲፯ ። ዮዲ ፲፬ ፡ ፱) ።

**ውውዓ** ፤ ጩኸት ፡ ውካታ ፤ እልልታ ፡ ድንፋታ ፤ ቡታ ፡ ዋይታ ። ውውዓ ፡ ቀትል ። ውውዓሆሙ ፡ ለሰብአ ፡ አፍራስ ። ውውዓ ፡ ኮነ ። ውውዓ ፡ እምውስጥ ፡ (ኤር፬ ፡ ፲፱ ፡ ፳፱ ። ማቴ፳፭ ፡ ፮ ። ሶፎ፩ ፡ ፲) ።

**ውዋዔ** ፤ መጮኽ ፤ አጯጯኽ ፤ ጩኸት ። ሰላም ፡ እብል ፡ በቃለ ፡ ስብሐት ፡ ወውዋዔ ፡ (ስንክ ፡ ታኅ፮) ።

**ወዚዝ ፤ (ወዘ ፤ ወዘዘ ። ወዝወዘ)** ፤ በቁሙ ፤ ዐማርኛ ።

**ዋዜማ ፤—በቁሙ ፤—ዜመ ፤ ወዝየመ ።**

**ወዘነ ፤—መዘነ ፤—ሚዛን ፤ መዝኖ ፡ መዘነ ።**

**ወዚፍ ፤ ፎት ፤ (ወዘፈ ፡ ይወዝፍ ፡ ይዘፍ ። ሱር ፡ ያዘፍ ፤ ተለወጠ)** ፤ ማጌጥ ፤ መለወጥ ፡ ሌላ ፡ መልክ ፡ ማውጣት ። መጽሐፍ ፡ ግን ፡ በወዘፈ ፡ ፈንታ ፡ ተወዝፈ ፡ ይላል ። እምተወዝፎቱኒ ፡ (አዋል) ። በቁሙ ፡ መወዘፍ ፡ ማስቀመጥ ፡ ማስቀረት ። ውዝፍ ፡ እንዲሉ ።

**ትውዝፍት** ፤ ትዕቢት ፡ ኵራት ፤ ከልብስና ፡ ከጌጥ ፡ የተነሣ ። የምንዝር ፡ ጌጥ ፡ መልክ ፡ የሚያድስ ፡ የሚለውጥ ፡ (ቀሌ) ።

—፤ ውዝፍንት ፡ ቀሪንት ። ዘወፈን ፡ እይ ፤ የዚህ ፡ ሞክሼ ፡ ነው ። ትውዝፍት ፡ በማለት ፡ ፈንታ ፡ ትዝውፍት ፡ ይላል ፡ (ገላ፭ ፡ ፳) ።

**ወዘረ ፤ (ዐረብ)** ፤ ለበጠ ፤ ሸለመ ፡ አስጌጠ ፤ የሕንጻ ። ወወዘሩ ፡ ኵሎ ፡ ንድቀ ፡ ማኅፈድ ፡ በዕፀ ።

—፤ አወየዘረ ፡ ሾመ ፡ አከበረ ፤ ራስ ፡ ቢትወደድ ፡ አደረገ ። መጽሐፍ ፡ ግን ፡ በወዘረ ፡ ፈንታ ፡ አስተውዘረ ፡ ይላል ። እስመ ፡ አክሳይሮስ ፡ አስተውዘረ ፡ ብእሴ ፡ ዘይብልዎ ፡ ሀማን ፡ (ዮሴፍ) ።

**ወዚር** ፤ ወይዘር ፡ ታላቅ ፡ መኰንን ፤ ራስ ፡ ቢትወደድ ፡ ባለሟል ። ሶበ ፡ ተሠይመ ፡ ሀማን ፡ ወዚረ ፡ ለአክሳይሮስ ፡ (ዮሴፍ) ። ተወዘረ ፡ ማለት ፡ ከዚህ ፡ ወጥቷል ።

**ዋሕዶ ፤ ዶት ፤ (ዋሐደ ፡ ይዋሕድ ፡ ይዋሕድ ። ዕብ ፡ ያሐድ)** ፤ መዋሐድ ፤ አንድ ፡ መኾን ፡ መተባበር ፤ አንዱ ፡ ካንዱ ፡ ጋራ ። እሒድን ፡ እይ ፤ መጽሐፍ ፡ ግን ፡ በዋሐደ ፡ ፈንታ ፡ ተውሕደ ፡ ተወሐደ ፡ ይላል ። ይትወሐዱ ፡ ክልኤሆሙ ፡ ይኩኑ ፡ አሐደ ፡ ሥጋ ። ናሁ ፡ ተዋሕደ ፡ ወተሰውጠ ፡ ቦቱ ፡ (ፍ ፡ ነ ፡ ፳ ፡ ፬ ። ፈ ፡ መ ፡ ፳፮ ፡ ፯) ።

**ዋሕድ ፤ ዉሑድ ፤ (ዳን ፡ ዳት ፤ ሕድ ፤ ድት ፤ ውሕድ ። ዕብ ፡ ያሒድ ። ዐረ ፡ ዋሒድ)** ፤ የተዋሐደ ፡ አንድ ፡ የኾነ ፤ የተባበረ ። አንድ ፡ ወጣት ፡ አንድ ፡ ቅንጣት ፤ ምንታዌ ፡ መንቲያ ፡ ወይም ፡ ተቀዳሚና ፡ ተከታይ ፡ የሌለው ፡ ፍጹም ፡ አንድ ። ውኅደን ፡ እይ ። ትቀትል ፡ ወልዳ ፡ ዋሕደ ። ወቦቱ ፡ ወለት ፡ ዋሕድ ፡ ት ። ወልድ ፡ ዋሕድ ፡ ዘሀሎ ፡ ውስተ ፡ ሕፅነ ፡ አቡሁ ። ክርስቶስ ፡ ዋሕድ ፡ (ዮሴፍ ። ሉቃ፰ ፡ ፵፪ ። ዮሐ፩ ፡ ፲፰ ። ስንክ ፡ የካ፬) ።

**ዋሕድ ፡ ወበኵር** ፤ ሥግው ፡ ቃል ፤ የሥግው ፡ ቃል ፡ ስም ። ይሰመይ ፡ ዋሕደሂ ፡ ወበኵረሂ ፡ (ቄር) ። ዋሕድ ፤ በወዲያኛው ፡ በአምላክነት ፡ በባሕርይ ፡ ልደት ፤ ወልድየ ፡ አንተ ፡ በተባለበት ። ወበኵር ፤ በወዲህኛው ፡ በሰውነት ፡ ሰው ፡ ኹኖ ፡ በነሣው ፡ በቅባት ፡ በግብር ፡ ልደት ፡ ወአነ ፡ ዮም ፡ ወለድኩከ ፤ አነ ፡ እከውኖ ፡ አባሁ ፡ ወውእቱ ፡ ይከውነኒ ፡ ወልድየ ፡ በተባለበት ። ውእቱ ፡ ይብለኒ ፡ አቡየ ፡ አንተ ፡ ወአነሂ ፡ በኵርየ ፡ እሬስዮ ። በኵረ ፡ ልደት ፡ ለኵሉ ፡ ፍጥረት ። በኵረ ፡ ልደት ፡ ኵሉ ፡ ተግባሩ ፡ (መዝ፹፰ ። ሃይ ፡ አበ ፡ ኄሬ ። ቄር) ።

**ዋሕድና** ፤ አንድነት ፤ አንድ ፡ ልጅነት ፤ አንድ ፡ ብቻ ፡ መኾን ።

**አዋሐደ ፤ አስተዋሐደ** ፤ በቁሙ ፤ አዋሐደ ፡ አወሓሐደ ፤ አስማማ ፡ አንድ ፡ አደረገ ። በበ ፡ አሐዱ ፡ ታዋሕድ ። ዘያስተዋሕደከ ፡ ምስለ ፡ እግዚ ። ወአስተዋሐደ ፡ ሥጋ ፡ እንተ ፡ ነሥአ ፡ ቃል ፡ እምኔሃ ፡ (አዋል ። አረጋ ፡ ድ፩ ። ሃይ ፡ አበ ፡ ጎር) ።

**መዋሕድ ፤ መስተዋሕድ** ፤ የሚያዋሕድ ፡ አዋሓጅ ፤ አንድ ፡ አድራጊ ።

**ሙሓድ ፤ ምስትውሓድ** ፤ መዋሐጃ ፤ ማዋሐጃ ፤ ቦታ ፡ መሣሪያ ።

**ተዋሐደ ፤ (ተደራራጊ)** ፤ በቁሙ ፤ ተወሓሐደ ፡ ተገናዘበ ፤ አንድ ፡ ኾነ ፤ ምንታዌ ፡ ዐጣ ። መዋሐድ ፡ ለኹለት ፡ ለሦስት ፡ ከዚያም ፡ ለሚበዛ ፡ ይነገራል ። ወተዋሕዶሂ ፡ ውእቱ ፡ ዘክልኤሆሙ ። ወኢኮነ ፡ ክርስቶስ ፡ እኅወ ፡ በግብር ፡ ሐዲስ ፤ አላ ፡ ለቢሶ ፡ ሥጋ ፡ ዚአነ ፡ በተዋሕዶ ፡ ዘኢይትነገር ። እስመ ፡ ተዋሕዶ ፡

ማዞር ፡ መዘወር ፤ ማሽከርከር ፤ የመኪና ፡ (ዐማርኛ) ።

**ዘዋሪ** ፤ (ሪት ፡ ርያን ፡ ያት) ፤ በቁሙ ፤ ጠባቂ ፡ ከባቢ ፤ የሚዞር ፡ የሚያዞር ፤ የሚዘውር ።

**መዘውር** ፤ (ርት ፡ ራን ፡ ራት) ፤ ዝኒ ፡ ከማሁ ፤ ዘዋሪ ። በቁሙ ፤ መኪና ፡ የሚዘወር ።

**ተዘወ(ው)ረ** ፤ ተዞረ ፡ ተከበበ ፡ ተጠበቀ ። ይዜወሩ ፡ ከመ ፡ አባግዕ ። ነፍስ ፡ ዝልፍት ፡ ኢትዜወር ፡ (ኢዮ፳፭ ፡ ፲፩ ። ሚራ፲፱ ፡ ፲፫) ።

**ዘውር** ፡ (ራት) ፤ ዙሪያ ፤ ከበብ ። ሠረገላሁ ፡ በረድ ፡ ወራሕበ ፡ ዘውሩ ፡ በእሳት ፡ ሕጹር ። ወይኩን ፡ ዘውረ ፡ አክሊሉ ፡ ስፉሐ ፡ ወስፉየ ፡ በሠላስ ፡ ማዕርጋተ ፡ ስፍየት ። አምጣነ ፡ ባዕል ፡ አነ ፡ ለኢየሩሳሌም ፡ በዘውራ ፤ ንዴት ፡ ውስተ ፡ ቤትየ ፡ ኢይበውእ ፡ ለግሙራ ፡ (ቅዳ ፡ ጎር ። ፈ ፡ መ ፡ ፴፭ ፡ ፭ ። ቅኔ) ፡ ይህን ፡ ቅኔ ፡ መርድ ፡ አዝማች ፡ አምኃየስ ፡ ንጉሥ ፡ በሚባል ፡ ሰው ፡ የዘረፉት ፡ ነው ፡ ይባላል ።

**ዜዉስ** ፤—ስመ ፡ ጣዖት ፤—ዘየዉስ ።

**ዘዘ** ፤ (ደቂቅ ፡ አገባብ) ፤ እየ ፤ እየቅል ፡ ልዩ ፡ ልዩ ። በዚኣ ፡ ዝርዝር ፡ እየገባ ፡ እንደሚስማማው ፡ ይፈታል ። ለለን ፡ እይ ፤ የዚህ ፡ ጎር ፡ ነው ። ዘዘ ፡ ዚኣሁ ፤ እየራሱ ፡ እየቅሉ ፡ እየብቻው ፡ እያንዳንዱ ። ይፈልጡሙ ፡ ዘዘ ፡ ዚኣሆሙ ። ተፋለጡ ፡ ዘዘ ፡ ዚኣሆሙ ። አስተራሕቅዎሙ ፡ ዘዘ ፡ ዚኣሆሙ ፡ (ማቴ፳፭ ፡ ፴፪ ። ግብ ፲፭ ፡ ፴፱ ። ዳን፩ ፡ ፶፩) ። ዘዘ ፡ ዚኣሁ ፡ ትምህርት ። ዘዘ ፡ ዚኣሁ ፡ ጸጋሁ ፤ ልዩ ፡ ልዩ ፡ (ኢዮ፴፰ ፡ ፴፮ ። ፩ቆሮ ፡ ፲፪ ፡ ፮) ።

**ዘሐብ** ፤ (ትግ ። ዕብ ። ዐረ) ፤ ወርቅ ፤ የወርቅ ፡ ገንዘብ ፡ ዕቃ ፡ መሣሪያ ።

**ዘሕዝሐ** ፤ ሐት ፤ (ዘሕዝሐ ፡ ይዘሐዝሕ ፡ ይዘሕዝሕ) ፤ መዘክዘክ ፡ መዘርገፍ ፤ ማራገፍ ።

**ዛሕዝሐ** ፤ ሐት ፤ (ዛሕዝሐ ፡ ይዛሐዝሕ ፡ ይዛሕዝሕ) ፤ መንዣዣት ፡ መብዛት ፤ መልቀቅ ፡ መትረፍ ፡ ከልክ ፡ ማለፍ ፤ መፍሰስ ፡ መዝረብረብ ፡ መንጠባጠብ ። መጽሐፍ ፡ ግን ፡ በዛሕዝሐ ፤ ፈንታ ፡ አዛሕዝሐ ፡ ይላል ። ወያዛሐዝሐኒ ፡ በሕቁ ፡ ማእስየ ፡ (ኢዮ፴ ፡ ፴) ። ናሕንሐን ፡ እይ ።

**ዝሕዙሕ** ፤ (ሓን ፡ ሓት ፡ ዝሕት) ፤ የተንዣዣ ፤ የተትረፈረፈ ፤ ጠብ ፡ ጠብ ፡ ርግፍ ፡ ርግፍ ፡ ያለ ፤ ከልክ ፡ ያለፈ ። መስፈርት ፡ ምሉእ ፡ ወዝሕዙሕ ፡ ወንሕኑሕ ። ትስረይ ፡ ሎቱ ፡ ጌጋዩ ፡ ዝሕዝሕተ ፡ ወምልእተ ፡ (ሉቃ፮ ፡ ፴፰ ። ቄድር) ።

**ዝሕዛሔ** ፤ መትረፍረፍ ፡ አተራረፍ ፤ ትርፍቻ ፡ ተረፍ ።

**ዝሒሕ** ፤ (ዘሕሐ ፡ ይዘሕሕ ፡ ይዝሐሕ) ፤ መስፈር ፡ መሰፋፈር ፤ ዘሕዝሐ ።

**ዝሒል** ፤ ሎት ፤ (ዝሕለ ፡ ይዝሕል ፡ ይዝሐል ። ዕብ ፡ ዛሐል ፤ ዳኸ ፡ ፈሰሰ) ፤ መዛግ ፡ መመረት ፡ ማደፍ ፤ ዐፈር ፡ መሬት ፡ ቅጠል ፡ መምሰል ። ወርቅክሙኒ ፡ ወብሩርክሙኒ ፡ ዝሕለ ። ህጉል ፡ ወርቅከ ፡ እምትህጉል ፡ ዐርክከ ፡ ወእምይዝሐል ፡ ውስተ ፡ መድፍን ፡ (ያዕ፩ ፡ ፫ ። ሚራ፳፱ ፡ ፲) ። በቁሙ ፤ መዛል ፡ መድከም ፤ መዝለፍለፍ ። (ግጥም ፤ በቴዎ ፡ ጊዜ) ፤ ብርቱ ፡ ነው ፡ ስትሉት ፡ ከውቤ ፡ ይልቅ ፤ ይኸው ፡ አ(ዐ)ሊዛለ ፡ የጁን ፡ እስኪለቅ ።

**ዘሓሊ** ፤ (ሊት ፡ ልያን ፡ ይት) ፤ የሚዝግ ፤ ል ፤ ዝገታም ። እምወርቅ ፡ ዘሓሊ ፡ ወእምብሩር ፡ ማሳኒ ፡ (ድጓ) ።

**ዝሑል** ፤ (ላን ፡ ላት ፡ ሕልት) ፤ የዛገ ፡ የመረተ ፤ የተበላሸ ፡ እድፋም ። ጽህርት ፡ ዝሕልት ። መጽሔት ፡ ዝሕልት ። ዝሑላነ ፡ ልእምሮ ፡ (ሕዝ፳፬ ፡ ፮ ። ሚራ፲፪ ፡ ፲፩ ። አፈ ፡ ድ፴፫) ።

**ዛሕል** ፤ (ላት) ፤ በቁሙ ፤ ዝገት ፤ እድፍ ። ከመ ፡ ዛሕለ ፡ ብርት ፡ እከየ ፡ ልቡ ። እንተ ፡ ኢሐብረትዋ ፡ ዛሕላ ። እፈትን ፡ ዛሕለኪ ፡ በከውር ፡ (ሚራ፲፪ ፡ ፲ ። ሕዝ፳፬ ፡ ፮ ። ኢሳ፩ ፡ ፳፭) ።

**አዝሐለ** ፤ አዛገ ፡ አሳደፈ ። አዛለ ፡ አደከመ ።

**አዝሓሊ** ፤ **መዝሕል** ፤ የሚያዝግ ፤ የሚያዝል ፡ አድካሚ ።

**ዙሐል** ፤ (ዐረብ) ፤ ስመ ፡ ኮከብ ፤ ፕላኔት ፡ ከሚባሉት ፡ ከ፯ቱ ፡ ዐበይት ፡ ከዋክብት ፡ አንዱ ፤ እንደ ፡ ምድር ፡ ያለ ። ጣዖት ፤ በምሳሌው ፡ የተሠራና ፡ በስሙ ፡ የሚጠራ ። ኮከብ ፡ ዙሐል ፡ (ስንክ ፡ ሠኔ፲፪ ። ዮሴፍ) ። ፍችውን ፡ ዳተኛ ፤ ዘአልቦ ፡ ብርሃን ፡ ይሉታል ፤ ዝሑል ፡ ከማለት ፡ ይስማማል ። በዙሐል ፡ ፈንታ ፡ ሱሐል ፡ ይላል ፤ የተሳሳተ ፡ ነው ። ሱሐል ፡ አብርሀ ፡ ላዕሌየ ፡ ዮም ፡ (ቄድር) ።

**ዝሕነ** ፤—ዘና ፤—ዝኂን ፡ ዝኅነ ።

**ዝሒቅ** ፤ ቆት ፤ (ዝሕቀ ፡ ዘሐቀ ፡ ይዝሕቅ ፡ ይዝሐቅ) ፤ መዛቅ ፤ አብዝቶ ፡ ማፈሥ ፡ መውሰድ ፡ (ዐማርኛ) ። መግፈፍ ፤ መላጥ ፡ መገሽለጥ ፤ መሸልቀቅ ፡ ቈርበትን ፡ ከሥጋ ፡ መለየት ፤ ስልቻ ፡ ማውጣት ። ሀበኒ ፡ መጥባሕተ ፡ እዝሐቅ ፡ ባቲ ፡ አነዳ ፡ ትፋሕ ። ዘባሒ ፡ ይዝሕቅ ፡ አነዳ ፡ እምዲበ ፡ ሥጋ ። አዘዘ ፡ መኰንን ፡ ይዝሐቁ ፡ አምእስቲሆሙ ። ሰብአ ፡ ህንደኬ ፡ ዘሐቁ ፡ አነዳሁ ፡ ለቶማስ ፡ (ዮሴፍ ። አፈ ፡ ድ፯ ። ስንክ ፡ ጥቅ፳፭ ። መጽ ፡ ምስ) ።

**ዝሕቅ** ፤ ዝቅ ፤ (ቃት ። ዐረ ፡ ዚቅ) ፤ የማስ ፡ የቈርበት ፡ ጋን ፡ ማድጋ ፡ ፊቀን ፡ ርኰት ፡ ራዎት ፡ ቀርበታ ፤ ቀረቦ ፡ ስልቻ ፡ ዳውላ ፤ የቈርበት ፡ መሣሪያ ። ዝቀ ፡ ማይ ። ዝቀ ፡ ወይን ። ይምልኡ ፡ ኖጻ ፡ ውስተ ፡ ዝቃት ፡ (ኩፋ ፡ ፲፯ ። ፩ነገ ፡ ፲ ፡ ፫ ። አፈ ፡ ተ፲፱) ።

**ዘሓቂ** ፤ (ቂት ፡ ቅያን ፡ ያት ፤ ሐቅት) ፤ የሚዝቅ ። የሚገፍ ፤ ገፋፊ ።

**ተዝሕቀ** ፤ ተዛቀ ። ተገፈፈ ፤ ተላጠ ። ተዝሕቀ ፡ አነዳሆሙ ፡ (ስንክ ፡ ሐም፭ ። ገድ ፡ አዳ) ።

**ዝሑቅ፤(ቃን፡ ቃት፡ ሒቅት)፤** የተዛቀ። የተገፈፈ፡ የተላጠ። ዝሑቀ፡ ማእስ። ማእስ፡ ዝሕቅት፡(ስንክ፡ የካ፲፫። ግን፳፯)።

**ምዝሓቅ፤(ቃት)፤** መዛቂያ፤ መግፈፊያ፤ ቦታ፡ ወይም፡ መማሪያ። ውስተ፡ አስኳተ፡ ሀገር፡ ወቦ፡ እለ፡ በምዝሓቅ፡ ወቦ፡ እለ፡ በመንኰራኵር፡ (መጽ፡ ምስ)።

**ዝኂን፤ኖት፤(ዝኅነ፡ ይዝኅን፡ ይዝኅን)፤** መዝናት፤ ማረፍ፡ መርጋት፤ ጸጥ፡ ማለት፤ አለመታወክ። ሀድአንና፡ ረመመን፡ እይ። ዝኅነ፡ ማዕበል። ሶበ፡ረከበ፡ዐቃቤ፡ሥራይ፡ይትፌወስ፡እምሕማሙ፡ ወይዝኅን፡ እምደዌሁ፡ (መጽ፡ ምስ። ገድ፡ ኪሮ)።

**ዝኁን፤(ናን፡ ናት፡ ኅንት)፤** የዘና፤ ያረፈ፡ የረጋ፤ ጸጥ፡ ያለ፡ ጸጥተኛ። ዝኁን፡መርሶ። ነፋስ፡ዝኁን። እንዘ፡ዝኁናን፡ንሕነ፡እምትንሣኤ፡ መዋግድ። ወበትእዛዛት፡ዝኁናት፡(ቄር። አፈ፡ ተ፴፪። መጽ፡ ምስ። ቄር፡ ገ፩)።

**ዝኅነት፤** መዝናት፤አዘናግ፡ ዝናት። ዕረፍት፡ ሀድአት፡ ጸጥታ፤ዝምታ። በዝኅነት፡መንግሥትክሙ፡ (ቄር፡ ገ፩)።

**ዛኅን፤** ዝናት፤ ዕረፍት፡ ሀድአት፡ ጸጥታ፤ የባሕር፡ ወደብ። ዛኅን፡ዐቢይ። ነቢር፡ ምስለ፡ ጠቢባን፡ሰላም፡ወዛኅን፡ወሀድአት፡ውእቱ። መርስ፡ ወዛኅን፡ ጥዑይ። ኀድፈኒ፡ ውስተ፡ዛኅን፡ ወመርስ። ዛኅኑ፡ ለባሕር፡ ወመርሶ፡ ለአሕማር፡ (ማቴ፰፡ ፳፮። ፈላስ። አፈ፡ ተ፲፰። ስንክ፡ ኅዳ፲። ድጓ)።

**ዝኖን፤ ዘኖን፤ (ናት)፤** በቁሙ፤ የታላቅ፡ አውሬ፡ ስም፡ ነጌ፤ ዝኁን፡ ማለት፡ ነው፤ ዝኖን፡ ያማርኛ፡ ነጌ፡ የግእዝ፤ ነግሀን፡ እይ። (ተረት፤ ስለ፡ ሆዳም)፤ በዝኖን፡ አፍ፡ ቅርፍት።

**አዝኀነ፤** አዘና፤ ዝም፡ አሰኘ፡ ጸጥ፡ አደረገ፤ አረጋ፡ አረጋጋ። አዝኅና፡ለባሕር፡በተግሣጸ፡ነፋሳት። ዘአዝኀንከ፡እምኔነ፡ማዕበላተ፡ውሒዛተ፡መናፍስት፡(መጽ፡ ምስ። ኪዳ)። በአዝኀነ፡ ፈንታ፡ አስተዝኀነ፡ ይላል፤ ፍችው፡ አንድ፡ ነው። ውስተ፡ ዘመድኅን፡ መርሶ፡ እንዘ፡ ታስተዝኅኖ፡ ንግደ፡ ስሐመርየ፡ (ስንክ፡ ጳጕ፩)። ዳግመኛም፡ በግልብጦ፡ አጣጣፍ፡ ቀሐመን፡ ቀምሐ፡ እንደሚለው፤ ዝኅነ፡ አዝኀነ፡ በማለት፡ ፈንታ፡ ነዝኀ፡ አንዝኀ፡ ይላል፤ የጣፊ፡ ስሕተት፡ ነው። ጸጋ፡እንተ፡ታነዝኆሙ፡ለቅዱሳን። ልቦ፡ ዘየሐውር፡ውስተ፡ምኔት፡አንስት፡ከመ፡ያንዝኅ፡ አኃተ፡(ፊልክ፡ ፹፱። ሥር፡ ጳጕ)።

**አዝኃኒ፤ መዝኅኒ፤ ኅን፤** የሚያዘና፡ የሚያጸና፡ የሚያጸናና፤ የሚያረጋጋ፤ ጸጥ፡ የሚያደርግ፡ ዝም፡ የሚያሰኝ፡ (አርጋ፡ ፫)።

**ዛኅነነ፤(ተቀ፡ ግ)፤** ዘኸነነ፤ ቀይ፡ ቀለም፡ አገባ፤ የእጅና፡ የእግር፡ የጭራ።

**ዝኅንን፤** ጭብር፡ ወይም፡ ምንጭርር፤ ቅጠሉ፡ ሸካራ፡ ቀለሙ፡ ጠንካራ፤ ደብተሮች፡ ጭራቸውን፡ ወይዛዝሮች፡ እጃቸውን፡ የሚያቀልሙበት። (ወንጌላዊ፡ ግጥም)፤ ይህ፡ነው፡ እጅታው፡ የወንጌል፡ ጭራ፤ የተቈነነው፡ ባምስት፡ እንጀራ። ሐዋርያትም፡ ታሪክ፡ ሲዘሩ፤ የንስንሱት፡ በያህጉሩ። ስማዕታትም፡ ተቀብለው፤ ዝኅንን፡ ያገቡት፡ በደማቸው። ዐለለን፡ እይ።

**ዝኂር፤ሮት፤(ዝኅረ፤ዘኅረ፡ይዝኅር፡ ይዝኅር። ዐረ፡ ዘኀረ)፤** መስፋት፡ መዘርጋት፤ ማበጥ፡ መነፋት፤ መዝለል፡ መገንፈል፡ መፍላት፤ ወደ፡ ላይ፡ መውጣት፤ ምስጢሩ፡ ከልክ፡ ማለፍ፡ ነው። ልዕልናን፡ ማሰብ፡ መመኘት፤ በዚህ፡ ደግሞ፡ ከዘከረ፡ ጋራ፡ ይገጥማል። ዘሀረንና፡ ዘከረን፡ እይ፤ የዚህ፡ ትሮች፡ ናቸው።

**አዝኀረ፤** አሰፋ፡ ዘረጋ፤ ነፋ። አዘረጋ፤ አሳበጠ፡ አስነፋ። አኰራ፡ አስታበየ፤ አስመካ።

**አዝኃሪ፤መዝኅር፤(ርት፡ራን፡ራት)፤** የሚያኰራ፡ የሚያስታብይ፡ አስመኪ። በዘጺ፡ ፈንታ፡ መዝኅርት፡ ይላል፡ (አዋል)።

**ተዝኅረ፤ተዘኅረ፤** ተዠረ፡ ታጀረ፤ተጓደደ፡ ተጐላመመ፤ ያከኼደ፡ ያለባበሰ። ተዝኅራ፡አዋልደ፡ጽዮን፡ወየሐውራ፡እንዘ፡ያገዝፋ፡ክሣዶን። ኢትዘኅር፡በሥነ፡አልባሲከ፡(ኢሳ፫፡ ፲፮። ሢራ፲፩፡ ፬)። ታበየ፡ ኰራ፡ ተመካ፤ የግብር፡ ያነጋገር። ተዘኅረት፡ ልብከ። ተዘኅሩ፡ፀርየ። ተዘኅሩ፡ላዕለ፡ብሔርየ። ለምንት፡ይዜኅር፡ኀያል፡በእከዩ፡(ዐብድ፡ ፫። ስቈ፩፡ ፫። ዘካ፪፡ ፰። መዝ፡ ፶፩)።

**ዝኁር፤(ራን፡ ራት፡ ኅርት)፤** የታጀረ፤ ዕቡይ፡ ኵሩ፤ ተከባሪ፡ ተመካኪ። ጸዓሊ፡ወዝኁር። ደቂቀ፡ዝኁራን። ኢትኩኑ፡ ዝኁራነ፡ (ኢሳ፪፡ ፲፪። ኢዮ፳፰፡ ፰። ዲድ፡ ፯)።

**ዝኁራዊ፤** ትቢተኛ፡ ኵራተኛ፤ ትምክሕታም፡ (ፊልክ፡ ፪፻፳፫)።

**ትዝኅርት፤(ታት)፤** በቁሙ፤ ትቢት፡ ኵራት፤ትምክሕት፡ ተግዳሮት። ለብዙኃን፡ አስሐቶሙ፡ ትዝኅርቶሙ። ትምክሕት፡ ወትዝኅርት፡ ያማስንዎ፡ ለባዕል፡(ሢራ፰፡ ፳፱። ፳፭፡ ፪)።

**ዝኅር፤(ራት። ዝክር)፤** መቃብር፤ ዝርግ፡ ሞላላ፡ ጕድጓድ፤ ሬሳ፡ የሚዘረጋበት። የሟች፡ መታሰቢያ፡ ዝክረ፡ ስም፤ በመቃብር፡ ላይ፡ የሚጣፍ፡ ጥፈት፤ የሚቆም፡ ሐውልት፤ የሚሠራ፡ ቤት። አውቀርከ፡ ለከ፡ ዝኅረ፡ ውስተ፡ ኰኵሕ። ዝኅር፡ ሐዲስ፡ ዘአልቦ፡ ዘተቀብረ፡ ውስቴቱ። ዝኅራት፡ ይትረኃዋ። ትነድቁ፡ መቃብሪሆሙ፡ ለነቢያት፡ ወታስተሣንዩ፡ ዝኅሮሙ፡ ለጻድቃን፡(ኢሳ፳፪፡ ፲፮። ዮሐ፲፱፡ ፵፩። ቄር። ማቴ፳፫፡ ፳፱)።

**ዛይ፤—ስመ፡ ፊደል፤—ዘዪን፡ ዜነ።**

**ዝየ፤(ዝ፡ የ)፤** የቦታ፡ ዐጸፋ፤ በዚህ፡ ከዚህ፤

ወዲሀ፡ ወደዚሀ። በ፡ እም፡ እስከ፡ ይሰማሙታል፤ ቅር ብን፡ አጠገብን፡ ግራና፡ ቀኝን፡ ያሳያል፤ የሀየ፡ አንጻር፡ ነው፤ ሀየ፡ የሩቅ፡ ዝየ፡ የቅርብ፤ የሀየን፡ ፍች፡ እይ። ዝየ፡ አንድር። መጺእከ፡ ዝየ። አምጽእዎን፡ ሊተ፡ ዝየ። በዝየ፡ ተፈጸመ። እምዝየ፡ ወእምዝየ። እ ስከ፡ ዝየ፡ ብጽሒ።

**ዝይ**፤ በቁሙ፤ ዳክዬ፡ አፈ፡ መሮ፡ የባሕር፡ ዶሮ፤ ዋንተኛን፡ እገሌ፡ ዝይ፡ ነው፡ እንዲሉ።

**ዘዪግ፤ ጎት፤ (ዜገ፡ ይዘይግ፡ ይዚግ)**፤ መዜግ፤ ዜጋ፡ መኾን፡ መገዛት፡ መዋረድ።

**ዜጋ፤ (ብ፡ አዝያግ)**፤ በቁሙ፤ ተገዥ፤ ገ ብር፡ ገባር፤ ጢሰኛ፡ ባላገር። ንባቡ፡ ለነዳይ፡ ወግዩር፡ ወዜጋ፡ አስተቃሰልኩ፤ ወንባበ፡ ባዕል፡ አልዐልኩ፡ (መጽ፡ ኑዛ)።

**ዘዪድ፤ ዶት፤ (ዜደ፡ ይዘይድ፡ ይዚድ)**፤ መዘየድ፤ ዘዴኛ፡ መኾን፡ (ዐማርኛ)።

**ዜዉስ፤ (ሮማይ፡ ዴዉስ)**፤ ስመ፡ ጣዖት፤ አምላክ፡ ማለት፡ ነው፤ ዜዉስና፡ ድዮስ፡ አንድ፡ ስም፡ ናቸው። ድካምስ፡ ለዕፀ፡ ንጢአት፡ ሥርዋ፤ ሳዕለ፡ አርጤምስ፡ ወዜዉስ፡ ነዋ፡ (ደራሲ)።



ዜዉስ፡

**ዚኸ፤ (ብ፡ አዝያኸ። ዐረ፡ ዚጅ፡ ግ)**፤ ሰንጠረዥ፡ የቍጥር፡ መጽሐፍ፤ የፀሓይና፡ የጨረቃ፡ ቀመር፡ የከዋክብት፡ መንገድና፡ አካኼድ፡ የተጣፈበት፡ ገጽ፡ ሰሌዳ። በብአ፡ አዝያኸ። የቍጥር፡ ሰዎች፡ ባለ ሰንጠረዦች፡ (አቡሻ፡ ፲፩። ፵፯)።

**ዘዪም፤ ሞት፤ (ዜመ፡ ይዘይም፡ ይ ዚም። ሱር፡ ዛም። ዕብ፡ ዛምዜም። ዐረ፡ ዘምዘመ)**፤ ማዜም፤ መጮኽ፡ መትመም፤ ማጕረም ረም። ቃሉ፡ ከንህብና፡ ከተርብ፡ ከጥንዝዛ፡ ከዝንብ፡ አጯጯኽ፡ የመጣ፡ ነው፤ ሲኼድ፡ ዕዝ፡ ጥዝ፡ እያለ፡ እንደሚጮኽው።

**ዘያሚ**፤ የሚያዜም፡ አዚያሚ፤ ጯኺ፡ ተ ማሚ።

**ዜማ፤ (ማት)**፤ በቁሙ፤ ስልት፡ ያለው፡ ጩ ኸት፤ የሐለይት፡ የንዋየ፡ ማሕሌት፡ ድምጥ። አዕዋፍ፡ ዘሠናይ፡ ዜማሆሙ። ይሴብሕዎ፡ በሠናይ፡ ዜማ፡ ወማሕሌት። ኀብረተ፡ ዜማ። ዜማ፡ ግእዝ፡ ወዕ ዝል፡ ወአራራይ። ዝብጠት፡ መሰንቆ፡ ወእንዚራ፡ እለ፡ ቦሙ፡ ሠናይ፡ ዜማ፡ (ጥበ፲፯፡ ፲፯። ቀሌ። አ ርጋ፡ ፱። ግንዘ። መቃ፡ ገ፴)። ዢማ፤ ታላቅ፡ ወንዝ፡ ኸረት፤ ጯኺ፡ ብዙ፡ ማለት፡ ነው። (ዐማርኛ)።

**ዜማዊ፤ (ዊት፡ ውያን፡ ያት)**፤ ዜመኛ፡ ባለዜማ፤ ዜማ፡ ዐዋቂ፡ የዜማ፡ ሰው።

**ወዜመ፤ (ይወዘይም፡ ይወዚም)**፤ ወ ዘመ፤ ዋዜማ፡ ቆመ፤ ዜማ፡ ዠመረ። ወ፡ ከዋይ፡ የመጣ፡ ባዕድ፡ ዘር፡ ነው፤ ነቀወ፡ ብሎ፡ በአንቀወ፡ ፈንታ፡ ሰን ቀወ፡ እንዲል፤ ይህም፡ እንደዚያ፡ ነው።

**ዋዜማ**፤ በቁሙ፤ መዠመሪያ፡ ዜማ፡ ከበዓሉ፡ በፊት፡ ማታዉን፡ የሚዜምና፡ የሚመራ፡ መዝሙር፤ ቅኔ። ዋዜማ፡ ዘሠርክ። እምድኅረ፡ ፍጻሜ፡ ዋ ዜማ፡ (ድጓ። ገድ፡ ተክ)። ውኸርሞ፡ ውኸርምኸርም፡ ማለት፡ ከዚህ፡ ይስማማል።

—፤ ድራር፤ ንኡስ፡ በዓል፤ ማኅትው፡ የሚቆምበት፡ ዋዜማ፡ የሚመራበት፡ ቀን። ማኅትው፡ የነግህ፡ መዝ ሙር፡ ነው። ዋይ፡ ዜማ፡ ሲል፡ ግን፡ ፪፡ ቃል፡ ነውና፤ ዋይን፡ ተመልከት።

**ዘይን፤ ኖት፤ (ዜነ፡ ይዘይን፡ ይዚን፤ አው፡ ዘይኖ፤ ዘየነ፡ ይዜይን፡ ይዘይን። ዕብ፡ ዛዬን። ዐረ፡ ዛነ)**፤ ማልበስ፡ ማስታጠቅ፤ መሸ ለም፡ ማስጌጥ፤ ማስለፍ፡ ማስጠረር፤ ጽሕምን፡ ራስን፡ መከርከም፡ ማበጠር።

**ዘያኒ፤ መዘይን፤ (ዐረ፡ ሙዘይን)**፤ የሚያለብስ፡ የሚያስጌጥ፡ አልባሽ፤ ጽራግ፡ ማሰሬ፡ ባለ ወግ። መዘይነ፡ ንጉሥ፡ (ዮሴፍ)።

**ዛይ፤ (ዕብ፡ ዛይን)**፤ ሰባተኛ፡ ፊደል፡ ዘ። ንዋየ፡ ሐቅል፡ የበዳ፡ ጸብት፤ ፍጹም፡ ጌጥ፡ ፍጹም፡ ሽልማት፡ ማለት፡ ነው። «እስመ፡ ኍልቈ፡ ሳብዕ፡ ፍ ጹም፡ ውእቱ፡ በኀበ፡ ዕብራውያን»፡ (ሃይ፡ አበ፡ ሳዊ)። ዛይ፡ ተዘከር፡ ቃለከ፡ ዘአሰፈውኮ፡ ለገብርከ፡ (መዝ፡ ፻፲፰፡ ሣ፱—፶፮። ሰቈ፩፡ ፯። ፪፡ ፯። ፫፡ ፲፱። ፬፡ ፯)።

**ዘዬ፤ (ዐማርኛ)**፤ የነገር፡ ጌጥ፡ አንዳንድ፡ ፈሊጥ፤ ሰው፡ ኹሉ፡ በየጨዎታው፡ እንደ፡ ዚቅና፡ እን ዳዝማች፡ አድርጎ፡ የሚያገባው። አኹንም፡ እንደኾን፤ እንግዲህ፡ እንሆ፤ ታዲያ፤ ይህን፡ የመሰለ።

**ዜነወ፤ (ተቀ፡ ግ፤ ዜነ፡ ወ)**፤ ነገረ፡ አ ወራ፤ [illegible]ማ፡ ሰበከ፡ አስተማረ፤ አረዳ፡ አበሠረ። ዜን ዎሙ፡ ለበሓውርት። ሠናይ፡ እግዚሆሙ፡ ለእለ፡ ይዜንዉ፡ ሠናየ፡ ዜና። ወንጌል፡ ቅዱስ፡ ዘዜነወ፡ ማቴዎስ። ወእንዘ፡ ይዜንዎ፡ መጽአ፡ ካልእ፡ ዘይ ዜንዎ፡ ወይቤሎ፡ መጺእኩ፡ እዜኑከ። ዜነዋ፡ ገብር ኤል፡ ለማርያም፡ (ዓሞ፫፡ ፱። ሮሜ፲፡ ፲፭። ቅዳ። ኢዮ፩፡ ፲፰፡ ፲፱። ድጓ)።

**ዜናዊ፤ (ዊት፡ ውያን፡ ያት)**፤ የሚነግር፡ የሚያወራ፡ አውሪ፡ ወሬ፡ ነጋሪ፤ ሰባኪ፡ አስተማሪ። ወ

ሬኛ ፡ ወሬያም ፡ ባለወሬ ፡ ባለምሥራች ፤ መልክተኛ ፤ ወግ ፡ ጠራቂ ፡ ታሪክ ፡ ዐዋቂ ፤ የወሬ ፡ ቋት ። ዜናዊ ፡ ዘነገረነ ፡ ጥበበ ። ዜናዌ ፡ ጥበብ ። ዜናዌ ፡ ትፍሥሕት ። ዜናውያን ፡ ጽዱቃን ፡ (ኪዳ ። ቅዳ ። ድጓ ። ፊልክ ፡ ፲፯) ።

**መዜንው፤(ውት ፡ ኑት ፤ ዋን ፡ ዋት)፤** ዝኒ ፡ ከማሁ ። ዛቲ ፡ መጽሐፍ ፡ መዜንወ ፡ ዘያስተፌሥሕ ፡ ትከውን ፡ ለከ ። ከመ ፡ ንኩን ፡ መዜንዋነ ፡ ኄራነ ፡ (ፊላስ ። ኪዳ) ።

**ዜና ፤ (ናት) ፤** በቁሙ ፤ ዝና ፡ ጨዎታ ፡ ወሬ ፤ የተባለ ፡ የተነገረ ፡ ቃል ፤ የኾነ ፡ የተደረገ ፡ ሥራ ፤ ሰው ፡ ከሰው ፡ አፍ ፡ ወይም ፡ ከመጽሐፍ ፡ የሚሰማው ፡ የሚቀበለው ፡ እንግዳ ፡ ነገር ፤ ትንቢት ፡ ብሥራት ፡ ስብከት ፤ ደኅንነት ፤ መርዶ ፡ ወግ ፡ ታሪክ ፡ ገድል ፤ ደብዳቤ ፡ መልክት ፡ የመሰለው ፡ ኹሉ ። ዛቲ ፡ ይእቲ ፡ ዜና ። ዜነ ዉነ ፡ ዜና ፡ ነቢያት ። እዜንወክሙ ፡ ዐቢየ ፡ ዜና ። አነ ፡ እልእክ ፡ ኀበ ፡ አቡከ ፡ ይንግርዎ ፡ ዜናከ ። በጽሐ ፡ ዜና ፡ ኀበ ፡ ዳዊት ፤ መርዶ ። ዜና ፡ እስክንድር ፤ ዜና ፡ አይሁድ ። በከመ ፡ ተጽሕፈ ፡ በዜናቲሆሙ ፡ ለቅዱሳን ፡ (፩ዮሐ ፡ ፩ ፡ ፭ ። ድጓ ። ሉቃ፪ ፡ ፲ ። ጦቢ፲ ፡ ፫ ። ፪ነገ ፡ ፲፫ ፡ ፴ ። ዮሴፍ ። ፊልክ ፡ ፻፺፬) ። ዜናዊ ፡ ላእክ ፡ መልአክ ፡ ሐዋርያ ፡ በማለት ፡ ፈንታ ፡ ዜና ፡ ይላል ፤ የመላሽና ፡ የጣፊ ፡ ስሕተት ፡ ነው ። ወመጽአ ፡ ዜና ፡ ኀበ ፡ ሳኦል ። ወዝንቱኒ ፡ ዜና ፡ መጽአ ፡ (፩ነገ ፡ ፳፫ ፡ ፳፯ ። ፪ነገ ፡ ፲፰ ፡ ፳፮) ።

**ተዜነወ፤(ይዜኖ)፤** ተወራ ፡ ተነገረ ፤ ቃሉ ። ተረዳ ፡ ተማረ ፡ ተበሠረ ፤ ሰውዮው ። ዕበየ ፡ ዝንቱ ፡ ጻድቅ ፡ ሶበ ፡ ተዜነወ ። ወነዳያን ፡ ይዜነዉ ፡ (ስንክ ፡ ሚያ፳ ። ማቴ፲፩ ፡ ፭) ።

**ዚንው፤(ዋን ፡ ዋት ፡ ኑት)፤** የተወራ ፡ የተነገረ ፤ የተረዳ ፡ ምሁር ።

**ተዝያነወ፤(ይዝያነው ፡ ይዝያነው)፤** ተነጋገረ ፤ ተጨዋወተ ። እንዘ ፡ ይዝያነዉ ፡ ዕበያቲሁ ፡ ለእግዚ ። ሶበ ፡ ንዝያነው ፡ በእንተ ፡ አሐዱ ፡ ብእሲ ። ዜና ፡ ይነብር ፡ ለዓለም ፡ ወይዝያነዉ ፡ ቦቱ ፡ ትውልድ ፡ እምድኅረ ፡ ትውልድ ። ወተዝያነዉ ፡ ዳኅናሃ ፡ ለኢየሩሳሌም ፡ (ስንክ ፡ የካ፫ ። አፈ ፡ ድ፩ ። ዮሴፍ ። መዝ ፡ ፻፵፮) ።

**አስተዝያነወ፤(ያስተዝያኑ)፤** አዋራ ፡ አጨዋወተ ።

**ዜቄነ፤(ዴቆነ)፤** ዛቄነ ፤ ዲያቆን ፡ ኾነ ። በዜቄነ ፡ ፈንታ ፡ ዝያቄነ ፡ ይላል ፤ (ቀኖ ፡ ኒቅ፩፯) ።

**አዜቄነ፤(ያዜቁን ፡ ያዜቁን)፤** አዛቄነ ፡ ዲቁና ፤ ሾመ ። (ተረት) ፡ ያዛቄነ ፡ ሳያቀስ ፡ አይለቅም ።

**ዝያቄን፤(ናት)፤** ዛቋኝ ፤ ዲያቆን ። እስመ ፡ ዘዝያቄን ፡ ሥርዐተ ፡ ዐቀበ ፡ (ድጓ) ። ደና ፡ ዘ ፡ በዐረብ ፡ (ዳል ፡ ዛል) ፡ ተወራራሾች ፡ ስለ ፡ ኾኑ ፡ ዝያቄን ፡ ይላል ። ዚቅ ፡ ማለት ፡ ከዚህ ፡ ወጥቷል ፤ ፍችው ፡ ተጨማሪ ፡ ተባባሪ ፡ መሰል ፡ አገልጋይ ፡ ማለት ፡ ነው ። ይህም ፡ ደብተሮች ፡ በመልክ ፡ መካከል ፡ እንደ ፡ ስፌጽ ፡ ጣልቃ ፡ እያገቡ ፡ የሚሉት ፡ ዜማ ፡ ነው ። በዕብራይስጥ ፡ ግን ፡ (ዚቅ ፤ ዚቃ) ፡ መብረቅ ፡ ነጸብራቅ ፤ ኹራታም ፡ ኮከብ ፤ ፍላጻ ፡ ይኾናል ።

**ዘይት ፤ (ታት ። ዕብ ፡ ዛይት ። ሱር ፡ ዛይታ ። ዐረ ፡ ዘይት) ፤** በቁሙ ፤ የተክል ፡ ዕንጨት ፤ የወይራ ፡ ወገን ፤ ፍሬው ፡ መልካም ፡ ቅባት ፡ የሚሰጥ ፡ የሚበላና ፡ የሚበራ ። ተክለ ፡ ዘይት ፡ ሐዲስ ። ትትከሊ ፡ ዘይተ ። ዕፀወ ፡ ዘይት ። ሕንባበ ፡ ዘይት ። አዕጻደ ፡ ዘይት ። ደብረ ፡ ዘይት ፡ (መዝ ፡ ፻፳፯ ። ሚክ፯ ፡ ፲፭ ። ፩ዜና ፡ ፳፯ ፡ ፳፰ ። ኢሳ፲፯ ፡ ፮ ። ዘዳ፮ ፡ ፲፩ ። ማቴ ፳፩ ፡ ፩) ።



ዘይት ፡

—፤ ቅባቱም ፡ ለብቻው ፡ ዘይት ፡ ይባላል ። ዘይት ፡ ዘቀንዲል ። ዘይት ፡ ማኅትት ። ይውሕዝ ፡ እምኔሁ ፡ ቅብዐ ፡ ዘይት ፡ ወዕፍረት ። በከመ ፡ ይትርአይ ፡ ዘይት ፡ በውስተ ፡ ማየው ፡ (ስንክ ፡ ታኅ፳ ። ሐም፴ ። ጥቅ ፳፱ ። ፳፯) ።

***ዘይቶን፤(ዐረ ፡ ዘይቱን)፤*** ዕፀ ፡ ዘይት ፤ የዘይት ፡ ዛፍ ፡ ተክል ፤ ሕንባብ ። ዘይቶን ፡ ወሆባዕና ። ፍሬ ፡ ዘይቶን ፡ (ስንክ ፡ መስ፫) ።

**ዝኩ ፤ ዝኮ ፤ ዝክቱ ፤ ዝስኩ፤(ዝ ፡ ኩ)፤** ዘክሃ ፤ የቅርብ ፡ ሩቅ ፡ ዐጸፋ ፤ እጅ ፡ የማይደርስበት ፡ ዐይን ፡ የሚያርፍበት ። ያ ፡ ያው ፡ ያኛው ፤ ርሱ ። የዝን ፡ አፈታት ፡ እይ ፤ ኩ ፡ ከሃ ፡ ከማለት ፡ መጥቷል ፤ ስለዚህ ፡ በዘ ፡ እንተ ፡ እለ ፡ እየገባ ፡ ለቅርብ ፡ ሩቆች ፡ ዐጸፋ ፡ ይኾናል ፤ በገቢርም ፡ ጊዜ ፡ ዝኰ ፡ እንትኰ ፡ እልኰ ፡ ይላል ። ነዋ ፡ ዝኩ ፡ ሐላሚ ። ዝኩ ፡ ቃለ ። እስመ ፡ ዝንቱ ፡ ዝክቱ ፡ ወዝክቱ ፡ ዝንቱ ። ዳኅንኑ ፡ ዝስኩ ፡ አረጋዊ ፡ አቡክሙ ፡ (ዘፍ፴፯ ፡ ፲፱ ። ሩእ፩ ፡ ፲፪ ። ቄር ፡ ጸላ ። ድጓ) ። እንትኩንና ፡ እልኩን ፡ እይ ።

**ዝኬ፤(ዝ ፡ ኬ)፤** ይህ ፡ ነዋ ፤ ይህ ፡ ነው ፡ እኮ ። ዝኬ ፡ ውእቱ ።

***ዘኪክ፤ከት፤(ዘከ ፡ ይዘክክ ፡ ይዝክክ ። ዕብ ፡ ዛክኽ)፤*** መንጻት ፡ መጥራት ፤ ንጹሕ ፡ ጽሩይ ፡ ብሩህ ፡ መኾን ፡ በግብር ፡ በነገር ። ዘካ ፡ ዘኬ ፡ ዘክዘክ ፡ ማለት ፡ ከዚህ ፡ ይወጣል ። ዘካ ፡ ያረብ ፤ ፍችው ፡ ዓሥራት ፤ ዘካ ፡ ጸሓፊ ፡ እንዲሉ ። ዘኬ ፡ ያማርኛ ፤ ፍችው ፡

ኵቸሮ ፡ ተረፈ ፡ ማእድ ፤ ተማሮች ፡ ከተዝካር ፡ ዐው ድማ ፡ የሚያነሡት ፤ ዓሥራት ፡ ኀብስት ። (ግጥም) ፤ ለመ ደችና ፡ ዘኬ ፡ ባልሟ ፤ ከተማሪ ፡ ቤት ፡ ኹለግዜ ፡ ኊሟ ። ደብተራ ፤ የዘኬ ፡ ጕተራ ።

**ዝኩኪት** ፡ (ዕብራ) ፤ ቅዘዝ ፡ መስተዋት ፡ የሥዕል ፡ የመስኮት ፡ መዝጊያ ።

**ዘከሮ ፤ ሮት ፤ (ዘከረ ፡ ይዜክር ፡ ይዘ ክር ፤ አው ፡ ዘኪር ፤ ዘከረ ፡ ይዘክር ፡ ይዝ ክር ። ዕብ ፡ ዛካር ። ሱር ፡ ዝካር ። ዐረ ፡ ዘከረ)** ፤ መዘከር ፤ ማሰብ ፡ መቍጠር ፤ በልብ ፡ ማኖር ፤ ባፍ ፡ ማ ውሣት ፡ መናገር ፤ ስም ፡ መጥራት ፡ እገሌ ፡ ማለት ፤ ሲ ጠብቅ ፡ የቀደሰ ፤ ሲላላ ፡ የቀተለ ፡ ቤት ፡ ነው ። ኢትዝ ክር ፡ ለነ ፡ አበሳነ ፡ ዘትካት ። ምንትኑ ፡ ሰብእ ፡ ከመ ፡ ትዝክሮ ። ወኢይዜክር ፡ አስማቲሆሙ ፡ በአፉየ ። ሖሎ ፡ ዘዘክርነ ። ዘአቅደምነ ፡ ዘክሮታ ፡ በጥንተ ፡ ዛቲ ፡ መጽሐፍ ፡ (መዝ ፡ ፸፱ ። ፰ ። ፲፰ ። መጽ ፡ ምስ ። ፈ ፡ መ ፡ ፪ ፡ ፲፩) ። ብዙው ፡ መጣፍ ፡ በዘከረ ፡ ፈንታ ፡ ተዘከረ ፡ ይላል ፤ አድራጊውን ፡ በተደራጊ ፤ ባለቅኔዎችም ፡ እንዲሁ ፡ ብለው ፡ ይገሉታል ፤ ባለመጣፎችም ፡ ስሕተ ትነቱን ፡ አላወቁለትም ። እለ ፡ ይዜክሩ ፡ እኩየ ። ተዘ ክሮ ፡ እከይ ። ተዘከረነ ፡ እግዚኦ ። ተዘከረ ፡ በእንተ ፡ ብሩር ። ወኢተዘከረ ፡ ይግበር ። ተዘከሮ ፡ እግዚኦ ፡ ለዳዊት ፡ (ምሳ ፲፪ ፡ ፳፰ ። ቅዳ ። ጦቢ ፬ ፡ ፩ ። መዝ ፡ ፻፰ ። ፻፴፩) ።

**ዘካሪ ፤ (ሪት ፡ ርያን ፡ ያት)** ፤ በቁሙ ፤ የ ሚዘክር ፡ የሚዘክር ፡ ዐሳቢ ፤ ቄስ ።

**አዘከረ** ፤ አሳሰበ ፤ አስወሣ ፡ አስታወሰ ። በዘአ ዘከረ ፡ ሎቱ ፡ ሞሐላ ፡ አበው ። አዘክሪ ፡ ድንግል ፡ ል ደቶ ፡ እምኔኪ ። አዘከራ ፡ እሳተ ፡ ገሃነም ። ወነዋ ፡ አዘከረ ፡ ዮሴፍ ፡ ወልደ ፡ ኮርዮን ፡ ከመ ። አዘክሮ ፡ ለፈርዖን ፡ በእንቲኣየ ፡ (ጥበ ፡ ፲፰ ፡ ፳፪ ። ቅዳ ። ስንክ ፡ የካ፫ ። ዮሴፍ ። ዘፍ፵ ፡ ፲፬) ። ዳግመኛም ፡ በአዘከረ ፡ ፈንታ ፡ ዘከረ ፡ ይላል ፤ የጣፊ ፡ ስሕተት ፡ ነው ። አነ ፡ እዜ ከረከ ፡ ሖሎ ። ከመ ፡ ኣንቅህክሙ ፡ በዘክሮ ። ዘክ ሮሙ ፡ ከመ ፡ ይትአዘዙ ፡ (ኩፋ ፡ ፴፪ ። ፪ጴጥ ፡ ፩ ፡ ፲፫ ። ፫ ፡ ፩ ። ቲቶ፫ ፡ ፩ ። ፪ጢሞ ፡ ፪ ፡ ፲፬) ።

**መዘክር ፤ (ርት ፡ ራን ፡ ራት)** ፤ የሚዘ ክር ፤ የሚያዘክር ፡ አዘካሪ ፤ ዐሳቢ ፡ አሳሳቢ ። ሹም ፤ ቄ ሳጨ ፤ ምስክር ። አ ፡ ድንግል ፡ አዘክሪ ፡ ኀበ ፡ መዘክር ፡ ዘኢይረስዕ ፡ ሖሎ ፡ (ቅዳ ፡ ሕር) ። ጸሓፊ ፡ በማለት ፡ ፈ ንታ ፡ ጸሓፌ ፡ ታሪክ ፡ እንደ ፡ ማለት ፡ መዘክር ፡ ይላል ፤ ምንም ፡ ምስጢሩ ፡ ቢገጥም ፡ ንባቡ ፡ ልዩ ፡ ነው ፡ (፪ነገ ፡ ፰ ፡ ፲፮ ። ፳ ፡ ፳፬ ። ፩ነገ ፡ ፲፰ ፡ ፲፰ ፡ ፴፯) ።

**መዝከር ፤ ምዝከር** ፤ ማሰቢያ ፤ ማሳሰቢያ ፤ ጊዜ ፡ ቦታ ፡ ምክንያት ። መስ(ዝ)ከረምን ፡ እይ ።

**ተዘክረ ፤ ተዘከረ** ፤ ታሰበ ፤ ትዝ ፡ አለ ፡ ተ ወሣ ፤ ተጠራ ፤ ተነገረ ። ልማዱ ፡ ግን ፡ እንደ ፡ ዘከረ ፡ አድራጊነት ፡ ነው ። ወተዘከረ ፡ ማህሎ ። ተዘከረኒ ፡ በ መንግሥትከ ። ተዘከርኩ ፡ በሌሊት ፡ ስመከ ፡ እያለ ፤ ገንዘቡን ፡ ተገብሮነትን ፡ ትቶ ፡ አለገንዘቡ ፡ ይነገራል ።

**ዝኩር ፤ (ራን ፡ ራት ፤ ክርት)** ፤ የታሰበ ፤ የተነገረ ፡ የተጠራ ፤ ዕውቅ ፡ ስመ ፡ ጥር ፤ አቦ ፡ እገሌ ፡ የሚባል ። ቀኖና ፡ ዘዝክርት ። መምህር ፡ ዝኩር ፡ ዲበ ፡ መሥዋዕት ። አብ ፡ ዝኩር ፡ (ፈ ፡ መ ፡ ፳፯ ፡ ፯ ። ስንክ ፡ ሠኔ፳፬ ። ፊልክ ፡ ፪፻፵፪) ። ዝኩር ፡ ባለው ፡ ስ ሙዕ ፡ ይላል ።

**ዝክረት ፤ (ታት)** ፤ ማሰብ ፤ መታሰብ ፤ አስ ተሳሰብ ፤ ዐሳቢነት ፡ ታሳቢነት ። ዕሰባ ፡ ዐሳብ ፡ ምክር ። እምዝክረታተ ፡ ሰይጣናት ፡ እኩያት ፡ (ፊልክ ፡ ፻፴፯) ።

**ዝክር ፤ (ራት)** ፤ በቁሙ ፤ ዐሳብ ፡ ትዝታ ፤ ጥሪ ፡ አጠራር ፡ ዜና ። እግዚ ፡ ያበስል ፡ ዝክረኪ ፡ እም ውስተ ፡ ልብየ ። ሙሴ ፡ ዘቡሩክ ፡ ዝክሩ ። በላም ፡ ለዝክረ ፡ ስምከ ፡ (ፊልክ ። ሚራ፵፭ ፡ ፩ ። ደራሲ) ።

—፤ መወሻ ፤ መታሰቢያ ፤ ስም ፡ የሚያስጠራ ፤ ነገር ፡ ምክ ንያት ፡ ሥራ ፤ የክፉ ፡ የበጎ ፡ (መክ፩ ፡ ፲፩ ። ፪ ፡ ፲፯ ። ፱ ፡ ፭) ። ርጉመ ፡ ይኩን ፡ ዝክሩ ። ወይጥፋእ ፡ እም ድር ፡ ዝክሩ ። ዝክረ ፡ ጻድቅ ፡ ለዓለም ፡ ይሄሉ ። ዝ ክረ ፡ ቅድሳቱ ፡ (ሚራ፳፫ ፡ ፳፯ ። መዝ ፡ ፻፰ ። ፻፲፩ ። ፳፱) ።

—፤ መቃብር ፤ የመቃብር ፡ ቤት ፡ ወይም ፡ ሐውልት ። ዝጎርን ፡ ተመልከት ።

—፤ የበዓል ፡ ድግስ ፤ ማኅበር ፡ ጩንቢ ፡ ባመትም ፡ በወ ርም ፡ የሚኾን ።

**ተዝካር** ፤ በቁሙ ፤ ዝኒ ፡ ከማሁ ፤ መታሰቢያ ፡ በዓል ፡ መሥዋዕት ፡ ጸሎት ፤ ንባብ ፡ ቃል ፡ ነገር ። ወከ መ ፡ ዝ ፡ ግበሩ ፡ ተዝካርየ ። ግበር ፡ ሎቱ ፡ ተዝካሮ ። ዘ ይሁብ ፡ ስኢነ ፡ ለተዝካርየ ። ተዝካረ ፡ ስእለት ፡ (ሉቃ ፳፪ ፡ ፲፱ ። ሚራ፴፰ ፡ ፳፫ ። ኢሳ፷፮ ፡ ፫ ። ጦቢ ፲፪ ፡ ፲፪) ።

—፤ ወግ ፡ ታሪክ ፡ ዜና ። መጽሐፈ ፡ ተዝካር ። ተዝ ካረ ፡ ኖብያት ። ጸሓፌ ፡ ተዝካር ፡ (ሚል፫ ፡ ፲፮ ። አስቴ ፡ ፩ ። ኢሳ፴፮ ፡ ፫) ። የዝክርና ፡ የተዝካር ፡ ዘይቤ ፡ በማና ቸውም ፡ ስልት ፡ ቢነገር ፡ ምስጢሩ ፡ ከመታሰቢያነት ፡ አይወጣም ።

**ተዝኪር ፤ (ዐረብ)** ፤ ገዳም ፤ የመነኰሴ ፡ ቦታ ፡ ቤት ፡ በኣት ፡ (ስንክ ፡ የካ፱) ። አንዳንድ ፡ መጣፍ ፡ በተዝኪር ፡ ፈንታ ፡ ተክዚር ፡ ይላል ፤ የተሳሳተ ፡ ነው ።

**ዝክቱ ፤—ዝክ ፡ ቱ ፤—ዝኩ ።**

**ዝልበ** ፤ ሳይቀረደድ ፡ የተቀቀለ ። ዘለበት ፤ የቀ በቶ ፡ ቍልፍ ፡ (ዐማርኛ) ።

**ዘሊግ ፤ ጎት ፤ (ዘለገ ፡ ይዘልግ ፡ ይዝ ልግ ። ዕብ ፡ ዛላግ)** ፤ መዝለግለግ ፡ መዝረብረብ ፤ መውረድ ፡ መንጠብ ፡ መንጠባጠብ ፤ መንጠፍጠፍ ፤ ከይ ንና ፡ ከፍንጫ ፡ ከፍ ፡ ከመሌሊት ።

—፤ መዝለግ ፤ ዘለግ ፡ ማለት ፡ ዘለግተኛ ፡ መኾን ፤ መር ዘም ፡ ማደግ ፡ (ዐማርኛ) ።

## ቊጥር ፡ በፊደልና ፡ በአኃዝ ።

| | | | | | | | | | | | | | | | | | | | |
|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|---|
| አ | በ | ገ | ደ | ሀ | ወ | ዘ | ሐ | ጠ | የ | ከ | ለ | መ | ነ | ሠ | ዐ | ፈ | ጸ | ቀ | ቈ | አ |
| ፩ | ፪ | ፫ | ፬ | ፭ | ፮ | ፯ | ፰ | ፱ | ፲ | ፳ | ፴ | ፵ | ፶ | ፷ | ፸ | ፹ | ፺ | ፻ | ፲፻ | ፼ |

## ፯ኛ ፡ ማዕርግ ።

## ስለ ፡ እጅ ፡ መኪና ፡ ፊደል ።

፴፪ ፤ ኤውሮፖች ፡ ፊደላቸውን ፡ ሳያሳንሱና ፡ ሳይከፍሉ ፡ እናሳንስም ፡ ሳይሉ ፡ መላውን ፡ ፊደል ፡ ፳፯ቱን ፡ ዘር ፡ ከነአኃዙና ፡ ከነጓዙ ፡ አሳክተውና ፡ አስማምተው ፡ በ እጅ ፡ መኪና ፡ እንዲጥፉ ፥ የኛም ፡ ፊደል ፡ በኤውሮፖች ፡ ልክ ፡ ፳፯ ፡ ዘር ፡ ነውና ፤ እንደ ፡ መዠመሪያው ፡ ማዕርግ ፡ ጭፍራውን ፡ ትቶ ፡ አበጋዙን ፡ ብቻ ፡ ግእዝ ፡ ግእዙን ፡ ባንድ ፡ አይቅር ፡ ሰብስቦ ፡ በ፯ ፡ ዋየል ፡ ቢያስኬዱት ፡ ከእጅ ፡ መኪና ፡ ተስማምቶ ፡ እንደ ነሱ ፡ ፊደል ፡ ይኼዳል ። አኃዙንም ፡ ፲ኛውን ፡ ዘሮ ፡ አድርጎ ፡ የላይ ፡ የታች ፡ ሠረዝ ፡ ቀርቶበት ፡ ከ፩ ፡ እስከ ፡ ፱ ፡ ያለውን ፡ በ፲ቱ ፡ ዘሮነት ፡ ቢያስኬዱት ፡ ከአኃዛቸው ፡ ይሰ ማማል ። ዘሮ ፡ ማለት ፡ የአኃዝ ፡ ዋየል ፡ ወይም ፡ ምእላድ ፥ ወላጤ ፡ ፍቅድ ፡ ወመፈ ድፍድ ፡ ማለት ፡ ነው ፤ ብቻውን ፡ ሲኾን ፡ ባዶ ፡ ጠፍ ፥ አኃዝ ፡ ሲከተለው ፡ አብዢ ፡ ይባላል ፤ ጥሬነቱም ፡ ዘረወንና ፡ ዘርዘረን ፡ ይመስላል ።

## ፊደልና ፡ ዋየል ፡ ከነአኃዙና ፡ ከነጓዙ ።

አ　በ　ገ　ደ　ሀ　ወ　ዘ　ሐ　ኀ　ጠ　የ　ከ　ለ
መ　ነ　ሠ　ዐ　ፈ　ጸ　ፀ　ቀ　ረ　ሰ　ተ　ጰ　ፐ ።

## ዲቃሎች ።

ጐ　ጀ　ዠ　ኈ　ጨ　ኰ　ኸ　ኘ　ቈ　ሸ　ቸ　።

## ዋየሎች ።

ኡ　ኢ　ኣ—ዋ　ኤ　እ　ኦ　።

## አኃዞች ።

፩　፪　፫　፬　፭　፮　፯　፰　፱　፲　።

## ምልክቶች ።

.　፡　፥　፤　፦　።　.　.　.　?　!　(　)　-　«　»　—　×　+

## ዐዋጅና ፡ አገባብ ።

፴፫ ፤ ግእዝ ፡ ፊደል ፡ በግእዝነት ፡ ዋየልም ፡ በፊደልነት ፡ ሲነገር ፡ ኹሉም ፡ ራሱን ፡ ችሎ ፡ በየጠባዩ ፡ ይነገራል ። ግእዝ ፡ ኹሉ ፡ ዋየል ፡ መፈለጉ ፡ ከካዕብ ፡ እስከ ፡

ሳብዕ ፡ ነው ፤ ዋየልም ፡ ድምፁን ፡ የሚያወርስ ፡ ለግእዝ ፡ ብቻ ፡ ነው ። ይህም ፡ ራሱን ፡ ችሎ ፡ ገደለ ፡ ተገደለ ፡ ቀበረ ፡ ተቀበረ ፡ እያለ ፥ በዋየልም ፡ ታዝሎ ፥ በኡ—ቡ ፡ በኢ—ቢ ፡ በኣ—ባ ፡ በዋ—ቧ ፡ በኤ—ቤ ፡ በእ—ብ ፡ በኦ—ቦ ፡ እያሰኘ ፡ ከገ ፡ እስከ ፡ ፐ ፡ ያሉትን ፡ የኹሉን ፡ አካኼድ ፡ ያሳያል ። ዋየልም ፡ በፊደልነቱ ፡ መነሻ ፡ መድረሻ ፡ መከከልም ፡ ቢኾን ፡ እንደ ፡ ግእዝ ፡ ራሱን ፡ ይችላል ፤ ይህም ፡ ኡረኡኤለእ—ኡሩኤል ፤ ኢየአ በእ—ኢዮብ ፤ አፈእኣ ፡ አፍኣ ፤ ኤለእየኣሰእ—ኤልያስ ፤ እነኤ—እኔ ፤ እኘኣ—እኛ ፤ ኦረኢተእ—ኦሪት ፡ እያሰኘና ፡ በቁም ፡ ቀሪነቱን ፡ መደብ ፡ አድርጎ ፡ ዋየልነቱንም ፡ ያሳያል ።  ዋ ፡ ደግሞ ፡ በመነሻና ፡ በመድረሻ ፡ ፊደል ፡ በአንቀጽ ፡ ሲገባ ፥ በጥሬ ፡ መነሻም ፡ ሲገባ ፡ ልዩነት ፡ የለውም ። ምሳሌ ፤ ጐዋጐረ—ጓጐረ ፡ ጐዋጐዋረኣ—ጓጓራ ፤ ተነእፈዋፈዋ—ተንፏፏ ፤ ፈዋፈዋተኤ—ፏፏቴ ። በጥሬ ፡ መድረሻ ፡ ሲገባ ፡ ግን ፡ የሩቅ ፡ ሴት ፡ ዝርዝር ፡ ይኾናል ። ምሳሌ ፤ በኣለዋ—ባሏ ፤ ለእጅዋ—ልጇ ፤ ዐመኣ ቹዋ—ዐማቿ ። የጥሬው ፡ መድረሻ ፡ ሣልስና ፡ ራብዕ ፡ ኃምስና ፡ ሳብዕ ፡ ሲኾንበት ፡ ርሱ ፡ ራሱ ፡ ብቻ ፡ ይበቃል ፤ ይህም ፡ ሰነእጠኢ—ሰንጢ ፡ ሰንጢዋ ፤ ከኣረኣዋ—ካራዋ ፤ ጐፈረኤዋ—ጐፈሬዋ ፤ መኢደኦዋ—ሚዶዋ ፡ ማለቱን ፡ ያሳያል ። ማእከል ፡ ኹኖ ፡ ግእዝ ፡ ሲቀድመውና ፡ ሲከታተል ፡ ግን ፥ ድምፁን ፡ ለግእዝ ፡ እንዳያወርስና ፡ በቁም ፡ ቀሪ ፡ ኹኖ ፡ እንዲነገር ፡ በራሱ ፡ ላይ ፡ ፪ ፡ ነቍጥ ፡ ይደረግበታል ፤ ይህም ፡ አስተዋ̈ለ ፤ ተዋ̈ዋለ ፤ ከኡ̈ረ ፥ ለኢ̈የ ፡ እያለ ፡ ሌላውን ፡ ኹሉ ፡ ያሳያል ። የኤውሮፓን ፡ ቋንቋ ፡ ተምረው ፡ ለሚጥፉና ፡ ለሚያነቡ ፡ ስላገር ፡ ቋንቋና ፡ ስለ ፡ እጅ ፡ መኪናም ፡ ለሚያ ስቡ ፡ ማመልከቻ ፡ ይኸው ፡ ይበቃል ። የአኃዙም ፡ ነገር ፡ ዐሥርቱ ፡ ዜሮ ፡ ስለ ፡ ኾነ ፡ ዐረቦች ፡ ከህንዶች ፡ ኤውሮፖች ፡ ካረቦች ፡ እንደ ፡ ወሰዱት ፡ እንደዚያው ፡ እንደ ፡ ህንዶች ፡ አኃዝ ፡ ይኼዳል ፤ ከመልክ ፡ በቀር ፡ ያካኼድ ፡ ልዩነት ፡ የለውም ። አኃዝነ ቱና ፡ ፊደልነቱም ፡ የጽርእና ፡ የቅብጥ ፡ እንደ ፡ ኾነ ፡ በ፫ኛው ፡ ማዕርግ ፡ ተነግሯል ፡ (ቍ፳፫ና ፡ ፳፬) ። የምልክቶችም ፡ አገባብ ፡ ከነስማቸው ፡ ገና ፡ ወደ ፡ ፊት ፡ ይነገራል ።

ያልተነገረውም ፡ ያራቱ ፡ ዐይነት ፡ ቍጥር ፡ ምልክት ፡ ይህ ፡ ነው ።

\+ የመደመር ፡

— የመቀነስ ፡

× የማብዛት ፡

÷ የማካፈል ።

የንባብ ፡ ማሳያ ።

መኣእ ፡ አነእበሰኣ ፡ ዘእ̈መእነገደ ፡ የእሀኡደኣ ፤ ቀደኣመኣወኢ ፡ ኀየእለ ፡ ሠእ ለኣሰኤ ፡ ሠእየኡመ ፡ እገእዘኢአበእሐኤረእ ፡ ነእገኡሠ ፡ ነገሠእተእ ፡ ዘኢ̈ተእየኦጰእ የኣ ።  ሞአ ፡ አንበሳ ፡ ዘእምነገደ ፡ ይሁዳ ፤ ቀዳማዊ ፡ ኀይለ ፡ ሥላሴ ፡ ሥዩመ ፡ እግ ዚአብሔር ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ ዘኢትዮጵያ ።  ፲፱፻፵ ፡ ወይም ፡ 1942 ፡ ፲፱፵፪ ፡ ዓ ፡ ም ፡

## የጥፈትና ፡ የመጻሕፍት ፡ መልክ ።

፴፬ ፤ ከንገት ፡ በላይ ፡ ባለው ፡ በፍጥረት ፡ ኹሉ ፡ መልክ ፡ በየራሱና ፡ በየገጹ ፡ ልዩ ፡ ልዩነት ፡ ያላቸው ፡ ብዙ ፡ ሕዋሳት ፡ እንዳሉ ÷ በመጻሕፍትም ፡ መልክ ፡ በያንዳንዱ ፡ ገጽ ፡ ብዙ ፡ ስም ፡ ያለው ፡ ክፍል ፡ አለበት ። ያልተቀጻው ፡ ብራና ፡ ወረቀት ፡ አንዳንዱ ፡ ጥቅል ፡ ሰሌዳ ÷ ወይም ፡ ሉሕ ፡ ይባላል ፤ ዝርግ ፡ ማለት ፡ ነው ። ከዚያ ፡ የሚቀጻው ፡ አንዳንዱ ፡ ክፍል ፡ ሳይታጠፍ ፡ ቅጽ ÷ ሲታጠፍ ፡ ቅጠል ፡ ይባላል ። ፪ኛ ፡ ቅጠል ፡ የሌለው ፡ እኩሌታ ፡ ቅጽ ፡ ሲኾን ፡ ጓላፍ ፡ ይባላል ። ፬ቱ ፡ ወይም ፡ ፭ቱ ፡ ቅጽ ፡ እየታጠፈ ፡ በንድነት ፡ ሲታሰር ፡ ጥራዝ ፡ ይባላል ። አንዱ ፡ ቅጽ ፡ ተሠምሮ ፡ ሲታጠፍ ፡ ባላ፬ ፡ ገጽ ፡ ከኾነ ፡ ዘንድ ፡ ባንድ ፡ ወገን ፡ ያለው ፡ የ፪ቱ ፡ ገጽ ፡ ስምና ፡ መልክ ፡ በየክፍሉ ፡ ይህ ፡ ነው ፤ ውግ ፡ ያለበት ፡ ክፍል ፡ ግራና ፡ ቀኙ ፡ ጠርዝ ÷ መግለጫውና ፡ መግለጫው ፡ ግልየት ÷ ላይኛው ፡ አርእስት ÷ ታችኛው ፡ ጎዳግ ÷ መካከለኛው ፡ ዐምድ ፤ ዕጥፋቱን ፡ እንደ ፡ ወንዝ ፡ አማክሎ ፡ ወደ ፡ ጥራዝ ፡ ያለው ፡ ማዶና ፡ ማዶው ፡ ምስማክ ፡ ይባላል ፤ መከዳ ፡ ማለት ፡ ነው ። በመካከልም ፡ በያንዳንዱ ፡ ውግ ፡ ፊት ፡ ወስፌውና ፡ ርሳሱ ፡ ያለፈበት ፡ ሰንበር ፡ ሰንበሩ ፡ ሚራክ ÷ ቀለም ፡ የሚወድቅበት ፡ ቃዳው ፡ ተለላው ፡ መሥመር ÷ በፊደልና ፡ በፊደል ፡ መካከል ፡ ያለው ፡ ክፍት ፡ ክፍቱ ፡ ኖኅት ÷ በየፊደሉ ፡ ውስጥ ፡ ያለው ÷ ከርሥ ፡ ይባላል ፤ የነጩ ፡ ስም ፡ ይህ ፡ ነው ። የመሥመርም ፡ ሥራ ፡ አብነቱ ፡ የተገኘና ፡ የተቀዳ ፡ ከሙዝ ፡ ቅጠልና ፡ ከጕናጕና ፡ ነው ፡ ይባላል ። የጥቍሩ ፡ ደግሞ ፡ አንዳንዱ ፡ ፊደል ÷ ቀለም ፡ ወይም ፡ ጎር(ወ)መት ፡ ይባላል ፤ ቅርጽ ፡ ማለት ፡ ነው ። ከነቍጥ ፡ እስከ ፡ ነቍጥ ፡ የሚሰደረው ፡ አንዳንዱ ፡ ስክ ፡ ንባብ ፡ ይባላል ፤ ቃል ፡ ማለት ፡ ነው ። ቃልንም ፡ ከቃል ፡ በየንባቡና ፡ በየስልቱ ፡ በየብልቱ ፡ ለይተው ፡ ነጥለው ፡ ዘርዝረው ፡ ደምረው ፡ ፭ ፡ ፈርጅ ፡ አድርገው ፡ የሚያሳዩ ፡ የቃል ፡ ምልክቶች ፡ ፬ ፡ ናቸው ፤ መልካቸውና ፡ ስማቸውም ፡ ይህ ፡ ነው ።

| መልካቸው ። | ስማቸው ። |
|---|---|
| . | ነጥብ ÷ አው ፡ (ወይም) ፡ ነቍጥ ÷ ማጥበቂያ ። |
| ፡ | ንኡስ ፡ ነጥብ ÷ አው ፡ ንጻል ፡ (ነጠላ) ። |
| ፤ ÷ | ንኡስ ፡ ሠረዝ ÷ አው ፡ ንጻል ። |
| ፤ | ዐቢይ ፡ ሠረዝ ÷ አው ፡ ክዑብ ፡ (ድርብ) ። |
| ። | ዐቢይ ፡ ነጥብ ÷ አው ፡ ክዑብ ። |

## ሐተታ ።

፴፭ ፤ ነጥብና ፡ ነቍጥ ፡ ፩ ፡ ስም ፡ ናቸው ፤ ነጥብ ፡ የግእዝ ፡ ብቻ ፡ ነቍጥ ፡ የዐረብና ፡ የዕብራይስጥ ፡ ነው ፤ ያውም ፡ አንዳንዱ ፡ ጠብታ ፡ ነው ፡ እንጂ ÷ ፪ቱና ፡ ፬ቱ ፡ አይዶለም ፤ ሲበዛ ፡ ነቍጣት ፡ ነጥባት ፡ ወይም ፡ ነጠብጣብ ፡ ያሰኛል ። የጥንቱ ፡ ነጥብ ፡ እንደ ፡ ዜማ ፡ ይዘት ፡ ፩ ፡ ቅንጣት ፡ ብቻ ፡ ነበረ ፡ ይባላል ፤ ፪ኛም ፡ በንዱ ፡ ነጥብ ፡ ፈንታ ፡ እንዳ፲ቱ ፡ ያለ ፡ ዘንግ ፡ ነበረ ፤ ፫ኛ ፡ ግን ፡ አንዱ ፡ ነጥብ ፡ የመጥበቅ ፡ ምልክት ፡ ስለ ፡

ኸነ ፡ እንዳይሞከሽ ፡ በዘንጉ ፡ ፈንታ ፡ ፪ ፡ ነጥብ ፡ ኹኗል ። ፪ቱን ፡ ፬ቱን ፡ ነቍጥ ፡ ነጥብ ፡ ብሎ ፡ ባንድነት ፡ ስም ፡ መጥራት ፡ በዚያው ፡ በጥንቱ ፡ ባንዱ ፡ ቅንጣት ፡ ልማድ ፡ ነው ፡ እንጂ ፤ በሰዋስው ፡ መንገድ ፡ አይዶለም ። ባማርኛ ፡ ፪ ፡ ነጥብ ፡ ፬ ፡ ነጥብ ፡ ተብሎ ፡ ከቅጽል ፡ ጋራ ፡ ይነገራል ፤ ጣፎችና ፡ ባለመጣፎች ፡ ግን ፡ ነቍጥን ፡ ለ፪ቱ ፡ ብቻ ፡ ነጥብን ፡ ላ፬ቱ ፡ ብቻ ፡ ሰጥተው ፡ አለቅጽል ፡ ፪ቱን ፡ ነቍጥ ፡ ፬ቱን ፡ ነጥብ ፡ ብለው ፡ በተለየ ፡ ስም ፡ ውስጠ ፡ ብዙ ፡ አድርገው ፡ ይጠሩታል ። ባለቅኔዎችም ፥ ቃልከ ፡ ነቍጥ ፡ እንዘ ፡ ክልኤቲ ፤ ልሳንከ ፡ አሐቲ ፡ ይእቲ ። ፍቅደ ፡ ነጥብ ፡ በዓላተ ፡ ወልድ ፡ ተስዐቱ ፡ ውእቱ ፡ እያሉ ፡ በውስጠ ፡ ብዙነት ፡ ያገቡታል ። ነጥብን ፡ ተስዐቱ ፡ ማለት ፡ ፭ ፡ ቀይ ፡ ሲጨመርበት ፡ ነው ።

## አገባባቸውም ፡ ይህ ፡ ነው ።

፴፮ ፤ ነቍጥ ፡ የንኡሳን ፡ ቃላት ፡ መለያ ፡ ነው ፤ በንባብ ፡ ኹሉ ፡ ራስ ፡ በያንዳንዱ ፡ ስክ ፡ ይገባል ። ነጠላ ፡ ወይም ፡ ንኡስ ፡ ሠረዝ ፡ ጠባዩ ፡ ፩ ፡ ሲኾን ፡ መልኩ ፡ ፪ ፡ ነው ፤ ልዩነት ፡ ስላላቸው ፡ እየራሳቸው ፡ በሚታሰሩና ፡ በማይጫፈሩ ፡ ባጫጭር ፡ ቃሎች ፡ ይገባል ። ምሳሌ ፤ አነ ፡ ቀዳማዊ ፤ ወአነ ፡ ደኃራዊ ፥ ርእስ ፡ ወማኅለቅት ፤ ጥንት ፡ ወተፍጻሜት ፤ አንተ ፡ ዘአሜሃ ፤ ወአንተ ፡ ዘይእዜ ፥ አንተ ፡ ዘእሙንቱ ፤ ወአንተ ፡ ዘለነ ። ተፈለጥ ፡ የማነ ፤ አው ፡ ፀጋመ ፥ ወእመ ፡ አኮ ፡ ግባእ ፡ ድኅረ ፤ ወኢትሑር ፡ ቅድመ ። ድርብ ፡ ወይም ፡ ዐቢይ ፡ ሠረዝ ፥ በፍጹም ፡ ቃል ፡ ማኸል ፡ በንዳንዱ ፡ ፈርጅ ፡ (ፍራዝ) ፡ ውስጥ ፡ እየራሱ ፡ በሚታሰርና ፡ በሚነገር ፡ ባስረጅና ፡ ባፍራሽ ፡ ይገባል ። ምሳሌ ፤ ወምድርሰ ፡ ኢታስተርኢ ፤ ወኢኮነት ፡ ድሉተ ፤ ወጽልመት ፡ መልዕልተ ፡ ቀላይ ፤ ወመንፈሰ ፡ እግዚ ፡ ይጼልል ፡ መልዕልተ ፡ ማይ ። ወይቤ ፡ እግዚ ፤ ለይኩን ፡ ብርሃን ፤ ወኮነ ፡ ብርሃን ። ነዐ ፡ ንበር ፡ ማእከሌነ ፡ ወንግረነ ፤ እስመ ፡ ኪያከ ፡ አልሀቀ ፡ እግዚ ። ፈርሀ ፡ ወደንገፀ ፤ ባሕቱ ፡ ኢጐየ ፡ ወኢገገጸ ። ነጥብ ፡ (።) ንኡስ ፡ ምዕራፍ ፡ ነው ፤ አንባቢን ፡ እንደ ፡ ልጓም ፡ ኹኖ ፡ ይገታል ። አንዱ ፡ ፍጹም ፡ ቃል ፡ ወይም ፡ አንዱ ፡ ፈርጅ ፡ ዐጭርም ፡ ረዥምም ፡ ቢኾን ፡ ተሳቢው ፡ ተከቶ ፡ ነገሩ ፡ ሲጨረስ ፡ እንደ ፡ ጕልላት ፡ በጫፉ ፡ በቍንጮው ፡ ይገባል ። ረዥም ፡ ቃል ፥ ወምድርሰ ፡ እንዳል ነው ፡ ያለ ፡ ነው ። ዐጭር ፡ ቃል ፥ በቀዳሚ ፡ ገብረ ፡ እግዚ ፡ ሰማያተ ፡ ወምድረ ። ያማርኛውም ፡ እንደ ፡ ግእዙ ፡ ነው ፤ ለብቻው ፡ የተለየ ፡ ዐዋጅ ፡ የለውም ።

፴፯ ፤ በነዚህ ፡ ባራቱ ፡ ላይ ፡ ደግሞ ፤ . . . . ነጠብጣብና ፡ ( ) ቀርን ፡ « » አቅርንት ፡ ሲጨመሩ ፡ ቍጥራቸው ፡ ፯ ፡ ይኾናል ፤ የነዚህም ፡ የ፫ቱ ፡ አገባብ ፡ እንዲህ ፡ ነው ። ነጠብጣብ ፡ ከያንዳንዱ ፡ ምዕራፍና ፡ አንቀጽ ፡ ፍሬ ፡ ፍሬው ፡ ጥቅስ ፡ በጥፈት ፡ ሲለቀም ፡ በቀሪው ፡ ቃል ፡ ፈንታ ፡ ይገባል ። ምሳሌ ፤ መጽሐፈ ፡ ልደቱ ፡ ለኢ ፡ ክር ፡ ወልደ ፡ ዳዊት ፡ ወልደ ፡ አብርሃም ። አብርሃም ፡ ወለዶ ፡ ለይሥሐቅ ፤ . . . . ወእሴይኒ ፡ ወለደ ፡ ዳዊትሀ ፡ ንጉሠ ፤ . . . . ወኵሎንኬ ፡ ትውልድ ፡ እምአብርሃም ፡ እስከ ፡ ዳዊት ፡ ዐሠርቱ ፡ ወአርባዕቱ ። ቀዳሚሁ ፡ ቃል ፤ . . . . ወውእቱ ፡ ቃል ፡ ሥጋ ፡ ኮነ ። ዳግመኛም ፡ በቋንቋ ፡ መጣፍ ፡ ውስጥ ፡ የተጣፈውን ፡ ቃል ፡ አንዱን ፡ ስም ፡ መላ

ልሰ ፡ በመጣፍ ፡ ፈንታ ፡ በቀሪው ፡ ፊደል ፡ ልክ ፡ ይገባል ። ምሳሌ ፤ ጎግ ፥ ማ . . ። ዳ
ዊት ፥ መዝሙረ ፡ . . . ። አምላክ ፥ ወልደ ፡ . . . . ። ቀርን ፡ እንደ ፡ ዋዌና ፡ እንደ ፡
አው ፡ ነው ፤ ሞክሼና ፡ በዕድ ፡ አስረጅ ፡ ወይም ፡ ተወላጅ ፡ ስለ ፡ ኹነ ፡ ተጥፎ ፡ በማይነ
በብ ፥ በ ፡ ዘይቤ ፡ በሚያሰኝ ፡ ነገር ፡ በትርፍ ፡ ንባብ ፡ ይገባል ። ምሳሌ ፤ ወንጌል ፡ ብሂል ፡
በልሳነ ፡ ጽርእ ፤ ወትርጓሜሃ ፡ ስብከት ፡ (ብሥራት) ። እስመ ፡ ክርስቶስ ፡ ብሂል ፡ ቅቡዕ ፡
(መሲሕ) ። ፲፱፻፴፬ ፡ (፵፪) ፡ ዓ ፡ ም ፡ በግስም ፡ ሲገባ ፡ ጽሒፍ ፤ (ጸሐፈ ፡ ይጽ
ሕፍ ፡ ይጽሐፍ) ፡ መጣፍ ፡ አጣጣፍ ። ጸሓፊ ፤ (ፊት ፡ ፍያን ፡ ያት ፤ ጸሐፍት) ፡ ያሰኛል ።
አቅርንት ፡ ያንዱን ፡ ደራሲ ፡ ቃል ፡ ከሌላው ፡ ድርሰት ፡ ለመለየት ፡ ባለድርሳኑ ፡ ሌሎች ፡
ከደረሱት ፡ ከድርሳን ፡ ከተግሣጽ ፡ አብዝቶ ፡ አሳንሶ ፡ በሚጠቅሰው ፡ ቃል ፡ በጥቅስና ፡
በስሯጽ ፡ ይገባል ፤ ጥቅስና ፡ ስሯጽ ፡ የንባብ ፡ የምስጢር ፡ የድርሰት ፡ ማቅኛ ፡ ስለ ፡
ኹኑ ፥ እነዚህ ፡ ፪ቱ ፡ ፩ ፡ ወገን ፡ ናቸው ። ምሳሌ ፤ ከመ ፡ ዝ ፡ ነአምን ፡ ወከመ ፡ ዝ ፡ ንት
አመን ፤ ወንበል ፡ ጸሎተ ፡ ሃይማኖት ። «ነአምን ፡ በአሐዱ ፡ አምላክ ፡ . . . . ። ወን
ሴፎ ፡ ትንሣኤ ፡ ሙታን ፤ ወሕይወተ ፡ ዘይመጽእ ፡ ለዓለመ ፡ ዓለም» ። ንግበእኬ ፡ ኀበ ፡
ጥንተ ፡ ነገር ።

፴፰ ፤ ጣፎችና ፡ ዐታሞች ፡ የፊደላትን ፡ ዘር ፡ በብራና ፡ ማሕፀናቸው ፡ በወረ
ቀት ፡ ሰፋድላቸው ፡ ከመምህራን ፡ እየተቀበሉ ፡ ፀንሰውና ፡ አምጠው ፡ በቀለም ፡ በብ
ርዕ ፡ የሚወልዱት ፡ የጥፈትና ፡ የመጻሕፍት ፡ መልክ ፡ ድርሰቱ ፡ መድበሉ ፡ ከምሉ ፡
በክፍሉ ፡ ይህ ፡ ነው ። ይህ ፡ የጣፍነው ፡ ኹሉ ፡ ስምና ፡ መልክ ፡ ታትሞ ፡ ተጥፎ ፡ ተጠ
ርዞና ፡ ታፍፎ ፥ ድጕሱና ፡ ማኅደሩ ፡ ተከናውኖ ፥ ግዙፍና ፡ ምእዙን ፡ ኹኖ ፡ ሥራው ፡
ከለቀለት ፡ በኋላ ፤ መጽሐፉ ፡ በጽላት ፥ ማኅደሩ ፡ በታቦት ፥ ዙሪያው ፡ በ፳ቱ ፡ ማእ
ዝን ፡ ይመሰላል ። ከዚያውም ፡ ዘንድ ፥ ቀኙ ፡ የምሥራቅ ፡ ግራው ፡ የምዕራብ ፥ ራሱ ፡
የሰሜን ፡ እግሩ ፡ የደቡብ ፤ ፬ቱ ፡ ቀርን ፡ በነዚህ ፡ ውስጥ ፡ ያለው ፡ የንኡስ ፡ ማእዝን ፡
ምሳሌ ፡ ነው ።

፴፱ ፤ ለንባቡም ፡ ትምርት ፥ ለስልቱና ፡ ለማዕርጉ ፡ እንዳ፭ቱ ፡ ጸዋትወ ፡ ዜማ ፡
፭ ፡ ክፍል ፡ አለው ፤ ፩ኛው ፡ ቊጥር ፥ ፪ኛው ፡ ግእዝ ፥ ፫ኛው ፡ ወርድ ፥ ፬ኛው ፡ ዐቢይ ፥
፭ኛው ፡ ድጋም ፡ ወይም ፡ ማነብነብ ፡ ይባላል ። እነዚህም ፡ ፭ቱ ፡ ክፍሎች ፡ ጸዋትወ ፡
ንባብ ፡ ተብለው ፡ ኹሉም ፡ በሕፃን ፡ አካኼድ ፡ ይመሰላሉ ፤ ቊጥር ፡ እንደ ፡ መንኛ
ቀቅ ፥ ግእዝ ፡ እንደ ፡ መዳኽ ፡ ነው ፤ እነዚህ ፡ ፪ቱ ፡ በሣር ፡ በሥንጥር ፡ ይነገራሉ ።
ቊጥር ፡ በኖኀትና ፡ በኖኀት ፡ መካከል ፡ ያለውን ፡ የያንዳንዱን ፡ ፊደል ፡ ራስ ፡ ራሱን ፡
በሣር ፡ እየነኩ ፥ ፩ ፡ ፪ ፡ ፫ ፡ እንደ ፡ ማለት ፡ ኹሉ ፡ ስም ፡ ስሙን ፡ ለይቶ ፡ መጥራት ፡
ነው ። ግእዝ ፥ ከነቊጥ ፡ እስከ ፡ ነቊጥ ፡ በያንዳንዱ ፡ ስክ ፡ ያሉትን ፡ ፊደሎች ፡ እንደ ፡
መሠረዝ ፡ ሣሩን ፡ በላያቸው ፡ እያሳለፉ ፡ በቅርብ ፡ በቅርቡ ፡ ማጋጠም ፡ ነው ።
ወርድ ፥ ዘርፍና ፡ ባለቤት ፡ ሳቢና ፡ ተሳቢ ፡ በማዛረፍና ፡ በማናበብ ፡ የሚወድቅና ፡ የሚ
ነሣ ፡ የሚጠብቅና ፡ የሚላላ ፡ ቀለም ፡ ለይቶ ፡ በሐዘንዚን ፡ ቃል ፡ እየጮኹና ፡ እያለፉ ፡
እየተደገፉ ፡ ማንበብ ፡ ነው ። ይኸውም ፡ እጅን ፡ ተይዞ ፡ አቱ ፡ ሥግሬ ፡ ታቱ ፡ ሥግሬ ፥
ወይም ፡ ዳዴ ፡ ዳዴ ፥ አንድ ፡ ኹለት ፡ እየተባሉ ፡ በመኼድና ፡ በመራመድ ፥ በማንገር

ገር ፡ በመወናከር ፡ ይመሰላል ። አቡጊዳና ፡ ወርድ ፡ ንባብ ፡ ለተማሪ ፡ በጣም ፡ ይጠቅማሉ ፤ እለነዚህ ፡ አለኹለቱ ፡ በፊደል ፡ በንባብ ፡ ቶሎ ፡ መሠልጠን ፡ አይቻልም ። ዐቢይ ፡ ንባብ ፥ ራስን ፡ ችሎ ፡ እየተቀናጡ ፡ ቶሎ ፡ ቶሎ ፡ እንደ ፡ መኼድ ፡ ኹሉ ፤ በነቍጥ ፡ በሠረዝ ፡ የተለየውን ፡ ቃል ፡ ከነጥብ ፡ እስከ ፡ ነጥብ ፡ እንደሚገባው ፡ እያሰሙ ፡ እያሰ ማሙ ፡ ማንበብ ፡ ነው ። ድጋም ፡ ከደጋሚው ፡ በቀር ፡ ሌላ ፡ የማይሰማው ፡ ስለ ፡ ኾነ ፡ በሩጫ ፡ አካኼድ ፡ ይመሰላል ። የሚጠብቅና ፡ የሚላላ ፡ ቀለም ፡ ያልነውም ፡ ልዩ ፡ ልዩነቱ ፡ በንባብ ፡ ብቻ ፡ አይዶለም ፥ በምስጢርም ፡ እንጂ ፤ መላላት ፡ የሥራ ውን ፡ ቀሊልነትና ፡ ገርነት ፥ መጥበቅ ፡ ግን ፡ ከባድነቱን ፥ በኀይልና ፡ በግድ ፡ መኾ ኑን ፡ ያሳያል ። ከግእዝም ፡ ይልቅ ፡ ዐማርኛ ፥ ገደለ ፡ ሰበረ ፥ ዐረሰ ፡ ቈፈረ ፥ ዐጨደ ፡ ነቀለ ፡ እያሰኘ ፡ አጥብቆ ፡ ያሳያል ፤ ዕብራይስጥም ፡ እንዳማርኛ ፡ ነው ። ጸዋትወ ፡ ፊደል ፡ የተባለው ፡ የሰዋስውና ፡ የግስ ፡ መቅድም ፡ እስከዚህ ፡ ነው ።

## የታሪክ ፡ መርገፍ ፡ የመቅድም ፡ አጫዋች ።

ውዳሴ ፡ ዕበያ ፡ ወክብራ ፡ ለብእሲተ ፡ ሰማይ ፡ ፊደል ፡ አርአያ ፡ ድንግል ።

፵ ፤ ንግባእኬ ፡ ኀበ ፡ ጥንተ ፡ ነገር ፡ ወባህል ፤ ወንሕትታ ፡ ካዕበ ፡ ለቅድስት ፡ ፊደል ፥ በዘዘ ፡ ዚአሁ ፡ አርአያ ፡ ወዘዘ ፡ ዚአሁ ፡ አምሳል ፡ እንዘ ፡ ኪያሃ ፡ ንሜስል ፡ ወናስተማስል ። በመኑ ፡ በአምሳለ ፡ መኑ ፡ ትትሜሰል ፡ ፊደል ፤ በምድረ ፡ ሎዛኑ ፡ ወዳቤር ፡ ሀገረ ፡ ሰዋስው ፡ ወመጽሐፍ ፥ ወሚመ ፡ በሲና ፡ ጉባኤ ፡ መላእክት ፡ አእ ላፍ ፤ አው ፡ በጽዮን ፡ ሀገረ ፡ ዳዊት ፥ ወእመ ፡ አኮ ፡ በኢየሩሳሌም ፡ ቅድስት ፤ ጽዮ ንሰ ፡ ወሳሌም ፥ መካነ ፡ ርእሱ ፡ ለአዳም ፥ ወመክፈልተ ፡ ርስቱ ፡ ለሴም ፤ እስመ ፡ እም ጽዮን ፡ ይወፅእ ፡ ሕግ ፡ ወቃለ ፡ እግዚአብሔር ፡ እምኢየሩሳሌም ፡ በከመ ፡ ጽሑፍ ። ፊደልሰ ፡ እሚን ፡ መሠረተ ፡ ነገር ፡ ወጥንት ፤ ወከልአኒሃ ፡ መጻሕፍት ፡ ሕንጻ ፡ ወንድቅ ፡ ከመ ፡ እንተ ፡ ምግባር ፡ ወትሩፋት ። ሥረዊሃ ፡ ሥርወ ፡ ቀለማት ፥ ዐቃቂረ ፡ ፈውስ ፡ ወመድኀኒት ፡ ዘመሀሮ ፡ ለኖኅ ፡ አሐዱ ፡ እመላእክት ፡ ዐቃቤ ፡ ሥራይ ፡ ታበት ፤ ወሥ ርወ ፡ ነገራ ፡ ይቀውም ፡ በስምዐ ፡ ሠለስቱ ፡ ገጻት ፡ ከመ ፡ ሥርወ ፡ እሴይ ፡ ወዳዊት ። ሠናይትኬ ፡ ሠናይት ፡ እምኵሎን ፡ ሠናያት ፥ ላሕየ ፡ ፈጣሪ ፡ ሕያው ፡ ወሥነ ፡ ኵሉ ፡ ፍጥ ረት ፤ እስመ ፡ ጐላቊሃ ፡ ዕሥራ ፡ ወክልኤት ፤ ወሱባዔሃኒ ፡ ፍጹም ፡ ሱባዔ ፡ ዕለት ፡ እም ዕለተ ፡ እሑድ ፡ ግእዝ ፡ እስከነ ፡ ሳብዕት ። አርአያሃኒ ፡ አዳም ፡ አርአያ ፡ ሥላሴ ፡ ቅድስት ፤ ወአምሳሊሃኒ ፡ ነዮሙ ፡ ዐሠርቱ ፡ ቃላት ፥ ወሰሌዳቲሃ ፡ ጽላት ። ጽሕፈታሂ ፡ መንክር ፡ ዘእ ግዚአብሔር ፡ ጽሕፈት ፡ በጸፍጸፈ ፡ ሰማይ ፡ ሳብዕ ፡ ሰሌዳ ፡ እሳት ፤ ወግብረታሂ ፡ ዕጹብ ፡ ግብረ ፡ መለኮት ፡ እምኀበ ፡ አልበ ፡ ማየ ፡ ሕመት ። ታቦታ ፡ ደቂቀ ፡ ሴት ፤ ወደብተራሃ ፡ ሰብአ ፡ ትካት ። አዕማዲሃሰ ፡ ኖኅ ፡ ወሴም ፡ ካም ፡ ወያፌት ፤ ወምዕማዲሃ ፡ ነቢያት ፡ ወካ ህናት ። አርእስቲሃ ፡ አብርሃም ፡ ይሥሐቅ ፡ ወያዕቆብ ፡ አርእስተ ፡ አበው ፡ ቀደምት ፤ ወደመና ፡ ርእሳ ፡ ብሩህ ፡ መንፈሰ ፡ ትንቢት ። አረፋቲሃ ፡ ዘዕንቍ ፡ አእባነ ፡ ልብሰ ፡ አሮን ፡ ሕስት ፤ ወመሠረታ ፡ ዘጽድቅ ፡ ኰኵሐ ፡ ሃይማኖት ፤ ወኰኵሕሰ ፡ ክርስቶስ ፡ ሊቀ ፡ ካህናት ፡ እብነ ፡ ርእሰ ፡ ኵሉ ፡ ማእዘንት ፡ ዘመነንዎ ፡ ነደቅት ። ቅድስተ ፡

ቅዱሳን፡አበው፡ንቅዐ፡ምስጢራት ፤ ወመንበረ፡ስብሐት፡ድልው፡እምአፈ፡ደቂቅ፡ ወሕፃናት ። ኵለንታሃ፡ወርቅ፡ተቋመ፡ማኅቶት ፥ ወመድሎተ፡ወርቃ፡ጽሩይ፡ መጠነ፡መክሊት ፤ አዕጹቂሃኒ፡አዕጹቀ፡ዘይት፡አምሳለ፡ሰብዐቱ፡ሀብታት ፥ ወመ ሳውሪሃ፡አእላፍ፡ብሩሃን፡አልባብ፡ጸሐፍት ። ጸዳለ፡ብርሃና፡ወሥና፡ብዝኀ፡ትም ህርት ፤ ወብርሃናስ፡ውእቱ፡ገባሬ፡ብርሃናት፡ዐበይት፡ዘበጸዳለ፡ብርሃኑ፡ሰሰለ፡ ጽልመት ።

፵፩ ፤ ጥብልልት፡ራእዩ፡ወፋእሙ፡ለበላዔ፡መጽሐፍ፡ሕዝቅኤል ፤ ወስቴ፡ ጽዋዑ፡ለዕዝራ፡ደመ፡ሕብረ፡እሳት፡አስካል፡ዘያውዒ፡ልበ፡ወያንበለብል ። ይእ ቲኬ፡ድንግል፡ወላዲተ፡ቃል፡በብሥራተ፡መልአክ፡ገብርኤል ፤ መጥበቢተ፡ አብዳን፡ኖሎት፡ወሰብአ፡ሰገል፡እለ፡ውስተ፡ዓለም፡ኀል ፤ እስመ፡ህላዌሁ፡ለቃል፡ ህላዌ፡ፊደል፡በከመ፡ተነበየ፡ዳንኤል፡ወፈከረ፡ላቲ፡በብዙኅ፡አምሳል ። ወኮከበኒ፡ ታው፡ጽዱል፡ኮከበ፡ወንጌል፡ዘቦቱ፡ትእምርተ፡መስቀል ። አበዊነሂ፡ይብ ልዋ፡በዘአበዊሆሙ፡ባህል፡ወለቱ፡ለሄኖስ፡ንእስተ፡አካል፡ወእኅተ፡አቡሁ፡ለመ ላልኤል ። ፍኅርቱ፡ለያሬድ፡ልሂቅ፡ብሉየ፡መዋዕል ፤ ወመፅመርተ፡ብርዑ፡ለሐ ኖክ፡ጸሓፌ፡ጥበቡ፡ለልዑል ። ሱታፌ፡ንባቡ፡ወቃሉ፡ለማቱሳላ፡ባዕል ፤ ወፍ ቅርተ፡ላሜኅ፡ወኖኅ፡ወራዙተ፡ኀይል ።

፵፪ ፤ ልህቅት፡ይእቲ፡እምሰብዓ፡ሊቃናት ፤ ወብሊት፡ዘእምቅድመ፡ብሉይ፡ ኦሪት ። ሐፃኒተ፡ሙሴ፡ሕፃን፡ዘአኮ፡ይብስተ፡አጥባት ፤ ወጥልልተ፡ርሥአን፡ ዕቤርት፡እሞን፡ለዕቤራተ፡ሕግ፡መጻሕፍት፡ወለአዋልድ፡ንኡሳት ፤ በከመ፡ተብ ህለ፡ስሳ፡እማንቱ፡ንግሥታት፡ወሰማንያ፡ዕቁባት ፥ አዋልድሰ፡እለ፡አልቦን፡ኍ ልቍ፡ወመስፈርት ። ወላዲቱ፡ለጥበብ፡ሕያው፡ወላዴ፡ሕይወት ፤ ወእምሔውቱ፡ ለነገረ፡ኵሎን፡በሓውርት ። ጽዕዳዌ፡ሥዕርታ፡ክርስቶስ፡ቅቡዐ፡መንፈስ፡ከመ፡ ፀምረ፡በግዕ፡ጌደዎን፡ወከመ፡ሚላተ፡ፍሑስ ፤ ወቂሐተ፡ገጻ፡ልሁብ፡መንፈሰ፡ ጸጋሁ፡ለአብ፡መስተፍሥሔ፡ልብ ። ድምድማሃ፡ድሉል፡በመሥዕርተ፡ብርዕ ፥ ወሕ ብረ፡ቀለማ፡ጸሊም፡ከመ፡ሕብረ፡ቋዕ ፤ ወቀይሕ፡ከመ፡ደመ፡በግዕ ። በእንተ፡ ዝ፡ትልሒ፡እምፀሓይ፡ወእምኵሉ፡ንብረተ፡ከዋክብት ። እንዘ፡ምስለ፡ብርሃን፡ ትትቃወም፡ትትረከብ፡ከመ፡ቀዳማዊት ፤ ወእንዘ፡በርሥእ፡ሀለወት፡ኵሎ፡ትሔ ድስ ፤ ወለትውልደ፡ትውልድ፡ውስተ፡ነፍስ፡ጻድቃን፡ትትፋለስ ።

፵፫ ፤ ይእቲ፡ትጌይስ፡እምዕንቍ፡ክቡር ፤ ወኵሉ፡ክብር፡ኢመጠና ። ላቲ፡ ምክር፡ወዕዘዝ ፤ ወላቲ፡ጽንዕ፡ወአእምሮ ። ባቲ፡ነገሥት፡ይነግሡ ፤ ወባቲ፡ኀያላን፡ ይጽሕፉ፡ጽድቀ ። ባቲ፡ዐቢያን፡ይከብሩ ፤ ወባቲ፡መኳንንት፡ይእኀዙ፡ምድረ ። እለ፡ያፈቅርዋ፡ታፈቅር ፥ ወእለ፡የዐቅብዋ፡ተዐቅብ ፤ ወእለ፡የኀሥዋ፡ላቲ፡ይረ ክቡ፡ሞገሰ ። ውስተ፡ፍናወ፡ጽድቅ፡ታንሶሱ ፤ ወውስተ፡አሠረ፡ጽድቅ፡ትትመ ያየጥ፡ከመ፡ተሀበሙ፡ለእለ፡የአምርዋ፡ጥሪተ፡ወመዛግብቲሆሙ፡ከመ፡ትምላእ፡ ተድላ ። ዘኵሎ፡የአምር፡ውእቱ፡የአምራ ፤ ወዘኵሎ፡ይመልክ፡ውእቱ፡አሠነየ፡

ፍኖታ ፡፡ ውእቱ ፡ ወሀቦ ፡ ለሄኖስ ፡ ቀኖልዔሁ ፡ ወለቃይናን ፡ ቅዱሱ ፡፡ ወእምዝ ፡ አስተርአየት ፡ ዲበ ፡ ምድር ፤ ወአንሶሰወት ፡ ውስተ ፡ ዕጓለ ፡ መሕያው ፡፡ ናሁ ፡ ሐነጸት ፡ ላቲ ፡ ቤተ ፤ ወአቀመት ፡ ሰብዐተ ፡ አዕማደ ፡፡ ዘብሐት ፡ ዘዚአሃ ፡ ጥብሐ ፥ ወቶስሐት ፡ ውስተ ፡ ስያሓ ፡ ዘዚአሃ ፡ ወይነ ፤ ወአስተዳለወት ፡ ዘዚአሃ ፡ ማእደ ፡፡ ወፈነወት ፡ ዘዚአሃ ፡ አግብርተ ፡ በነዋኅ ፡ ሰብከት ፡ እንዘ ፡ ትብል ፡ ዘአብድ ፡ ውእቱ ፡ ይትገሐሥ ፡ ኀቤየ ፤ ወለእለሂ ፡ የሐጽሙ ፡ አእምሮ ፡ ትጼውዕ ፡ እንዘ ፡ ትብል ፥ ንዑ ፡ ብልዑ ፡ ኅብዝትየ ፡ ወስተዩ ፡ ወይንየ ፤ ወኅድግዋ ፡ ለእበድ ፡ ወሕየዉ ፡፡ ፊደልሰ ፡ ውእቱ ፡ እግዚአብሔር ፡ ዘለክአ ፡ ወእደ ፡ መንፈሱ ፡ ቅዱስ ፡ ዘአስተናበሮ ፡ ወሠርዖ ፥ ዲበ ፡ ዕፀ ፡ መስቀል ፡ ይኩን ፡ ስፉሐ ፡ ሰሌዳ ፡ ተሰብአ ፥ ወምስለ ፡ ኃጥአን ፡ ይትኈለቍ ፡ በሱባዔ ፡ ኅለት ፡ ተኰርዖ ፥ ኢየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ አልፋ ፡ ወዖ ፤ በበ ፡ ስብዕ ፡ ስብዐ ፡ እንበለ ፡ አጽርዖ ፡ እስመ ፡ ኵሉ ፡ ትውልድ ፡ ያስተበፅዖ ፥ በአሐዱ ፡ ቃለ ፡ አውሥአ ፡ እንዘ ፡ ይብል ፡ እግዚእ ፡ እግዚእ ፡፡ ሎቱ ፡ ስብሐት ፡ ወአኰቴት ፡ ዕበይ ፡ ወበርከት ፥ ውዳሴ ፡ ወማሕሌት ፤ ክብር ፡ ወብዕል ፡ ዕዘዝ ፡ ወኀይል ፡ ለልዑል ፡ ወሃቤ ፡ ፊደል ፤ ይእዜኒ ፡ ወዘልፈኒ ፡ ወለዓለመ ፡ ዓለም ፤ አሜን ፡፡ ወለእለሂ ፡ ነሥእዋ ፡ እምኔሁ ፡ በአሚን ፡ ከመ ፡ ጽላተ ፡ ሕግ ፡ ወኪዳን ፡ ወከመ ፡ ቅዱስ ፡ ቍርባን ፥ ለርእሰ ፡ ነቢያት ፡ ሄኖስ ፡ ወለበኵረ ፡ ነገሥት ፡ ቃይናን ፤ እስመ ፡ ከመ ፡ ሙሴ ፡ ወአሮን ፡ ክቡዳን ፡ ክልኤ ፡ አቅርንት ፡ ወአምርሕተ ፡ ሠናይ ፡ ፍኖት ፡ ለዕዉራን ፡ ልብ ፡ ሰብአ ፡ ትካት ፡፡ ፍኖትሰ ፡ ፊደል ፡ ፅንስተ ፡ ወንጌል ፥ ወስፍሕተ ፡ ማሕፀን ፡ ትንቢት ፡ ለወሊደ ፡ ተስፋ ፡ ሥግው ፡ እምኍልቄ ፡ ዕሥራ ፡ ወክልኤቱ ፡ ዘመደ ፡ ፍጥረት ፡ አበው ፥ ወእምዘርዐ ፡ ያዕቆብ ፡ ሰዋስው ፡፡

## ዐጭርና ፡ ቍርጭኝ ፡ ሰዋስው ፡

የመምህራን ፡ ዐይን ፡ ያዕቆብ ፡ እንደ ፡ ረኸሙ ፡ አጥርቶና ፡ ቀምሎ ፡
ያላየው ፥ ቀርበም ፡ እንደ ፡ ሐኪም ፡ ያልዳሰሰውና ፡ ያልፈወሰው ፡፡

ሰዋስው ፡ ማለት ፡ ዘይቤው ፡ መሰላል ፡ ማለት ፡ ነው ፤ እሙን ፡ ትርጓሜው ፡ ግን ፡ የግእዝ ፡ ቋንቋ ፡ ዐዋጅ ፥ ያሰከኩና ፡ ያጣጣፉ ፡ ያነጋገሩ ፡ ፈርጅ ፥ የንባቡ ፡ ኹሉ ፡ እጅና ፡ ፍንጅ ፥ አስተሳሰሩና ፡ አፈታቱ ፡ ተለይቶ ፡ የሚታወቅበት ፡ የትምርት ፡ ደንብ ፡ ፍርድና ፡ አገባብ ፡ ማለት ፡ ነው ፤ ፍትሐ ፡ ነገሥት ፡ እንደ ፡ ማለት ፡ ኹሉ ፡፡

አዝመራ ፡ ታጭዶ ፡ ሲሰበሰብ ፡ ብዙው ፡ አገዳ ፡ ፩ ፡ እስር ፡ ነዶ ፥ ብዙው ፡ ነዶ ፡ ፩ ፡ ሙሉ ፡ ዕቅፍ ፥ ብዙው ፡ ዕቅፍ ፡ ፩ ፡ ጕቻ ፥ ብዙው ፡ ጕቻ ፡ ፩ ፡ ታላቅ ፡ ክምር ፡ እንዲኾን ፤ የሰዋስውም ፡ ክፍል ፡ እንዲህ ፡ ነው ፤ ምዕራፍ ፡ በታላቅ ፡ ክምር ፡ ይመሰላል ፡፡ ብዙው ፡ ብትን ፡ ቃል ፡ እንደ ፡ ሥነ ፡ ፍጥረት ፡ በየወገኑና ፡ በያይነቱ ፡ ሲሰበሰብና ፡ ሲለቀም ፡ ነዶውና ፡ ዕቅፉ ፡ ጕቻው ፡ በ፫ ፡ ዐይነት ፡ ቍጥር ፡ ተቈጥሯል ፤ ብትኑ ፡ ቃል ፡ በነዶው ፡ ቍጥር ፥ ነዶው ፡ ቃል ፡ በዕርከን ፥ ዕርከንም ፡ በዐቢይ ፡ ክፍል ፡ ተጠቅልሎ ፡ ፯ ፡ ብቻ ፡ ኹኗል ፡፡ በያንዳንዱ ፡ ክፍል ፡ ውስጥ ፡ የሚገኝ ፡ አርእስተ ፡ ቃል ፡ ንኡስ ፡

ክፍል ፡ እንደ ፡ መኾኑ ፡ ዕርከን ፡ ተብሏል ፤ ፩ ፡ ክፍል ፡ ትምርት ፡ ማለት ፡ ነው ፤ ፩ ፡ ሙሉ ፡ ዕቅፍ ፡ እንደ ፡ ማለት ። ከ፯ቱ ፡ ደግሞ ፡ ፬ቱና ፡ ፫ቱ ፡ አንዳንድ ፡ ወገን ፡ ኹነው ፡ በ፪ ፡ ምዕራፍ ፡ ይከፈላሉ ፤ ክፍላቸውና ፡ ስማቸውም ፡ ይህ ፡ ነው ።

## የሰዋስው ፡ ክፍሎች ፡ ስምና ፡ ተራ ።

### መዠመሪያ ፡ ምዕራፍ ፡ በላ፬ ፡ ክፍል ።

፩ኛ ፡ ክፍል ፡ ጸዋትወ ፡ ቅምር ፡ ባለብዙ ፡ ሕብር ።
፪ኛ ፡ ክፍል ፡ ጸዋትወ ፡ ርባ ፡ የሰዋስው ፡ ሆድና ፡ ዠርባ ።
፫ኛ ፡ ክፍል ፡ ጸዋትወ ፡ ጥሬ ፡ የርባታ ፡ ቅንጣትና ፡ ፍሬ ።
፬ኛ ፡ ክፍል ፡ ጸዋትወ ፡ ቅጽል ፡ ባለቤት ፡ አከል ።

### ፪ኛ ፡ ምዕራፍ ፡ ባለ፫ ፡ ክፍል ።

፭ኛ ፡ ክፍል ፡ ጸዋትወ ፡ ንባብ ፡ ሳቢና ፡ ተሳቢ ፡ ተናባቢ ።
፮ኛ ፡ ክፍል ፡ ጸዋትወ ፡ አገባብ ፡ የዘርና ፡ የነባር ፡ ሕንባብ ።
፯ኛ ፡ ክፍል ፡ ጸዋትወ ፡ ቅኔ ፡ የሠምና ፡ የወርቅ ፡ ዥርጓኔ ።

### ፫ኛ ፡ ምዕራፍ ፡ ጸዋትወ ፡ ግስ ፡

### ባለ፳፮ ፡ ክፍልና ፡ ራስ ፡ ከአ ፡ እስከ ፡ ፐ ፡ ድረስ ።

ጸዋትውም ፡ ማለት ፡ ጓዝና ፡ ወገን ፡ ቤት ፡ ሰብ ፡ ማለት ፡ ነው ፤ ጸዋትወ ፡ ቀዳሴ ፡ እንዲሉ ። ያጭሩ ፡ ሰዋስው ፡ ልክና ፡ መልክ ፥ ወርዱና ፡ ቁመቱ ፡ አርእስቱ ፡ ይህ ፡ ነው ። የቀረውን ፡ በየነዶውና ፡ በየቅፉ ፡ በየጕቾው ፡ ቃል ፡ ተመልከት ፤ አንዱ ፡ ክፍል ፡ ላንዱ ፡ መቅድምና ፡ አርእስት ፡ እየኾነ ፡ ሰዋስውነቱን ፡ ስንስለት ፡ አድርጎ ፡ ያሳይ ኻል ። ከዚህም ፡ ሰዋስው ፡ የቀረውን ፡ ረዥም ፡ ትምርት ፡ ጎሊናችን ፡ ዐጥሮ ፡ ስላልደረሰበት ፡ ለኋላ ፡ ልጆች ፡ ትተነዋል ፡ (ማቴ፯ ፡ ፯ና ፡ ፰) ።

## መዠመሪያ ፡ ምዕራፍ ፡ ባለ፬ ፡ ክፍል ፡ ጎረ ፡ ቤት ፡ ወንጌል ።

### ፩ኛ ፡ ክፍል ።

### የሰዋስው ፡ ዐዋጅ ፡ ርባ ፡ ቅምር ።

የፍጥረት ፡ ኹሉ ፡ ዐይነት ፡ ፪ ፡ ፪ ፡ ብቻ ፡ እንደ ፡ ኾነ ፡ ያውም ፡ ወንድና ፡ ሴት ፡ ተባትና ፡ እንስት ፡ እንዲባል ፤ ሰዋስው ፡ ተብሎ ፡ የሚጠራ ፡ የቋንቋም ፡ ዐይነት ፡ ፪ ፡ ነው ፤ ዘርና ፡ ነባር ፥ ወይም ፡ ስምና ፡ ግብር ። ወንድና ፡ ተባት ፡ ሴትና ፡ እንስት ፡ አንዳንድ ፡ ወገን ፡ ኹነው ፡ በ፪ነት ፡ እንዲታዩ ፥ እነዚህም ፡ ፬ቱ ፡ ስሞች ፡ ዘርና ፡ ግብር ፡ ነባርና ፡ ስም ፡ አንዳንድ ፡ ወገን ፡ ናቸው ። ፪ኛም ፡ የመሰላል ፡ ዕርከን ፡ ብዙ ፡ ሲኾን ፡ በ፪ ፡ አዕማድ ፡ እንዲወሰን ፤ የቋንቋም ፡ ትምርት ፡ ስሙና ፡ ክፍሉ ፥ ስልቱና ፡ ባህሉ ፡ ብዙ ፡ ሲኾን ፡ ዐይነቱና ፡ ሕብሩ ፡ አርእስተ ፡ ነገሩ ፡ በነዚህ ፡ በ፪ቱ ፡ ብቻ ፡ ተወስኗል ፤ ከስ ምና ፡ ከግብር ፡ አይወጣም ። ሲዘረዘሩ ፡ ግን ፡ አንቀጽና ፡ ርባታ ፥ ዝርዝር ፥ ቅጽልና ፡

ጥሬ ፣ አገባብ ፣ ሠምና ፡ ወርቅ ፣ ሙሻዘር ፣ ሠረዝ ፣ አንጻር ፡ ተብለው ፡ ፲ ፡ ይኾናሉ ፤ ዝርዝር ፡ ከርባታ ፣ አገባብ ፡ ከጥሬ ፡ ሲደረቡ ፡ ግን ፡ ፰ ፡ ብቻ ፡ ኹነው ፡ ይቀራሉ ። የሰዋስውን ፡ ክፍል ፡ ዝቅ ፡ ብለው ፡ ፫ና ፡ ፬ ፡ ፯ ፣ ከፍ ፡ ብለው ፡ ፲፪ና ፡ ፲፰ ፡ የሚሉ ፡ አሉ ።

## መዠመሪያ ፡ ዕርከን ፡ ወይም ፡ ቀዳማይ ።

### የዘርና ፡ የነበር ፡ ጠባይ ።

### ዘር ።

፩ ፤ ነጠላ ፡ ግስን ፡ ከነርባው ፡ የሚያስገኝ ፣ ጥሬ ፡ ዘርን ፡ ኹሉ ፡ የሚወልድ ፡ በሊዕ ፡ ሰትይ ፡ ጸጊብ ፡ ሰኪር ፡ መዊት ፡ ሐዪው ፡ እያለ ፡ በሦስት ፡ ፊደል ፡ በቅሎ ፡ የሚኼድ ፣ ይህን ፡ የመሰለ ፡ ኀጠተ ፡ ቃል ፣ አባት ፡ ዘር ፡ ይባላል ፤ አባትነቱም ፡ አዳምን ፡ ይመስላል ። አባት ፡ ዘር ፣ ርሱ ፡ ራሱ ፡ እንደ ፡ ሥር ፡ ኹኖ ፡ ሌላውን ፡ ፍሬ ፡ ቃል ፡ ቢያስገኝ ፡ እንጂ ፡ ለርሱ ፡ አስገኝና ፡ አባት ፡ የለውም ። ፪ኛም ፡ ሥረ ፡ ነገር ፡ መሠረተ ፡ ቃል ፡ ስለ ፡ ኾነ ፣ አርእስት ፡ ይባላል ። ፫ኛም ፡ ዐጕል ፡ አንቀጽ ፡ ስለ ፡ ኾነ ፣ ንኡስ ፡ ይባላል ። ስሞቹ ፡ እንደ ፡ ፊደሎቹ ፡ ፫ ፡ ናቸው ፤ አባት ፡ ዘር ፣ አርእስት ፣ ንኡስ ፡ አንቀጽ ።

፪ ፤ ዘር ፡ በቋንቋ ፡ ኹሉ ፡ የግስ ፡ ጥንት ፡ የርባ ፡ መሠረት ፡ ስለ ፡ ኾነ ፣ ከአናቅጽ ፡ በፊት ፡ ይጣፋል ፤ ከርባታ ፡ በፊት ፡ ይነገራል ። ጣፊም ፡ አንባቢም ፡ ወንጌል ፡ ዘዮሐንስ ፡ ሳይል ፡ ቀዳሚሁ ፡ ቃል ፡ እንዳይል ፤ አርእስትን ፡ በጥፈትም ፡ በመነገርም ፡ ንባብ ፡ እንዳይቀድመው ፣ ዘርንም ፡ አንቀጽና ፡ ጥሬ ፡ አይቀድሙትም ። የዚህ ፡ መጽሐፈ ፡ ግስ ፡ ቀዋሚ ፡ ግብሩ ፡ ደገኛ ፡ ነገሩ ፡ ይህ ፡ ነው ፤ እናት ፡ ዘር ፡ ሳትቀበል ፡ እንዳት ፀንስ ፡ ርሱም ፡ ዘር ፡ ሳያስቀድም ፡ አንቀጽ ፡ አይጥፍም ። ምንጩን ፡ አሳይቶ ፡ ውሃውን ፣ ዛፉን ፡ አሳይቶ ፡ ፍሬውን ፡ እንደ ፡ መስጠት ፡ ኹሉ ፣ ዘሩን ፡ በፊት ፡ አንቀጹን ፡ በኋላ ፡ ያመጣዋል ፤ ባፊ ፡ ታሪክም ፡ የቀድሞ ፡ መምህራን ፡ ዘር ፡ ሳያስቀድሙ ፡ አይገሱም ፡ ነበር ፡ ይባላል ።

፫ ፤ ዘር ፡ መባሉም ፡ በምሳሌ ፡ ነው ፤ ዘር ፡ በዘሩት ፡ ጊዜ ፡ አንዱ ፡ ቅንጣት ፡ ብዙ ፡ ቅንጣቶች ፡ እንዲያፈራ ፣ ንኡስ ፡ አንቀጽም ፡ ባረቡትና ፡ በገሰሱት ፡ ጊዜ ፡ አንዱ ፡ ቃል ፡ ብዙ ፡ ቃላት ፡ ያፈራልና ፤ ስለዚህ ፡ ዘር ፡ ተባለ ፡ (ዮሐ ፲፪ ፡ ፳፬) ። በዕብራይስጥም ፡ ሸሬሽ ፡ ምቆር ፡ ይባላል ፤ ሥርው ፡ ነቅዕ ፡ ማለት ፡ ነው ፤ ዘር ፡ ከማለት ፡ ጋራ ፡ ይሰማማል ። አማናዊው ፡ የባሕርይ ፡ ስሙ ፡ ግን ፡ ግብር ፡ ይባላል ፤ ግብርነቱም ፡ ሠራተኛው ፡ ያልታወቀለት ፣ ለሠራተኛ ፡ ያልተሰጠ ፣ ገና ፡ ወደ ፡ ፊት ፡ የሚሰጥ ፣ በኋላፊና ፡ በትንቢት ፡ መካከል ፡ የቆመ ፡ ዐጓጕል ፡ ማእከላዊ ፡ ነው ። ዳግመኛም ፡ ካባት ፡ ዘር ፡ የሚገኝ ፡ ጥሬ ፡ ዘር ፣ ስምና ፡ መስም ፣ ርሱም ፡ እንዳባቱ ፡ ሲገሰስ ፣ ዘርነቱ ፡ ወዳንቀጽነት ፡ ተለውጦ ፡ ጥሬ ፡ ግስ ፡ ይኾናል ። ካባቱ ፣ አባት ፡ የመሰለ ፡ የ፫ ፡ ፊደል ፡ ግስ ፡ እንዲገኝ ፣ ከጥሬውም ፡ ጥሬ ፡ የመሰለ ፡ ይገኛል ፤ አገኛኘቱንም ፡ በግስ ፡ አርእስት ፡ ውስጥ ፡ ባ፵፬ ፡ ቍጥር ፡ ተመልከት ።

፬ ፤ በ፫ ፡ ፊደል ፡ እግር ፡ የቆሙ ፡ ዘርና ፡ ግስ ፡ የሚነሡባቸው ፡ ፊደላት ፡ ወይም ፡ ቀለማት ፡ ፫ ፡ ናቸው ፤ ባላገባቦች ፡ መራኁት ፡ ይሏቸዋል ፤ መክፈቾች ፡ ማለት ፡ ነው ። እሊሁም ፡ ግእዝ ፡ ራብዕ ፡ ኃምስ ፡ ሳድስ ፡ ሳብዕ ፡ ናቸው ፤ ዘርና ፡ ግስ ፡ በነዚህ ፡ ብቻ ፡ ቢነሡ ፡ እንጂ ፡ በካዕብ ፡ በሣልስ ፡ አይነሡም ። የዘርና ፡ የግስ ፡ አነሣሥ ፥ አካኼድና ፡ አገሣገሥ ፡ እንዴት ፡ እንደ ፡ ኾነ ፡ በግስ ፡ አርእስት ፡ ተመልከት ። የዘር ፡ መድረሻ ፡ ወይም ፡ መጨረሻ ፡ ፪ ፡ ናቸው ፤ ሳድስና ፡ ሳብዕ ፥ ይህም ፡ ነዋም ፡ ነቂህ ፥ ሰብሖ ፡ ዘምሮ ፡ እያለ ፡ በነዚህ ፡ ብቻ ፡ መድረሱን ፡ ያሳያል ። ግስ ፡ ግን ፡ ምንም ፡ እንደ ፡ ዘር ፡ በላ፫ ፡ መነሻ ፡ ቢኾን ፥ ባላንድ ፡ መድረሻ ፡ ነውና ፤ ቀደሰ ፡ ባረከ ፡ ሤመ ፡ ጥሕረ ፡ ሖረ ፡ እያለ ፡ በግእዝ ፡ ብቻ ፡ ይጨርሳል ፤ ይኸውም ፡ የሩቅ ፡ ወንድ ፡ አንቀጽ ፡ ስለ ፡ ኾነ ፡ ነው ፤ ግእዝ ፡ የሩቅ ፡ ዝርዝር ፡ ነውና ። ሲረባና ፡ ሲዘረዘር ፡ ግን ፡ ከኃምስ ፡ በቀር ፡ በሌሎቹ ፡ ኹሉ ፡ ይጨርሳል ።

፭ ፤ አባት ፡ ዘር ፡ ከ፫ቱ ፡ ልጆቹ ፡ (ቀዳማይ ፡ ካልኣይ ፡ ሣልሳይ) ፡ ከዐበይት ፡ አና ቅጽ ፡ በኋላ ፡ ፬ኛ ፡ ንኡስ ፡ አንቀጽ ፡ ኹኖ ፥ ቀቲል ፡ ቀቲሎት ፥ ቀድሶ ፡ ቀድሶት ፥ ባርኮ ፡ ባርኮት ፥ ብሂል ፡ ብሂሎት ፡ እያለ ፡ በደጊመ ፡ ቃል ፡ መነገሩና ፡ ምእላድ ፡ ፊ ደል ፡ ትን ፡ እየጨመረ ፡ መኼዱ ፥ ለመዘርዘርና ፡ ለማዛረፍ ፡ ለማብዛትና ፡ ለማብለጥ ፡ ንባብ ፡ ለማስጌጥ ፡ ነው ። በዝርዝር ፡ ጊዜ ፥ ቀቲልሁ ፡ ቀቲሎቱ ፥ ቀድሶሁ ፡ ቱ ፥ ባር ኮሁ ፡ ቱ ፥ ብሂልሁ ፡ ብሂሎቱ ፡ ቢል ፡ እንጂ ፥ ቀቲሉ ፡ ቀድሱ ፡ ባርኩ ፡ ብሂሉ ፡ ብሎ ፡ በዘመድ ፡ አይዘረዝርም ፤ ይህ ፡ በለ ፡ ሲያዛርፍ ፡ ነው ። በዘና ፡ በግእዝ ፡ ሲያዛርፍ ፡ ግን ፡ እንዳለ ፡ ይገባል ፤ ይህም ፡ ቀቲል ፡ ዘዳዊት ፥ ዘዳዊት ፡ ቀቲሎት ፥ ቀቲለ ፡ ዳዊት ፡ ቀቲሎተ ፡ ዳዊት ፡ ጎልያድሀ ፡ እያለ ፡ ሌላውን ፡ ኹሉ ፡ ያሳያል ። ባላገባቦችም ፡ ለብ ሂል ፡ ለ ፡ የለው ፥ ለብሂሎት ፡ ዘ ፡ የለው ፡ ብለው ፡ ያውጃሉ ፤ ይህም ፡ ብሂሉ ፡ ለዳ ዊት ፥ ብሂሎት ፡ ዘዳዊት ፡ አለማለቱን ፡ ያሳያል ፤ በብሂል ፡ ኹሉን ፡ መናገር ፡ ነው ። ሲያበዛና ፡ ሲዘረዝርም ፥ ሀልዎታት ፡ ሀልዎታቱ ፡ ቲሁ ፡ ያሰኛል ።

፮ ፤ ዘር ፡ ጥንቱን ፡ ሲፈጠር ፡ ሲታነጽ ፡ ሲቀረጽ ፡ ከ፫ ፡ ፊደል ፡ ባሕርይ ፡ መገኘ ቱና ፡ በ፫ ፡ ፊደል ፡ ብቻ ፡ መመሥረቱ ፥ ወደ ፡ ፪ና ፡ ወዳ፬ ፡ አለመውረድ ፡ አለመው ጣቱ ፡ ስለ ፡ ምን ፡ ነው ፡ ብትል ፤ እግዜር ፡ በ፮ኛ ፡ ቀን ፡ ንግበር ፡ ሰብአ ፡ በአርአያነ ፡ ወበአምሳሊነ ፡ ብሎ ፡ አዳምን ፡ ሲፈጥር ፡ ቋንቋውንም ፡ አርአያና ፡ አምሳል ፡ አድርጎታ ልና ፥ ስለዚህ ፡ ነው ። ይኸውም ፡ አነ ፡ ውእቱ ፡ አልፋ ፡ ወዖ ፡ ወይም ፡ አሌፍ ፡ ወታው ፡ በለው ፡ ይታወቃል ፡ (ራእ፳፪ ፡ ፲፫) ። ኋላም ፡ በባቢሎን ፡ ንዑ ፡ ንረድ ፡ ወንክዐው ፡ ሀየ ፡ ነገሮሙ ፡ ከመ ፡ ኢይስማዕ ፡ ብእሲ ፡ ከንፈረ ፡ ቢጹ ፡ ብሎ ፡ የልጆቹን ፡ ቋንቋ ፡ ሲለያይ ፡ ይህ ፡ የአዳም ፡ ቋንቋ ፡ በሴም ፡ ብቻ ፡ ቀርቷል ፡ (ዘፍ፲፩ ፡ ፳፯ ። ፲፩ ፡ ፯) ። በሴም ፡ ዘር ፡ የቀረ ፡ ቋንቋው ፡ ብቻ ፡ አይዶለም ፤ ተስፋውና ፡ ሃይማኖቱም ፡ እንጂ ። ስለዚህ ፡ ነገር ፡ የሴም ፡ ቋንቋ ፡ ኹሉ ፡ ዘሩ ፡ ሥረ ፡ ነገሩ ፥ ዋሕደ ፡ ቃል ፡ ሥሉስ ፡ ፊደል ፡ እየ ኾነ ፡ በ፫ ፡ ፊደላት ፡ ተወስኗል ፤ ከ፫ ፡ ቅንጣት ፡ ፊደል ፡ አይወጣም ፤ ወደ ፡ ፪ ፡ ፊደል ፡ አይወርድም ። ከዚህ ፡ የተነሣ ፡ ፊደሉ ፡ አርአያ ፡ አካላት ፥ ቃሉ ፡ አምሳለ ፡ መለኮት ፡ ተብሏል ።

፯ ፤ ግእዝም ፡ ከላይ ፡ ከአዳም ፡ የነቃ ፡ ከታችም ፡ ከኖኅ ፡ የፈለቀ ፡ ሴማዊና ፡ አዳማዊ ፡ ቋንቋ ፡ ስለ ፡ ኾነ ፥ ዘሩን ፡ በኖኅ ፡ ልጆች ፡ አምሳል ፡ ሲሰፍርና ፡ ሲቈጥር ፡ ከ፫ ፡ ፊደላት ፡ አያበልጥም ፤ አያሳንስም ። ቀቲል ፡ ገቢር ፥ ቀዊም ፡ ሐዊር ፥ ሣርሮ ፡ ሐድሶ ፥ ሐውጾ ፡ ገሥጾ ፡ እያለ ፡ እንደ ፡ ወንድሞቹ ፡ እንዳረብና ፡ እንደ ፡ ሱርስት ፡ እንደ ፡ ዕብራይስጥ ፡ በ፫ ፡ ፊደላት ፡ ይኼዳል ።

«ዋዜማ ፡ ዘሰሚቴ ፡ ሠርጸ ፡ ድንግል ።

አካልከ ፡ ነጋዴ ፡ ሕግ ፡
ለአጥርዮ ፡ ሕማም ፡ ሲሳዩ ፡ ውስተ ፡ ቀራንዮ ፡ ወረደ ፤
ጊዮርጊስ ፡ መብረቀ ፡ ስባሔ ፡ ዘትጸውር ፡ ነደ ።
ወበውስተ ፡ ዓለም ፡ ይዝራዕ ፡ ገቢረ ፡ ተአምር ፡ ዘመደ ፡
ከማድከ ፡ ኖኅ ፡ ሠለስተ ፡ ወለደ ፤
ወበእሉ ፡ ኢወሰከ ፡ ባዕደ» ።

፰ ፤ መጻሕፍት ፡ ከጽርእ ፡ ወደ ፡ ግእዝ ፡ ሲመለሱ ፡ ያን ፡ ጊዜ ፡ የገባ ፡ የሰባ ፡ የኖባ ፥ የጽርእ ፡ የቅብጥ ፡ ቃል ፡ የኋላ ፡ ቅጥል ፡ ካልኾነ ፡ በቀር ፥ ከለዳዊና ፡ ዮቅጣናዊ ፡ ሕምያራዊ ፡ ለሚባለው ፡ ለጥንታዊው ፡ ግእዝ ፡ ከዕብራይስጥ ፡ ልዩነት ፡ የለውም ። ኋላ ፡ ግን ፡ በታደሰ ፡ ጊዜ ፡ ብዙ ፡ ባዕድ ፡ ቋንቋ ፡ ገብቶበታል ፤ ባዕድ ፡ የተባለም ፡ የካ ምና ፡ የያፌት ፡ ቋንቋ ፡ ነው ። የሴም ፡ ቋንቋ ፡ ግን ፡ ምንም ፡ ከ፫ ፡ ከ፬ ፡ ቢከፈል ፡ ነቍ ሥር ፡ መሠረቱ ፡ እንደ ፡ ምንጭ ፡ እንደ ፡ ዛፍ ፡ እንደ ፡ ሕንጻ ፡ አንድ ፡ ስለ ፡ ኾነ ፥ ርስ ፡ በርሱ ፡ ይሰማማልና ፤ አንዱ ፡ ላንዱ ፡ ዘመድ ፡ እንጂ ፥ ባዕድ ፡ አይባልም ። የጐደለው ንም ፡ አንዱ ፡ ካንዱ ፡ ቢወስድ ፡ ብድር ፡ አይኾንም ፥ ገንዘቡ ፡ ነውና ፤ የቅርብ ፡ ዘመድ ፡ ወንድም ፡ እኅት ፡ ወዳጅ ፡ ጎረ ፡ ቤት ፡ እያለ ፡ ከባዕድ ፡ መበደር ፡ አይገባም ፥ ታላቅ ፡ ስንፍና ፡ ነው ፤ ሳይቸገሩም ፡ መበደር ፡ ዝሙት ፡ ይባላል ።

ነባር ።

፱ ፤ ዘርነት ፡ የሌለው ፥ ከዘር ፡ ከአንቀጽ ፡ የማይገኝ ፡ የቋንቋ ፡ ቤት ፡ ሰብ ፡ እየ ኾነ ፡ በውጥንቅጥነት ፡ የሚገኝ ፡ ጥሬ ፡ ቃል ፡ ኹሉ ፡ ነባር ፡ ይባላል ፤ ትርጓሜውም ፡ የማይፈልስ ፡ የማይናወጥ ፡ የማይጠፋ ፡ የማይለወጥ ፡ ስም ፡ ማለት ፡ ነው ። ከነባር ፡ የሚገኝ ፡ ስም ፡ ብቻ ፡ አይዶለም ፥ አንቀጽና ፡ አገባብም ፡ እንጂ ፤ ከዘሩ ፡ ዘር ፡ የመሰለ ፡ አንቀጽ ፡ እንዲገኝ ፥ ከነባሩም ፡ ነባር ፡ የመሰለ ፡ ይገኛል ። ካባት ፡ ዘር ፡ የሚገኝ ፡ ጥሬ ፡ ዘር ፥ አንቀጽ ፡ እየኾነ ፡ እንዲገሰስ ፡ ግስነቱም ፡ ዲቃላ ፡ እንዲባል ፥ ከነባርም ፡ ጥሬ ፥ አንቀጽ ፡ እየኾነ ፡ የሚገሰስ ፡ ብዙ ፡ ስም ፡ አለ ፤ ነባር ፡ ስም ፡ ኹሉ ፡ እንደ ፡ ዘር ፡ ኹኖ ፡ ሊረባ ፡ ሊገሰስ ፡ አንቀጽ ፡ ሊወጣለት ፡ ይቻላል ። ይህም ፡ ሰብእ ፡ ብሎ ፡ ተሰብአ ፥ ወይን ፡ ወየነ ፡ አውየነ ፥ እብን ፡ አበነ ፡ አእበነ ፥ ክርስቲያን ፡ ክረስተነ ፥ ደብተራ ፡ ደብ ተረ ፡ ተደብተረ ፡ እያለ ፡ ሌላውን ፡ ኹሉ ፡ ያሰያል ። ከተጸውዖ ፡ ስም ፡ በቀር ፡ የማይበ ዛና ፡ የማይረባ ፡ የማይገሰስ ፡ ስም ፡ የለም ፤ ከነባር ፡ ስም ፡ የሚወጣ ፡ አንቀጽ ፡ ነባር ፡ ግስ ፡ ይባላል ።

፲ ፤ ነባር ፡ መባሉም ፡ ሥሩና ፡ ምንጩ ፡ ስላልታወቀ ፡ እንጂ ፥ ዘር ፡ የሌለው ፡ ኹኖ ፡ አይዶለም ፤ ልጅ ፡ አላባት ፡ አለናት ፡ እንዳይገኝ ፥ ነባርም ፡ አለዘር ፡ በቅሉ ፡ አይገኝም ። ጥሬ ፡ ዘር ፡ እንደ ፡ ሚስት ፡ ልጅ ፡ ነው ፤ ነባር ፡ ግን ፡ ከባት ፡ ከናቱ ፡ እንደ ሚጣልና ፡ ሌሎች ፡ አንሥተው ፡ እንደሚያሳድጉት ፥ ወይም ፡ እናቱ ፡ ታውቃ ፡ አባቱ ፡ እንደማይታወቅ ፡ ዲቃላ ፡ ነው ። ከዘር ፡ አንቀጽም ፡ እየተዴቀለ ፡ ስሙና ፡ ጠባዩ ፡ ተለውጦ ፡ ነባር ፡ አንቀጽ ፡ የሚባል ፡ አለ ፤ ሐሰወ ፡ ሐሰ ፥ ነዐወ ፡ ነዐ ፥ አበየ ፡ እንቢ ፤ የመሰለው ፡ ኹሉ ፤ የቀረውን ፡ በደቂቅ ፡ ርባታ ፡ ተመልከት ።

፲፩ ፤ ለጥሬ ፡ ለነባር ፡ እንደ ፡ ዘር ፡ እንደ ፡ ግስ ፡ የፊደል ፡ ውሳኔ ፡ የለውም ፤ ከግእዝ ፡ እስከ ፡ ሳብዕ ፡ ባሉት ፡ በ፯ቱ ፡ ኹሉ ፡ ተነሥቶ ፡ ከግእዝ ፡ በቀር ፡ በ፮ቱ ፡ ኹሉ ፡ ይጨርሳል ። ያገባብም ፡ ቃል ፡ አመ ፡ ሶበ ፡ ከመ ፡ ሌላውም ፡ ኹሉ ፡ መድረሻው ፡ ግእዝ ፡ መኾኑ ፡ ሲናበብ ፡ ነው ፡ እንጂ ፥ ሲያርፍና ፡ ሲወድቅ ፡ ሳድስ ፡ ነው ። ከዚህም ፡ አካኼድ ፡ የተነሣ ፡ ነባር ፡ ከዘርና ፡ ከግስ ፡ ተዛንቆ ፥ የፊደሉን ፡ ተራ ፡ ጠብቆ ፥ ተባብሮ ፡ ተጫፍሮ ፡ በንድነት ፡ ይጣፋል ፡ እንጂ ፤ ለብቻው ፡ የተለየ ፡ ቦታ ፡ የለውም ። ያለም ፡ ቋንቋ ፡ ኹሉ ፡ ሲጣፍ ፡ ሲነገር ፡ እንደዚህ ፡ ነው ፤ ነባርን ፡ ከዘር ፡ አይለየውም ። የፊደሉም ፡ ተራ ፡ ሥሩን ፡ መነሻውን ፡ እንጂ ፥ እንደ ፡ መልክና ፡ እንደ ፡ ቅኔ ፡ እንደ ፡ ሙሾና ፡ እንደ ፡ ዘፈን ፡ ግጥም ፡ ጫፉን ፡ መድረሻውን ፡ አይሻም ።   ባለቅኔዎች ፡ ግን ፡ ከቅኔያቸው ፡ እንዲስማማላቸው ፡ መነሻውን ፡ ትተው ፡ መድረሻውን ፡ ብቻ ፡ ይሻሉ ፤ ግሱንም ፡ ሎሐ ፡ ለብሐ ፡ ለስሐ ፡ እያሉ ፡ በቅኔያቸው ፡ መንገድ ፡ ስላስኬዱት ፤ የርባታው ፡ መንገድ ፡ የዘሩና ፡ የነባሩ ፡ አካኼድ ፡ የጥፈቱ ፡ ረገድ ፡ ተበላሽቶ ፡ ካለም ፡ ቋንቋ ፡ መንገድ ፡ ወጥቷል ። የሐ ፡ ግስ ፡ የሚባል ፡ በሐ ፡ የሚነሣ ፡ ነው ፡ እንጂ ፥ በሌላ ፡ ተነሥቶ ፡ በሐ ፡ የሚጨርስ ፡ አይዶለም ፤ የሌላውም ፡ ፊደል ፡ እንዲሁ ፡ ነው ። ዳግመኛም ፡ ፊደልና ፡ ግስ ፡ ፩ ፡ ወገን ፡ ነውና ፤ ፪ቱንም ፡ ያፋለሷቸው ፡ ሰባክያን ፡ ናቸው ፡ ይባላል ፥ አስቀድመን ፡ እንደ ፡ ተናገርን ፡ (መቅ ፡ ፲፰) ።

፲፪ ፤ የርባታውም ፡ መበላሸትና ፡ መሳሳት ፡ በዚህ ፡ ይታወቃል ፤ አመረ ፡ በመላላቱ ፡ የቀተለ ፡ ቤት ፡ ሲኾን ፤ አመረ ፡ (የአምር ፡ ይእምር ፤ አሚር ፡ አሚሮት) ፡ ዐወቀ ፡ በማለት ፡ ፈንታ ፤ አስደራጊውን ፡ አእመረን ፡ መደበኛ ፡ ያ፬ ፡ ፊደል ፡ ግስ ፡ አድርጎ ፤ አእመረ ፡ (የአምር ፡ ያእምር ፤ አእምሮ ፡ ሮት) ፡ አሳወቀ ፡ እንደ ፡ ማለት ፡ ኹሉ ፡ ዐወቀ ፡ እያሉ ፡ በደንገፀ ፡ ቤት ፡ መግሰስና ፡ ማርባት ፡ የስሕተት ፡ ስሕተት ፡ ነው ። አስደራጊውን ፡ መደበኛ ፡ ትንቢቱን ፡ ኀላፊ ፡ ስላሉት ፡ የአእመረና ፡ የይቤ ፡ ርባታ ፡ ከሥር ፡ እስከ ፡ ጫፍ ፡ ተበላሽቷልና ፤ ሌላውንም ፡ እንደነዚህ ፡ እየው ። አእኰተ ፡ አግመረ ፡ አድምዐ ፡ አጥብዐ ፡ አጥመቀ ፡ አልጸቀ ፡ አይድዐ ፡ አርመመ ፡ አዕረፈ ፡ አፍቀረ ፤ ተገበረ ፡ ተወከለ ፡ ተለዐለ ፡ ተሰፈወ ፡ ይህን ፡ የመሰለ ፡ ዐመል ፡ ያለበት ፡ ግሡ ፡ ኹሉ ፡ እንደ ፡ ይቤና ፡ እንደ ፡ አእመረ ፡ ያልታረመ ፡ ያልተጠነቀቀ ፡ ሕገ ፡ ወጥ ፡ ነው ።

፲፫ ፤ አንቀጽ ፡ የሌላቸው ፡ አገባቦችና ፡ የመጠሪያ ፡ ስሞች ፡ ፊደልና ፡ አኃዝም ፡ አንዳንድ ፡ ቅንጣት ፡ ዘሮች ፡ ስለ ፡ ኾኑ ፡ ቍጥራቸውና ፡ ክፍላቸው ፡ ከነባሮች ፡ ነው ። ዘርና ፡ ነባርን ፡ በጥፈት ፡ በትምርት ፡ ለመለየት ፡ በግእዝ ፡ ንባብ ፡ ውስጥ ፡ ያለ ፡ ቍጥ

ርን፡አሐድ፡ዱ፤ክልኤት፡ቱ፤ዐሥርት፡ቱ፡እያሉ፡ኹሉን፡በፊደል፡ብቻ፡እንጂ፡በአኃዝ፡ብቻ፡፩፡፪፡፲፡ብሎ፡ወይም፡አኃዝና፡ፊደል፡አቈራኝቶ፡፩ዱ፡፪ቱ፡፲ቱ፡ይልቁንም፡፳ኤል፡እያሉ፡መጣፍ፡አይገባም፤የንባቡና፡የትርጓሜው፡የምስጢሩ፡ጣዕም፡ይበላሻል ። በአኃዝ፡ሊጣፍ፡የሚገባው፡ምዕራፍና፡ክፍል፡በውስጡ፡ያለው፡ነዶ፡ቃል፡ያማርኛ፡ንባብ፡ነው፡እንጂ፤ለግእዝ፡ቋንቋ፡አይስማማውም ።

## ፪ኛ፡ዕርከን ።

## የግስ፡ዐመሎች ።

፲፩ ፤ ግስ፡ማለት፡የቋንቋ፡ጓዝ፡የዘርና፡የነባር፡እክት፡ወይም፡ዕቃ፡ግሴት፡ማለት፡ነው፤ሰማይ፡ከነግሱ፡ምድር፡ከነልብሱ፡እንዲሉ÷ከነጓዙ፡ሲሉ ። የሚያጠግበውና፡የሚያረካው፡እሙን፡ትርጓሜው፡ግን፡ተወራራሽና፡ተመላላሽ፡ቃል፡ማለት፡ነው ። ፩ዱ፡አንቀጽ፡እስከ፡፻፡ጥሬው፡እስከ፡፲፡መደብ፡መረባቱና፡መዘርዘሩ፡ያንዱ፡ለብዙ፡የወንዱ፡ለሴት፡የሩቁ፡ለቅርብ፡እየተሰጠ፡በመፋለስና፡በመዋረስ፡በመመላለስ፡ነውና ። በገሲስ፡ዘይቤም፡ሲፈቱት፡መደቦችና፡መደበኞች፡ኹነው፡የሚዳሰሱና፡የሚያዙ፡ዐሥሩን፡ሰራዊት፡ያሳያል፡(ቍ፶፯) ። ለግስ፡አከፋፈል፡ብዙ፡ስም፡አለው ። መዥመሪያ፡ትርጓሜና፡አፈታት፡እንደ፡ገጠመው፡ሲነገር፡ከተማ፡ግስ፤፪ኛ፡እንደ፡ተገኘ፡ሲነገር፡መንደር፡ግስ፤፫ኛ፡እንደ፡ፊደሉ፡ተራ፡በየወገኑና፡በየቤቱ፡በየሰራዊቱ፡ሲነገር፡ተራ፡ግስ፡ይባላል ። የቀረውም፡ኋላ፡በ፯ኛ፡ዕርከን፡ይመጣል ።

፲፪ ፤ ነጠላ፡ግስ፡ከ፪፡ፊደል፡አይወርድም፤ከ፬፡ፊደል፡አይወጣም፤ልማድና፡በዕድ፡ሲጨመር፡ግን፡፭ም፡፮ም፡፯ም፡ይኾናል፤ከ፯፡በላይ፡ግን፡አይወጣም፤ይህን፡ኋላ፡በቦታው፡እናመጣዋለን ። በግስ፡ያሉ፡ዐመሎች፡፫፡ናቸው፤አና፡ሀ÷ወና፡የ÷ደጊመ፡ቃል ። አና፡ሀ፡ስላንድ÷ወና፡የ፡ስላንድ፡ይቈጠራሉ፤ደጊመ፡ቃል፡ግን፡ለብቻው፡፩፡ነው፤እሊህ፡፫ቱ፡ዐመሎች፡ያሉበት፡ግስ፡ቤቱን፡ሳይለቅ፡ድምጥና፡መንገድ፡ይለውጣል ። ዐመሎችን፡ሕርመት፡ወይም፡ጸዋትው፡የሚሉ፡አሉ ።

### ከመላላት፡በቀር፡መጥበቅ፡የሌላቸው፡አ—ዐ፡ሀ—ሐ—ኀ ።

አና፡ሀ፡በመካከሉ፡ያሉበት፡ግስ፡የቀተለ፡ሰርዌ፡አርእስቱ፡በግእዝ፡ይነሣ፡የነበረውን፡ለውጦ፡ሳድስ፡ያደርጋል፤ይህም፡ልኢክ፡ለአከ÷ልሒኮ፡ለሐኰ፡ጽዒል፡ጸዐለ÷ምሂር፡መሀረ÷ግሒሥ፡ገሐሠ÷ዝኂር፡ዘኀረ፡እያለ፡ሌላውን፡ኹሉ፡ያሳያል ። አንዳንድ፡ጊዜም፡አንቀጹ፡ሳይቀር፡፪ቱንም፡በሳድስ፡ያስነሣል፤ይህም፡ንኢድ፡ንእደ÷ጥዒም፡ጥዕመ÷ብሂል፡ብህለ÷ጥሒር፡ጥሕረ÷ጐሒቍ፡ጐሕቈ÷ድኂን፡ድኅነ፡እያለ፡መኼዱን፡ያሳያል ። አና፡ሀ፡ማእከል፡ኹነው፡እንዲህ፡ካለወጡት፡በቀር፡ዘርና፡አንቀጽ፡በሳድስ፡ፊደል፡አይነሣም ። ዳግመኛም፡በመካከሉ፡ዐመል፡ያለበት፡ግስ፡እንደ፡ኅሥሥት፡የሚለዋወጥ፡ስለ፡ኾነ፡

ተዝኅረ ፡ ተዘኅረ ፥ ተልዕለ ፡ ተለዐለ ፥ ተውዕረ ፡ ተወዐረ ፥ ተምህረ ፡ ተመሀረ ፥ ተክዕወ ፡ ተከዐወ ፡ እያለ ፡ ይገኛል ። በክህለም ፡ ያለ ፡ ህ ፡ እስከ ፡ ፹ ፡ ሰራዊት ፡ በካልአይ ፡ ኹሉ ፡ ይታጣል ፤ ይህም ፡ ክህለ ፡ ይክል ፥ ክህልከ ፡ ትክል ፥ ክህልኩ ፡ እክል ፡ እያለ ፡ ጭራሽ ፡ መታጣቱን ፡ ያሳያል ። የብህለም ፡ አካኼድ ፡ እንደ ፡ ክህለ ፡ ነው ፤ ህን ፡ በካልአይ ፡ ኹሉ ፡ ይውጣል ። ይህም ፡ ብህለ ፡ ይብል ፥ ብህልኩ ፡ እብል ፥ ብህልነ ፡ ንብል ፡ ማለቱን ፡ መደብ ፡ አድርጎ ፡ ይብህል ፡ እብህል ፡ ንብህል ፡ አለማለቱን ፡ ያሳያል ። በቤለ ፡ አካኼድ ፡ ግን ፡ መሪና ፡ ተከታይ ፡ የሌለው ፡ ባሕታዌ ፡ ፍኖት ፡ ነው ፤ ቤለን ፡ ተመልከት ።

፲፮ ፤ ፫ኛም ፡ ከቀተለ ፡ እስከ ፡ ማህረከ ፡ ባሉት ፡ በ፯ቱ ፡ አርእስት ፡ አና ፡ ሀ ፡ መድረሻ ፡ ሲኾኑ ፡ ፩ኛው ፡ ፊደል ፡ ወይም ፡ ፫ኛው ፡ ግእዝ ፡ ይኾን ፡ የነበረውን ፡ ለውጠው ፡ ሳድስ ፡ ያደርጉታል ። ይህም ፡ ገብአ ፡ ፈርሀ ፥ ጸውዐ ፡ ሰብሐ ፥ ሰርሐ ፡ ሣርኀ ፡ ባልሐ ፥ ቈቅሐ ፡ ቶስሐ ፡ ሞቅሐ ፥ ገፍትዐ ፡ ቀሕቅሐ ፥ ላዕልዐ ፡ ላሕልሐ ፡ እያለ ፡ ሌላውን ፡ ኹሉ ፡ ያሳያል ። ፯ቱ ፡ አርእስቶች ፡ ማን ፡ ማን ፡ እንደ ፡ ኾኑ ፡ ባመል ፡ መጨረሻ ፡ ተመልከት ። ፪ኛም ፡ በ፫ ፡ ፊደል ፡ ግስ ፥ ከዚያውም ፡ በቀተለ ፡ ቤት ፡ በሣልሳይ ፡ አንቀጽ ፡ ሳድስ ፡ ይኾን ፡ የነበረውን ፥ ይግበእ ፡ ይፍራህ ፥ ይብላዕ ፡ ይክላሕ ፡ ይበእ ፡ ይፃእ ፡ ይብዛኅ ፡ እያሰኙ ፡ ወደ ፡ ራብዕ ፡ ይለውጡታል ። ፩ነታቸው ፡ ስላንድ ፡ የሚቈጠር ፡ የአና ፡ የሀ ፡ ግብር ፡ ይህ ፡ ነው ።

ወና ፡ የ ።

፲፯ ፤ የወና ፡ የየ ፡ ዐመል ፡ መጕረድና ፡ ድምጥ ፡ መለወጥ ፡ ነው ፤ ራሳቸውን ፡ እየጐረዱና ፡ እየዋጡ ፥ ወይም ፡ በጥፈት ፡ እየታጡ ፡ እየተዋጡ ፡ ለሌሎቹ ፡ መወልጣነ ፡ ድምፅ ፡ ይኾናሉ ። የድምጣቸውም ፡ ስልት ፡ በፊደላት ፡ ጠባይ ፡ በ፲ኛው ፡ ቍጥር ፡ በመቅድም ፡ ውስጥ ፡ እንደ ፡ ተነገረ ፡ ፩ ፡ ፩ ፡ ነው ፤ የወ ፡ ካዕብና ፡ ሳብዕ ፡ ማድረግ ፥ የየ ፡ ሣልስና ፡ ኃምስ ፡ ማድረግ ።

ወ ።

፲፰ ፤ ወ ፡ መድረሻ ፡ ወይም ፡ መጨረሻ ፡ ሲኾን ፥ ከልአዩ ፡ ሳድስ ፡ ይኾን ፡ የነበረውን ፡ ጕርዶ ፡ ካዕብና ፡ ሳብዕ ፡ ያደርጋል ፤ ይህም ፥ በገቢር ፡ ዘረወ ፡ ይዘሩ ፥ ሠረወ ፡ ይሤሩ ፥ ፈነወ ፡ ይፌኑ ፡ ማለቱን ፤ በተገብሮም ፡ ተዘርወ ፡ ይዘሮ ፥ ተሠረወ ፡ ይሤሮ ፥ ተፈነወ ፡ ይትፌኖ ፡ ማለቱን ፡ ያሳያል ። ደጊም ፡ ሲኾን ፡ በጭራሽ ፡ አይጐርድም ፤ ይህም ፥ ከወወ ፡ ይከውው ፥ ለወወ ፡ ይለውው ፥ ጌወወ ፡ ይጌውው ፡ እያለ ፡ መኼዱን ፡ ያሳያል ። ሳድስ ፡ ቅጽሉንም ፡ መከከሉ ፡ ካዕብ ፡ ይኾን ፡ የነበረውን ፡ ሳድስ ፡ ያደርጋል ፤ ይህም ፡ ዝርው ፡ ሥርው ፡ ፍንው ፡ ህልው ፡ ቅንው ፡ ጊውው ፡ ምጥው ፡ ማለቱን ፡ ያሳያል ።

፲፱ ፤ ኹለተኛም ፡ ወ ፡ በቀተለ ፡ ሰርዌ ፡ ማእከል ፡ ሲኾን ፡ ያንቀጹ ፡ መነሻ ፡ ግእዝ ፡ ይኾን ፡ የነበረውን ፡ ጕርዶ ፡ ሳብዕ ፡ ያደርጋል ፤ ይህም ፡ ሀዊብ ፡ ሆበ ፡ የሀውብ ፡ ይሁብ ፥ ሐዊር ፡ ሖረ ፥ ጸዊር ፡ ጾረ ፥ ነዊም ፡ ኖመ ፥ ቀዊም ፡ ቆመ ፡ እያለ ፡ መኼዱን ፤

እንዳርእስቱ ፡ ሀወበ ፡ ሐወረ ፡ ጸወረ ፡ ነወመ ፡ ቀወመ ፡ አለማለቱን ፡ ያሳያል ። በ፩ ፡ ፊደል ፡ ግስ ፡ ማእከል ፡ ሲኾን ፡ ግን ፡ ያርእስቱንም ፡ ጣፍ ፡ እንደ ፡ ሥሩ ፡ ሳብዕ ፡ ያደርጋል ። ይህም ፡ ኖልዎ ፡ ኖለወ፥ሰስዎ ፡ ሰሰወ፥ቶስሖ ፡ ቶስሐ፥ቆጽሮ ፡ ቆጸረ ፡ እያለ ፡ በ፫ ፡ ፊደል ፡ ብቻ ፡ መኼዱን ፤ ነውልዎ ፡ ነውለወ፥ሰውስዎ ፡ ሰውሰወ፥ተውስሖ ፡ ተውስሐ፥ቀውጽሮ ፡ ቀውጸረ ፡ አለማለቱን ፡ ያሳያል ።

፳ ፤ ሦስተኛም ፡ ወ ፡ ለሦስት ፡ ፊደል ፡ ግስ ፡ መነሻ ፡ ሲኾን፥ጥሬ ፡ ዘሩ ፡ ፩ ፡ ፊደል ፡ ይኾን ፡ የነበረውን ፡ ጕርዶ ፡ ፫ ፡ ፊደል ፡ ብቻ ፡ ያደርጋል ። ይህም ፡ ወጊስ ፡ ወገሰ ፡ ብሎ ፡ ሞገስ ፤ ወጥሖ ፡ ወጥሐ ፡ ብሎ ፡ ሞጥሕ ፤ ወቂሕ ፡ ወቅሐ ፡ ብሎ ፡ ሞቅሕ ፤ ወጊድ ፡ ወገደ ፡ ብሎ ፡ ሞገድ ፤ ወገረ ፡ ሙጋር፥ወደየ ፡ ሙዳይ፥ወድቀ ፡ ሙዳቅ፥ውሕዘ ፡ ሙሓዝ፥ወለደ ፡ ሙላድ ፡ ማለቱን ፡ ያሳያል ። ሳቢ ፡ ዘሩ ፡ ግን፥ልደት ፡ ፀአት ፡ ድቀት ፡ ርደት ፡ እያለ ፤ ወይም ፡ ሳይጕርድ ፡ ውግረት ፡ ውኅደት ፡ ውኅጠት ፡ ውጥነት ፡ ውዕፈት ፡ እያለ ፡ ይኼዳል ። ኃልሳዩንም ፡ ከቀደሰና ፡ ከበረከ ፡ ቤት ፡ በቀር ፡ ኹሉን ፡ ይጕርዳል ፤ ይህም ፡ ወሀበ ፡ ይውህብ ፡ ብሎ ፡ የሀብ ፤ ይገስ ፡ ይቃሕ ፡ ይገድ ፡ ይገር ፤ ይደቅ ፡ የሐዝ ፡ ይለድ ፡ ይፈጥ፥ይፀፍ ፡ ይረድ ፡ ማለቱን ፡ ያሳያል ።

፳፩ ፤ አራተኛም ፡ ከ፪ቱ ፡ ዐመሎች ፡ ሲገናኝ ፡ አርእስቱ ፡ ሳድስ ፡ ይኾን ፡ የነበረውን ፡ ወደ ፡ ራብዕ ፡ ይለውጠዋል ፤ ይህም ፡ ዋሕይ ፡ ዋሕዮት፥ዋሐየ ፡ ይዋሒ ፡ ይዋሒ ፡ እያለ ፡ መኼዱን ፡ ያሳያል ። ዳግመኛም ፡ ውዕይ ፡ ውዕዮት ፡ ውዕየ ፡ ወይም ፡ ወዐየ ፡ ይውዒ ፡ የዐይ ፡ ይላልና፥ዋሐየም ፡ እንደ ፡ ውዕየ ፡ ሊኼድ ፡ ይችላል ፤ ይህም ፡ አካኼድ ፡ በቀተለ ፡ ቤት ፡ ነው ። በቀደሰና ፡ በበረከ ፡ ቤት ፡ ግን ፤ ወደሰ ፡ ይዌድስ ፡ ይወድስ፥ወጥሐ ፡ ይዌጥሕ ፡ ይወጥሕ፥ወሠረ ፡ ይዌሥር ፡ ይወሥር፥ዋሐደ ፡ ይዋሕድ ፡ ይዋሕድ፥ዋከየ ፡ ይዋኪ ፡ ይዋኪ፥ዋነየ ፡ ይዋኒ ፡ ይዋኒ ፡ ይላል ፡ እንጂ ፤ እንደ ፡ ቀተለ ፡ ቤት ፡ አይጕርድም ። ወ ፡ መነሻም ፡ መድረሻም ፡ ማእከልም ፡ ኹኖ ፡ ከልጕረደው ፡ በቀር፥የግእዝ ፡ ቋንቋ ፡ ግስ ፡ በሳብዕ ፡ ቀለም ፡ አይነሣም ፤ <u>በካዕብ</u> ፡ <u>በሳብዕ</u> ፡ <u>አይጨርስም</u> ፤ ጥሬ ፡ ዘሩም ፡ በካዕብ ፡ በሳብዕ ፡ አይነሣም ። ከዚህ ፡ የቀረውን ፡ የወን ፡ ጠባይና ፡ ዐመል ፡ እኹል ፡ ገብ ፡ ፊደል ፡ መኾኑን ፡ በበታው ፡ ተመልከት ።

የ ።

፳፪ ፤ የ ፡ መድረሻ ፡ ወይም ፡ መጨረሻ ፡ ሲኾን፥ከልአዩ ፡ ሳድስ ፡ ይኾን ፡ የነበረውን ፡ ጕርዶ ፡ ኃልስ ፡ ያደርጋል ፤ ያርእስቱንም ፡ ማእከል ፡ ኃልስ ፡ ይኾን ፡ የነበረውን ፡ ለውጦ ፡ ሳድስ ፡ ያደርጋል ። ይህም፥ሐቅይ ፡ ሐቀየ ፡ የሐቂ ፤ ሰቅይ ፡ ሰቀየ ፡ ይሰቂ ፤ ፈድይ ፡ ፈደየ ፡ ይፈዲ ፤ ገንይ ፡ ገነየ ፡ ይገኒ ፤ ኀርይ ፡ ኀረየ ፡ የኅሪ ፡ እያለ ፡ ሌላውን ፡ ኹሉ ፡ ያሳያል ። በበዝ ፡ አንቀጽም ፡ እንዲሁ ፡ ነው ፤ ኃልስ ፡ ይሆን ፡ የነበረውን ፡ ሳድስ ፡ ያደርጋል ። ወርእያ ፡ ደንገፀት ፤ በሊዖ ፡ ወሰትዮ ፤ አዕሚቆ ፡ ወኀልዮ ፡ እንዲል ።

፳፫ ፤ ፪ኛም ፡ የ ፡ በቀተለ ፡ ሰርዌ ፡ በ፫ ፡ ፊደል ፡ ግስ ፡ ማእከል ፡ ሲኾን ፡ መነሻው ፡ ግእዝ ፡ ይኾን ፡ የነበረውን ፡ ለውጦና ፡ ጕርዶ ፡ ኃምስ ፡ ያደርጋል ። ይህም ፡ ገዪሥ ፡

ጌሠ ፥ ጠዪስ ፡ ጤሰ ፥ መዪጥ ፡ ሜጠ ፥ ሠዪም ፡ ሤመ ፥ ዐዪል ፡ ዔለ ፥ በዪል ፡ ቤለ ፡ እያለ ፡ መኼዱን ፡ መደብ ፡ አድርጎ ፤ እንዳርእስቱ ፥ ገየሠ ፡ ጠየሰ ፥ መየጠ ፡ ሠየመ ፤ ዐየለ ፡ በየለ ፡ አለማለቱን ፡ ያሳያል ። በ፩ ፡ ፊደል ፡ ግስ ፡ ማእከል ፡ ሲኾን ፡ ግን ፡ አርእስቱንም ፡ እንዳንቀጹ ፡ በኃምስ ፡ ያስነሣል ፤ ይህም ፡ ዼግኖ ፡ ዼገነ ፥ ጌግዮ ፡ ጌገየ ፥ ሌልዮ ፡ ሌለየ ፥ ቄቅዮ ፡ ቄቀየ ፥ ሴስዮ ፡ ሴሰየ ፡ ማለቱን ፡ መደብ ፡ አድርጎ ፤ ደይግኖ ፡ ደይገነ ፥ ገይግዮ ፡ ገይገየ ፥ ለይልዮ ፡ ለይለየ ፥ ቀይቅዮ ፡ ቀይቀየ ፥ ሰይስዮ ፡ ሰይሰየ ፥ አለማለቱን ፡ ያሳያል ። የ ፡ ማእከልና ፡ መድረሻ ፡ እየኾነ ፡ ካልጐረደው ፡ በቀር ፥ ግስ ፡ በኃምስ ፡ ፊደል ፡ አይነሣም ፤ በሣልስ ፡ ፊደል ፡ አይጨርስም ፤ ጥሬና ፡ ነባርም ፡ እንደዚህ ፡ ነው ።

ሐተታ ፡ ስለ ፡ ብህለና ፡ ስለ ፡ ቤለ ።

፹፩ ፤ ሀሎ ፡ የሀለወ ፡ ክፋይ ፡ ወይም ፡ ካዕቡ ፥ መንቲያው ፡ ድርቡ ፡ እንደ ፡ ኾነ ፤ ቤለም ፡ የብህለ ፡ ካዕብ ፡ መንቲያና ፡ ድርብ ፡ ይባላል ፤ ያንዱ ፡ ቅንጣት ፡ ዘር ፡ ግስ ፡ ባለ፪ ፡ ዐመል ፡ ስለ ፡ ኾነ ፡ በሀና ፡ በየ ፡ ስልት ፡ በ፪ቱ ፡ አካኼድ ፡ ይኼዳል ። የሀውን ፡ አካኼድ ፡ በሀ ፦ ተናግረናል ፤ የየውም ፡ አካኼድ ፡ እንዲህ ፡ ነው ። በሀ ፡ ማእከልነት ፡ ብሂል ፡ ብሂሎት ፡ ብህለ ፦ የተባለው ፤ ፪ኛ ፡ ደግሞ ፡ በየ ፡ ማእከልነት ፥ በዪል ፡ በዪሎት ፡ ቤለ ፡ ተብሎ ፥ አስደራጊውንም ፥ አበለ ፡ ያብል ፡ እያሰኘ ፡ ልውጥና ፡ ግልብጥ ፡ ሕገ ፡ ወጥ ፡ አካኼድ ፡ ይኼዳል ፤ ብህለም ፡ ቤለ ፡ መባሉ ፡ በወዲያኛው ፡ ትግሬ ፡ በሐባቦች ፡ ቋንቋ ፡ ይታወቃል ፤ በወዲህኛውም ፡ ትግሬኛ ፥ ሐማሴኖች ፡ የለ ፥ አኵስሞችና ፡ ዐዶች ፡ በለ ፡ ይሉታል ። ያካኼዱም ፡ ሕገ ፡ ወጥነት ፡ ይህ ፡ ነው ፤ ቤለ ፡ ይበይል ፡ ይቢል ፡ ብሎ ፥ እንደ ፡ ዔለና ፡ እንደ ፡ ሤመ ፡ ፊት ፡ ለፊት ፡ በመኼድ ፡ ፈንታ ፥ ቤለ ፡ ይቤ ፡ ይበል ፡ ይበል ፤ ቤልከ ፡ ትቤ ፡ ትበል ፡ በል ፤ ቤለት ፡ ትቤ ፡ ትበል ፡ ትበል ፤ ቤልኩ ፡ እቤ ፡ እበል ፡ እበል ፤ ቤልነ ፡ ንቤ ፡ ንበል ፡ ንበል ፡ እያለ ፡ በነዚህ ፡ በ፳ቱ ፡ ሰራዊት ፡ ለን ፡ እያሰገደ ፥ የን ፡ እየጐረደ ፡ በዔለና ፡ በሤመ ፡ አካኼድ ፡ ግእዝ ፡ ይኾን ፡ የነበረውን ፡ በ ፥ በካልኣይ ፡ ኹሉ ፡ ኃምስ ፡ ያደርጋል ። በቀሩት ፡ ደግሞ ፡ በ፳ቱ ፡ ኹሉ ፥ ቤሉ ፡ ይቤሉ ፡ ይበሉ ፡ ይበሉ ፤ ቤልክሙ ፡ ትቤሉ ፡ ትበሉ ፡ በሉ ፤ ቤላ ፡ ይቤላ ፡ ይበላ ፡ ይበላ ፤ ቤልክን ፡ ትቤላ ፡ ትበላ ፡ በላ ፤ ቤልኪ ፡ ትቤሊ ፡ ትበሊ ፡ በሊ ፡ እያሰኘ ፡ የን ፡ በመጕረዱ ፡ ላይ ፡ ለን ፡ እየጨመረ ፡ ይኼዳል ። ትንቢትነቱንም ፥ ይቤ ፡ ትቤ ፡ እቤ ፡ ንቤ ፡ ብሎ ፡ በሥርወ ፡ ቀለሙ ፡ ያስረዳል ፤ ይህነንም ፡ በአሥራውና ፡ በብሂል ፡ አፈታት ፡ ተመልከት ። ባላገባቦች ፡ ግን ፡ ባለመጽሐፎችም ፡ ሳይቀሩ ፥ የይቤ ፡ ቀዳማይ ፡ ቤለ ፡ መኾኑን ፡ ስላላስተዋሉ ፤ ፪ኛም ፡ ቀዳማይ ፡ አንቀጽ ፤ ሥርወ ፡ ፊደል ፡ አለመለወጡን ፥ በሣልስ ፡ በኃምስ ፡ አለመጕረዱን ፥ አጥብቀው ፡ አጥልቀው ፡ ስላልመረመሩ ፥ ይቤን ፡ በቤለ ፡ ፈንታ ፦ ቀዳማይ ፡ አንቀጽ ፡ አድርገው ፥ እኩሉ ፡ ዘርና ፡ አርእስት ፡ የሌለው ፡ ለብቻው ፡ የቆመ ፡ ነበር ፡ ቀዳማይ ፡ ነው ፤ እኩሉም ፡ የቀዳማይ ፡ አንቀጽ ፡ የብህለ ፡ ድርብ ፡ ነው ፡ እያሉ ፡ በቀዳማይነት ፡ ስላቆሙት ፥ ርባታውና ፡ አፈታቱ ፡ ከሥር ፡ እስከ ፡ ጫፍ ፡ ተበላሽቷል ፡ (ቍ፲፪) ።

፹፪ ፤ የአንና ፡ የሀን ፥ የወንና ፡ የየን ፡ የነዚህን ፡ የኹለቱን ፡ ስልት ፥ የመንገዳቸውን ፡ ልዩነት ፥ ያካኼዳቸውን ፡ መጥፎነት ፥ ነውጠኞችና ፡ ዐመለኞች ፡ ኹነው ፡ የግ

ስን፡ ቤት፡ ኹሉ፡ ማናወጣቸውን፥ ጠባይና፡ ዘር፡ ማስለወጣቸውን፡ ለማስተዋልና፡ ለመመርመር፡ ይህ፡ የጣፍነው፡ ብቻ፡ ይበቃል፤ ከዚህ፡ የቀረውን፡ የየን፡ ጠባይና፡ ዐመል፡ በቦታው፡ ተመልከት ። በመካከሉ፡ እነዚህ፡ ዐመሎች፡ የሌሉበት፡ ግስ፡ በግእዝ፡ በራብዕ፡ ቢነሣ፡ እንጂ፥ በኃምስ፡ በሳድስ፡ በሳብዕ፡ ፊደል፡ አይነሣም ። በግእዝ፡ መነሣት፡ የዐረብ፥ በራብዕ፡ መነሣት፡ የሱርስትና፡ የዕብራይስጥ፡ ነው፤ ግእዝም፡ የዐረብ፡ የሱርስት፡ የዕብራይስጥ፡ ወንድም፡ ስለ፡ ኾነ፥ በነዚህ፡ አካኼድ፡ ይኼዳል ። የነዚህም፡ ያራቱ፡ ልሳናት፡ ዘራቸውና፡ ነባራቸው፥ ንባባቸውና፡ ምስጢራቸው፡ እንደ፡ ወንጌላት፡ ቃል፡ ይገጥማል፤ ልዩነቱ፡ ጥቂት፡ ጥቂት፡ ነው ።

## ደጊመ፡ ቃል ።

፹፮፤ ደጊመ፡ ቃል፡ ያለው፡ የ፫፡ ፊደል፡ ግስ፡ ከዚያውም፡ የቀተለ፡ ሰርዌ፡ እንደ፡ ወና፡ እንደ፡ የ፡ ይጐርዳል፤ አጐራረዱ፡ ግን፡ እየቅል፡ ነው ። ፪ኛው፡ ፊደል፡ ፫ኛውን፡ ውጦ፡ ከዕብና፡ ሳብዕ፡ ወይም፡ ሣልስና፡ ኃምስ፡ ሳይኾን፡ እየጠበቀ፡ የ፪፡ ፊደል፡ ግስ፡ ይኾናል ። ይህም፡ ጠቢብ፡ ጠበ፥ ነቢብ፡ ነበ፥ ነዲድ፡ ነደ፥ ጸኒን፡ ጸነ፥ ቀሊል፡ ቀለ፥ ቈሪር፡ ቈረ፥ ተኒን፡ ተነ፡ እያለ፡ መኼዱን፡ ያሳያል ። ወና፡ የ፡ ደጊመ፡ ቃል፡ እሊህ፡ ፫ቱ፡ ዐመሎች፡ ካልጐረዱት፡ በቀር፡ የ፫፡ እንጂ፡ የ፪፡ ፊደል፡ ግስ፡ አይገኝም ።

፹፯፤ ዕጥፍ፡ ደጊመ፡ ቃል፡ ያለውም፡ በኊበኈ፥ ጐድጐደ፥ ደግደገ፥ ጠብጠበ፥ ከብከበ፥ በልበለ፥ ቀልቀለ፥ ፈልፈለ፥ ጸንጸነ፥ ተንተነ፥ እንደዚህ፡ ያለ፡ ይህን፡ የመሰለ፡ ኹሉ፡ ፊተኛውና፡ ፫ኛው፡ ስላንድ፡ ተቈጥሮ፡ የ፫፡ ፊደል፡ ግስ፡ ይባላል፤ ምንም፡ ቅንጣቱ፡ ፬፡ ቢኾን፡ ፊደሉ፡ ፪፡ ነውና፥ ግስነቱም፡ ደጊመ፡ ቃል፡ ካለው፡ ከ፪፡ ፊደል፡ ግስ፡ የወጣ፡ ተቀጥላ፡ ግስ፡ ነውና፥ ባ፩፡ ግስ፡ ፩፡ ብቻ፡ እንጂ፡ ፪፡ ደጊመ፡ ቃል፡ አይኾንም ።

፹፰፤ ደጊመ፡ ቃል፥ ገሰሰ፡ ኀሠሠ፥ አረረ፡ ሣረረ፥ ኰነነ፡ መነነ፥ ሐተተ፡ ፈተተ፡ እያለ፡ ፫ኛ፡ ሲኾን፡ ለብቻው፡ በራሱ፡ ይቈጠራል፤ ገብሰሰ፡ ደምሰሰ፥ ደንገገ፡ ፈርገገ፥ ጠንቀቀ፡ ሐንቀቀ፡ እያለ፡ ፬ኛ፡ ፊደል፡ ሲኾን፡ ግን፡ ፬ኛው፡ ዲቃላ፡ ነውና፥ ከ፫ኛው፡ ጋራ፡ ስላ፩፡ ተቈጥሮ፡ የ፫፡ ፊደል፡ ግስ፡ ይባላል፤ አርእስቱ፡ ግን፡ ደንገፀ፡ ነው ።

፹፱፤ ያ፬፡ ፊደል፡ ግስ፡ ያልናቸውም፡ ኖለወ፥ ሎለወ፥ ሶሰወ፥ ጌገየ፥ ሴለየ፥ ቄቀየ፥ ሴሰየ፡ እሊህን፡ የመሰሉ፡ ኹሉ፡ በምስጢር፡ በውሳጣይ፡ ቍጥር፡ ያ፬፡ ፊደል፡ ግስ፡ ሲኾኑ፡ የተጐረደው፡ ፪ኛውና፡ ያልተጐረደው፡ ፬ኛው፡ ፊደል፡ ስላንድ፡ ተቈጥሮ፡ የ፫፡ ፊደል፡ ግስ፡ ይባላሉ ። ይኸውም፡ ከ፬፡ አንዱ፡ ፊደል፡ ተጐርዶ፡ ፫፡ ብቻ፡ ስለ፡ ቀረ፡ ነው ። ደጊመ፡ ቃልም፡ ባይኖር፡ ወና፡ የ፡ ያሉበት፡ ቶስሐን፡ ዴገነን፡ የመሰለ፡ ያ፬፡ ፊደል፡ ግስ፡ ወና፡ የ፡ በንባብ፡ በጥፈት፡ ተውጠው፡ ተጐርደው፡ ስለ፡ ቀሩ፡ ፪ኛው፡ ፊደል፡ ከፊተኛው፡ ጋራ፡ ስላንድ፡ ተቈጥሮ፡ የ፫፡ ፊደል፡ ግስ፡ ይባላል ።

፴ ፤ በትናጋ ፡ የሚነገሩም ፡ ፫ቱ ፡ ፊደላት ፡ ገ ፡ ከ ፡ ቀ ፤ በምላስ ፡ ከሚነገሩትም ፡ ነ ፡ እነዚህ ፡ ፬ቱ ፡ የግስ ፡ መድረሻ ፡ ሲኾኑ ፡ ከና ፡ ነ ፡ ደግሞ ፡ መድረሻና ፡ ትራስ ፡ እየ ኾኑ ፡ በምእላድነት ፡ ሲጨመሩ ፡ ገና ፡ ቀ ፡ ተወራራሾች ፡ ናቸውና ፤ ከ ፡ ባለባቸው ፡ በ፫ቱ ፡ ቅርቦች ፡ ላይ ፡ አቅራቢውን ፡ ከ ፡ ደጊመ ፡ ቃልነት ፡ ስላለው ፡ ውጠውና ፡ ጕር ደው ፡ በንባብ ፡ በጥፈት ፡ ያስቀሩታል ። ይህም ፡ (ዐረግከ ፡ ሰበክከ ፡ ጠየቅከ) ፡ በማለት ፡ ፈንታ ፡ ዐረገ ፡ ውስተ ፡ አርያም ፤ ሰበከ ፡ ለነ ፡ ልደተ ፡ እግዚእ ፤ ጠየቀኑ ፡ አ ፡ ፍቁር ፡ እያለ ፡ ሌላውን ፡ ኹሉ ፡ ያሳያል ። ነ ፡ ደግሞ ፡ የንሕነ ፡ ዝርዝር ፡ ስለ ፡ ኾነ ፡ (ከንነ ፡ ድ ኅንነ ፡ አመንነ) ፡ በማለት ፡ ፈንታ ፡ ከነ ፡ ድኅነ ፡ አመነ ፡ እያለ ፡ በመጥበቅ ፡ ደጊሙን ፡ ይጐርዳል ። በተና ፡ በደ ፡ በጠ ፡ የሚጨርስ ፡ ግስ ፡ ባንዲቱ ፡ ሴት ፡ ሳድስ ፡ ቅጽልና ፡ በመድበል ፡ ቅጽል ፡ ሳይጐርድም ፡ እየጐረደም ፡ እንዲሁ ፡ ይጠብቃል ። ይህም ፡ ት ሑት ፡ ብሎ ፡ ትሕት ፤ ሐታቲ ፡ ሐተት ። ብዑድ ፡ ፍሉጥ ፡ ብሎ ፡ ብዕድ ፡ ፍልጥ ። ዐ ጻዲ ፡ መሣጢ ፡ ብሎ ፡ ዐጻድ ፡ መሠጥ ፡ እያለ ፡ ሌላውን ፡ ኹሉ ፡ ያሳያል ።

## ፫ኛ ፡ ዕርከን ።

## የግስ ፡ ልማድ ፡ ባላ፭ ፡ አዕማድ ።

፴፮ ፤ በኋላፊ ፡ አንቀጽ ፡ ላይ ፡ ተውሳክ ፡ እየኾኑ ፡ የግስን ፡ ጾታ ፡ ያንቀጽን ፡ ርባታ ፡ በየቤቱና ፡ በየሰራዊቱ ፡ ለይተው ፡ የሚመሩና ፡ የሚያስኬዱ ፡ የግስ ፡ ልማዶች ፡ እንዳ፭ቱ ፡ አዕማድ ፡ ፭ ፡ ናቸው ፤ አ ፡ ተ ፡ አስተ ፡ አን ፡ አስ ። ካ፭ቱ ፡ ደግሞ ፡ መደበኞቹ ፡ አና ፡ ተ ፡ ፪ቱ ፡ ናቸው ። ስና ፡ ን ፡ ስሯጽ ፡ ይባላሉ ፤ ፭ ፡ አዕማድ ፡ የተባሉም ፡ አድራጊ ፡ አስደራጊ ፡ ተደራጊ ፡ ተደራራጊ ፡ አደራራጊ ፡ ናቸው ። አ ፡ እነፈለሰን ፡ በሚመስሉ ፡ ባንጕል ፡ ግሶች ፡ ላይ ፡ ሲገባ ፡ ባንድ ፡ ጊዜ ፡ የማድረግና ፡ የማስደረግ ፡ ልማድ ፡ ይኾ ናል ፤ ይህም ፡ አምጽአ ፡ ብሎ ፡ አመጣ ፡ አስመጣ ፡ ማለቱን ፡ ያሳያል ፤ እነቀተለን ፡ በሚ መስል ፡ በገቢር ፡ ግስ ፡ ግን ፡ የማስደረግ ፡ ብቻ ፡ ይኾናል ።

፴፯ ፤ ተ ፡ የመደረግና ፡ የመደራረግ ፡ ልማድ ፡ ነው ፤ በጥርስ ፡ በምላስ ፡ ከሚነገሩ ፡ ከሥራንዱ ፡ ፊደላት ፡ በ፮ቱ ፡ ብቻ ፡ (ደ ፡ ዘ ፡ ጠ ፡ ሠሰ ፡ ጸፀ ፡ ተ) ፡ ለሚነሡ ፡ ግሶች ፡ ልማድ ፡ ሲኾን ፡ ግን ፡ በሩቆችና ፡ አነ ፡ ንሕነ ፡ በሚል ፡ በትንቢት ፡ በዘንድ ፡ በትእዛዝ ፡ ኹሉ ፡ ተውጦ ፡ ተጐርዶ ፡ ይቀርና ፡ በ፬ቱ ፡ ቅርቦች ፡ በትእዛዝ ፡ ብቻ ፡ ይገኛል ። ይ ህም ፡ ተድኅረ ፡ ይዴኀር ፡ ይደኀር ፤ ተዘብጠ ፡ ይዘበጥ ፤ ተጠውመ ፡ ይጠወም ፤ ተሠ ይመ ፡ ይሠየም ፤ ተፀምደ ፡ ይፀመድ ፤ ተፀመድኩ ፡ ነ ፡ እፀመድ ፡ ንፀመድ ፡ ካለ ፡ በኋላ ፡ ያራቱን ፡ ቅርቦች ፡ ተፀመድ ፡ ዲ ፡ ዱ ፡ ዳ ፡ እያለ ፡ መኼዱን ፡ ያሳያል ፤ በንዱ ፡ የኹሉ ፡ ይታወቃል ።

፴፰ ፤ አስተ ፡ መደቡ ፡ የማደራረግ ፡ ድርቡ ፡ የማድረግና ፡ የማስደረግ ፡ የመደ ረግም ፡ ነው ፤ አስተ ፡ የማደራረግ ፡ ልማድና ፡ መደብ ፡ መኾኑ ፡ ባስደራጊው ፡ ልማድ ፡ በአና ፡ በተ ፡ መካከል ፡ ስ ፡ ስሯጽ ፡ ኹኖ ፡ ስለ ፡ ገባ ፡ ነው ፤ ይኸውም ፡ ሥርወ ፡ ቀለ ሙን ፡ አስተቃተለ ፡ ብሎ ፡ ራብዕ ፡ በማድረግ ፡ ይታወቃል ፤ የማያሳስት ፡ መለዮውና ፡ ምልክቱ ፡ ይህ ፡ ነው ። የማድረግና ፡ የማስደረግ ፡ የመደረግ ፡ ልማድ ፡ መኾኑም ፡

## ንኡስ ፡ አገባብ ።

፻፲ ፤ በነባር ፡ በዘማች ፥ በዐቢይ ፡ በንኡስ ፥ በአናቅጽ ፡ ኹሉ ፡ እየገባ ፡ ማሰሪያ ነትን ፡ የማያስለቅቅ ፤ ጥያቄና ፡ አንክሮ ፥ ደስታና ፡ ሐዘን ፥ ልመናና ፡ ምኞት ፥ አሉታና ፡ አፍራሽ ፡ ዕሽታና ፡ እንቢታ ፥ ሌላም ፡ ይህን ፡ የመሰለ ፥ ልዩ ፡ ልዩ ፡ ነገር ፡ የሚያሳይ ፡ ፊደልና ፡ ቃል ፥ ንኡስ ፡ አገባብ ፡ ይባላል ፤ ከዐቢይ ፡ አገባብ ፡ ተለይተው ፡ ንኡስ ፡ አገ ባቦች ፡ የሚባሉም ፡ እነዚህ ፡ ናቸው ።

| | | | |
|---|---|---|---|
| ሁ ፡ | ኑ ፡ | ሐዊሳ ፡ | እንቋዕ ፡ |
| እም ፡ | አሌ ፡ | እስኩ ፡ | ጥቀ ፡ |
| መ ፡ ሚ ፡ | ወይ ፡ ዋይ ፡ | ዮጊ ፡ | እንከ ፡ |
| እፎ ፡ በእፎ ፡ | ወይሌ ፡ | እንጋ ፡ | ኦ ፡ |
| አይ ፡ ምንት ፡ ተ ፡ | አሀ ፡ አሀሀ ፡ | ክመ ፡ ጽመ ፡ | ሶ ፡ |
| ሁ ፡ ኑ ፡ በኑ ፡ | ሰይ ፡ ዬ ፡ | ኣ ፡ | ኬ ፡ |
| አይ ፡ መኑ ፡ | አይ ፡ አይቴ ፡ | አይ ፡ ማእዜ ፡ | ስፍን ፡ |
| አሉታ ፤ ......... | አል ፡ | ኢ ፡ | አከ ፡ |
| አማራጭ ፤ ....... | አው ፡ ዮጊ ፡ ሚመ ፡ እመ ፡ ኦከ ፡ ሶበ ፡ አከ ፡ | | |
| አጫፋሪ ፤ ....... | ወ ፡ ሂ ፡ ኒ ፡ ዓዲ ፡ | | |
| ከፋይ ፤ ........ | ወ ፡ ሂ ፡ ኒ ፡ ሰ ፡ ባሕቱ ፡ | | |
| አጋናኝ ፤ ....... | ወ ፡ ሂ ፡ ኒ ፡ ጥቀ ፡ | | |
| ጕድና ፡ ድንቅ ፤ | ዕጹብ ፡ ግሩም ፡ ተአምር ፡ ግናይ ። | | |

## የጊዜ ፡ ጥሬዎች ።

| | | |
|---|---|---|
| ቅድመ ፡ ቅድም ፡ | ትማልም ፡ | ጌሠም ፡ ሳኒታ ፡ |
| ትካት ፡ ዓለም ፡ | አሚር ፡ ዮም ፡ | ወትረ ፡ ዘልፈ ፡ |
| አስፌር ፡ | ኀሪፍ ፡ | ለዝሉ(ላ)ፉ ፡ |
| ናሁ ፡ | ይእዜ ፡ | ግሙራ ፡ ለግሙራ ፡ |
| ማእዜ ፡ | ወትር ፡ ዘልፍ ፡ | ለፍጻሜ ። |

## የብዙ ፡ ብዙና ፡ ጭራሽ ፡ የሚያሳዩ ።

፻፲፩ ፤ ጥቀ ፡ ፈድፋደ ፡ ብዙኅ ፡ ይሙኑ ፤ በሕቁ ፡ በፍድፋዴ ። ለዓለም ፡ ለዝሉፉ ፤ ለፍጻሜ ፥ ግሙራ ፡ ለግሙራ ። ምንት ፡ ጽመ ፡ ክመ ፥ እምድሩ ፡ በምልኡ ፡ ስብዐ ። ዳግመኛም ፡ መድረሻቸው ፡ ግእዝ ፡ እየሆነ ፥ ወይም ፡ በ ፡ ወድቆባቸው ፡ በሳድስነት ፡ ንኡስ ፡ አገባብ ፡ የሚኾኑ ፡ ሳድስ ፡ ቀጽሎች ፡ ከምሉ ፡ በክፍሉ ።

| | | | |
|---|---|---|---|
| ፍጹመ ፡ | በፍጹም ፡ | ጥዩቀ ፡ | በጥዩቅ ፡ |
| ጥንቁቀ ፡ | በጥንቁቅ ፡ | ሕቀ ፡ | በሕቅ ፡ |

| | | | |
|---|---|---|---|
| ሀልወ ፡ | በሀልው ፡ | ኀዳጠ ፡ | በኀዳጥ ፡ |
| ድቡተ ፡ | በድቡት ፡ | ውኁደ ፡ | በውኁድ ፡ |
| ሀዱአ ፡ | በሀዱእ ፡ | ንስቲተ ፡ | በንስቲት ፡ |
| ክቡተ ፡ | በክቡት ፡ | ፍድፉደ ፡ | በፍድፉድ ፡ |
| ኅቡአ ፡ | በኅቡእ ፡ | ንሕኑሐ ፡ | በንሕኑሕ ፡ |
| ክሡተ ፡ | በክሡት ፡ | ብዙኀ ፡ | በብዙኅ ፡ |
| ግሁደ ፡ | በግሁድ ፡ | ርቱዐ ፡ | በርቱዕ ፡ |
| መፍትወ ፡ | በመፍትው ፡ | ድልወ ፡ | በድልው ። |

በነዚህ ፡ አምሳል ፡ ንኡስ ፡ አገባብ ፡ እየኾነ ፡ ለሚነገር ፡ ቅጽል ፡ ውሳኔ ፡ የለውም ። ፫ኛም ፡ ነበር ፡ አንቀጽ ፡ የሚሰማባቸው ፡ ጥሬዎችና ፡ ቅጽሎች ፥ ወይም ፡ ውስጠ ፡ ውእቱዎች ። ድልወት ፡ መፍትው ፤ ብዉሕ ፡ ርትዕ ። መፍቅድ ፡ ፈቃድ ፡ ፍትወት ፡ ጸሕቅ ፡ ሥምረት ፡ ማኅሠሥ ። ግብር ፡ ዅርሀ ፡ ግድ ፡ ግዱድ ። ፬ኛም ፡ ጽድቅና ፡ አሉታ ፡ አንቀጽ ፡ የሚሰማባቸው ፡ የጥሬና ፡ ያንቀጽ ፡ ልቃሞች ፥ ወይም ፡ እንጥብጣቦች ። ናሁ ፡ ዮጊ ፡ ነዋ ፡ ዬ ፤ እንሆ ። ነዮ ፡ (ያ ፡ ዮሙ ፡ ዮን ፤ ነየከ ፡ ኪ ፡ ክሙ ፡ ክን ፤ ነየ ፡ ነየነ) ፤ እንሆት ፤ እንሆለት ። እወ ፡ አሜን ፡ አማን ፤ አዎን ፡ እውነት ። እንዳዒ ፡ እንጃ ፤ እንጃ ። አሆ ፡ እንቢ ፡ (ቍ፺፬) ። አሀ ፡ አሀሀ ፥ አሀ ፡ አሀ ፤ ወዲያ ፡ ወዲያ ። ብሥራት ፤ ብሥራትከ ፡ (ኪ ፡ ክሙ ፡ ክን) ፤ የምሥራች ፥ ደስ ፡ ይበልኽ ፤ ተፈሣሕ ፡ ወተሐሠይ ። ፭ኛም ፡ ከትእዛዝ ፡ እየተጨመሩ ፡ ንኡስ ፡ አገባብ ፡ የሚኾኑ ፡ ትእዛዝ ፡ አንቀጾች ። ሀብ ፤ ሀቡ ፤ ሀቢ ፤ ሀባ ፡ (ወሀበ) ። ሀብኬ ፡ ንትኃሠሥ ። ነዐ ፤ ነዑ ፤ ነዒ ፤ ነዓ ፡ (ነዐወ) ። ነዑ ፡ ንረድ ፤ ነዑ ፡ ንምሳሕ ። ሕንክ ፡ ክሙ ፡ ሕንኪ ፡ ካ ፡ (ሐነከ) ። ሕንክሙ ፡ ብልዑ ።

## ደቂቅ ፡ አገባብ ።

፪፲፪ ፤ በብትን ፡ ሰዋስው ፡ ባራት ፡ ሰራዊት ፡ በሩቅ ፡ በሩቆች ፡ እየገባ ፡ በሥር ፡ መደብ ፡ የሚዘረዝር ፡ ደቂቅ ፡ አገባብ ፡ ይባላል ፤ በተገናኝ ፡ የባለቤትን ፡ ኹነታና ፡ ሥራ ፡ ለመግለጥ ፡ በብትን ፡ ላይ ፡ የሚጨመር ፡ ቃል ፡ ማለት ፡ ነው ፤ ተረፈ ፡ ንኡስ ፡ እንደ ፡ ማለት ። ለዚህም ፡ ፪ ፡ ዐይነት ፡ አለው ፤ መድረሻውን ፡ የሚለውጥና ፡ የማይለውጥ ። መድረሻቸውን ፡ የማይለውጡ ፡ ደቂቅ ፡ አገባቦች ፡ ከዚህ ፡ ቀጥሎ ፡ ባ፬ ፡ ረድፍ ፡ የተጣፉት ፡ ናቸው ።

| | | | |
|---|---|---|---|
| ቤዛ ፡ | ፍና ፡ | ውስተ ፡ ጠ ፡ | ለ ፡ ለለ ፡ |
| ዐስበ ፡ | ዲቡ ፡ | ውሳጤ ፡ | በ ፡ በበ ፡ |
| ዕሴተ ፡ | ላዕለ ፡ | ቅድመ ፡ | ዘ ፡ ዘዘ ፡ |
| ተክለ ፡ | መልዕልተ ፡ | ማእከለ ፡ | ምስለ ፡ ከመ ፡ |
| በይነ ፡ | ታሕተ ፡ | አፍአ ፡ | አርአያ ፡ |
| አፈ ፡ | መትሕተ ፡ | ዝየ ፡ ለፌ ፡ | ሀየ ፡ ከሃ ። |

## መድረሻቸውን፡የሚለውጡና፡የማይለውጡ፡የቦታና፡የጊዜ፡ጥሬዎች ።

### የቦታ፡ጥሬ ።

ላዕል፡መልዕልት፡ላዕሊት ። ታሕት፡መትሕት፡ታሕቲት ። ትርአስ፤ትርጋፅ፤ አፍአ፤ውስጥ፡ውሳጢ፡ውሳጢት ። ቅድም፡ፍጽም፡ገጽ፤አንጻር፡ምንጻር ። ድኅሬት፡ከዋላ፤ግንጽሊት፡ግፍትዒት፡ቍልቍሊት ። የማን፡ይምን፤ፀጋም፡ፅግም ። ጽንፍ፡ክንፍ፡ከንፈር፡ሐይቅ፤ድንጋግ፡ወሰን ። አድያም፡ደወል፡ብሔር ። ዝየ፡ ህየ፡ለፌ፡ከሃ ። ጥቃ፡ጎር፡ሕፅን፡ገቦ፡ጕንድ፡ጽጕ፡ጽጕጕ፤ዐውድ፡ዘውር፡ ግድም፡ኑኅ፡ኰለኄ ።

### የጊዜያት፡ጥሬ ።

ቅድም፡ቀዲሙ፡አቅዲሙ፤ቀዳሚ፡መቅድም ። ድኅር፡ደኃሪ፡ከዋላ ። ምዕር፡ ወትር፡ዘልፍ ። ኵሎ፡ጊዜ፡ኵሎ፡ሰዓ፡ኵሎ፡ዕለተ፥ኵሎ፡አሚረ፥ኵሎ፡ዘመነ ። ንእስ፡ናእስ፤ውርዙት፡ውርዛዌ ። ርሥእ፡ርሥእና፡ርሥአን ። ትካት፡ጥንት፡መሠረት፤ፍጻሜ፡ተፍጻም፡ተፍጻሜት ። ዐቢይና፡ንኡስ፡ደቂቅ፡የተባሉት፡እነዚህ፡ኹሉ፡ያገባብ፡ጥሬዎች፡እንዲህ፡እንደሸት፡ተመርጠው፥ታሽተው፡ተፈልፍለው፡በ፫፡ማእሰረ፡ክፍል፡የታሰሩ፡ኋላ፡እንዲፈቱ፡ነውና፤ግቢያቸውንና፡ባህላቸውን፡አፈታታቸውን፡በየተራቸው፡በ፭ኛው፡ክፍል፡ተመልከት ።

### ፬ኛ፡ክፍል ።

### ጸዋትወ፡ቅጽል፡ወአኃዝ፡የሰዋስው፡ባለቤትና፡ጓዝ ።

### ፲፬ኛ፡ዕርከን ።

፻፲፫፤ቅጽል፡ማለት፡ተጨማሪ፡ቃል፡ማለት፡ነው፤መለዮ፡ምልክት፡እንደ፡ማለት፤ምስጢሩ፡ግን፡የባለቤትን፡ስምና፡ግብር፥ጠባይና፡አኳኋን፥መልኩን፡ዐይነቱን፥ወርዱን፡ቁመቱን፡ስፍሩን፡ቍጥሩን፤ሌላውንም፡ኹሉ፡የሚያሳይ፡የስምና፡የግብር፡ፍካሬ፥ወይም፡ጽጌና፡ፍሬ፡ማለት፡ነው፤(እስመ፡እምፍሬሁ፡ይትዐወቅ፡ዕፅ)። የቅጽልም፡ዐይነት፡እንደ፡ሰዋስው፡ክፍል፡፪፡ነው፤፩ኛው፡ዘር፥፪ኛው፡ነባር፡ይባላል፤ዘር፡ቅጽል፡አንቀጽ፡ያለው፥ነባር፡ግን፡አንቀጽ፡የሌለው፡ነው ።

፻፲፬፤ ዘር፡ቅጽሎች፡፫፡ናቸው፤ውስጠ፡ዘና፡መስም፥ጥሬ፡ዘርና፡ወገን፡ቅጽል፥አኃዝ ። ለዘር፡ቅጽል፡ኹሉ፡ውስጠ፡ዘነት፡አለው፤የውስጠ፡ዘም፡ነገር፡በ፹፫፡ቍጥር፡ከመስም፡ጋራ፡ተነግሯል ። የጥሬ፡ዘርም፡ውስጠ፡ዘነት፥ዘርፍ፡እየያዘ፡ሲቀጸል፡ነው፤ዘርፍ፡የሌለው፡ጥሬ፥ነጠላ፡ስም፡እንጂ፡ቅጽል፡አይባልም ። በአንቀጽ፡በብትን፡እየገቡ፡የልክ፡ቅጽልና፡አገባብ፡የሚኾኑ፡መጠንና፡አምጣን፡ዐቅም፥እነዚህ፡ኹሉ፡ዘር፡ቅጽሎች፡ናቸው ። ወገን፡ቅጽሎች፡የተባሉም፡አስቀድመን፡በ፮፡ቍጥር፡እንዳርእስት፡የተናገርናቸው፡ዊና፡ይ፡ናቸው፤

(ቀዳማዊ ፡ ይ ፥ ወደኃራዊ ፡ ይ) ፤ እነዚህ ፡ ፪ቱ ፡ ምእላዶች ፥ ዘርፍ ፡ አያያዥነት ፡ ባላ
ቸው ፡ በ፬ቱ ፡ ፊደላትና ፡ (ግእዝ ፡ ራብዕ ፡ ኃምስ ፡ ሳብዕ) ፡ በ፪ቱ ፡ አገባብ ፡ በለ ፡ በዘ ፡
ፈንታ ፡ እየገቡ ፥ የዘርፍና ፡ የቅጽል ፡ አፈታት ፡ ስላገኙ ፥ ከቅጽሎች ፡ ጋራ ፡ ተቈጥረ
ዋል ፤ ስማቸውም ፡ የሙሻዘር ፡ ውስጠ ፡ ዘ ፡ ይባላል ። ወገንነታቸው ፡ በወገን ፡ ጥሬ ፡
ሲገቡ ፡ ነው ። ምድር ፡ ምድራዊ ፥ ሰማይ ፡ ሰማያዊ ፥ ኢትዮጵያዊ ። አኃዝ ፡ ቅጽልም ፡
ካንድ ፡ እስከ ፡ ምእልፊት ፡ ያለ ፡ ቍጥር ፡ ነው ፤ ኋላ ፡ በቦታው ፡ ይነገራል ።

፻፲፭ ፤ ነባር ፡ ቅጽሎችም ፥ እንደ ፡ ዘር ፡ ቅጽሎች ፡ ፫ ፡ ናቸው ፤ ነባር ፡ ጥሬና ፡
ግልጸ ፡ ዘ ፥ የቦታና ፡ የጊዜ ፡ ቅጽሎች ፥ ንኡስና ፡ ደቂቅ ። ነባር ፡ ጥሬ ፥ የሚበዛና ፡ የማ
ይበዛ ፡ ስም ፡ ነው ፤ የሚበዛ ፡ ስም ፥ እብን ፡ አእባን ፤ ይህን ፡ የመሰለ ። የማይበዛ ፡ የመ
ጠሪያ ፡ ስም ፡ ነው ፤ ዳዊት ፡ ሰሎሞን ፥ የመሰለው ፡ ኹሉ ። ግልጸ ፡ ዘ ፡ የሚባል ፡ ዐበ
ይት ፡ አገባቦች ፡ ዘ ፡ እንተ ፡ እለ ፡ የገቡበት ፡ ዘማች ፡ አንቀጽና ፡ ነባር ፡ አንቀጽ ፡ ነው ፤
የዘ ፡ እንተ ፡ እለም ፡ ዝርዝር ፡ ምስጢሩ ፡ ዘርፍ ፡ አያያዥነት ፡ ስለ ፡ ኾነ ፡ ግልጸ ፡ ዘ ፡ ይባ
ላል ፤ ዘ ፡ ያንድ ፥ እንተ ፡ ያንዲት ፥ እለ ፡ የብዙ ፡ ቅጽል ፡ ነው ። የቦታና ፡ የጊዜ ፡ ቅጽ
ሎች ፡ የተባሉም ፡ የዘንና ፡ የበን ፡ ዐማርኛ ፡ ይዘው ፡ የሚፈቱ ፡ ዐበይት ፡ አገባቦች ፡
ናቸው ፤ የዘን ፡ ዐማርኛ ፡ መያዛቸው ፡ በባለቤቱ ፡ ላይ ፡ አገባብ ፡ ሳይኖር ፡ ነው ፤ አገ
ባብ ፡ ሲኖር ፡ ግን ፡ የዘ ፡ ዐማርኛ ፡ የ ፡ ተበዝብዞ ፡ ይቀራል ፡ እንጂ ፤ አይነገርም ።

፻፲፮ ፤ የቦታ ፡ ቅጽሎች ፡ ኀበና ፡ መንገለ ፡ ውእደ ፡ ናቸው ፤ እነዚህ ፡ ፫ቱ ፡ አገ
ባብ ፡ በሌለው ፡ ሲቀጸሉ ፤ መካን ፡ ኀበ ፡ ይትገበር ፡ መንገለ ፡ ይትገበር ፡ ውእደ ፡ ይት
ገበር ፡ መሥዕተ ፡ ቅዳሴ ፡ ቅዱስ ፡ ውእቱ ፤ የሚደረግበት ፡ ቦታ ። አገባብ ፡ በለውም ፡
ሲቀጸሉ ፤ ውስተ ፡ መካን ፡ ኀበ ፡ ቆመ ፡ መንገለ ፡ ቆመ ፡ ውእደ ፡ ቆመ ፡ እግረ ፡ እግዚእነ ፤
የጌታችን ፡ እግር ፡ ከቆመበት ፡ በቆመበት ፡ ቦታ ፡ ያሰኛሉ ። በነባር ፡ አንቀጽም ፡ ሲገቡ ፤
በምድረ ፡ በድው ፡ ኀበ ፡ አልቦ ፡ መንገለ ፡ አልቦ ፡ ውእደ ፡ አልቦ ፡ ዕፅ ፡ ወማይ ፤ ዕንጨ
ትና ፡ ውሃ ፡ በሌለበት ፡ እያሰኙ ፡ ሌላውን ፡ ኹሉ ፡ ያሳያሉ ። የጊዜም ፡ ቅጽሎች ፡
የሚባሉ ፡ በኀላፊና ፡ በትንቢት ፡ በነባር ፡ አንቀጽ ፡ እየገቡ ፡ የዘን ፡ ዐማርኛ ፡ የበን ፡ ዝር
ዝር ፡ ይዘው ፡ የሚፈቱ ፡ ዐበይት ፡ አገባቦች ፡ አመ ፡ ሶበ ፡ ጊዜ ፡ ሰዓ ፡ ሰዓተ ፡ ዕለተ ፡
መዋዕለ ፡ ዓመተ ፡ ናቸው ። ሲገቡም ፡ በኀላፊ ፡ አመ ፡ ተእኀዘ ፡ ሶበ ፡ ተእኀዘ ፡ እግዚ
እነ ፤ ጌታችን ፡ የተያዘበት ። በትንቢት ፡ አመ ፡ ይብሉ ፡ ሶበ ፡ ይብሉ ፡ ጊዜ ፡ ይብሉ ፡
ብፁዓት ፡ መካናት ፤ መካኖች ፡ ምስጉኖች ፡ ናቸው ፡ የሚሉበት ። በነባርም ፡ አመ ፡ ቦ ፡
ወአመ ፡ አልቦ ፡ እያለ ፡ ይገባል ። የቀሩትም ፡ ሰዓ ፡ ሰዓተ ፡ ዕለተ ፡ መዋዕለ ፡ ዓመተ ፡ ምስጢ
ራቸውን ፡ ይዘው ፡ እየገቡ ፡ ሰዓት ፡ ቀን ፡ ቀኖች ፡ ዘመኖች ፡ ወራት ፡ ዓመት ፡ ተብለው ፡
በያማርኛቸው ፡ ይፈታሉ ። ይህም ፡ በመዋዕለ ፡ ትኤብስ ፤ በምትበድልበት ፡ ወራት ።
በዓመተ ፡ ሞተ ፡ ዖዝያን ፡ ንጉሥ ፤ ንጉሡ ፡ ዖዝያን ፡ በሞተበት ፡ ዓመት ፡ ማለቱን ፡ ያሳ
ያል ። የልክ ፡ ቅጽሎች ፡ የሚባሉም ፡ በኀላፊና ፡ በትንቢት ፡ በነባር ፡ አንቀጽ ፡ እየገቡ ፡
ያኽል ፡ ተብለው ፡ የሚፈቱ ፡ ዐበይት ፡ አገባቦች ፡ መጠነ ፡ አምጣነ ፡ ዐቅመ ፡ ናቸው ።
ሲገቡም ፡ በኀላፊ ፡ ከብረ ፡ ዮሴፍ ፡ መጠነ ፡ አምጣነ ፡ ዐቅመ ፡ ተዋረደ ፡ ወከነ ፡ ገብረ ፤
ዮሴፍ ፡ የተዋረደና ፡ ባሪያ ፡ የኾነውን ፡ ያኽል ፡ ከበረ ። በትንቢት ፥ መጠነ ፡ ይክል ፡

አፉየ ፡ አስተበፅዕ ፡ ዕበየኪ ። በነባርም ፥ መጠነ ፡ ብየ ፡ እሁብ ፤ ያለኝን ፡ ያለብኝን ፡ ያኽል ፡ እሰጣለኹ ፡ ያሰኛል ። የቀረውን ፡ ፍች ፡ በአኃዝ ፡ ቅጽል ፡ መጨረሻና ፡ ባቢይ ፡ አገባብ ፡ ውስጥ ፡ ተመልከት ።

፻፲፯ ፤ ንኡስ ፡ ቅጽልም ፡ የሚባሉ ፡ በንኡስ ፡ አገባብ ፡ የሚገኙ ፡ የጥያቄና ፡ ያንክሮ ፡ ጥሬዎች ፡ አይ ፡ ምንት ፥ አይ ፡ መኑ ፥ አይ ፡ ማእዜ ፥ አይ ፡ አይቴ ፥ አይ ፡ አያት ፥ ስፍን ፡ እስፍንት ፡ ናቸው ። አይ ፡ ምንት ፤ ምን ፡ ምንድር ፤ አያት ፡ ምንታት ፥ ምኖች ፡ ምንድሮች ፤ የነገር ፡ ቅጽሎች ፡ ናቸው ፤ አይ ፡ አያት ፡ ላካልም ፡ ይኾናል ። አይ ፡ መኑ ፥ ማን ፤ አያት ፡ እለ ፡ መኑ ፥ እነማን ፤ ያካል ፡ ቅጽሎች ፡ ናቸው ። አይ ፡ ማእዜ ፥ መች ፡ መቼ ፤ የጊዜ ፡ ቅጽሎች ። አይ ፡ አይቴ ፥ ሐኤት ፡ ወዴት ፤ የቦታ ፡ ቅጽሎች ። አይ ፡ አያት ፥ ማነኛው ፡ ማናቸው ፤ ማነኛቸው ፤ ማናቻቸው ፤ ከፋዮች ። ስፍን ፡ እስፍንት ፥ ስንት ፡ ምን ፡ ያኽል ፤ ቍጥር ፡ ጠያቆች ። የጥያቄያቸውም ፡ ተሰጦና ፡ ምስጢር ፡ አኃዝ ፡ ቅጽል ፡ ነው ፤ አንክሮም ፡ ይኾናል ። አይ ፡ አይቴ ፡ ከአየየ ፥ ስፍን ፡ እስፍንት ፡ ከሰፈነ ፡ የወጡ ፡ ናቸው ፤ ነባርነታቸው ፡ በጠባይ ፡ ነው ፡ እንጂ ፥ በትውልድ ፡ አይዶለም ፡ (ቍ ፲) ። ከማእዜ ፡ በቀር ፡ ኹሉም ፡ ባ፲ ፡ መደብ ፡ ይረባሉ ፤ አኃዝ ፡ ቅጽልም ፡ ከደቂቅ ፡ በኋላ ፡ ይመጣል ።

ደቂቅ ፡ ቅጽል ።

፻፲፰ ፤ በ፳፬ ፡ ቍጥር ፡ በደቂቅ ፡ ርባታ ፡ ቃጥተን ፡ የተውናቸው ፡ ደቂቅ ፡ ቅጽሎች ፡ ከነርባታቸው ፡ ከናፈታታቸው ፡ እሊህ ፡ ናቸው ።

(ሩቅና ፡ ድብቅ) ።

| | |
|---|---|
| ውእቱ ፡ | ርሱ ፡ |
| ይእቲ ፡ | ርሷ ፡ |
| ውእቶሙ ፡ እሙንቱ ፡ | ርሳቸው ፡ እነርሱ ፡ |
| ውእቶን ፡ እማንቱ ፡ | ዝኒ ፡ ከማሁ ። |

(ቅርብ ፡ ፊት ፡ ለፊት ፡ ያለ) ።

| | |
|---|---|
| አንተ ፡ | በቁሙ ፡ አንተ ፡ |
| አንቲ ፡ | አንቺ ፡ ች ፡ |
| አንትሙ ፡ | እላንተ ፡ ት ፡ |
| አንትን ፡ | ዝኒ ፡ ከማሁ ። |

(ነባቢ ፡ ወነባቢት) ።

| | |
|---|---|
| አነ ፡ | እኔ ፡ (ወንድና ፡ ሴት) ፡ |

(ነባብያን ፡ ወነባብያት) ።

| | |
|---|---|
| ንሕነ ፡ | እኛ ፡ (ወንዶችና ፡ ሴቶች) ፡ |

ጭብጥ ፡ ቅጽል ፡ ወይም ፡ አማሬ ፡፡
(የቅርብ ፡ ሩቅ ፡ የሚታይ) ፡፡

| | |
|---|---|
| ዝኩ ፡ ዝስኩ ፡ ዝክቱ ፡ | ያ ፡ ያኛው ፡ |
| እንትኩ ፡ እንታክቲ ፡ | ያች ፡ ያችኛዋ ፡ ይቱ ፡ |
| እልኩ ፡ እልክቱ ፡ | እሊያ ፡ እሊያኞች ፡ ቹ ፡ |
| እልክን ፡ እልክቶን ፡ | ዝኒ ፡ ከማሁ ፡፡ |

(የቅርብ ፡ ቅርብ ፡ የሚዳሰስ) ፡፡

| | |
|---|---|
| ዝ ፡ ዝንቱ ፡ | ይህ ፡ |
| ዛ ፡ ዛቲ ፡ | ይህች ፡ |
| እሉ ፡ እሎንቱ ፡ | እሊህ ፡ |
| እላ ፡ እሎን ፡ እላንቱ ፡፡ | ዝኒ ፡ ከማሁ ፡፡ |

ዝኩ ፡ ዝስኩ ፡ በዮች ፡ አነና ፡ ንሕነ ፡ ስለ ፡ ኹኑ ፡ ርባታው ፡ በ፳ ፡ መደብ ፡ ተወስኗል ፤ ሲዘረዘር ፡ ግን ፡ ከውእቱ ፡ እስከ ፡ ንሕነ ፡ ላሉት ፡ ዘርፍ ፡ አያያዥ ፡ ኹኖ ፡ ይቀጸላል ፡፡

ዚአሁ ፡ እንቲአሁ ፡ እሊአሁ ፡ (ሃ ፡ ሆሙ ፡ ሆን) ፡ — የርሱ ፡ የርሱን ፡ የርሱ ፡ ነው ፡፡
ዚአከ ፡ እንቲአከ ፡ እሊአከ ፡ (ኪ ፡ ክሙ ፡ ክን) ፡ — ያንተ ፡ ያንተን ፡ ያንተ ፡ ነው ፡፡
ዚአየ ፡ (ነ) ፡ — የኔ ፡ የኔን ፡ የኔ ፡ ነው ፡፡ ኹሉን ፡
እንዲህ ፡ ፍታ ፡፡

፬፻፶፱ ፤ የገቢር ፡ ቅጽልና ፡ ዐጸፋ ፡፡ ኪያ ፡ (ዐረብ ፡ ኢያ) ፡ ርስን ፡ ራስን ፡፡
ኪያሁ ፡ (ሃ ፡ ሆሙ ፡ ሆን) ፡ — ርሱን ፡ ራሱን ፡፡
ኪያከ ፡ (ኪ ፡ ክሙ ፡ ክን ፡ የ ፡ ነ) ፡ — አንተን ፡ ራስኽን ፡፡

የተገብሮ ፡ ቅጽልና ፡ ዐጸፋ ፡፡ ለል ፡ (ለለ) ፡ ርስ ፡ ቅል ፡ ራስ ፡፡
ለሊሁ ፡ (ሃ ፡ ሆሙ ፡ ሆን) ፡ ርሱ ፡ ቅሉ ፡ ራሱ ፡ በለቤቱ ፡፡
ለሊከ ፡ (ኪ ፡ ክሙ ፡ ክን ፤ ልየ ፡ ሊነ) ፡ አንተ ፡ ቅልኽ ፡ ራስኽ ፡፡

ደምላይና ፡ ጠቅላይ ፡ ውስጠ ፡ ብዙ ፡፡ ኵል ፡ (ክሉል) ፡ ድምር ፡ ጥቅል ፡፡
ኵሉ ፡ (ላ ፡ ሎሙ ፡ ሎን) ፡ ኵ=ኹሉ ፡ መላው ፡ ጠቅላላው ፡ ፩ ፡ ሳይቀር ፡፡
ኵልከ ፡ (ኪ ፡ ክሙ ፡ ክን ፤ ልየ ፡ ልነ) ፡ ኹልኽ ፡ መላኽ ፡፡
ኵለንታ ፤ (የሕዋሳት ፡ ቅጽል) ፡ ኹለንተና ፡ ኹለመና ፡ ከራስ ፡ እስከ ፡ እግር ፡፡
ኵለንታሁ ፡ (ሃ ፡ ሆሙ ፡ ሆን ፡፡ ከ ፡ ኪ ፡ ክሙ ፡ ክን ፤ የ ፡ ነ) ፡ ኹለንተ(መ)ናው ፡፡

ባሕቲት ፡ (ብሕተ ፡ ባሕተወ) ፡ ብቻ ፡ ብቻነት ፡ ነጠላነት ፡፡
ባሕቲቱ ፡ (ታ ፡ ቶሙ ፡ ቶን ፡፡ ትከ ፡ ኪ ፡ ክሙ ፡ ክን ፤ የ ፡ ነ) ፡ ብቻው ፡ ራሱ ፡፡

ዕራቅ ፤ ዕራቍትነት ፡ ባዶ ፡ ብቻ ፡ ነጠላ ፡ መለመላ ፡ አንዳች ፡ የሌለበት ፡፡
ዕራቁ ፡ (ቃ ፡ ቆሙ ፡ ቆን ፡፡ ቅከ ፡ ኪ ፡ ክሙ ፡ ክን ፤ የ ፡ ነ) ፡ ዕራቍቱ ፡ ባዶው ፡ ብቻው ፡፡

በይን ፡ በይናት ፤ ብቻ ፡ ርስ ፡ ራስ ፡፡ በበይናት ፤ ርስ ፡ በርስ ፡፡
በበይናቲሁ ፡ (ሃ ፡ ሆሙ ፡ ሆን ፡፡ ከ ፡ ክሙ ፡ ክን ፡ ትኪ ፡ ትየ ፡ ቲነ) ፡ ርስ ፡ በርሱ ፡፡

ከንቱ ፤ በቁሙ + ብላሽ ፡ የዝም ፡ ብሎ + ዋጋ ፡ የሌለው ።

በከ ፤ ዝኒ ፡ ከማሁ ፤ ከንቱ ፡ ብላሽ ፡ ጠፍ ። በከት ፡ ሙቶ ፡ ያደረ + ቢያክ ፡ ቢያክ ፡ የሚባል ፡ የሚያስጠይፍ ። የዝርዝሮችም ፡ ጠባይ + ስማቸውና ፡ መልካቸው + ዘመድና ፡ ባዕድ ፡ መባላቸው ፡ ዐጸፋና ፡ ቅጽል ፡ መኾናቸው ፡ ባ፺፯ ፡ ቍጥር ፡ ተነግሯል ፤ ከነባር ፡ ቅጽልም ፡ መቈጠራቸው + በስም ፡ ዐጸፋነት ፡ እየገቡ ፡ ሩቅና ፡ ቅርብ ፡ ፩ና ፡ ብዙ ፡ ወንድና ፡ ሴት ፡ የሚለያዩና ፡ የሚያሳዩ ፡ ስለ ፡ ኾኑ ፡ ነው ።

## ፲፭ኛ ፡ ዕርከን ።

## አኃዝ ፡ ቅጽል ።

፻፳ ፤ አኃዝ ፡ ዘርና ፡ ነባር ፡ ስለ ፡ ኾነ ፡ በዘርነቱ ፡ ከዘር ፡ ቅጽሎች ፡ እንዲስማማ + በነባርነቱም ፡ ከነባር ፡ ቅጽሎች ፡ ከንኡስ ፡ ከደቂቅ ፡ ይሰማማልና ፤ ቍጥሩ ፡ ከ፪ቱም ፡ ነው ። ነባርነቱ ፡ ብ፲፫ኛ ፡ ቍጥር ፡ ተነግሯል ፤ ዘርነቱም ፡ በዝርዝር ፡ ፊደል ፡ ሲጣፍ ፡ ነው ። አኃዝ ፡ ካንድ ፡ እስከ ፡ ምእልፊት ፡ ያለ ፡ የቍጥር ፡ ኹሉ ፡ ጠቅላይ ፡ ስም ፡ ነው ፤ አኃዝ ፡ ማለት + መያዣ ፡ ዐረበን + ወይም ፡ ዥምርና ፡ ውጥን ፡ ማለት ፡ ነው ፤ መያዣው ፡ አንዳንድ ፡ ቅንጣት ፡ ፊደል ፡ (፩ ፡ ፪ ፡ ፫—አ ፡ በ ፡ ገ) ፡ ውጥኑም ፡ ቃል ፡ ነው ፤ አንድ ፡ ኹለት ፡ ሦስት ፡ ማለት ። ከ፺ ፡ እስከ ፻ ፡ ምንም ፡ በየክፍሉ ፡ ፍጹም ፡ ቢሆን ፡ ያንዱ ፡ ቤት ፡ ላሥር + ያሥሩ ፡ ለመቶ + የመቶው ፡ ለሺሕ + የሺሑ ፡ ለእልፍ + የእልፉ ፡ ለምእልፊት ፡ ውጥን ፡ ይባላል ፤ ፲ሩ ፡ የርበታ ፡ መደብ ፡ ለ፻ው ፡ መደብ ፡ ውጥን ፡ እንዲባል ። አኃዝ ፡ ሲባል ፡ ኹሉም ፡ ውስጠ ፡ ዘና ፡ ውስጠ ፡ ብዙ ፡ ስም ፡ ነው ፤ ስፍን ፡ ስፍናዊ ፡ ብሎ ፡ ለሚጠይቅ + ወይም ፡ ለሚያስብ + የብትኖችን ፡ ማነስና ፡ መብዛት + ስንትነትና ፡ ስንተኛነት ፡ ዘርዝሮ ፡ ደምሮ ፡ ለማሳየት ፡ ከባለቤት ፡ በፊት ፡ እየገባ ፡ ዐብሮ ፡ የሚነገር + ባለቤትም ፡ ባይኖር ፡ ርሱው ፡ ራሱ ፡ በቂ ፡ ስለ ፡ ኾነ ፡ ቅጽል ፡ ይባላል ። ርስ ፡ በርሱም ፡ ይቀጻጸላል ። ካንድ ፡ እስከ ፡ ምእልፊት ፡ ያለ ፡ አኃዛዊ ፡ ቍጥር ፡ ባንድ ፡ ረዥም ፡ ገመድ ፡ ሲመሰል ፡ ቤቱና ፡ ክፍሉ ፡ ፩ ፡ ፩ ፡ ይኾኑለታል ፤ ቤት + ፩ ፡ ፲ ፡ ፪ ፡ ፲፪ ፡ ፻ ። ክፍል + መዘርጋት ፡ መተርተር ፡ መክፈል ፡ ማጠፍ ፡ መጠቅለል ፡ ናቸው ። መዘርጋት + ብዛትንና ፡ ስንትነትን ፡ እንደ ፡ ነዶና ፡ እንደ ፡ ቸቦ ፡ አስሮ ፡ ሰብስቦ ፡ የሚያሳይ ፡ የጅምላ ፡ ቍጥር ፡ ነው ። ምሳሌ ፤ ፩ ፡ ፪ ፡ ፲ + እንዲሁ ። መተርተር + ስንትነታቸው ፡ ከታወቀ ፡ ከብዙዎች ፡ ማኸል ፡ ስንተኛነትን ፡ ለይቶ ፡ የሚያሳይ ፡ የተራ ፡ ቍጥር ፡ ነው ። ምሳሌ ፤ ፩ኛ ፡ ፪ኛ ፡ ፲ኛ + እንዲሁ ። መክፈል + የክፍሎችን ፡ ስም ፡ እንደ ፡ ተራ ፡ ቍጥር ፡ እየለየ ፡ በየማዕርጉ ፡ የሚያሳይ ፡ ክፍላዊ ፡ ቍጥር ፡ ነው ። ምሳሌ ፤ መንፈቅ ፡ ሣልሲት ፡ ራብዒት + ወከማሁ ። ማጠፍ ፡ ጅምላውን ፡ ቍጥር ፡ ዐጥፎ ፡ ደርቦ ፡ እያሳየ ፡ በመንታ ፡ መንገድ ፡ የሚወስድ ፡ ያጸፋ ፡ ቍጥር ፡ ነው ። ምሳሌ ፤ አሐዳት + አው ፡ ከዕበተ ፡ አሐዱ + ፩ ፡ ዕጽፍ ። ክልኤታት + አው ፡ ከዕበተ ፡ ክልኤቱ + ፪ ፡ ዕጽፍ + ፬ ፡ ነጠላ ፤ ወከማሁ ። መጠቅለል + እንዳራቱ ፡ ክፍሎች ፡ አኃዝ ፡ ሳይኖረው + በቅጽልነቱ ፡ ማነስና ፡ መብዛት ፡ ሕጸጽና ፡ ምልአት ፡ የሚያሳይ + የአኃዝ ፡ ቅጽ

ሎች ፡ ሰብሳቢና ፡ ከታች ፡ የሚኸን ፡ መድበል ፡ ቍጥር ፡ ነው ፤ ያውም ፡ ኅዳጥ ፡ ብዙኅ ፡ ሁሉ ፡ [illegible] የመሰለ ።

፻፳፩ ፤ ሥራቸውንና ፡ ማፋቸውን ፡ በገመድ ፡ ዘይቤ ፡ ስበን ፡ ጐትተን ፡ መዘር ጋት ፡ መተርተር ፡ ያልናቸው ፡ ጅምላና ፡ ተራ ፡ አከኼዳቸው ፡ እንደ ፡ የዋህና ፡ እንደ ፡ መሠሪ ፡ ርባ ፡ ስለ ፡ ኸነ ፡ ስማቸው ፡ የዋህ ፡ ቍጥርና ፡ መሠሪ ፡ ቍጥር ፡ ይባላል ፤ የዋሁ ፡ ጅምላ ፡ መሠሪው ፡ ተራ ፡ ነው ፤ የቀሩትም ፡ ሦስቱ ፡ መክፈልና ፡ ማጠፍ ፡ መጠቅለል ፡ ያልናቸው ፡ ከፋይና ፡ ዐጣፊ ፡ ጠቅላይ ፡ ይባላሉ ። ጅምላና ፡ ተራ ፡ ካንድ ፡ እስከ ፡ ኻያ ፡ ወንድና ፡ ሴት ፡ እየለዩ ፡ ከዚያ ፡ በላይ ፡ ግን ፡ ሳይለዩ ፡ ዕሥራ ፡ ሠላሳ ፡ በማለት ፡ እያስ ተባበሩ ፡ ይኼዳሉ ፤ ይኸውም ፡ ምእላድ ፡ ሳይኖር ፡ ነው ፤ ምእላድ ፡ ሲኖር ፡ ግን ፡ ዕሥራ ፡ ሠላሳ ፡ ያለውን ፡ ዕሥራዊ ፡ ዊት ፡ ሠላሳዊ ፡ ዊት ፡ ያሰኛልና ፤ ከመለየት ፡ በቀር ፡ ማስ ተባበር ፡ የለም ። የጅምላ ፡ ቍጥር ፡ አጣጣፍና ፡ አፈታት ፡ ፪ ፡ ዐይነት ፡ ነው ፤ አጣጣፍ ፡ በአኃዝ ፡ በፊደል ፤ አፈታት ፡ እንደ ፡ ንባቡ ፡ አንድ ፡ አንዱ ፡ ኹለት ፡ ኹለቱ ፡ እያሉ ፡ በሳድስ ፡ በካዕብ ፡ መጨረስ ፡ ነው ። የሴቶችም ፡ ቍጥር ፡ ካንድ ፡ እስከ ፡ ኻያ ፡ ከፊደል ፡ እንጂ ፡ ከአኃዝ ፡ ጋራ ፡ አይስማማም ፤ ዱብና ፡ ቅል ፡ ነው ። ስለዚህ ፡ አሐት ፡ አሐቲ ፡ ክልኤ ፡ ክልኤቲ ፡ ሠላስ ፡ አርባዕ ፡ ኀምስ ፡ እያለ ፡ በፊደል ፡ ብቻ ፡ ይጣፋል ። አኃዝ ፡ ቅጽል ፡ ዘርና ፡ ነባር ፡ ስለ ፡ ኾነ ፡ ርባታውና ፡ ዝርዝሩ ፡ እስከ፲ ፡ መደብ ፡ ነው ።

፻፳፪ ፤ የወንዶች ፡ ጅምላና ፡ የሴቶች ፡ ጅምላ ፡ ቍጥር ።

| | የወንዶች ። | | የሴቶች ። |
|---|---|---|---|
| ፩ ፡ | አሐድ ፡ ዱ ፡ | አንድ ፡ ዱ ፡ | አሐ(ድ)ት ፡ ቲ ፡ |
| ፪ ፡ | ክልኤ ፡ ት ፡ ቱ ፡ | ኹለት ፡ ቱ ፡ | ክልኤ ፡ ቲ ፡ |
| ፫ ፡ | ሠለስት ፡ ቱ ፡ | | ሠላስ ፡ |
| ፬ ፡ | አርባዕት ፡ ቱ ፡ | | አርባዕ ፡ |
| ፭ ፡ | ኀምስት ፡ ቱ ፡ | ዐምስት ፡ ቱ ፡ | ኀምስ ፡ |
| ፮ ፡ | ሰድስት ፡ ቱ ፡ | | ስሱ ፡ |
| ፯ ፡ | ሰብዐት ፡ ቱ ፡ | | ሰብዑ ፡ |
| ፰ ፡ | ሰምንት ፡ ቱ ፡ | | ሰማኑ ፡ ኒቱ ፡ |
| ፱ ፡ | ተስዐት ፡ ቱ ፡ | ዘጠኝ ፡ ኙ ፡ | ተስዑ ፡ |
| ፲ ፡ | ዐሥርት ፡ ቱ ፡ | ዐሥር ፡ ሩ ፡ | ዐሥሩ ፡ |
| ፲ወ፩ ፡ | ዐሥርት ፡ ወአሐድ ፡ ዱ ፡ | | ዐሥር ፡ ወአሐት ፡ ቲ ፡ |
| ፲ወ፪ ፡ | ዐሥርት ፡ ወክልኤት ፡ ቱ ፡ | | ዐሥር ፡ ወክልኤ ፡ ቲ ፡ |
| ፲ወ፫ ፡ | ዐሥርት ፡ ወሠለስት ፡ ቱ ፡ | | ዐሥር ፡ ወሠላስ ፡ |
| ፲ወ፬ ፡ | ዐሥርት ፡ ወአርባዕት ፡ ቱ ፡ | | ዐሥር ፡ ወአርባዕ ፡ |
| ፲ወ፭ ፡ | ዐሥርት ፡ ወኀምስት ፡ ቱ ፡ | | ዐሥር ፡ ወኀምስ ፡ |
| ፲ወ፮ ፡ | ዐሥርት ፡ ወሰድስት ፡ ቱ ፡ | | ዐሥር ፡ ወስሱ ፡ |
| ፲ወ፯ ፡ | ዐሥርት ፡ ወሰብዐት ፡ ቱ ፡ | | ዐሥር ፡ ወሰብዑ ፡ |
| ፲ወ፰ ፡ | ዐሥርት ፡ ወሰምንት ፡ ቱ ፡ | | ዐሥር ፡ ወሰማኑ ፡ ኒቱ ፡ |

| | | | |
|---|---|---|---|
| ፲ወ፱ ፡ | ዐሥርት ፡ ወተስዐት ፡ ቱ ፡ | | ዐሥር ፡ ወተስዑ ፡ |
| ፳ ፡ | ዕሥራ ፤ ኻያ ፡ ካያ ፥ ካዕበተ ፡ ዮድ ። | | ዕሥራ ፤ ፪ ፡ ጊዜ ፡ ፲ ። |

በወንዶች ፡ ዕሥራ ፡ ወአሐድ ፡ ዱ ፤ በሴቶች ፡ ወአሐት ፡ ቲ ፡ እያለ ፡ እስከ ፡ ፳፱ ፡ እንዲሁ ፡ ተጣፍሮ ፡ ይኼዳል ።

| | | | |
|---|---|---|---|
| ፴ ፡ | ሠላሳ ፡ | በቁሙ ፡ | ሦስት ፡ ዐሥር ፡ |
| ፵ ፡ | አርብዓ ፡ | አርበ ፡ | አራት ፡ ዐሥር ፡ |
| ፶ ፡ | ኀምሳ ፡ | ዐምሳ ፡ | ዐምስት ፡ ዐሥር ፡ |
| ፷ ፡ | ስ(ድ)ሳ ፡ | በቁሙ ፡ | ስድስት ፡ ዐሥር ፡ |
| ፸ ፡ | ሰብዓ ፡ | ሰባ ፡ | ሰባት ፡ ዐሥር ፡ |
| ፹ ፡ | ሰማንያ ፡ | ሰማኒያ ፡ | ስምንት ፡ ዐሥር ፡ |
| ፺ ፡ | ተስዓ ፡ | ዘጠና ፡ | ዘጠኝ ፡ ዐሥር ፡ |
| ፻ ፡ | ምእት ፡ | መቶ ፡ | ዐሥር ፡ ዐሥር ፡ |
| ፲፻ ፡ | አምአት ፥ አው ፡ ዐሥርቱ ፡ ምእት ፡ | | ዐሥር ፡ መቶ ፥ ፩ ፡ ሺሕ ፡ |
| ፳፻ ፡ | ዕሥራ ፡ ምእት ፡ | | ኹለት ፡ ሺሕ ፡ |
| ፴፻ ፡ | ሠላሳ ፡ ምእት ፡ | | ሦስት ፡ ሺሕ ፡ |
| ፵፻ ፡ | አርብዓ ፡ ምእት ፡ | | አራት ፡ ሺሕ ፡ |
| ፶፻ ፡ | ኀምሳ ፡ ምእት ፡ | | ዐምስት ፡ ሺሕ ፡ |
| ፷፻ ፡ | ስሳ ፡ ምእት ፡ | | ስድስት ፡ ሺሕ ፡ |
| ፸፻ ፡ | ሰብዓ ፡ ምእት ፡ | | ሰባት ፡ ሺሕ ፡ |
| ፹፻ ፡ | ሰማንያ ፡ ምእት ፡ | | ስምንት ፡ ሺሕ ፡ |
| ፺፻ ፡ | ተስዓ ፡ ምእት ፡ | | ዘጠኝ ፡ ሺሕ ፡ |
| ፼ ፡ | እልፍ ፡ | (መቶ ፡ ጊዜ ፡ መቶ) ፡ | ዐሥር ፡ ሺሕ ፡ |
| ፲፼ ፡ | ዐሥርቱ ፡ እልፍ ፥ አው ፡ አእላፍ ፡ | | መቶ ፡ ሺሕ ፡ |
| ፳፼ ፡ | ዕሥራ ፡ እልፍ ፥ ሠላሳ ፡ እልፍ ፡ እያለ ፡ እስከ ፡ ፺፱፼ ፡ ይኼዳል ። | | |
| ፻፼ ፡ | አእላፋት ፡ | መቶ ፡ እልፍ ፥ ወይም ፡ ፲፻ ፡ ሺሕ ፡ (ሚልዮን) ፡ | |
| ፲፻፼ ፡ | ትእልፊት ፡ | ሺሕ ፡ እልፍ ፥ ወይም ፡ እልፍ ፡ ሺሕ ፡ (፲ ፡ ሚልዮን) ፡ | |
| ፳፻፼ ፡ | ዕሥራ ፡ ምእት ፡ እልፍ ፡ | እንዲህ ፡ እያለ ፡ እስከ ፡ ፺፻ ፡ ይኼዳል ። | |
| ፼፼ ፡ | ምእልፊት ፡ | እልፍ ፡ ጊዜ ፡ እልፍ ፡ (፻ ፡ ሚልዮን) ። | |

ሐዲስ ፡ ሐሳብ ፡ እንግዳ ፡ ቍጥር ፥ በምእልፊት ፡ ላይ ፡ የሚጨመር ፥ የቢልዮንና ፡ የትሪልዮን ፡ አንጻር ።

ምእልፊትን ፡ ደግሞ ፡ እንደ ፡ እልፍ ፡ ፲ ፡ ፻ ፡ ፲፻ ፡ ፼ ፡ እያሉ ፡ በ፬ቱ ፡ ቅጽሎች ፡ ሲያበዙት ፡ አንድ ፡ የነበረው ፡ ፼ ፡ ምእልፊት ፡ ይኾናል ። ኹለተኛም ፡ በሚልዮንና ፡ በቢልዮን ፡ ተራ ፡ ሲያወርዱት ፥ ትሪልዮን ፡ ከሚባለው ፡ ቍጥር ፡ ይሰማማል ። ከእልፍና ፡ ከአእላፍ ፡ በላይ ፡ ያለ ፡ ቍጥር ፡ በውሱኔም ፡ አለውሱኔም ፡ ይነገራልና ፤ ውሱኔው ፡ ይህ ፡ ነው ። ያለውሱኔ ፡ ግን ፡ ሲነገር ፥ አእላፈ ፡ አእላፋት ፡ ወትእልፊተ ፡ አእላፋት ፡ ምእልፊት ፡ ይላል ፤ ብዛቱ ፡ እንዳሸዋና ፡ እንደ ፡ ኮከብ ፡ ሰፍሮ ፡ ቈጥሮ ፡ ሊያው

ቁት፡የማይቻል፥ከፈጣሪ፡በቀር፡ሰፉሪ፡ቈጣሪ፥ልክና፡መጠን፡የሌለው፡የብዙ፡
ብዙ፡ማለት፡ነው፤ አባይን፡በጫልፋ፡እንዲሉ፡(ዘፍ፲፫፡፲፮። ፲፭፡፭) ።

ሐተታ፡ስላንድ፡ቤት፡ቍጥር ።

፻፳፫ ፤ ሠለስት፡የተባለው፡ሦስት፡መኾኑ፡ለ፡ስለ፡ላላ፡ነው፤ሲጠብቅ፡ግን፡(ሠላሲ፡ሲት፡ስያን፡ያት)፡ሠለስት፡መድበል፡ቅጽል፡ኹኖ፡፫፡የሚያደርጉ፡፫፡አድራጎች፡ያሰኛል፡እንጂ፥፫ነትን፡ወይም፡፫፡መኾንን፡አያሳይምና፤ ከማጥበቅ፡ተጠንቀቅ ። ሰድስት፡ያልነውም፡ስድስት፡ተብሎ፡እንዳማርኛው፡በሳድስ፡ሲነሣ፡ያንዲት፡ሴት፡ውስጠ፡ዘ፡ነውና፥ውስጠ፡ብዙነቱ፡ምንም፡ርግጥ፡ቢኾን፥በሰዋስው፡ሕግ፡ለውስጠ፡ብዙ፡ወንድ፡ሊነገርና፡ጅምላ፡ቍጥር፡ሊኾን፡አይችልም ። አጥብቀን፡ሰምንትና፡ዐሥርት፡ያልናቸውም፡(ሰማኒ፡ኒት፡ንያን፡ያት)፡ዐሣሪ፡ሪት፡ርያን፡ያት)፡ሰመንትና፡ዐሠርት፡ሲባሉ፥አድራጊነትን፡ቢያሳዩ፡እንጂ፥ኂኝነትን፡አያሳዩምና፤ በሰምንትና፡በዐሥርት፡ፈንታ፡ሰመንትና፡ዐሠርት፡ከማለት፡ተጠንቀቅ፤ካንድ፡እስካሥር፡ያሉ፡አኃዞች፡ኹሉም፡በውስጠ፡ብዙነት፡ከተደራጊ፡አንቀጽ፡እንደ፡ወጡ፡አፈታታቸው፡ያስረዳኻል ።

፻፳፬ ፤ ዳግመኛም፡ከክልኤት፡እስከ፡ዐሥርት፡ያለው፡ት፡ምእላድ፡መኾኑን፡የአኃዞችም፡ሥር፡ከሦስት፡ቅንጣት፡ፊደል፡ወዳራት፡አለመውጣቱን፡አስተውል፤ይኸውም፡ምእላድ፡በሌለው፡በአሐድና፡በጊዜያት፡አኃዝ፡ይታወቃል። ት፡ምእላድ፡ኹኖ፡በሳድስነት፡መጨመሩ፡የወንዱን፡ከሴት፡ለመለየትና፡ለማብዛት፥ለመዘርዘርም፡እንዲመች፡ነው ። የዝርዝሩ፡ካዕብነት፡ቱ፡ብእሲሁ፡እንደ፡ማለት፡ኹኖ፡ዐጸፋን፡ብቻ፡ያሳያል፤ዝርዝሩ፡ዐጸፉ፡ባይኾን፡ግን፡በገቢር፡ጊዜ፡የሳድስ፡ወራሽ፡ግእዝ፡እንደ፡ኾነ፥የካዕብም፡ወራሽ፡ሳብዕ፡ነውና፤ አሐዱ፡ክልኤቱ፡ያለውን፡አሐደ፡ክልኤተ፡በማለት፡ፈንታ፡አሐዶ፡ክልኤቶ፡ያሰኝ፡ነበር ። አርባዕት፡ባዕድ፡ከምእላድ፥አርብዓም፡ባዕድ፡ዘር፡ይባላል፤ ባዕድ፡ኹኖ፡ባዕድ፡ያሰኘውም፡አ፡ነው ።

ተራ፡ቍጥር፡በፊደል፡ብቻ ።

፻፳፭ ፤ የተራ፡ቍጥር፡መነሻ፡ኹሉም፡ራብዕ፡ፊደል፡ነው፤ በራብዕ፡ተነሥቶ፡ምእላድ፡ሳይጨምር፡በ፫፡በ፫፡ፊደል፥እየጨመረም፡በ፬፡በ፬፡ፊደል፡ይኼዳል፤ የምእላዶቹም፡(ዊ፡ይ፡ት)፡ሻያ፡መዘርዘርና፡ዐጸፋ፡መኾን፡ነው፤ አንደኛ፡አንደኛው፥አንደኚት፡አንደኛይቱ፡እያልኽ፡ኹሉን፡እንዲህ፡ፍታ፤ ንባቡ፡መንታ፡እንደ፡ኾነ፡ፍችውም፡መንታ፡ነው ። በጅምላና፡በተራ፡ቍጥር፡ከአሐዱና፡ከክልኤቱ፡የሚተባበሩ፥ስለነርሱም፡የሚነገሩ፡ቅጽሎች፡እሊህ፡ናቸው፤ ዋሕድ፡ግእዝ፡አኃዝ፡ጥንት፡መሠረት፡ቀዳም፡ቀዳሚ፡በኵር፥የአሐዱ ። ዳግም፡ካዕብ፡መንታ፡ዘውግ፡ፅምድ፥የክልኤቱ፡ናቸው ።

፻፳፩ ፤ የወንዶችና ፡ የሴቶች ፡ ተራ ፡ ቍጥር ፡፡

| የወንዶች ፡፡ | የሴቶች ፡፡ |
|---|---|
| አሐድ ፡ አሐዳይ ፡ ዊ ፡ | አሐ(ድ)ት ፡ አሐቲ ፡ |
| (ግእዝ ፡ ጥንት ፡ ቀዳሚ ፡ በኵር) ፡ | (ቀዳሚት ፡ ማዪት) ፡ |
| ክልእ ፡ ክልኣይ ፡ ዊ ፡ | ክልእት ፡ ክልኣዪ(ዊ)ት ፡ |
| (ካዕብ ፡ ዳግም ፡ ዳግማይ ፡ ዊ) ፡ | (ዳግምት ፡ ሚት ፡ ማዪት) ፡ |
| ሣልስ ፡ ሣልሳይ ፡ ዊ ፡ | ሣልስት ፡ ሣልሳዊ(ዪ)ት ፡ |
| ራብዕ ፡ ራብዓይ ፡ ዊ ፡ | ራብዕት ፡ ራብዓዊ(ዪ)ት ፡ |
| ኃምስ ፡ ኃምሳይ ፡ ዊ ፡ | ኃምስት ፡ ኃምሳዊ(ዪ)ት ፡ |
| ሳድስ ፡ ሳድሳይ ፡ ዊ ፡ | ሳድስት ፡ ሳድሳዊ(ዪ)ት ፡ |
| ሳብዕ ፡ ሳብዓይ ፡ ዊ ፡ | ሳብዕት ፡ ሳብዓዊ(ዪ)ት ፡ |
| ሳምን ፡ ሳምናይ ፡ ዊ ፡ | ሳምንት ፡ ሳምናዊ(ዪ)ት ፡ |
| ታስዕ ፡ ታስዓይ ፡ ዊ ፡ | ታስዕት ፡ ታስዓዊ(ዪ)ት ፡ |
| ዓሥር ፡ ዓሥራይ ፡ ዊ ፡ | ዓሥርት ፡ ዓሥራዊ(ዪ)ት ፡ |

በወንዶች ፡ ዓሥር ፡ ወአሐድ ፡ ወክልእ ፡ ወሣልስ ፡ እያለ ፡ እስከ ፡ ታስዕ ፥ በሴቶችም ፡ እንደዚሁ ፤ ዕሥራዊ ፡ ት ፡ ሠላሳዊ ፡ ምእታዊ ፡ እልፋዊ ፡ እያለ ፡ እስከ ፡ ምእልፊት ፡ ይኼዳል ፡፡ ሲበዛም ፡ አበዛዙ ፡ ይህ ፡ ነው ፡፡

ቀደምት ፡ ቀዳም(ማው)ያን ፡ ያት ፡ የወንዶችና ፡ የሴቶች ፡፡
ደኅርት ፡ ክልኣን ፡ ኣት ፥ ክልኣው(ይ)ያን ፡ ያት ፡
(ዳግማን ፡ ት ፥ ዳግማው(ይ)ያን ፡ ያት) ፡
ሣልሳን ፡ ት ፥ ሣልሳው(ይ)ያን ፡ ያት ፡
ራብዓን ፡ ት ፥ ራብዓይ(ው)ያን ፡ ያት ፡
ኃምሳን ፡ ት ፥ ኃምሳው(ይ)ያን ፡ ያት ፡
ሳድሳን ፡ ት ፥ ሳድሳው(ይ)ያን ፡ ያት ፡
ሳብዓን ፡ ት ፥ ሳብዓይ(ው)ያን ፡ ያት ፡
ሳምናን ፡ ት ፥ ሳምናው(ይ)ያን ፡ ያት ፡
ታስዓን ፡ ት ፥ ታስዓይ(ው)ያን ፡ ያት ፡
ዓሥራን ፡ ት ፥ ዓሥራው(ይ)ያን ፡ ያት ፡፡

፻፳፪ ፤ የብዙዎች ፡ አኃዝ ፡ በብዙዎቹ ፡ ብቻ ፡ በሦስት ፡ ሰራዊት ፡ በእሙንቱና ፡ በአንትሙ ፡ በንሕነ ፡ ይዘረዘራል ፤ አነሣሡም ፡ አሐዱን ፡ አይሽም ፤ ካንድ ፡ የወጣ ፡ ብዙ ፡ ስለ ፡ ኾነ ፡ ከ፪ ፡ ይነሣል ፡፡ ክልኤሆሙ ፡ ን ፥ ክልኤቶሙ ፡ ን ፥ ክልኤቲሆሙ ፡ ን ፡፡ ክልኤክሙ ፡ ን ፥ ክልኤት ፡ ቲ ፡ ክሙ ፡ ን ፥ ክልኤነ ፡ ክልኤትነ ፡፡ ሠለስቶሙ ፡ ቲሆሙ ፡ ን ፡፡ ሠለስቲክሙ ፡ ክን ፥ ሠለስትነ ፤ እንዲህ ፡ እያለ ፡ እስከሥር ፥ ፍችውም ፡ ሦስታችን ፡ ሦስትነታችን ፡ ያሰኛል ፡፡ ወደ ፡ ተራ ፡ ቍጥር ፡ ሲለወጥ ፡ ግን ፡ አሐዱን ፡ መሠረት ፡ አድርጎ ፡ አሐዶሙ ፡ ክልኦሙ ፡ ሣልሶሙ ፡ እያለ ፡ በራብዕ ፡ ይነሣል ፡፡ ከግእዝ ፡ እስከ ፡ ሳብዕ ፡ ያሉ ፡ የ፯ቱ ፡ ፊደላት ፡ ስምና ፡ ቍጥር ፡ ከወንዶች ፡ ተራ ፡ ስለ ፡ ወጣ ፡ ኹሉም ፡ በወንድነት ፡ ይጠራሉ ፡፡

## የክፍል ፡ ቍጥር ።

፻፳፫ ፤ የብዙዎች ፡ ቍጥር ፡ አሐድን ፡ ትቶ ፡ ከክልኤት ፡ እንደ ፡ ተነሣ ፥ የክፍልም ፡ ቍጥር ፡ ከመንፈቅ ፡ ይነሣል ፤ ተከፋዩ ፡ አሐዱ ፡ ነውና ። ምንም ፡ አካኼዱ ፡ እንደ ፡ ተራ ፡ ቢኾን ፡ ልዩነት ፡ አለው ፤ ለበታና ፡ ለጊዜም ፡ ሲነገር ፡ እንደ ፡ ጅምላ ፡ ነው ።

| | |
|---|---|
| መንፈቅ ፡ ንፍቅ ፡ ክልኢት ፡ | እኩል ፡ እኩሌታ ፡ ፪ኛ ፡ እጅ ፡ |
| ሣልሲት ፡ | ሦስተኛት ፡ ሦስቲያ ፡ ሢሶ ፡ |
| ራብዒት ፡ | ርቢት ፡ አራቲያ ፡ ርቦ ፡ ሩብ ፡ |
| ኃምሲት ፡ | ዐምስተኛት ፡ ዐምስቲያ ፡ ዐምሾ ፡ |
| ሳድሲት ፡ | ስድስተኛት ፡ ስድስቲያ ፡ |
| ሳብዒት ፡ | ሰባተኛት ፡ ሰባቲያ ፡ |
| ሳምኒት ፡ | ስምንተኛት ፡ ስምንቲያ ፡ |
| ታስዒት ፡ | ዘጠነኛት ፡ ዘጠኚያ ፡ |
| ዓሥሪት ፡ | ዐሥረኛት ፡ ዐሥሪያ ፡ ከሥር ፡ አንድ ። |

ሲበዛም ፡ ክልኢታት ፡ ሣልሲታት ፡ ዓሥሪታት ፡ ያሰኛል ። ከ፲ ፡ በላይ ፡ ግን ፡ ክፍልነቱን ፡ ገልጦ ፡ ዐሥርቱ ፡ ወአሐዱ ፡ ክፍል ፡ ዕሥራ ፡ ወክልኤቱ ፡ ክፍል ፡ እያለ ፡ በጅምላና ፡ በየዋህ ፡ ቍጥር ፡ ይኼዳል ። ከክልኢት ፡ እስከ ፡ ዓሥሪት ፡ ያሉ ፡ ስሞች ፡ ኹሉም ፡ በ፲ ፡ በ፲ ፡ መደብ ፡ ይረበሉ ፤ ይህም ፡ መንፈቁ ፡ ቃ ፡ ቆሙ ፡ ቆን ፤ ክልኢቱ ፡ ታ ፡ ቶሙ ፡ ቶን ፥ ትከ ፡ ኪ ፡ ክሙ ፡ ክን ፡ ትን ፡ ማሰኘታቸውን ፡ ያሳያል ። በጅምላም ፡ አካኼድ ፡ ሲነገሩ ፡ ስማቸው ፡ እጅ ፡ ክፍል ፡ እየተባለ ፡ ስንትነታቸውን ፡ ይገልጣል ።

| | |
|---|---|
| ምእሕዲት ፡ | ፩ ፡ እጅ ፡ ፩ ፡ ክፍል ፤ እጅና ፡ ክፍል ፡ ፩ ፡ ወገን ፡ ናቸው ። |
| ምክልኢት ፡ ምክዕቢት ፡ | ፪ ፡ እጅ ፡ ዕጥፍ ፡ ድርብ ፡ |
| ምሥልሲት ፡ | ፫ ፡ እጅ ፡ ፫ ፡ ክፍል ፡ |
| ምርብዒት ፡ | አራት ፡ እጅ ፡ |
| ምኅምሲት ፡ | ዐምስት ፡ እጅ ፡ |
| ምስድሲት ፡ | ስድስት ፡ እጅ ፡ |
| ምስብዒት ፡ | ሰባት ፡ እጅ ፡ |
| ምስምኒት ፡ | ስምንት ፡ እጅ ፡ |
| ምትስዒት ፡ | ዘጠኝ ፡ እጅ ፡ |
| ምዕሥሪት ፡ | ዐሥር ፡ እጅ ፡ |

ሲበዙም ፡ እጅነታቸው ፡ ዕጽፍ ፡ ኹኖ ፥ ምእሕዲታት ፡ ፩ ፡ ዕጽፍ ፡ ፪ ፡ ቀንጃ ። ምክልኢታት ፡ ፪ ፡ ዕጽፍ ፡ ፬ ፡ ቀንጃ ፡ ፬ ፡ ነጠላ ። ምዕሥሪታት ፡ ፲ ፡ ዕጽፍ ፡ ፲ ፡ ጥንድ ፡ ፳ ፡ ነጠላ ፡ ፳ ፡ ቀንጃ ፡ እየተባሉ ፡ እንዲህ ፡ በዕጽፍነት ፡ ይፈታሉ ። እጅ ፡ ማለትና ፡ ዕጽፍ ፡ ማለት ፡ ልዩ ፡ እንደ ፡ ኾነ ፡ አስተውል ። ለበታም ፡ ሲቀጸል ፥ ምእሕዲት ፡ ብሎ ፡ ፩ ፡ ክፍል ፡ ፩ ፡ አውራጃ ፡ ፩ ፡ ጋሻ ፡ ወይም ፡ ቀላድ ፤ ፩ ፡ ወገን ፡ ፩ ፡ ፈት ፡ ፩ ፡ እመም ፡ ፩ ፡

ገዝም ፡ ፩ ፡ አፍታ ፡ ፩ ፡ ወረሬ ፡ ፩ ፡ ፈፋ ፡ ፩ ፡ ቃዳ ፡ ፩ ፡ ተለላ ፡ ያሰኛል ። ከምክልኢት ፡ እስከ ፡ ምዕሥሬት ፡ ኹሉን ፡ እንዲህ ፡ ፍታ ።

፻፹፱ ፤ (በጥሬነታቸው ፡ የክፍልን ፡ ኹነታ ፡ የሚያሳዩ ፡ ጥሬዎች) ።

| | | |
|---|---|---|
| ትእሕ(ድ)ዲት ፡ እሕድና ፡ | አንድነት ፡ | ፩ኛነት ፡ |
| ትክልእት ፡ ክላኤ ፡ | ኹለትነት ፡ | ፪ኛነት ፡ |
| ትሥልስት ፡ ሥላሴ ፡ | ሦስትነት ፡ | ፫ኛነት ፡ |
| ትርብዕት ፡ ርባዔ ፡ | አራትነት ፡ | ፬ኛነት ፡ |
| ትኀምስት ፡ ኀማሴ ፡ | ዐምስትነት ፡ | ፭ኛነት ፡ |
| ትስድስት ፡ ስዳሴ ፡ | ስድስትነት ፡ | ፮ኛነት ፡ |
| ትስብዕት ፡ ስባዔ ፡ | ሰባትነት ፡ | ፯ኛነት ፡ |
| ትስምንት ፡ ስማኔ ፡ | ስምንትነት ፡ | ፰ኛነት ፡ |
| ትስዒት ፡ ትሳዔ ፡ | ዘጠኝነት ፡ | ፱ኛነት ፡ |
| ትዕሥርት ፡ ዕሣሬ ፡ | ዐሥርነት ፡ | ፲ኛነት ፡ |

## የዕለታት ፡ አኃዝ ።

፻፺ ፤ አሚር ፡ በጽርእና ፡ በቅብጥ ፡ (ኢሜራ) ፡ ዕለት ፡ ነው ፡ እንጂ ፥ አኃዝ ፡ አይ ዶለም ፤ ስለዚህ ፡ ቅጽል ፡ አይኾንም ። ሰኑይም ፡ በዕብራይስጥ ፡ (ሼኒ) ፡ ተራ ፡ ቍጥር ፡ ነው ፤ ፪ኛ ፡ ያሰኛል ፡ እንጂ ፥ ፪ ፡ አያሰኝም ፤ አሚርና ፡ ሰኑይ ፡ እነዚህ ፡ ፪ቱ ፡ በኣሐ ድና ፡ በክልእ ፡ ቦታ ፡ ስለ ፡ ገቡ ፡ በነዚያ ፡ ዘይቤ ፡ ይፈታሉ ። የእሑድና ፡ የቅዳሜም ፡ ስማቸው ፡ ተፋልሷል ፤ እሑድን ፡ አሐድ ፡ ቀዳም ፡ ቀዳሚት ፡ በማለት ፡ ፈንታ ፡ በው ስጠ ፡ ዘ ፡ ንባብ ፡ እሑድ ፡ ብሎ ፡ አንደኛ ፡ ማለት ፤ ቅዳሜንም ፡ ሰቡዕ ፡ ሳብዕት ፡ በማ ለት ፡ ፈንታ ፡ ቀዳም ፡ ቀዳሚት ፡ ብሎ ፡ በእሑድ ፡ ስም ፡ መጥራት ፡ የመሳሳት ፥ ቋንቋ ፡ ያለማስተዋል ፡ ጓዝ ፡ ነው ፡ እንጂ ፤ የታረመ ፡ ግእዝ ፡ አይዶለም ። አይሁድም ፡ ሰኑ ይን ፡ ሼኒ ፡ (፪ኛ) ፡ ማለታቸው ፡ እሑድን ፡ ሪሾን ፡ (ቀዳም ፡ ቀዳሚ) ፡ ብለው ፡ ነው ። ፮ኛውም ፡ ቀን ፡ እንደ ፡ ሸማኔ ፡ ዕቃ ፡ ዐርብ ፡ መባሉ ፡ የፊት ፡ ግንዱን ፡ እሑድ ፡ ተጠ ግቶ ፡ ከሰኞ ፡ እስከሙስ ፡ ያሉትን ፡ ልብ ፡ ባለማድረግ ፡ ነው ፡ እንጂ ፤ ዐሥርነት ፡ ባለው ፡ በመዘራዝሩ ፡ በተራ ፡ ቍጥር ፡ ሕግ ፡ አይዶለም ። የዐርብ ፡ ዘይቤ ፡ በግእዝም ፡ በዕብራ ይስጥም ፡ ሠርክ ፡ ነውና ፤ አኃዝ ፡ ኹኖ ፡ ዕለት ፡ ከመባል ፥ ወይም ፡ የዕለት ፡ ስምና ፡ ቅጽል ፡ ከመኾን ፡ አይገባም ። ከሰኑይ ፡ እስከ ፡ ዐሡር ፡ ያሉ ፡ የዕለታት ፡ ስሞች ፡ ከሣ ልስና ፡ ከሳድስ ፡ ውስጠ ፡ ዘ ፡ ስለ ፡ ተዴቀሉ ፡ በግእዝ ፡ ተነሥተው ፡ ከዕብ ፡ እያስከ ተሉ ፡ በሳድስ ፡ ይጨርሳሉ ፤ አፈታታቸውም ፡ ፪ ፡ ነው ፤ እንደ ፡ ጅምላና ፡ እንደ ፡ ተራ ። እሑድ ፡ አሐድ ፡ አሚር ፤ አንድ ፡ አንደኛ ፡ መበቻ ፡ መዠመሪያ ። ሰኑይ ፡ ሠሉስ ፡ ረቡዕ ፡ ኀሙስ ፡ ሰዱስ ፡ ሰቡዕ ፡ ሰሙን ፡ ተሱዕ ፡ ዐሡር ፤ ዐሥር ፡ ዐሥረኛ ፥ ኹሉን ፡ እንዲህ ፡ ፍታ ። አመና ፡ በ ፡ ሲጨመሩባቸው ፡ መድረሻቸውን ፡ እየዘረዘሩ ፡ ከወርኃ ፡ ተስማም ተው ፡ በሳድሱ ፡ ለጽልመት ፡ ወርኃ ። አመ ፡ ዐሡሩ ፡ ወአሚሩ ፥ አመ ፡ ዕሥራ ፡ ወሰኑዩ ፡

እያሰኙ ፡ እስከ ፡ ፴ ፡ ይኼዳሉ ፤ ጥፈታቸውም ፡ ከፊደል ፡ እንጂ ፡ ከአኃዝ ፡ ጋራ ፡ አይተ ባበርም ፤ የጊዜያትም ፡ ክፍል ፡ እንዲሁ ፡ ነው ።

፻፴፩ ፤ የጊዜያት ፡ አኃዝ ።

| | | |
|---|---|---|
| እሕድ ፡ ምዕር ፡ | እሕደ ፡ ምዕረ ፡ | ፩ ፡ ጊዜ ፥ በ፩ ፡ ጊዜ ፡ |
| ክልኢ ፡ | ክልአ ፡ | |
| ሥልስ ፡ | ሥልሰ ፡ | |
| ርብዕ ፡ | ርብዐ ፡ | |
| ኅምስ ፡ | ኅምሰ ፡ | |
| ስድስ ፡ | ስድሰ ፡ | |
| ስብዕ ፡ | ስብዐ ፡ | |
| ስምን ፡ | ስምነ ፡ | |
| ትስዕ ፡ | ትስዐ ፡ | |
| ዕሥር ፡ | ዕሥረ ፡ | ዐሥር ፡ ጊዜ ፥ በሥር ፡ ጊዜ ። |

ዳግመኛም ፡ አሐደ ፡ ጊዜ ፡ ክልኤተ ፡ ጊዜ ፥ ሰብዐተ ፡ ጊዜያተ ፡ እያሰኘ ፡ በጅምላ ፡ ቍጥር ፡ ይነገራል ፤ ከሥራንድም ፡ በላይ ፡ እንደዚሁ ።

፻፴፪ ፤ የዕጽፍ ፡ ቍጥር ።

| | |
|---|---|
| አሐዳት ፥ አው ፡ ከዕበተ ፡ አሐዱ ፡ | ፩ ፡ ዕጽፍ ፡ |
| ክልኤታት ፥ አው ፡ ከዕበተ ፡ ክልኤቱ ፡ | ፪ ፡ ዕጽፍ ፡ |
| ሠለስታት ፥ ከዕበተ ፡ ሠለስቱ ፡ | ፫ ፡ ዕጽፍ ፡ |
| አርባዕታት ፥ ከዕበተ ፡ አርባዕቱ ፡ | ፬ ፡ ዕጽፍ ፡ |
| ኀምስታት ፥ ከዕበተ ፡ ኀምስቱ ፡ | ፭ ፡ ዕጽፍ ፡ |
| ሰድስታት ፥ ከዕበተ ፡ ሰድስቱ ፡ | ፮ ፡ ጥንድ ፡ |
| ሰብዐታት ፥ ከዕበተ ፡ ሰብዐቱ ፡ | ፯ ፡ ጥንድ ፡ |
| ሰምንታት ፥ ከዕበተ ፡ ሰምንቱ ፡ | ፰ ፡ ጥንድ ፡ |
| ተስዐታት ፥ ከዕበተ ፡ ተስዐቱ ፡ | ፱ ፡ ጥንድ ፡ |
| ዐሥርታት ፥ ከዕበተ ፡ ዐሥርቱ ፡ | ፲ ፡ ዕጽፍ ። |

ዐሥርታት ፡ ወአሐዳት ፥ ወይም ፡ ከዕበተ ፡ ዐሥርቱ ፡ ወአሐዱ ፤ ፲፩ ፡ ዕጽፍ ። ዕሥራት ፥ ከዕበተ ፡ ዕሥራ ፤ ሠላሳት ፡ ከዕበተ ፡ ሠላሳ ፡ እያለ ፡ እስከ ፡ ምእልፊት ፡ ይኼዳል ። የጊ ዜም ፡ አኃዞች ፡ እሕዳት ፡ ምዕራት ፡ ሲባሉ ፡ እንደ ፡ ምእሕዲታት ፡ ዕጽፍ ፡ ያሰኛሉ ፤ ክልኣት ፡ ሥልሳት ፡ ርብዓት ፡ ኅምሳት ፡ ስድሳት ፡ ስብዓት ፡ ስምናት ፡ ትስዓት ፡ ዕሥ ራት ፡ እያሰኙ ፡ ኹሉም ፡ ዕጽፍ ፡ ይኾናሉ ።

ሳድስ ፡ ውስጠ ፡ ዘ ።

| | |
|---|---|
| እሑድ ፤ ዋሕድ ፡ (ዳን ፡ ት ፡ ሕድ) ፡ | የታነደ ፡ እንድ ፥ አንድ ፡ የኾነ ፡ አንድ ፡ አን ዲዮ ፡ ውስጠ ፡ ብዙ ፤ ኹሉን ፡ እንዲህ ፡ ፍታ ። |
| ክሉእ ፡ (ኣን ፡ ኣት ፡ ልእት) ፡ | የተኾለተ ፡ ኹልት ፥ ኹለቶ ፡ ኹለቲዮ ፡ |

| | |
|---|---|
| ምንትው ፡ (ዋን ፡ ዋት ፡ ቱት) ፡ | የመነታ ፥ መንቶ ፡ መንቲዮ ፡ |
| ሥሉስ ፡ (ሳን ፡ ሳት ፡ ልስት) ፡ | የተሠለሰ ፡ ሥልስ ፥ ሦስቶ ፡ ሦስቲዮ ፡ |
| ርቡዕ ፡ (ዓን ፡ ዓት ፡ ብዕት) ፡ | የታረተ ፡ እርት ፥ አራቶ ፡ አራቲዮ ፡ |
| ኀሙስ ፡ (ሳን ፡ ሳት ፡ ምስት) ፡ | የታመሰ ፡ ዕምስ ፥ ዐምስቶ ፡ አምስቲዮ ፡ |
| ስዱስ ፡ (ሳን ፡ ሳት ፡ ድስት) ፡ | የተሰደሰ ፡ ስድስ ፥ ስድስቶ ፡ |
| ስቡዕ ፡ (ዓን ፡ ዓት ፡ ብዕት) ፡ | የተሰበተ ፡ ስብት ፥ ሰባቶ ፡ ቲዮ ፡ |
| ስሙን ፡ (ናን ፡ ናት ፡ ምንት) ፡ | የተሰመነ ፡ ስምን ፥ ስምንቶ ፡ |
| ትሱዕ ፡ (ዓን ፡ ዓት ፡ ስዕት) ፡ | የተዘጠነ ፡ ዝጥን ፥ ዘጠኞ ፡ ኒዮ ፡ |
| ዕሡር ፡ (ራን ፡ ራት ፡ ሥርት) ፡ | የታሠረ ፡ ዕሥር ፥ ዐሥሮ ፡ ዐሥሪዮ ፡ ብሎ ፡ |

በዚሁ ፡ ይቆማል ፤ ከሥር ፡ አይወጣም ።

## የመስፈሪያና ፡ የሚዛን ፡ ዕጽፍ ።

| | |
|---|---|
| መእሕድ ፡ | ፪ቱን ፡ ፩ ፡ የሚያደርግ ፡ |
| መክልእ ፡ | ፬ቱን ፡ ፪ ፡ የሚያደርግ ፡ |
| መሥልስ ፡ | ፮ቱን ፡ ፫ ፡ የሚያደርግ ፡ |
| መርብዕ ፡ | ፰ቱን ፡ ፬ ፡ የሚያደርግ ፡ |
| መኀምስ ፡ | ፲ሩን ፡ ፭ ፡ የሚያደርግ ፡ |
| መስድስ ፡ | ፲፪ቱን ፡ ፮ ፡ የሚያደርግ ፡ |
| መስብዕ ፡ | ፲፬ቱን ፡ ፯ ፡ የሚያደርግ ፡ |
| መስምን ፡ | ፲፮ቱን ፡ ፰ ፡ የሚያደርግ ፡ |
| መትስዕ ፡ | ፲፰ቱን ፡ ፱ ፡ የሚያደርግ ፡ |
| መዕሥር ፡ | ፳ውን ፡ ፲ ፡ የሚያደርግ ። |

፪ኛ ፡ መንገድ ፥ መእሕድ ፤ ብዙውን ፡ ፩ ፡ የሚያደርግ ። መክልእ ፤ አንዱን ፡ ፪ ። መሥልስ ፤ አንዱን ፡ ፫ ። መዕሥር ፡ አንዱን ፡ ፲ ፡ የሚያደርግ ፡ እያሉ ፡ አንድን ፡ ተከፋይ ፡ አድርጎ ፡ ሲፈቱት ፡ ዕጽፍነቱ ፡ ቀርቶ ፡ ዝርዝርና ፡ ብትን ፡ ይኾናል ። ሲበዛም ፡ መአሕድ ፡ መክልእ ፡ መሣልስ ፡ እያለ ፡ እስከ ፡ መዓሥር ፡ ይኼዳል ፤ መ ፡ ባይኖር ፡ ግን ፡ ከእሕድ ፡ እስከ ፡ ዕሥር ፡ ኹሉም ፡ የጊዜ ፡ አኃዝ ፡ ናቸው ።　　የአኃዝ ፡ ነገር ፡ እስከ ዚህ ፡ ነው ።

## ደምላይና ፡ ጠቅላይ ፡ መድበላዊ ፡ ቍጥር ።

፪፻፫ ፤ ኵል ፡ ኵሉ ፤ ኹሉ ፡ መላው ፡ ጠቅላላው ፥ ካንድ ፡ እስከ ፡ ምእልፊት ፡ ያለው ፤ ወይም ፡ በየክፍሉ ፡ ፍጹምነት ፡ ያለው ፡ ያ፫ቱ ፡ ቤት ፡ ቍጥር ፡ አንዱም ፡ አንዱም ፡ ኹሉ ። ስፍርና ፡ ቍጥር ፡ ለሌለውም ፡ ከታች ፡ ይባላል ፤ ርባታው ፡ በደቂቅ ፡ ቅጽል ፡ ተነግሯል ፡ (ቍ፪፲፱) ። ኵል ፡ ኵሉ ፡ ማለት ፡ አሐድ ፡ አሐዱ ፡ እንደ ፡ ማለት ፡ ነው ፤ አሐዱና ፡ ኵሉ ፡ ይዋረሳሉ ፤ ኵሉ ፡ አሐዱ ፡ በማለት ፡ ፈንታ ፡ አሐዱ ፡ አሐዱ ፡ ወይም ፡ ብእሲ ፡ ብእሲ ፡ ይላል ፤ ኵሉ ፡ ብእሲ ፡ ማለት ፡ ነው ። ኵሉን ፡ የመሰሉ ፡ ቅጽሎች ፤ ምሉእ ፡ ፍጹም ፡ ብዙኅ ፡ ንሕኑሕ ፡ ዝሕዙሕ ፡ ፍድፉድ ፤ ከፋዮቻቸውም ፡

ንኡስ ፡ ሕጹጽ ፡ ኅዳጥ ፡ ውሑድ ፥ ንስቲት ፡ ሕቅ ፡ መጠን ፡ አምጣን ፡ ዐቅም ፡ ናቸው ። ኵል ፡ የክሉል ፡ ክፋይ ፡ ነው ፤ ሲዘረዘርም ፥ ኵሉ ፡ ኵላ ፡ ሎሙ ፡ ሎን ፤ ኵልክ ፡ ኪ ፡ ክሙ ፡ ክን ፥ ኵልየ ፡ ኵልነ ፡ እያሰኘ ፡ ጠብቆ ፡ ይነገራል ። ዕብራውያንም ፡ እንደዚሁ ፡ ባ፲ ፡ ሰራዊት ፡ ይዘረዝሩታል ፤ አንዳንድ ፡ ባላገባቦች ፡ ግን ፡ ከ፲ቱ ፡ በቀር ፥ አንተ ፡ አንቲ ፡ አነ ፡ ባለው ፡ በነዚህ ፡ በ፫ቱ ፡ የለውም ፡ ብለው ፡ ያውጃሉ ።

፪፻፩ ፤ መጠንና ፡ አምጣን ፡ ዐቅም ፡ የልክ ፡ ቅጽልና ፡ አገባብ ፡ ተብለው ፡ ከበዕድ ፡ ቅጽሎችና ፡ ከበይት ፡ አገባቦች ፡ ተቈጥረዋል ። ምስጢራቸው ፡ የአኃዝ ፡ ግምት ፡ ስለ ፡ ኾነ ፥ በስፍር ፡ በቍጥር ፡ በአኃዝ ፡ ፈንታ ፡ እየገቡ ፡ ያኽል ፡ ተብለው ፡ ሲፈቱ ፡ ግምታቸው ፡ ምሉእና ፡ ሕጹጽ ፡ ያሳያል ። ምሉእ ፥ መጠኑ ፡ ለረድእ ፡ ከመ ፡ ሊቁ ፥ በአምጣነ ፡ ብሒሩ ፡ ዘርዐ ፤ ዐቅመ ፡ ቆመ ፡ ብእሲ ። ሕጹጽ ፥ መጠነ ፡ ትክል ፡ ጹር ፤ መጠነ ፡ በ ፡ ውስተ ፡ እዴከ ፤ ወነበረት ፡ ማርያም ፡ ኀቤሃ ፡ መጠነ ፡ ሠለስቱ ፡ አውራኅ ። ዳግመኛም ፡ ቅጽል ፡ ሲኾኑ ፡ አገባቦች ፥ አገባብ ፡ ሲኾኑ ፡ ቅጽሎች ፡ ኹነው ፡ ይገኛሉ ፤ ይህም ፥ ተዋረደ ፡ ፈርዖን ፡ አምጣነ ፡ (መጠነ ፡ ዐቅመ) ፡ አስተዋረዶሙ ፡ ለእስራኤል ፡ ባለው ፡ ይታወቃል ። ሲፈታም ፡ በገባብነቱ ፥ እስራኤልን ፡ አዋርዷቸዋልና ፥ እንዳዋረዳቸው ፡ መጠን ፥ ባዋረዳቸው ፡ ልክ ፡ ስላዋረዳቸው ፡ አሰኝቶ ፥ በቅጽልነቱም ፡ ያዋረዳቸውን ፡ ያኽል ፡ ያሰኛልና ፥ መታወቂ ፡ ይህ ፡ ነው ፤ የቀረውን ፡ ባገባብ ፡ ተመልከት ። ፬ቱን ፡ ክፍል ፡ እንዳ፬ ፡ ጣት ፡ ፲፫ቱን ፡ ዕርከን ፡ እንደ ፡ ቀለበት ፡ አድርጎ ፥ የሰዋስውን ፡ ሕዋሳትና ፡ ጌጥ ፡ ንዋያተ ፡ ውስጥ ፡ ሰፍሮና ፡ ቈጥሮ ፡ ዘርዝሮ ፡ ደምሮ ፡ ለ፪ኛው ፡ ምዕራፍ ፡ የሚያስረክብና ፡ የሚሰጥ ፡ የሚያስተላልፍ ፡ ፩ኛው ፡ ምዕራፍ ፡ ተፈጸመ ። ያለፈው ፡ ንባብ ፤ የሚመጣው ፡ መትርጒም ።

## ፪ኛ ፡ ምዕራፍ ፡ ባለ፫ ፡ ክፍል ፡ ኅረ ፡ ቤተ ፡ ሥሉስ ፡ አካል ።

ጸዋትወ ፡ ክፍሉም ፡ ጸዋትወ ፡ ንባብ ፤ ጸዋትወ ፡ አገባብ ፤ ጸዋትወ ፡ ቅኔ ፤ የሠምና ፡ የወርቅ ፡ አንጥረኞች ፡ እነተዋኔ ፥ እንደነኤልያብ ፡ ስለ ፡ ደብተራ ፡ ሕግ ፡ ሥልጣኔ ፥ በመንፈስ ፡ ጥበብ ፡ የሠሩት ፡ የንባብ ፡ ሽልማት ፡ ውሳኔ ፤ የጸያፎችም ፡ መታጠቢያ ፡ ጥሩ ፡ ፈሳሽ ፡ ትምርት ፡ ማየ ፡ ቤተ ፡ ግእዝ ፡ ብለኔ ። ወይም ፡ የሰዋስው ፡ ሥዕርተ ፡ ርእስ ፥ ከ፺ ፡ ቀለም ፡ ቀንድ ፡ በተሠራው ፡ በፊደላት ፡ ሚዶ ፡ በጥሩ ፡ ግስ ፥ የሚበጠርና ፡ የሚነቀስ ፤ ከሎታ ፡ ንባቡ ፡ የዕንቍ ፥ ወለባ ፡ ምስጢሩ ፡ የወርቅ ፥ የሚያንጸባርቅ ። መምህራንም ፡ የግእዝን ፡ ቋንቋ ፡ አልብኪ ፡ ነውር ፡ ወኢምንትኒ ፡ ላዕሌኪ ፡ እያሉ ፡ እንደ ፡ መርዓዊና ፡ እንደ ፡ መርዓት ፡ ሸልመው ፡ አስጊጠው ፡ አንቈጥቍጠው ፡ ለተማሮች ፡ የሚድሩበት ።

## ፫ኛ ፡ ክፍል ።

ጸዋትወ ፡ ንባብ ፥ የሰዋስው ፡ ግቢ ፡ ቤተ ፡ ሰብ ፥ ርስ ፡ በርሱ ፡ የሚዛረፍና ፡ የሚናበብ ፥ ተናበና ፡ ወድቆም ፡ የሚሳሳብ ፤ ሳቢ ፡ ከተሳቢ ፡ ዘርፍ ፡ ከባለቤት ፥ ቅጽል ፡ ከባ

ለቤት ፡፡ እነዚህም ፡ ፫ቱ ፡ አርእስቶች ፡ በ፫ኛውና ፡ በ፬ኛው ፡ ክፍል ፡ ነጠላና ፡ ቀንጃ ፡ እየኾኑ ፡ ኹሉም ፡ ብቻ ፡ ብቻቸውን ፡ ተነግረዋል ፡፡ የሳቢና ፡ የተሳቢ ፡ ዐዋጅ ፤ ለመ ምህርና ፡ ለተማሪ ፡ ለቅኔ ፡ ፈጣሪ ፡ መንገድ ፡ የሚጠርግ ፡ የሚያዘጋጅ ፤ ለባለመጽሐ ፍም ፡ ለተርጓሚ ፡ ላንባቢ ፡ ለሰሚ ፡ የሚበጅ ፡፡ ዝርዋን ፡ ቃላት ፡ እንደ ፡ ድባና ፡ እንደ ፡ ማርዳ ፡ እንደ ፡ ድሪ ፡ እንደ ፡ ሰንሰለት ፥ ወይም ፡ እንደ ፡ ዋንጫ ፡ እንደ ፡ ሕዋ ሳት ፡ ርስ ፡ ብርሳቸው ፡ የሚያያዙና ፡ የሚሳኩ ፡ የሚሳመኩ ፡ በ፮ ፡ ነገር ፡ ነው ፤ በዘ ርፍ ፥ በቅጽል ፥ በባለቤት ፡ በዝርዝር ፥ በሳቢና ፡ በተሳቢ ፥ በገባብ ፥ በሠምና ፡ በወርቅ ፡፡ የነዚህንም ፡ ሕግ ፡ ለውጠው ፡ በልዩነት ፡ የሚነገሩ ፡ ፬ቱ ፡ ባህሎች ፥ ብትን ፥ ሙሻ ዘር ፡ ሠረዝና ፡ አንጻር ፡ እንደኒሁ ፡ ናቸው ፤ ኋላ ፡ በቦታቸው ፡ ይነገራሉ ፡፡ አንቀጽን ፡ ቅጽልን ፡ ዝርዝርን ፡ ከባለቤት ፡ ጋራ ፡ በሩቅና ፡ በቅርብ ፥ ባንድና ፡ በብዙ ፥ በወንድና ፡ በሴት ፡ አስማምቶ ፡ ለመናገርና ፡ ለመጣፍ ፥ የተጣፈውንም ፡ ድርሰትና ፡ ቅኔ ፡ ለማመ ስገንና ፡ ለመንቀፍ ፡ ፍጹም ፡ ጥንቃቄ ፡ ያስፈልጋል ፡፡ መጽሐፍ ፡ ግን ፡ በመላሾችና ፡ በጣፎች ፡ ስሕተት ፡ የሰዋስውን ፡ ሕግ ፡ ሳይጠብቅ ፡ ሩቁን ፡ በቅርብ ፡ ቅርቡን ፡ በሩቅ ፥ አንዱን ፡ በብዙ ፡ ብዙውን ፡ ባንድ ፥ ወንዱን ፡ በሴት ፡ ሴቱን ፡ በወንድ ፡ እያደባለቀ ፡ ይናገራል ፤ አነጋገሩም ፡ ይህ ፡ ነው ፡፡ ተባዕተ ፡ ወአንስተ ፡ ፈጠሮሙ ፤ ሜጡ ፡ ለተባ ዕት ፡ ኀምሳ ፥ ወለአንስትሰ ፡ ሜጣ ፡ ሠላሳ ፤ ፀር ፡ እኩይ ፥ ቢጽ ፡ ሀካይ ፡ ብሎ ፡ ስላንድ ፡ የተናገረውን ፡ መልሶ ፡ ደግሞ ፡ ስለ ፡ ብዙ ፥ አእንስት ፡ ወይም ፡ አንስትያት ፥ አፅራር ፥ አብያጽ ፡ በማለት ፡ ፈንታ ፥ ጠባባት ፡ አንስት ፡ ሐነጻ ፡ አብያተ ፤ ተጋብኡ ፡ ፀር ፡ እኩ ያን ፥ ወቢጽ ፡ ሐሳውያን ፤ ይቤሎሙ ፡ ለቢጹ ፡ አርዳእ ፡ ይላል ፡፡ አንባቢ ፡ ሆይ ፡ በመጻሕፍት ፡ ውስጥ ፡ ይህን ፡ የመሰለ ፡ ብዙ ፡ ዐይነት ፡ ጸያፍ ፡ አለና ፤ አሕጻከ ፡ ስሑል ፥ ዘእንበለ ፡ ይቁም ፡ አድባር ፥ ተቈጣዕክዎሙ ፡ ለይእቲ ፡ ትውልድ ፡ እያለ ፡ አላገባቡ ፡ ገብቶና ፡ ተጥፎ ፡ ብታገኝ ፡ እንደዚህ ፡ ያለው ፡ ጸያፍ ፡ ንባብ ፡ ኹሉ ፡ የመላሽና ፡ የጸ ሓፊ ፡ ስሕተት ፡ እንደ ፡ ኾነ ፥ የግእዝ ፡ ሕግና ፡ የሰዋስው ፡ ሥርዐት ፡ እንዳይዶለ ፡ አስ ተውል ፡፡ መተርጕማን ፡ ግን ፡ የተቀዳበትን ፡ ጽርኡንና ፡ ዐረቡን ፡ ዕብራይስጡንም ፡ ስላላዩት ፥ መጽሐፍ ፡ ምስጢር ፡ ብቻ ፡ እንጂ ፡ ሕገ ፡ ሰዋስው ፡ አይጠብቅም ፥ አንድና ፡ ብዙ ፡ ወንድና ፡ ሴት ፡ ቅርብና ፡ ሩቅ ፡ አይጠነቀቅም ፡ ብለው ፡ ያውጁና ፥ ጸያፍን ፡ ኹሉ ፡ ልማደ ፡ መጻሕፍት ፡ ይሉታል ፡፡ በገድል ፡ በታምር ፡ በቅኔ ፡ በመልክና ፡ በሰላምታ ፡ ድርሰት ፡ ብዙ ፡ ጸያፍ ፡ አለመገኘቱ ፡ ስለ ፡ ምን ፡ ነው ፡ ብትል ፥ ሥሩና ፡ ምንጩ ፡ ግእዝ ፡ ብቻ ፡ ስለ ፡ ኾነለት ፥ አበባውም ፡ ድርሰት ፡ ከግእዝ ፡ መምህራን ፡ ስለ ፡ ፈነዳና ፡ ከሌላ ፡ ቋንቋ ፡ ስላልተቀዳ ፡ ነው ፡፡ የዘ ፡ እንተ ፡ እለም ፡ ጥንቃቄ ፡ ኋላ ፡ በዘርፍ ፡ በቅጽል ፡ ይነ ገራል ፡፡

## ፲፮ኛ ፡ ዕርከን ፡፡

## ሳቢና ፡ ተሳቢ ፡ የሰዋስው ፡ ኵንቢ ፡፡

፩ ፤ ሳቢና ፡ ተሳቢ ፡ ማለት ፡ ዘርፍና ፡ ባለቤት ፡ ወይም ፡ ቅጽልና ፡ ባለቤት ፡ እንደ ፡ ማለት ፡ ነው ፤ ሳቢው ፡ አንቀጽ ፡ ተሳቢው ፡ ባለቤት ፡ ነውና ፡፡ የባለቤትም ፡ ጓዝ ፡ ዘር ፍና ፡ ቅጽል ፡ ሌላውም ፡ ኹሉ ፡ በተሳቢነት ፡ ይከተታል ፡፡ በገቢር ፡ አንቀጽ ፡ አደረገ ፡

አላደረገም ፥ በተግብሮ ፡ ተደረገ ፡ አልተደረገም ፥ ባጕል ፡ አንቀጽ ፡ ኾነ ፡ አልኾነም ፥ በነባር ፡ አንቀጽ ፡ ነው ፡ አይዶለም ፡ ተብሎ ፡ የሚነገርለ(በ)ት ፡ አካል ፥ ወይም ፡ ፩ ፡ ሌላ ፡ ነገር ፥ በንቀጽ ፡ የሚሳብ ፡ ስለ ፡ ኾነ ፡ ተሳቢ ፥ ማሰሪያ ፡ ተቀባይ ፡ ስለ ፡ ኾነ ፡ ባለቤት ፡ ይባላል ። በተሳቢነቱ ፡ አንቀጽ ፡ ቀድሞት ፡ ወይም ፡ ተከትሎት ፡ ሲነገር ፡ አገባብ ፡ አይ ወድቅበትም ፤ ስሙም ፡ ነባር ፡ ካልኾነ ፡ በቀር ፥ ሳድስ ፡ ሣልስ ፡ ካዕብ ፡ ኹኖ ፡ በቊሙ ፡ ይነ ገራል ፡ እንጂ ፤ ተለውጦ ፡ ግእዝና ፡ ኃምስ ፡ ሳብዕ ፡ አይኾንም ። ምሳሌ ፤ ሐዋርያት ፡ ሰበኩ ፥ ወይም ፡ ሰበኩ ፡ ሐዋርያት ፡ ወንጌለ ፡ እምኢየሩሳሌም ፡ እስከ ፡ በሓውርተ ፡ አሕ ዛብ ፡ ሲል ፡ ኹሉም ፡ እያንዳንዱ ፡ ሰበኩ ፡ ባለው ፡ ይሳባል ። ዐቢይ ፡ አንቀጽም ፡ ዐቢይ ፡ አገባብ ፡ ሳይወድቅበት ፡ ከሚስበው ፡ ባለቤትና ፡ ቃል ፡ ቀድሞ ፡ ተከትሎ ፡ ሲነገር ፥ ስሙ ፡ ማሰሪያ ፡ ይባላል ። አገባብ ፡ ወድቆበት ፡ ተሳቢ ፡ ሲኾን ፡ ግን ፡ አንቀጽ ፡ እንጂ ፡ ማሰሪያ ፡ አይባልም ። ባለቤትን ፡ ማሰሪያ ፡ ተቀባይ ፡ ማለት ፡ ስለዚህ ፡ ነው ። ባንድነት ፡ ቃስረው ፡ የሚነገሩ ፡ ፍጹማን ፡ ቃላት ፡ ከ፪ ፡ አያንሱም ፤ ማነሳቸውና ፡ መብዛታቸ ውም ፡ ከንቀጽ ፡ ቍጥርና ፡ ከተሳቦቹ ፡ ማጠር ፡ ነው ።

፪ ፤ የሳቢና ፡ የተሳቢ ፡ አርእስት ፡ ፮ ፡ ናቸው ፤ መኾን ፥ ወይም ፡ ኋኝነት ፤ መደ ረግ ፥ ማድረግ ፥ ማስደረግ ፥ መደራረግ ፡ ማደራረግ ። መኾን ፡ ኺኙን ፡ አካል ፡ ብቻ ፡ የሚ ስብ ፡ ያጕል ፡ አንቀጽ ፡ ነው ፤ ፈለሰ ፡ ነገደ ፡ ዐርገ ፡ ወረደ ፡ ጕሕቈ ፡ ረትዐ ፡ ደክመ ፡ ጸንዐ ፥ ይህን ፡ የመሰለ ። ኋኝ ፡ ብቻ ፡ ሳይኾን ፡ አኋኝና ፡ ኺኝ ፡ ፍሉጠ ፡ ርእስ ፡ የሦ ስት ፡ ፊደል ፡ ግስ ፡ ስለ ፡ ኾነ ፡ ምንም ፡ የመደረግ ፡ ልማድ ፡ ተ ፡ ፬ኛ ፡ ኹኖ ፡ ባይገባ በት ፡ አሳሳቡና ፡ አገባቡ ፡ እንደ ፡ መደረግ ፡ ነው ። በነዚህም ፡ በ፮ቱ ፡ አርእስት ፡ የሚ ገቡ ፡ ደቂቅ ፡ አገባቦች ፡ በ ፡ እም ፡ ለ ፡ ኀበ ፡ መንገለ ፡ ውእደ ፡ እንተ ፡ ውስተ ፡ እስከ ፡ እንዳንቀጹ ፡ ስልት ፡ ልዩ ፡ ልዩ ፡ ስም ፡ አላቸው ፤ ይህም ፡ በ ፡ እንደሚስበው ፡ አንቀጽ ፡ መኾኛ ፡ መደረጊያ ፥ ማድረጊያ ፡ ማስደረጊያ ፥ መደራረጊያ ፡ ማደራረጊያ ፥ እም ፡ ሰጭ ፥ ለ ፡ ተቀባይ ፡ ይባላሉ ። ሖረ ፡ ተመይጠ ፡ ወፅአ ፡ ወረደ ፡ በሚያሰኙ ፡ አናቅጽ ፡ ሲሳቡ ፡ ግን ፥ እም ፡ መነሻ ፡ ለ ፡ ኀበ ፡ መንገለ ፡ ውእደ ፡ ውስተ ፡ መገሥገሻ ፥ እስከ ፡ መድረሻ ፡ ይባላሉ ።

፫ ፤ መኾን ፡ ኋኝን ፡ መኾኛን ፥ መደረግ ፡ ተደራጊን ፡ መደረጊያን ፥ መነሻን ፥ መገሥገሻን ፥ ወይም ፡ መድረሻን ፥ መነሻና ፡ መድረሻም ፡ ቢቀሩ ፡ ሰጭን ፥ ተቀባይን ፡ ማሰሪያ ፡ የሚያስለቅቅ ፡ ዐቢይ ፡ አገባብን ፥ ዘንድን ፥ ንኡስ ፡ አንቀጽን ፡ ይስባል ። ማሰ ሪያ ፡ የማያስለቅቅ ፡ አገባብ ፡ ግን ፡ መደረጊያ ፥ መነሻ ፥ መገሥገሻ ፡ ተቀባይ ፡ ከተበ ሉት ፡ ጋራ ፡ ዐቢይ ፡ አገባብም ፡ ቢኾን ፡ ዐብሮ ፡ ይቈጠራል ። መኾን ፡ ኺኝና ፡ መኾኛን ፡ መደረግም ፡ ተደራጊንና ፡ መደረጊያን ፡ ከቢይ ፡ አገባብ ፡ ጋራ ፡ ሲስብ ፥ (ረትዐት) ፡ ተወሰ ነት ፡ ሃይማኖት ፡ ኦርቶዶክሳዊት ፡ በጉባኤ ፡ ኒቅያ ፡ በአፈ ፡ ሠለስቱ ፡ ምእት ፡ አመ ፡ ነግሠ ፡ ቈስጠንጢኖስ ፡ ይላል ። መነሻ ፡ መገሥገሻ ፥ ወይም ፡ መድረሻ ፡ ተደራጊ ፡ አገ ባብ ፡ ሲስብ ፥ (ፈለሱ ፡ አው ፡ ወፅኡ) ፡ ተፈነዉ ፡ ሐዋርያት ፡ እምኢየሩሳሌም ፡ ውስተ ፡ ኵሉ ፡ ብሔረ ፡ አሕዛብ ፡ ሰበ ፡ ፈቀዱ ፡ ፈጽሞተ ፡ ቃሉ ፡ ለእግዚእነ ፡ ይላል ። ተደራ ጊን ፡ ሰጭን ፡ ተቀባይን ፡ አገባብን ፡ ሲስብ ፥ (በርሀ) ፡ ተሰብከ ፡ ሃይማኖት ፡ እምቃለ ፡

ሐዋርያት ፡ ለአሕዛብ ፡ ድኅረ ፡ ዐርገ ፡ እግዚእነ ፡ ይላል ። ጊቱን ፡ ኹሉ ፡ ሲስብ ፥ (ተመ ሥጠ) ፡ ዐርገ ፡ ኤልያስ ፡ እምድር ፡ ውስተ ፡ ገነት ፡ በሠረገላ ፡ እሳት ፡ እምድኅረ ፡ ተአ ምረ ፡ ዐቂቦቱ ፡ ሕገ ፡ እግዚአብሔር ፡ ይንበር ፡ ህየ ፡ ይላል ። በዚህ ፡ ላይ ፡ በማድረግ ፡ ጊዜ ፡ አድራጊን ፥ በማስደረግ ፡ ጊዜ ፡ አስደራጊን ፡ ጨምር ። (መሠጦ) ፡ አዕረጎ ፡ እግ ዚአብሔር ፡ ለኤልያስ ፡ አዕርጎተ ፡ ፍቅር ።

፬ ፤ መደራረግ ፡ ተደራራጊን ፡ መደራረጊያን ፡ ተደራጊን ፡ መነሻን ፡ መገሥገሻን ፡ ወይም ፡ መድረሻን ፡ ንኡስ ፡ አንቀጽን ፡ አገባብን ፡ ይስባል ። ሲገባም ፥ ተራወጹ ፡ ተቃ ሓውያን ፡ ሩጸተ ፡ እመካን ፡ እስከ ፡ መካን ፡ ዘወሰኑ ፡ ሎሙ ፡ ባዕዳን ፡ በመርሕብ ፡ በዕ ለተ ፡ አዕረፉ ፡ እምተግባረ ፡ ሥጋ ፡ ይክሥቱ ፡ ፍጥነተ ፡ እግሮሙ ። ፪ኛም ፡ መደራረግ ፡ ተደራራጊን ፡ መደራረጊያን ፡ አገባብን ፡ ሲስብ ፥ ተቃተለ ፡ ዳዊት ፡ ምስለ ፡ ጎልያድ ፡ በመካነ ፡ ዔላ ፡ ሶበ ፡ ዐርጉ ፡ ኢሎፍላውያን ፡ ኀበ ፡ ደቂቀ ፡ እስራኤል ፡ ይላል ። ተደራ ጊንም ፡ ሲጨምር ፥ ተራወጹ ፡ አብያጽ ፡ ተቃሓውያን ፡ ሩጸተ ፡ በመርሕብ ፡ በዕለተ ፡ አዕረፉ ፡ እምተግባረ ፡ ሥጋ ፡ ይላል ። መነሻንና ፡ መገሥገሻንም ፡ ሲጨምር ፥ ይትራ ወጹ ፡ ሩጸተ ፡ መንፈሳዌ ፡ ሐዋርያት ፡ ወአርድእት ፡ እምኢየሩሳሌም ፡ ኀበ ፡ እስከ ፡ ብሔረ ፡ አሕዛብ ፡ ወእምህየ ፡ ኀበ ፡ ሳሌም ፡ እንዘ ፡ ይሰብኩ ፡ ወንጌለ ፡ ይላል ። በማደ ራረግም ፡ ጊዜ ፡ በዚህ ፡ ላይ ፡ አደራራጊን ፡ ጨምር ፤ አስተራወጸ ፡ እግዚእነ ፡ ሐዋር ያተ ፡ ወአርድእተ ።

፭ ፤ ዳግመኛም ፡ መደረግ ፡ ተደራጊን ፥ መደራረግ ፡ ተደራራጊን ፥ ግእዝ ፡ ኃምስ ፡ ሳብዕ ፡ አድርገው ፡ ይስባሉ ። ራብዕ ፡ ግን ፡ ለገቢርና ፡ ለተገብሮ ፡ ስለ ፡ ተመቸ ፡ ኹሉ ፡ ይስቡታል ፤ ይህም ፡ በልዐ ፡ ሥጋ ፡ ወመና ፥ ተበልዐ ፡ ሥጋ ፡ ወመና ፡ ማለቱን ፡ ያሳ ያል ። ስመ ፡ ተጸውዖም ፡ በገቢር ፡ አንቀጽ ፡ ተደራጊ ፡ ተሳቢ ፡ ኹኖ ፡ ሲነገር ፡ የግእዝ ፡ ወራሽ ፡ ሀ ፡ ይጨመርበታል ፤ ይህም ፡ ጸውዐ ፡ ሊተ ፡ ናታንሀ ፡ ነቢየ ፡ ወሳዶቅሀ ፡ ካህነ ፡ ወብንያስሀ ፡ ባለው ፡ ይታወቃል ። መደረግ ፡ ሳድስን ፡ ካዕብን ፡ ሣልስን ፡ ሲስብ ፡ ተቀ ትለ ፡ ፀር ፡ አው ፡ ፀሩ ፡ ወሚመ ፡ ጸላኢ ፡ ይላል ። ማድረግ ፡ ግእዝን ፡ ሳብዕን ፡ ኃምስን ፡ ሲስብ ፥ ቀተለ ፡ ፀረ ፡ አው ፡ ፀሮ ፡ ወሚመ ፡ ጸላኤ ፡ ይላል ። በማስደረግ ፡ ጊዜ ፡ አቅተለ ፡ በማደራረግ ፡ ጊዜ ፡ አስተቃተለ ፡ በል ። መደረግ ፡ በነባርነት ፡ ያሉ ፡ የማድረግን ፡ ተሳ ቦች ፡ ይወርሳል ፤ ይህም ፡ ተቀሥመ ፡ ጽጌ ፡ ወፍሬ ፥ ተዘብጠ ፡ ከበሮ ፡ ወመሰንቆ ፡ ማ ለቱን ፡ ያሳያል ። ማድረግም ፡ በጐልትነት ፡ ያሉ ፡ የመደረግን ፡ ተሳቦች ፡ ይወርሳል ። ይህም ፡ አክበረ ፡ አቡሁ ፥ ከሠተ ፡ አፉሁ ፥ አፍቀረ ፡ ፈጣሪሁ ፥ አፈቅር ፡ መድኅንየ ፡ ማለቱን ፡ ያሳያል ።

፮ ፤ ማናቸውም ፡ አንቀጽ ፡ በንኡስ ፡ አገባብ ፡ ፈንታ ፡ ጥሬዎቹን ፡ ግእዝ ፡ አድ ርጎ ፡ ሲስብ ፡ ማሰሪያ ፡ አጐላማሽ ፡ ነው ፡ እንጂ ፤ እውነተኛ ፡ ተሳቢ ፡ አይዶለም ። ይ ህም ፡ ፈቲወ ፡ ፈተውክዎ ፥ ወፈተዉ ፡ ፍትወተ ፥ ልህበ ፡ ልህበተ ፥ ተዐጽበ ፡ ዕጽበተ ፡ ሲል ፥ አካቶ ፡ ፈጽሞ ፡ ጭራሽ ፡ እያሰኘ ፡ ሌላውን ፡ ኹሉ ፡ ያሳያል ። ፪ኛም ፡ በደቂቅ ፡ አገባብ ፡ ፈንታ ፡ ዐርገ ፡ ሰማየ ፡ ወረደ ፡ ቀላየ ፥ ተሰቅለ ፡ ቀትረ ፥ ተዛበጠ ፡ በትረ ፡ እያለ ፡ ባዕድ ፡ ጥሬ ፡ ሲስብ ፡ ግእዝነቱ ፡ የብትን ፡ ሰዋስው ፡ ነውና ፤ ኋላ ፡ በቦታው ፡ ይነገራል ።

መደረግ ፡ በጕልትነት ፡ ካሉ ፡ ከነባሮችና ፡ ግእዝ ፡ አድርጎ ፡ ከሚስባቸው ፡ ከራሱ ፡ ጥሬዎች ፡ በቀር ፡ ማድረግ ፡ የሚስባቸውን ፡ ግእዝና ፡ ኃምስ ፡ ሳብዕ ፡ አይስብም ፤ ግንዘበቹን ፡ ብቻ ፡ ካዕብና ፡ ሣልስ ፡ ሳድስ ፡ ቢስብ ፡ እንጂ ። ይህም ፡ ተላጸየ ፡ ርእስ ፡ ሱ ፤ ተመትረ ፡ ክሣድ ፡ ዱ ፥ ተሀይደ ፡ ንዋይ ፡ ዩ ፥ ተእኅዘ ፡ ሰራቂ ፡ ማለቱን ፡ መደብ ፡ አድርጎ ፡ ርእሰ ፡ ሶ ፥ ክሣደ ፡ ዶ ፥ ንዋየ ፡ ዮ ፥ ሰራቄ ፡ አለማለቱን ፡ ያሳያል ። መጽሐፍ ፡ ግን ፡ የገቢሩን ፡ ለተገብሮ ፡ ሰጥቶ ፡ ተላጸየ ፡ ርእሶ ፥ ተመትረ ፡ ክሣዶ ፥ ተሀይደ ፡ ንዋዮ ፡ ወብእሲቶ ፡ ይላል ፤ የመላሽና ፡ የጣፊ ፡ ስሕተት ፡ ነው ። ባላገባቦችም ፡ የሚያሰኝ ፡ መስኋቸው ፡ አብነት ፡ አድርገው ፡ ይጠቅሱታል ። ዐዋቆችና ፡ ጠንቃቆች ፡ ግን ፡ ስንኳን ፡ ግእዙን ፡ ዐማርኛውንም ፡ ይነቅፋሉ ፤ ተላጨ ፡ ተቈረጠ ፡ ተቀማ ፡ ብሎ ፡ ራሱን ፡ ዐንገቱን ፡ ገንዘቡን ፡ ሚስቱን ፡ ማለት ፡ ልውጥና ፡ ግልብጥ ፡ ነውና ። ተገብሮ ፡ ግእዝ ፡ የሚስብ ፡ ገቢሩ ፡ እንደነመሀረ ፡ ፪ ፡ ግእዝ ፡ ሲስብለት ፡ ነው ፡ (ተምህረ ፡ መጽሐፈ) ። ይህነንም ፡ ኋላ ፡ በተራው ፡ እናመጣዋለን ።

፯፤ ሳቦች ፡ አናቅጽ ፡ ፰ ፡ ናቸው ፤ ፫ቱ ፡ ዐበይት ፥ ፭ቱ ፡ ንኡሳት ፡ (ቍ፶፰) ። በጠባይና ፡ በሳሳብ ፡ ግን ፡ ገቢር ፡ ተገብሮ ፡ ተብለው ፡ በ፪ ፡ ይከፈላሉ ፡ (ቍ፶፭) ። ዐበይት ፡ አናቅጽ ፡ የሚባሉት ፡ ኀላፊና ፡ ትንቢት ፡ ትእዛዝ ፥ ከንኡሳትም ፡ ዘንድና ፡ ቦዝ ፡ እነዚህ ፡ ፭ቱ ፡ በፊት ፡ ኹነው ፡ ወደ ፡ ኋላ ፥ በኋላም ፡ ኹነው ፡ ወደ ፡ ፊት ፡ ሲስቡ ፡ ዐርፈው ፡ እንጂ ፡ ተናበው ፡ አይስቡም ። ይህም ፡ በፊት ፡ ሲኾኑ ፥ በልዐ ፡ ኅብስተ ፡ ይበልዕ ፡ ኅብስተ ፡ ይብላዕ ፡ ኅብስተ ፤ ሖረ ፡ ይብላዕ ፡ ኅብስተ ፥ በሊዖ ፡ ኅብስተ ። በኋላም ፡ ሲኾኑ ፡ ኅብስተ ፡ በልዐ ፡ ይበልዕ ፡ ይብላዕ ፤ ኅብስተ ፡ ይብላዕ ፡ ሖረ ፤ ኅብስተ ፡ በሊዖ ፡ ማለቱን ፡ ያሳያል ፤ በቀሩትም ፡ ባራቱ ፡ አዕማድ ፡ አሳሳባቸው ፡ እንዲሁ ፡ ነው ፤ አይለወጥም ። አርእስትና ፡ ሳቢ ፡ ዘር ፡ ውስጠ ፡ ዘ ፡ እነዚህ ፡ ሦስቱ ፡ ዐርፈው ፡ ተናበው ፡ በለ ፡ ተያይዘው ፡ በፊትም ፡ በኋላም ፡ ኹነው ፡ ይስባሉ ። ዐርፈው ፡ በፊት ፡ ኹነው ፡ ሲስቡ ፥ በሊዕ ፡ በሊዖት ፤ በሊዖት ፡ ኅብስተ ፥ በላዒ ፡ ኅብዝተ ። በኋላም ፡ ኹነው ፡ ሲስቡ ፡ ኅብዝተ ፡ በሊዕ ፡ ዖት ፡ ብልዐት ፡ በላዒ ፡ ያሰኛሉ ። ተናበው ፡ ሲስቡ ፥ በሊዐ ፡ ኅብስት ፡ በሊዖተ ፡ ኅ ፡ ብልዐተ ፡ ኅ ፡ በላዔ ፡ ኅብዝት ። በለ ፡ ተያይዘው ፡ ወደ ፡ ፊት ፡ ሲስቡ ፥ በሊዕሁ ፡ በሊዖቱ ፡ ብልዐቱ ፡ በላዒሁ ፡ ለኅብዝት ። ወደ ፡ ኋላም ፡ ሲስቡ ፥ ለኅብዝት ፡ በሊዕሁ ፡ በሊዖቱ ፡ ብልዐቱ ፡ በላዒሁ ፡ ያሰኛሉ ። የቀረ ፡ ተሳቢ ፡ ሲጨምሩና ፡ አገባብ ፡ ሲጫናቸው ፡ ግን ፡ ወደ ፡ ፊት ፡ ብቻ ፡ እንጂ ፡ ወደ ፡ ኋላ ፡ አይስቡም ። ይህም ፡ በሊዐ ፡ ኅብዝት ፡ በማእድ ፡ ቢል ፡ እንጂ ፡ በማእድ ፡ በሊዐ ፡ ኅ ፡ በላዔ ፡ ኅ ፡ አይልም ። ሲያያዝም ። በሊዖቱ ፡ ለኅብዝት ፡ በማእድ ፡ ቢል ፡ እንጂ ፡ በማእድ ፡ በሊዖቱ ፡ ለኅብዝት ፡ አይልም ፤ አገባብም ፡ ሲጫነው ፡ ለበሊዕ ፡ ኅብዝተ ፡ ለበላዔ ፡ ኅብዝት ፡ ቢል ፡ እንጂ ፥ ኅብዝተ ፡ ለበሊዕ ፡ ወይም ፡ ለበላዒ ፡ አይልም ፤ በቀሩትም ፡ እንደዚሁ ፡ ነው ።

፰፤ ኹለት ፡ ግእዝ ፡ የሚስቡ ፡ አናቅጽ ፥ ረሰየ ፡ መሀረ ፡ ጸውዐ ፡ ሰመየ ፡ ብህለ ፡ መልአ ፡ ቀብዐ ፡ ከደነ ፡ ዐጸፈ ፡ ናቸው ፤ እነዚህን ፡ የመሰሉ ፡ ኹሉ ፡ ፪ ፡ ግእዝ ፡ ስበው ፡ ሲገኙ ፡ ፩ኛው ፡ ተሳቢ ፡ ኹኖ ፡ በራሱ ፥ ፪ኛው ፡ ባገባብ ፡ ፈንታ ፡ ይነገራል ፤ ረሰዮ ፡ ለማይ ፥ ወይም ፡ ረሰየ ፡ ማየ ፡ ወይነ ፡ ቢል ፥ ከመ ፡ ወይን ፡ ማለት ፡ ነውና ፤ የረሰየ ፡ ምስ

ጢር ፡ እንዲህ ፡ እንዳ'ኹኑ ፡ ውላጤ ፡ ሲ'ኾን ፡ ተገብሮውንም ፡ ኮነ ፡ ይወርሰዋል ፤ ጥዒሞ ፡ አንከረ ፡ ውእተ ፡ ማየ ፡ ዘኮነ ፡ ወይነ ፡ እንዲል ። መሀረም ፡ ትምርቱንና ፡ ተማሪውን ፡ 'ኹለቱንም ፡ በግእዝ ፡ ሲስብ ÷ መሀረ ፡ ፊደለ ፡ ሕፃናተ ፡ ቢል ፡ የተቀባይን ፡ ን ፡ አገባብ ፡ ለን ፡ ግእዝ ፡ ሲወርሰው ፡ ነው ፤ ስትፈታም ፡ ለሕፃናት ፡ በል ፡ እንጂ ፡ ሕፃናትን ፡ አት በል ። ፪ኛም ፡ መሀሮሙ ፡ ፊደለ ፡ ለሕፃናት ፤ ወትፈቅዱ ፡ ይምሀሩክሙ ፡ ቀዳሚ ፡ መጽ ሐፈ ፡ እያሰኘ ፡ ተቀባዩን ፡ ባገባብና ፡ በዝርዝር ÷ ተሰጭን ፡ በግእዝ ፡ ሲስብ ÷ ፩ ፡ አን ቀጽ ፡ ከ፩ ፡ ገቢር ፡ በቀር ፡ ፪ኛ ፡ ገቢር ፡ እንዳይስብ ፡ በግልጥ ፡ ያስረዳል ። ተገብሮውና ፡ ሳድስ ፡ ቅጽሉም ÷ ተምህረ ፡ መጽሐፈ ÷ ብእሲ ፡ ምሁር ፡ መጽሐፈ ፡ እያሰኘ ፡ ገቢር ፡ የሳበውን ፡ መልሶ ፡ በግእዝ ፡ ይስባል ።

፶ ፤ ጸውዐና ፡ ሰመየም ፡ ባለስምን ፡ በዝርዝርና ፡ በጠቃሽ ÷ ስምን ፡ በግእዝ ፡ ሲ ስቡ ÷ ወጸውዑ ፡ ስሞ ፡ ኢየሱስሀ ፤ ወሰመዮ ፡ ለብርሃን ፡ መዓልተ ፡ ወለጽልመት ፡ ሌ ሊተ ፡ ያሰኛሉ ። ተገብሯቸውም ÷ ተጸውዐ ፡ ተጠራ ፡ ሲ'ኾን ፡ ሳድስ ፡ እንጂ ፡ ግእዝ ፡ አይስብም ፤ ተሰምየ ፡ ግን ፡ ተባለ ፡ ሲ'ኾን ፡ ግእዝና ፡ ነባር ፡ ይስባል ። ተሰመይኪ ፡ እመ ፡ ወአመተ ፤ ተሰምየ ፡ አምላክ ፡ ውእቱ ፡ ክርስቶስ ፤ አምላክ ፡ ነው ፡ ተባለ ። ተሰምየ ፡ ብሎ ፡ ስሙ ፡ ካላለ ፡ ግእዝ ፡ እንጂ ፡ ሳድስ ፡ አይስብም ፤ መጽሐፍ ፡ ግን ፡ ተሰምየ ፡ ዐማ ኑኤል ፤ ወዓዲ ፡ ይሰመይ ፡ ኢየሱስሀ ፡ ይላል ። ሰመየም ፡ በግእዝ ፡ ፈንታ ፡ ሳድስ ፡ እየ ሳበ ፡ ይገኛል ። ሰመዮ ፡ ለስምዖን ፡ ጴጥሮስ ። ብህለና ፡ ይቤም ፡ ፩ ፡ ወገን ፡ 'ኹኖ ፡ ጥሬ ዎችን ፡ እንደነሰመየ ፡ ሲስብ ÷ መነ ፡ ትብል ፡ ርእሰከ ፤ መነ ፡ ይብለኒ ፡ ሰብእ ፡ ይላል ። በውእቱም ፡ ፈንታ ÷ ቦ ፡ እለ ፡ ይብሉከ ፡ ኤልያስሀ ፡ አው ፡ ኤርምያስሀ ፤ እለ ፡ ይብሉ ፡ ርእሶሙ ፡ ሐዋርያተ ፡ እያለ ፡ ግእዝ ፡ ይስባል ። በተለየም ፡ አንቀጽና ፡ አገባብ ፡ ሲስብ ፡ ይቤሎ ፡ እግዚእ ፡ ለእግዚእየ ፡ ንበር ፡ በየማንየ ፤ ኢትበል ፡ ለየማን ፡ ወኢለፀጋም ፡ ይላል ። መልእና ፡ ቀብዐ ፡ ከደነና ፡ ዐጸፈም ፡ ፪ ፡ ግእዝ ፡ ስበው ፡ ሲገኙ ፡ ፪ኛው ፡ ባገ ባብ ፡ ፈንታ ፡ ነው ፤ ተገብሯቸውም ፡ ተመልአ ፡ ጥበበ ÷ ተቀብዐ ፡ ዘይተ ÷ ተከድነ ፡ ሠቀ ÷ ተዐጽፈ ፡ ርትዐ ፡ እያሰኘ ፡ እንደነመሀረ ፡ ግእዝ ፡ ይስባል ።

፲ ፤ የነባር ፡ አንቀጽም ፡ አሳሳብ ፡ እንዲህ ፡ ነው ፤ ውእቱ ፡ በአንቀጽነቱ ፡ ነው ፡ ተብሎ ፡ ሲፈታ ፡ የነባርና ፡ የጥሬ ፡ ዘር ፡ የሣልስና ፡ የሳድስ ፡ ቅጽል ፡ ያርእስትና ፡ የሳቢ ፡ ዘር ፡ ማሰሪያ ፡ ይ'ኾናል ። መሓሪ ፡ ውእቱ ፡ እግዚአብሔር ፤ ሠናይ ፡ ውእቱ ፡ ሕግ ፤ መንፈስ ፡ ይእቲ ፡ ነፍስ ፤ መሬት ፡ ውእቱ ፡ ሥጋ ፡ እያለ ፡ በሚስበውና ፡ በሚያስረው ፡ 'ኹሉ ፡ የባለቤትን ፡ በሕርይና ፡ ግብር ፡ ሌላውንም ፡ ይተረጕማል ። ተገልጦም ፡ ባልተ ነገረበት ÷ ሕይወቱ ፡ ለነዳይ ፡ ስኢለ ፡ ምጹት ፤ ወተስፋሁ ፡ ጻጊብ ፡ ኅብስት ፤ ፈጢር ፡ ዘእግዚአብሔር ፤ ወተፈጥሮ ፡ ዘሰማይ ፡ ወምድር ፡ እያሰኘ ፡ በየደጁ ፡ ይመረመራል ። አኮና ፡ ኢ ፡ ደግሞ ፡ አይዶለም ፡ ተብለው ፡ ሲፈቱ ፡ አካ'ኼዳቸው ፡ እንደ ፡ ውእቱ ፡ ነው ፤ ርሱ ፡ የሚስባቸውን ፡ ይስባሉ ። ይህም ፡ አኮ ፡ ወይም ፡ ኢመፍትው ፡ አድልዎ ፡ በፍትሕ ፤ አኮ ፡ ወይም ፡ ኢሕዝብየ ፡ እሉ ። ተነስሐቱ ፡ ለይሁዳ ፡ አኮ ፡ ወይም ፡ ኢከመ ፡ ተነስሐቱ ፡ ለጴጥሮስ ፡ ማለቱን ፡ ያሳያል ።

፲፩ ፤ ቅጽል ፡ ከባለቤት ፡ ሲርቅ ፡ ወይም ፡ በውእቱ ፡ ሲፈረቀቅ ፡ ስሙ ፡ ተለዋጭ ፡ ይባላል ፤ ተለዋጭም ፡ ባሕርይና ፡ ግብር ፡ ስምና ፡ ነገር ፡ ይተረጐማል ፤ አካልም ፡ ያመጣል ። አካልም ፡ ኹኖ ፡ ቅጽልም ፡ ኹኖ ፡ ማሰሪያ ፡ ከወደቀበት ፡ በግድ ፡ ተለዋጭ ፡ ይኾናል ፤ አካል ፡ ሲያመጣ ፡ አምላክ ፡ ውእቱ ፡ ዘለብሰ ፡ ሥጋ ፡ ብሎ ፡ ሥጋ ፡ የለበሰ ፡ አካል ፡ ያሰኛል ፤ ግብርም ፡ ሲተረጐም ፡ ማርያም ፡ ይእቲ ፡ ኪሩቤል ፡ ይላል ። ከሥሩ ፡ መደብ ፡ ፬ቱ ፡ ሩቆች ፡ በቂና ፡ አንቀጽ ፡ እየኾኑ ፡ ራሳቸውን ፡ ይችላሉ ። ምሳሌ ፤ ውእቱ ፡ ዘፈጸመ ፡ ሕገ ። ይእቲ ፡ እንተ ፡ ወለደት ፡ አምላከ ። ውእቶሙ ፡ አው ፡ እሙንቱ ፡ እለ ፡ ሰበኩ ፡ ወንጌለ ፤ ውእቶን ፡ አው ፡ እማንቱ ፡ እለ ፡ ብዙኀ ፡ ተጋደላ ። ዘ ፡ እንተ ፡ እለም ፡ ባልገቡበት ፡ ቅጽልና ፡ ጥሬ ፡ ማሰሪያ ፡ ሲኾኑ ፡ ውእቱ ፡ ሕያው ፥ ወአከ ፡ ምዉት ፤ ውእቱ ፡ አብርሃም ፥ ወይእቲ ፡ ሳራ ፤ እሙንቱ ፡ ደቂቅ ፥ ወእማንቱ ፡ አዋልድ ፡ እያሰኙ ፡ ሌላውን ፡ ኹሉ ፡ ያሳያሉ ።

፲፪ ፤ ፮ቱ ፡ ቅርቦች ፡ ግን ፡ የሩቁን ፡ አንቀጽ ፡ ውእቱን ፡ ይደርባሉ ። ውእቱም ፡ ለዋጭ ፡ ተለዋጭ ፡ እንደ ፡ መኾኑ ፡ በወንድና ፡ በሴት ፡ ባንድና ፡ በብዙ ፡ የቅርብ ፡ አፈታት ፡ ይፈታል ። ምሳሌ ፤ አንተ ፡ ውእቱ ፡ ዘትገብር ፡ መንክረ ። አንቲ ፡ ውእቱ ፡ እንተ ፡ ወለድኪ ፡ አምላከ ። አንትሙ ፡ ውእቱ ፡ እለ ፡ ዖድክሙ ፡ አህጉረ ። አንትን ፡ ውእቱ ፡ እለ ፡ አፍቀርክን ፡ ንጽሐ ። አነ ፡ ውእቱ ፡ ዘአአምን ፡ በክርስቶስ ። ንሕነ ፡ ውእቱ ፡ እለ ፡ ንትፋቀር ፡ በበይናቲነ ። ወይም ፡ በብዙ ፡ አንትሙ ፡ እሙንቱ ፥ አንትን ፡ እማንቱ ፥ ንሕነ ፡ እሙንቱ ፤ ባንዲቱም ፡ አንቲ ፡ ይእቲ ፡ እያሰኘ ፡ ሩቆቹን ፡ ኹሉ ፡ ይደርባል ። በግልጠ ፡ ዘ ፡ ብቻ ፡ ያይዶለ ፡ በሌላውም ፡ ቅጽልና ፡ ጥሬ ፡ እንዲሁ ፡ ናቸው ፤ አንተ ፡ ውእቱ ፡ ክርስቶስ ። አንቲ ፡ ውእቱ ፡ ምሥራቅ ። አንትሙ ፡ ውእቱ ፡ ዘርዕ ፡ ክቡር ። አነ ፡ ውእቱ ፡ እግዚአብሔር ፡ ይላል ። ፪ኛም ፡ ሩቁን ፡ ትተው ፡ ቅርቡን ፡ ብቻ ፡ ይደርባሉ ። ምሳሌ ፤ አንተ ፡ መኑ ፡ አንተ ። አንቲሰ ፡ እብድ ፡ አንቲ ። አንትሙ ፡ ኢለባውያን ፡ አንትሙ ። አንትንሰ ፡ ጠባባት ፡ አንትን ። እስመ ፡ አነ ፡ ኄር ፡ አነ ። ንሕነሰ ፡ አግብርቲከ ፡ ንሕነ ። ፫ኛም ፡ ሩቅና ፡ ቅርብ ፡ ሳይደርቡ ፡ ብቻ ፡ ብቻቸውን ፡ ራሳቸውን ፡ ይችላሉ ። ምሳሌ ፤ አንተ ፡ ዘትፈትን ፡ ልበ ፡ ወኵልያተ ፤ አንተ ፡ ካህኑ ፡ ለዓለም ። አንቲ ፡ በአማን ፡ ምክሐ ፡ ዘመድነ ። አንትሙ ፡ ጼው ፡ ለምድር ። አንትን ፡ አዋልደ ፡ መኑ ። አነሰ ፡ ቃለ ፡ ዐዋዲ ። ወንሕነ ፡ ሰማዕቱ ።

፲፫ ፤ ውእቱ ፡ በግብር ፡ ለውጥ ፡ ሩቁን ፡ በቅርብ ፥ ቅርቡን ፡ በሩቅ ፥ አንዱን ፡ በብዙ ፥ ብዙውን ፡ ባንድ ፥ ወንዱን ፡ በሴት ፥ ሴቱን ፡ በወንድ ፡ ያናግራል ። አንተ ፡ ውእቱ ፡ ዘይገብር ፡ ኵሎ ። ማርያም ፡ ኪሩቤል ፡ ይእቲ ፤ ወኪሩቤል ፡ እሙንቱ ፡ ማርያም ፡ በ ፡ ለ ፡ እም ፡ በእንተ ፡ ጸዊረ ፡ አምላክ ። በአካልም ፡ ለውጥ ፡ ሲገባ ፡ በየራሱ ፡ ያናግራል ፤ ወይም ፡ ተለዋጭ ፡ ይኾናል ። እመ ፡ አምላክ ፡ ይእቲ ፡ ማርያም ፤ ማርያም ፡ ይእቲ ፡ እመ ፡ አምላክ ። በባሕርይም ፡ ለውጥ ፥ እብን ፡ ዘአርአዮ ፡ ሰይጣን ፡ ለእግዚእነ ፡ ኅብዝት ፡ ውእቱ ፤ ኅብዝት ፡ ዘአርአዮ ፡ ሰይጣን ፡ ለእግዚእነ ፡ እብን ፡ ውእቱ ፡ ያሰኛል ። አኮና ፡ ኢ ፡ ደግሞ ፡ የውእቱ ፡ አሉታ ፡ እየኾኑ ፡ እስካኹን ፡ በገባው ፡ ይገባሉ ።

፲፬ ፤ በ ፡ በነባርነቱ ፡ አለ ፡ ኖረ ፡ ነበረ ፡ ተብሎ ፡ እንደ ፡ ውእቱ ፡ ሲፈታ ፤ በ ፡ አዳም ፡ ውስተ ፡ ገነት ፡ እምቅድመ ፡ ዕልወት ፡ መጠነ ፡ ሰብዐቱ ፡ ዓመት ፡ እያሰኘ ፡ ባለ

ቤት ፡ ካገባብ ፡ ይስባል ። በዝርዝርነቱም ፡ በ ፡ በቱ ፡ አለው ፡ ኖረው ፡ ነበረው ፡ ተብሎ ፡
ሲፈታ ፥ ወበ ፡ እኅት ፡ ሠናይት ፡ ለአቤሴሎም ። ወበቲ ፡ ለርብቃ ፡ እኅ ፡ እያሰኘ ፡ ገን
ዘብና ፡ ባለገንዘብን ፡ ከናገባቡ ፡ ይስባል ። ዝርዝሩ ፡ በቂና ፡ ዐጸፋ ፡ ሲኾን ፡ ግን ፡ ዘበ ፡
ክልኤ ፡ ክዳናት ። ወቦቱ ፡ ብርሃን ፡ ዘኢይጠፍእ ፡ እያለ ፡ ገንዘብን ፡ ብቻ ፡ ይስባል ።
አሉታውም ፡ አልቦ ፡ አልቦቱ ፡ እንደ ፡ ጽድቁ ፡ ነው ። በ ፡ ነባር ፡ ከዝርዝር ፡ እንደ ፡
ኾነ ፥ ቦቱ ፡ ግን ፡ ዝርዝር ፡ ብቻ ፡ እንደ ፡ ኾነ ፡ አስተውል ። ሎ ፡ ሎቱ ፡ ደግሞ ፡ አለው ፡
አለለት ፡ ተብሎ ፡ ሲፈታ ፡ እንደ ፡ ቦቱ ፡ አድርጎ ፡ ይስባል ፤ ማይሰ ፡ ሎሙ ፡ አረፍት ፡
በይምን ፡ ወአረፍት ፡ በፅግም ። ሎሙ ፡ ሕግ ፡ ወሎሙ ፡ ሥርዐት ፡ እንዲል ።     ሐሰ ፡
በለ ፡ ሲዘረዘር ፡ ዘንድና ፡ አርእስት ፡ ሳቢ ፡ ዘር ፡ ይስባል ። እግዚአ ፡ ታጥፍአነ ፡ ሐሰ ፡
ለከ ። ሐሰ ፡ ሊተ ፡ እግበር ፡ እኩየ ፤ አው ፡ ገቢረ ፡ እኩይ ፡ ግብረተ ፡ እኩይ ። ሳይዘረ
ዝርም ፡ እንደነአከ ፡ ብቻውን ፡ ይገባል ። ገደፎሙኑ ፡ እግዚ ፡ ለሕዝቡ ፤ ሐሰ ።

፲፫ ፤ የኮነም ፡ አካኼድ ፡ እንደ ፡ ውእቱ ፡ ነው ፤ ያርእስትና ፡ የሳቢ ፡ ዘር ፡ የቅ
ጽልና ፡ የጥሬ ፡ ማሰሪያ ፡ ይኾናል ። አንቀጽነቱ ፡ ዐጕል ፡ ስለ ፡ ኾነ ፡ የረሰየና ፡ የገብረ ፡
መደረግ ፡ ይባላል ፤ የረሰየ ፡ ሲኾን ፡ በሚለወጥና ፡ በማይለወጥ ፡ ነገር ፡ ግእዝና ፡ ራብዕ ፡
ኃምስና ፡ ሳብዕ ፡ ይስባል ። ምሳሌ ፤ ሌሊተ ፡ ኮነ ፡ ቀትር ፤ ቃል ፡ ሥጋ ፡ ኮነ ፤ ይስማኤል ፡
ኮነ ፡ ነዳፌ ፤ ኮንኪ ፡ ታቦቶ ፡ ለፈጣሪ ። የገብረ ፡ መደረግ ፡ ሲኾን ፡ ግን ፡ ሳድስ ፡ እንጂ ፡
ግእዝ ፡ አይስብም ፤ ይህም ፡ ከብካብ ፡ ኮነ ፡ በቃና ፤ ዮም ፡ ኮነ ፡ ሕይወት ፡ ለዝንቱ ፡
ቤት ። ኢዐቀብነ ፡ ወኢገበርነ ፡ በከመ ፡ አዘዝከነ ፡ ከመ ፡ ይኩን ፡ ሠናይ ፡ ላዕሌነ ፡ ማለ
ቱን ፡ ያሳያል ። በሚለወጥ ፡ ነገር ፡ መደረግ ፡ ሲኾን ፡ በማይለወጠው ፡ ማድረግ ፡ ይኾ
ናል ፤ በሚለወጥ ፡ ማለት ፥ ለዋጩ ፡ ሌላ ፡ ተለዋጩ ፡ ሌላ ፡ ሲኾን ፡ ነው ፤ እንደ ፡ ማየ ፡
ግብጽ ፡ እንደ ፡ ማየ ፡ ቃና ። በማይለወጥ ፡ ማለት ፡ ግን ፡ ዐጕል ፡ አንቀጽ ፡ ከኗኙ ፡
በቀር ፡ ሌላ ፡ አይስብምና ፤ የራሱ ፡ አድራጊ ፡ ኺኙም ፡ አኺኙም ፡ ርሱ ፡ ራሱ ፡ ብቻ ፡
ሲኾን ፡ ነው ፤ ይህም ፥ ቃል ፡ ሥጋ ፡ ኮነ ፡ ብሎ ፡ ወኅደረ ፡ ውስቴትነ ፡ ባለው ፡ ይታ
ወቃል ።

፲፬ ፤ ዳግመኛም ፡ በወ ፡ ከፋይነትና ፡ አያያዥነት ፡ የነገር ፡ የታሪክ ፡ ማንሻና ፡
መነሻ ፡ ሲኾን ፡ እንደ ፡ ብህለና ፡ እንደ ፡ ይቤ ፡ አንቀጽ ፡ ይስባል ። ይህም ፥ ወኮነ ፡ እም
ድኅረ ፡ ሞተ ፡ ሙሴ ፤ ይቤሎ ፡ እግዚ ፡ ለኢያሱ ። ወኮነ ፡ በመዋዕለ ፡ ሄሮድስ ፡ ንጉሥ ፤
ሀሎ ፡ አሐዱ ፡ ካህን ። ወኮነ ፡ በውእቱ ፡ መዋዕል ፤ ወፅአ ፡ ትእዛዝ ፡ እያለ ፡ ሌላውን ፡
ኹሉ ፡ ያሳያል ። ጽንዕም ፡ ሲኾን ፥ አካኼዱ ፡ እንደ ፡ ሀለወ ፡ ነው ፤ ከትንቢት ፡ አን
ቀጽ ፡ እየተደረበ ፡ ነበር ፡ ተብሎ ፡ ይፈታል ። አገባቡንም ፡ በ፳ኛ ፡ ዕርከን ፡ ተመልከት ፡
(ቍ፳) ።     ሀለወ ፡ ደግሞ ፥ ሀሎ ፡ ይጽሕፍ ፡ አው ፡ ይጽሕፍ ፡ ሀሎ ፡ እያሰኘ ፡ የትን
ቢት ፡ ትርአስና ፡ ትርጋፅ ፡ ሲኾን ፡ ይጥፋል ፡ ብሎ ፡ ያኹኑን ፥ ይጥፍ ፡ ነበር ፡ ብሎ ፡
ያለፈና ፡ የሚመጣ ፡ ጊዜ ፡ ያሳያል ። ተዘርዝሮም ፥ ሀለዎሙ ፡ ይእመኑ ፡ ቦቱ ፥ ዘሀለዎ ፡
ይኩን ፡ ፍጡነ ፥ እስመ ፡ ሀለዎ ፡ ይሙት ፡ እያሰኘ ፡ ዘንድ ፡ አንቀጽ ፡ ሲስብ ፥ ወደ ፡ ፊት ፡
የሚመጣ ፡ እንጂ ፡ ያለፈ ፡ አያሳይም ። የሳቢና ፡ የተሳቢ ፡ ነገር ፡ ባጭሩ ፡ ይህ ፡ ነው ።

## መጨረሻ ፡ ዐዋጅ ።

፲፯ ፤ ግእዝ ፡ ኃምስ ፡ ሳብዕ ፡ የሚኾነውን ፥ ሳድስ ፡ ሣልስ ፡ ካዕብ ፡ ከማድረግ ፥ ሳድስ ፡ ሣልስ ፡ ካዕብ ፡ የሚኾነውን ፥ ግእዝ ፡ ኃምስ ፡ ሳብዕ ፡ ከማድረግ ፡ ተጠንቀቅ ። በባለቤትና ፡ በዘርፍ ፡ በቅጽል ፡ መካከል ፡ ሌላ ፡ እንዳይገባ ፥ በሳቢና ፡ በተሳቢም ፡ ማኸል ፡ ባዕድ ፡ አይገባም ። ይህም ፡ በማእድ ፡ ነዳይ ፡ በሊዐ ፡ ኅብዝት ፡ አለማለቱን ፡ ያሳያል ። ሳቢና ፡ ተሳቢ ፡ ማስተላለፍ ፡ ብርቱ ፡ ጸያፍ ፡ ነው ። እምአርዑተ ፡ ኀጢአት ፡ ኢየሱስ ፡ ዘአግዐዘ ፡ ትዝምደ ፡ ሰብእ ፤ ወይም ፡ ለተቀንዎ ፡ አምላክ ፡ ዘኢያኀጽርከ ፡ አእጋረ ፡ አያሰኝም ። የዚህ ፡ ዐይነት ፡ ጸያፍ ፡ ስሙ ፡ ግሥግሥ ፡ ይባላል ፤ ኅብስተ ፡ ለበሊዕ ፡ አይልም ፡ ያልነውም ፡ መከታ ፡ ይባላል ፤ መከታውም ፡ ለ ፡ ነው ።

## ፲፯ኛ ፡ ዕርከን ።

## ዘርፍና ፡ ባለቤት ፥ ተናባቢና ፡ ተያያዥ ።

፲፯ ፤ ዘርፍ ፡ ማለት ፥ ዘይቤው ፡ ዘፈረ ፡ ቃል ፥ ትርጓሜው ፡ ዐጭር ፡ ቅጽል ፥ ምስጢሩ ፡ ግን ፡ ባለወገንና ፡ ባለገንዘብ ፥ የስም ፡ ተውሳክ ፡ የባለቤት ፡ ምስማክ ፡ ማለት ፡ ነው ። ባለቤትም ፡ ማለት ፥ ባለዘርፍ ፡ የዘርፍና ፡ የቅጽል ፡ ጌታ ፥ ዘርፉን ፡ ተቈራኝቶ ፡ እንደ ፡ ኵታ ፡ ዐብሮ ፡ የሚታሰር ፡ የሚፈታ ፡ ማለት ፡ ነው ። አገናኝቶም ፡ ዘርፍና ፡ ባለቤት ፡ ሲሉት ፥ ነፍስና ፡ ሥጋ ፡ ወይም ፡ ባልና ፡ ሚስት ፡ እንደ ፡ ማለት ፡ ኹኖ ፡ ዕሙርነቱን ፡ ያሳያል ። ዘርፍ ፡ ኹሉ ፡ የርሱን ፡ ስምና ፡ ባለገንዘብነት ፡ መደብ ፡ አድርጎ ፡ የባለቤቱን ፡ ገንዘብነት ፡ ስሙና ፡ ግብሩን ፡ ወገኑን ፡ ዐይነቱን ፡ ገልጦ ፡ የሚያሳይ ፡ ዐጭር ፡ ቅጽል ፡ እንደ ፡ መኾኑ ፥ ባስተሳሰሩና ፡ ባፈታቱ ፡ የዘ ፡ እንተ ፡ እለን ፡ ዐማርኛ ፡ የን ፡ አይለቅም ።

፲፰ ፤ ዘርፍና ፡ ባለቤት ፡ የሚባሉ ፡ በ፪ ፡ አገባብ ፡ በለና ፡ በዘእንተእለ ፡ ተያይዘው ፥ ወይም ፡ በ፬ ፡ ፊደል ፡ በግእዝ ፡ በራብዕ ፥ በኃምስ ፡ በሳብዕ ፡ ተናበው ፡ የሚጣፉና ፡ የሚጠሩ ፥ ተከታትለው ፡ የሚነገሩ ፡ ፪ ፡ ስሞች ፡ ናቸው ፤ አምላክ ፥ ሰማይ ፥ እነዚህን ፡ የመሰለ ፡ ኹሉ ። ፪ቱ ፡ ቀንጃ ፡ ስም ፡ በገባብ ፡ በፊደል ፡ ሲያያዝና ፡ ሲናበብ ፥ አምላኩ ፡ ለሰማይ ፥ አምላክ ፡ ዘሰማይ ፥ አምላከ ፡ ሰማይ ፥ ደብተራ ፡ አሪት ፡ ፍሬ ፡ በለስ ፡ ገቦ ፡ ኢየሱስ ፡ አሰኝቶ ፡ ፍችውንም ፡ የሰማይ ፡ አምላክ ፡ የኦሪት ፡ ድንኳን ፡ የበለስ ፡ ፍሬ ፡ የኢየሱስ ፡ ጐን ፡ እያሰኘ ፡ ኹሉን ፡ ያሳያል ። መንታ ፡ ዘርፍም ፡ ሲኾን ፡ አምላክ ፡ ሰማይ ፡ ወምድር ፥ እግዚአ ፡ መላእክት ፡ ወሰብእ ፥ ነቢያተ ፡ ይሁዳ ፡ ወሰማርያ ፡ ወባቢሎን ፡ እያሰኘ ፡ በወ ፡ ያጫፍራል ። ባለቤትም ፡ መንታ ፡ እየኾነ ፡ በዋዌ ፡ ተጫፍሮ ፡ ባንዳንድ ፡ ዘርፍ ፡ ላይ ፡ ይናበባል ። ኅሩያነ ፡ ወሠናያነ ፡ ሊባኖስ ። ተምያጠ ፡ ወተውላጠ ፡ ህላውያት ፤ ጽጌያተ ፡ ወፍሬያተ ፡ ትሩፋት ። ሦስት ፡ እየኾነም ፡ ሲጫፈር ፡ ጥንተ ፡ ወተፍጻመ ፡ ወማእከለ ፡ መዋዕል ። ድምፀ ፡ ወጣሕረ ፡ ወግርማ ፡ አራዊት ፡ ይላል ። ይህም ፡ አካኼድ ፡ በመጽሐፍ ፡ እንጂ ፡ በቅኔ ፡ አልተለመደም ።

፳ ፤ ያ፩ኛው ፡ አገባብ ፡ የለ ፡ ፊደሉ ፡ ፩ ፡ እንደ ፡ ኾነ ፡ ዐዋጁም ፡ ፩ ፡ ነው ፤ ይኸውም ፡ ላንድና ፡ ለብዙ ፡ ለወንድና ፡ ለሴት ፡ አያያዥ ፡ መኾን ፡ ነው ። ዘ ፡ እንተ ፡ እለ ፡

ግን ፡ ምንም ፡ በማያያዝ ፡ እንዘ ፡ ሠለስቱ ፡ አሐዱ ፡ ቢባሉ ፡ የንባብና ፡ የምስጢር ፡ ልዩ ነት ፡ ስላላቸው ፥ ዐዋጃቸውም ፡ እንደ ፡ ንባባቸው ፡ ፫ ፡ ነው ፤ ዘ ፡ ላንድ ፡ ወንድ ፡ ብቻ ፥ እንተ ፡ ላንዲት ፡ ሴት ፡ ብቻ ፥ እለ ፡ ለ፪ቱም ፡ ወገን ፡ ብዙዎች ፡ ለወንዶች ፡ ለሴቶች ፡ ተብለው ፡ ይነገራሉ ፤ በቅጽልነትም ፡ እንዲሁ ፡ ናቸው ። ይህም ፡ ዐዋጅ ፡ ያዋቆችና ፡ የጠንቃቆች ፥ ያይናሞችና ፡ የልባሞች ፡ እንጂ ፡ የኹሉ ፡ አይደለም ፤ የሌሎቹስ ፡ ዐ ዋጅ ፡ ወንድና ፡ ሴት ፡ ሳይለይ ፥ እንተ ፡ ላንድ ፡ ዘ ፡ ላንድና ፡ ለብዙ ፡ እለ ፡ ለብዙ ፡ ተ ብሎ ፡ በሽፍንነት ፡ ይነገራል ።

፷፩ ፤ ለ ፡ ላንድና ፡ ለብዙ ፥ ለወንድና ፡ ለሴት ፡ አያያዥ ፡ ሲኾን ፥ ጥበቡ ፡ ጥበባ ቲሁ ፡ ለሰሎሞን ፤ ምክሮሙ ፡ ምክራቲሆሙ ፡ ለጠቢባን ፤ ዕበያ ፡ ዕበያቲሃ ፡ ለድንግል ፤ ክብሮን ፡ ክብራቲሆን ፡ ለአንስት ፡ ያሰኛል ። የዘርፉንም ፡ ዘርፍ ፡ ቀስተ ፡ መሐላሁ ፡ ለኖኅ ፤ ደቀ ፡ ጽርሑ ፡ ለዳዊት ፡ ወመገብተ ፡ ቤቱ ፡ ያሰኛል ። ደፍቶም ፡ ሲያያይዝ ፥ ለኖኅ ፡ ሐመሩ ፥ ለአሮን ፡ በትሩ ፥ ለጌዴዎን ፡ ፀምሩ ፡ ያሰኛል ። የዘርፉንም ፡ ሲደፋ ፥ ለዳዊት ፡ መሰንቆ ፡ መዝሙሩ ፥ ለሰሎሞን ፡ መንበረ ፡ ክብሩ ፥ ለፍሬ ፡ ስብሐት ፡ መጸሩ ፡ ያሰኛል ፤ አንዳንድ ፡ መምህራን ፡ ለ ፡ ለዘርፍ ፡ ብቻ ፡ እንጂ ፥ ለዘርፍ ፡ ዘርፍ ፡ ደፊነት ፡ የለውም ፡ ይላሉ ። ዘ ፡ እንተ ፡ እለም ፡ ሲያያይዙ ፥ መዝሙር ፡ ዘዳዊት ፥ መዘምራን ፡ እለ ፡ ዳዊት ፥ ብእሲት ፡ እንተ ፡ ዳዊት ፥ ዕቁባት ፡ እለ ፡ ሰሎሞን ፤ ወይም ፡ ደፍተው ፡ ዘዳዊት ፡ መዝሙር ፡ እለ ፡ ዳዊት ፡ መዘምራን ፤ እንተ ፡ ዳዊት ፡ ብእሲት ፥ እለ ፡ ሰሎ ሞን ፡ ዕቁባት ፡ ያሰኛሉ ።

፷፪ ፤ ዘርፍና ፡ ባለቤት ፡ ተሳቢ ፡ ኹኖ ፡ በ፪ ፡ አገባብ ፡ ሲያያዝ ፥ የባለቤቱ ፡ መድ ረሻ ፡ ነባር ፡ ፊደል ፡ ካልኾነ ፡ በቀር ፡ እንዳንቀጹ ፡ ጠባይ ፡ በመወራረስ ፡ ይነገራል ። ይህም ፡ ቀተለ ፡ ኢዮአብ ፡ ብሎ ፥ ፀረ ፡ ዳዊት ፥ አፅራረ ፡ እለ ፡ ዳዊት ፥ ዕቤረ ፡ እንተ ፡ ዳዊት ፤ ፀሮ ፡ አፅራሮ ፡ ዕቤሮ ፡ ለዳዊት ፤ ወይም ፡ ደፍቶ ፡ ዘዳዊት ፡ ፀረ ፥ እለ ፡ ዳዊት ፡ አፅራረ ፥ እንተ ፡ ዳዊት ፡ ዕቤረ ፤ ለዳዊት ፡ ፀሮ ፡ አፅራሮ ፡ ዕቤሮ ፡ ይላል ፡ እንጂ ፤ ፀር ፡ አፅራር ፡ ዕቤር ፥ ፀሩ ፡ አፅራሩ ፡ ዕቤሩ ፡ አይልም ፤ ጸላኢ ፡ ባለውም ፡ እንዲሁ ፡ ነው ። ዳግመኛም ፡ ተቀትለ ፡ ብሎ ፡ ፀር ፡ ፀሩ ፥ ተቀትሉ ፡ ብሎ ፡ አፅራር ፡ አፅራሩ ፥ ተቀትለት ፡ ብሎ ፡ ዕቤር ፡ ዕቤሩ ፡ ቢል ፡ እንጂ ፥ ፀረ ፡ ፀሮ ፥ አፅራረ ፡ አፅራሮ ፡ ዕቤረ ፡ ዕቤሮ ፡ አይ ልም ። ካዕብና ፡ ሳብዕ ፡ መዋረሳቸው ፡ ዝርዝሩ ፡ እንዲህ ፡ እንዳኹኑ ፡ ዘመድ ፡ ሲኾን ፡ ነው ፤ ባዕድ ፡ ሲኾን ፡ ግን ፥ ጕልትነትና ፡ ስያፍነት ፡ ያስቀርባቸዋል ፤ ይህም ፡ ጸላኢሁ ፡ ብሎ ፡ ቀተለ ፡ ተቀትለ ፥ አፅራሪሁ ፡ ብሎ ፡ ቀተሉ ፡ ተቀትሉ ፡ እያሰኘ ፡ ሌላውን ፡ ኹሉ ፡ ያሳያል ።

፷፫ ፤ ዘርፍ ፡ ከባለቤት ፡ በ፪ ፡ አገባብ ፡ ሲያያዝ ፡ የባለቤትን ፡ ፍጻሜ ፡ በገቢርና ፡ በተገብሮ ፡ ለይተው ፡ የሚያስታውቁ ፡ ፊደላት ፡ ግእዝና ፡ ሳድስ ፡ ካዕብና ፡ ሳብዕ ፡ ሣል ስና ፡ ኃምስ ፡ እነዚህ ፡ ፮ቱ ፡ ተቃራንያን ፡ ይባላሉ ፤ ተወራራሾች ፡ ማለት ፡ ነው ፤ (መቅ ፡ ቍ፷) ። መድረሻው ፡ ፊደል ፡ ግን ፡ ነባር ፡ ሲኾን ፥ ዓሣ ፡ ባሕር ፡ ብሎ ፡ አሥገረ ፥ ወይም ፡ ተሠግረ ፤ አርዌ ፡ ምድር ፡ ብሎ ፥ ቀተለ ፥ ወይም ፡ ተቀትለ ፤ ስብከ ፡ ዕፅ ፡ ብሎ ፡ ሰበረ ፡ ወይም ፡ ተሰብረ ፡ እያሰኘ ፥ ገቢር ፡ ተገብሮ ፡ ያሰማማል ፤ እነዚህም ፡ ፫ቱ ፡ ፊደ

ላት ፡ (ሣ ፡ ዌ ፡ ክ) ፡ ተፋቃርያን ፡ ይባላሉ ። ባ፬ ፡ ፊደልም ፡ ሲናበብ ፡ ፪ቱ ፡ በዝርዝር ነት ፡ ፪ቱ ፡ በነባርነት ፡ ገቢር ፡ ተገብሮ ፡ ያሰማሙለታል ፤ ዝርዝርነቱም ፡ ሳድሱን ፡ ግእዝ ፥ ሣልሱን ፡ ኃምስ ፡ ማድረግ ፡ ነው ። ግእዝና ፡ ኃምስ ፡ በዝርዝርነት ፡ እየተና በቡ ፡ ሲያሰማሙ ፤ ሃይማኖተ ፡ ወንጌል ፡ ብሎ ፡ ሰበከ ፡ ወይም ፡ ተሰብከ ፤ ጸላኤ ፡ ዳዊት ፡ ብሎ ፡ ሞአ ፡ ወይም ፡ ተሞአ ፡ ያሰኛሉ ። ለራብዕና ፡ ለሳብዕ ፡ ግን ፡ ነባርነት ፡ እንጂ ፡ ዝርዝርነት ፡ የላቸውም ፤ የነባርም ፡ ምስጢር ፡ ጕልትነት ፡ ነው ።

፺፬ ፤ ዘርፍና ፡ ባለቤት ፡ በ፪ ፡ አገባብ ፡ ሲያያዙና ፡ ባ፬ ፡ ፊደላት ፡ ሲናበቡ ፡ የሚ ያሳዩትና ፡ የሚያሰሙት ፡ ምስጢር ፡ ብዙ ፡ ነው ፤ ፩ኛው ፡ ገንዘብነትና ፡ ባለገንዘብነት ። ይህም ፡ መዝሙር ፡ ዘዳዊት ፥ መዝሙሩ ፡ ለዳዊት ፥ መዝሙረ ፡ ዳዊት ፡ ብሎ ፥ የዳ ዊት ፡ መዝሙር ፡ እያሰኘ ፡ መዝሙር ፡ ገንዘብ ፥ ዳዊት ፡ ባለገንዘብ ፡ መኾኑን ፡ ያሳያል ። ማሳየቱም ፡ ዘርፍ ፡ እንዲህ ፡ እንዳኹኑ ፡ ነባቢ ፡ አካል ፡ ኹኖ ፥ ባለቤት ፡ ኢነባቢ ፡ ስም ፡ ሲኾን ፡ ነው ። ፪ኛም ፥ ባለቤት ፡ ነባቢ ፡ ዘርፍ ፡ ኢነባቢ ፡ ኹኖ ፥ መልአከ ፡ ሰማይ ፡ ብእሴ ፡ ምድር ፡ ሲል ፥ ወገንና ፡ ባለወገንን ፡ ያሳያል ፤ መልአክና ፡ ብእሲ ፡ ወገን ፥ ሰማ ይና ፡ ምድር ፡ ባለወገን ። መናበብና ፡ መያያዝም ፡ ሲቀር ፡ መልአክ ፡ ሰማያዊ ፡ ብእሲ ፡ ምድራዊ ፡ እያሰኘ ፡ ወገን ፡ ቅጽል ፡ ኹኖ ፡ ይነገራል ። ዘርፎችን ፡ በዘርፍነታቸው ፡ አቁሞ ፡ ባለገንዘብና ፡ ባለወገን ፡ የሚያደርጋቸው ፡ በለ ፡ መያያዝ ፡ ነው ፤ ዘ ፡ እንተ ፡ እለና ፡ መናበብ ፡ ግን ፡ ግልጠ ፡ ዘና ፡ ውስጠ ፡ ዘ ፡ ኹነው ፡ አንቀጽ ፡ እየሰጡ ፡ ዘርፍን ፡ ኹሉ ፡ ወደ ፡ ቅጽልነት ፡ ይስባሉ ።

፺፭ ፤ ፫ኛም ፡ ዘርፍና ፡ ባለቤት ፡ ፪ቱም ፡ ኢነባብያን ፡ ሲኾኑ ፡ ዝርዝርና ፡ ለን ፡ አያስገቡምና ፥ ባንድ ፡ አገባብ ፡ ብቻ ፡ በዘ ፡ እንተ ፡ እለ ፡ ተያይዘው ፥ ባ፬ ፡ ፊደላት ፡ ተናበው ፡ ሲዛረፉና ፡ ሲነገሩ ፡ ቅጽልና ፡ ባለቤት ፡ ኹነው ፡ ሥራንና ፡ መሥሪያን ፡ ያሳ ያሉ ። ይህም ፡ ተቋም ፡ ዘወርቅ ፥ ልብሰ ፡ ወርቅ ፥ ወልታ ፡ ወርቅ ፥ አርዌ ፡ ብርት ፥ ስብከ ፡ ዕፅ ፡ ብሎ ፡ ተቋሙ ፡ ልብሱ ፡ ወልታሁ ፡ ለወርቅ ፥ አርዌሁ ፡ ለብርት ፡ ስብከሁ ፡ ለዕፅ ፡ አለማሰኘቱን ፡ መደብ ፡ አድርጎ ፡ ተቋምና ፡ ልብስ ፡ ወልታና ፡ አርዌ ፡ ስብከ ፡ ሥራ ፡ እንደ ፡ ኾኑ ፡ ወርቅና ፡ ብርት ፡ ዕፅ ፡ መሥሪያ ፡ እንደ ፡ ኾኑ ፡ ያሳያል ። ሲፈታም ፡ ዘግ ቡር ፡ እምወርቅ ፥ ዘልቡጥ ፡ በወርቅ ፥ ግቡረ ፡ ብርት ፡ ዘተገብረ ፡ እምዕፅ ፡ እያሰኘ ፡ ቅጽል ፡ ይኾናል ፤ ስሙም ፡ ሥረ ፡ ወጥ ፥ ወይም ፡ ዘመድ ፡ ዘርፍ ፡ ይባላል ።

፺፮ ፤ ፬ኛም ፡ የባሕርይ ፡ ስም ፡ ከህላዌ ፡ ስም ፡ ተናቦ ፡ ሲዛረፍ ፡ የህላዌ ፡ ስም ፡ ለባሕርይ ፡ ስም ፡ መፍቻና ፡ ቅጽል ፡ እየኾነ ፡ ባሕርይና ፡ መልክን ፡ ያሳያል ። ይህም ፡ ዕፀ ፡ አውልዕ ፡ ብሎ ፡ ወይራ ፡ የሚባል ፡ ዕንጨት ፥ የወይራ ፡ ዕንጨትነት ፥ ወይም ፡ ወይራው ፡ ዕንጨት ፡ እያሰኘ ፡ የዕፅን ፡ ባሕርይነትና ፡ የርሱን ፡ ህላዌነት ፡ ያስረዳል ። ዕፅ ፡ ብሕርዩና ፡ የባሕርይ ፡ ስሙ ፡ ነው ፤ አውልዕም ፡ ከዕፀዋት ፡ ኹሉ ፡ ተለይቶ ፡ የሚ ታወቅበት ፡ ህላዌውና ፡ የህላዌው ፡ ስም ፡ ነው ። ህላዌም ፡ ማለት ፡ አናዎር ፡ ጠባይ ፡ ግዘፈ ፡ ባሕርይ ፥ የተፈጥሮ ፡ ልክ ፡ ዐይነትና ፡ መልክ ፡ ማለት ፡ ነው ፤ አካል ፡ እንደ ፡ ማለት ። ህላዌ ፡ አስተጋባኢ ፡ ስም ፡ ስለ ፡ ኾነ ፡ ለፈጣሪም ፡ ሳይቀር ፡ ለፍጡራን ፡ ኹሉ ፡

ይነገራል ፤ አካል ፡ ግን ፡ እኔ ፡ እገሌ ፡ ብሎ ፡ ስሙንና ፡ ግብሩን ፡ ለሚናገር ፡ ለነባቢ ፡ በሕርይ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ ለኢነባብያን ፡ አይኾንም ።

፳፯ ፤ ፫ኛም ፡ የግብር ፡ ስም ፡ ከተጸውዖ ፡ ስም ፡ ሲናበብ ፡ ዘርፉ ፡ ለባለቤት ፡ ቅጽል ፡ እየኾነ ፡ እንዲሁ ፡ ይፈታል ፤ ይህም ፡ ነቢየ ፡ ሙሴ ፡ ብሎ ፡ ሙሴ ፡ የሚባል ፡ ነቢይ÷ወይም ፡ ነቢዩ ፡ ሙሴ ፡ ማለቱን ፡ ያሳያል ። የተቀብዖም ፡ ስም ፡ ካህነ ፡ አሮን ፡ ብሎ ፡ እንዲሁ ፡ ይፈታል ፤ በዘርፍም ፡ አፈታት ፡ ሲቃኙት ፡ የሙሴ ፡ ነቢይነት ፡ የአሮን ፡ ክህንነት÷ክህን ፡ መኾኑ ፡ ክህን ፡ መባሉ ፡ እያሰኘ ፡ በሕርይና ፡ ግብርን ፡ ያሳያል ። የተጸውዖ ፡ ስም ፡ ማናቸውም ፡ ስም ፡ ተናበበት ፡ ዘርፍ ፡ ይኾናል ፡ እንጂ÷ርሱ ፡ በሌላ ፡ ስም ፡ ተናበ ፡ የዘርፍ ፡ ባለቤት ፡ አይኾንም ፤ ይህም ፡ ዳዊት ፡ መንግሥት ፡ አሮን ፡ ክህነት ፡ አለማሰኘቱን ፡ ያሳያል ። ያገርም ፡ ስም ፡ ቢኾን ፡ እንደዚሁ ፡ ነው ፤ ናዝሬት ፡ ኢየሱስ÷ወይም ፡ ኢየሱሰ ፡ ናዝሬት ፡ አያሰኝም ፤ ናዝሬት ፡ እንተ ፡ ኢየሱስ÷ ኢየሱስ ፡ ናዝራዊ ፡ ቢያሰኝ ፡ እንጂ ። በዘ ፡ እንተ ፡ እለም ፡ ሲያያዝ ፡ ጊዮርጊስ ፡ ዘልዳ÷ ማርያም ፡ እንተ ፡ ዕፍረት ፡ ቢል÷ዘርፉ ፡ ልዳዊ ፡ ብእሴ ፡ ልዳ÷ዕፍረታዊት ፡ በዓልተ ፡ ዕፍረት ፡ እያሰኘ ፡ ወገን ፡ ቅጽል ፡ ይኾናል ፡ እንጂ ፤ ባለወገን ፡ ዘርፍ ፡ አይኾንም ።

፳፰ ፤ የባሕርይም ፡ ስም ፡ ብእሲ ፡ ዘለምጽ÷ዕደው ፡ እለ ፡ ለምጽ ፤ ወይም ፡ ብእሴ ፡ ለምጽ÷ዕደወ ፡ ለምጽ ፡ ብሎ ፡ ሲያያዝና ፡ ሲናበብ ፡ ለምጻዊ ፡ ልሙጽ ፡ ዘቦቱ ፡ ለምጽ ፤ ልሙጻን ፡ እለ ፡ በሙ ፡ ለምጽ ፡ እያሰኘ ፡ በቅጽልነት ፡ ይፈታል ፤ ሲደፋም ፡ ዘብእሲ ፡ ማቴዎስ ፡ ቢል ፡ ፍችው ፡ እንደዚሁ ፡ ነው ። ዘርፍን ፡ ከቅጽል ፡ ለይቶ ፡ ዘርፍ ፡ የሚያሰኘው ፡ መያያዝና ፡ መናበብ ፡ ብቻ ፡ ነው ፤ ባፈታትና ፡ በምስጢር ፡ ግን ፡ ከቃላቅ ፡ ወንድሙ ፡ ከቅጽል ፡ ልዩነት ፡ የለውም ። እስካኹን ፡ ድረስ ፡ በነጠላነት ፡ የተነገረው ፡ ዘርፍ ፡ ፪ ፡ ዐይነት ፡ ነው ፤ ፩ኛው ፡ ባለገንዘብና ፡ ባለወገን÷፪ኛው ፡ ዘመድ ፡ ወይም ፡ ሥረ ፡ ወጥ ፤ አካኼዱም ፡ የመጽሐፍ ፡ ንባብ ፡ ነው ፤ ለቅኔም ፡ ይኾናል ። የዘርፍና ፡ የባለቤት ፡ ጠባይ ፡ በሠምና ፡ በወርቅ ፡ አካኼድ ፡ ስሙና ፡ ጓዙ ፡ ስለ ፡ በዘ ፡ ጸዋትወ ፡ ቅኔ ፡ ተብሎ ፡ ለብቻው ፡ ፩ ፡ ወገን ፡ ተጠቅሎ ፡ በልዩነት ፡ ተጽኝልና ፤ ከዚህ ፡ የቀረውን ፡ በ፫ኛው ፡ ክፍል ፡ ተመልከት ። አርእስትና ፡ ሳቢ ፡ ዘርም ፡ ውስጠ ፡ ዘ ፡ ሳይቀር ፡ ሳቢና ፡ ተሳቢ ፡ በመኾን ፡ ዘርፍና ፡ ባለቤት ፡ ኹነው ፡ እየተናበቡ ፡ ገቢር ፡ ተገብሮ ፡ ያሳያሉና ፤ ይህም ፡ በሳቢና ፡ በተሳቢ ፡ ቦታ ፡ ተነግሯል ። የዘርፍ ፡ ነገር ፡ ከምሉ ፡ በክፍሉ ፡ ይህ ፡ ነው ።

## ፲፰ኛ ፡ ዕርከን ።

## ቅጽልና ፡ ባለቤት ።

፳፱ ፤ ቅጽል ፡ ማለት ፡ ከባለቤት ፡ ጋራ ፡ እንደ ፡ ዘርፍ ፡ ሳይያያዝና ፡ ሳይናበብ ፡ የባለቤትን ፡ ጠባይና ፡ አኗዎር ፡ ለመግለጥ ፡ ዐብሮት ፡ የሚነገር ፡ ማለት ፡ ነው ፤ ባለሟል ፡ ወይም ፡ አስተርጓሚ ፡ እንደ ፡ ማለት ፡ (ቍ፱፲፫) ። ቅጽልም ፡ እንደ ፡ ዘርፍ ፡ ፪ ፡ ዐይነት ፡ ነው ፤ ዘመድ ፡ ቅጽልና ፡ ባዕድ ፡ ቅጽል ። ሲዘረዘር ፡ ግን ፡ ስሙ ፡ ፰ ፡ ነው ፤ ውስጠ ፡ ዘ÷

ግልጠ ፡ ዘ ÷ ወገን ፡ ቅጽል ÷ መስም ÷ ጥሬ ÷ ንኡስ ÷ ደቂቅ ÷ አኃዝ ፡ ይባላል ። ዘመድና ፡ ባዕድ ፡ ያሰኘውም ፡ ጌታውንና ፡ ባለቤቱን ፡ መምሰልና ፡ አለመምሰል ፡ ነው ።

## ዘመድ ፡ ቅጽል ።

፴፤ ውስጠ ፡ ዘ ፤ መንፈስ ፡ (ሰ) ፡ ናዝዚ ፡ (ዜ) ፤ መልአክ ፡ (ከ) ፡ ፍንው ፡ (ወ) ፤ አምላክ ፡ (ከ) ፡ ዐቢይ ፡ (የ) ፤ ብእሲ ፡ (ሴ) ፡ መካሕ ፡ (ሐ) ፡ (ቊ፳፩—፳፫) ። ግልጠ ፡ ዘ ፤ ጳውሎስ ፡ ዘተጸውዐ ÷ ፊቤን ፡ አንተ ፡ ትትለአክ ÷ አርድእት ፡ እለ ፡ ተኀርዩ ። ወገን ፤ አብርሃም ፡ (ሀ) ፡ ከለዳዊ ፡ (ዌ) ። መስም ፤ ዳዊት ፡ መዘምር ፡ ዳዊትሀ ፡ መዘምረ ፤ ሰሎሞን ፡ (ሀ) ፡ ማእምር ፡ (ረ) ። ጥሬ ፤ ወንጌል ፡ ጽንዐ ፡ ሃይማኖት ፤ ክርስቶስ ፡ አክሊለ ፡ ሰማዕት ። ንኡስ ፤ አይ ፡ አፍ ፡ ወአይ ፡ ከናፍር ÷ አይ ፡ አኰቴት ። ደቂቅ ፤ ውእቱ ፡ ሚካኤል ፤ ይእቲ ፡ ማርያም ፤ ዝኩ ፡ ብእሲ ፤ እንታክቲ ፡ ብእሲት ። አኃዝ ፤ አሐዱ ፡ እግዚአብሔር ÷ ወአሐቲ ፡ ሃይማኖት ።

፴፩፤ ቅጽል ፡ ከባለቤት ፡ ቀድሞ ፡ ወይም ፡ ተከትሎ ፡ ይነገራል ፤ ይህም ፡ ክቡር ፡ አምላክ ÷ አምላክ ፡ ክቡር ፡ እንደ ፡ ማለት ፡ ነው ። ቅጽል ÷ ባለቤት ፡ ሲቀር ፡ በቂ ፡ ይኾናል ፤ ይህም ፡ ድንግል ፡ ወለደት ፡ አምላከ ፤ ዘተወልደ ፡ እምድንግል ፡ አድኅነ ፡ ዓለመ ፡ እንደ ፡ ማለት ፡ ነው ። ቅጽል ፡ ከባለቤቱ ፡ አይርቅም ፤ ቢርቅ ፡ ግን ፡ ማሰሪያ ፡ አስፈላጊ ፡ ወይም ፡ መመርመሪያ ፡ ይኾናል ፤ ይህም ፡ እግዚአብሔር ፡ ክቡር ፡ በኀበ ፡ እስራኤል ፡ ሲል ፡ ቅጽልነቱን ፤ እግዚ ፡ በኀበ ፡ እስራኤል ፡ ክቡር ÷ ወይም ፡ ዘከብረ ፡ ሲል ÷ ማሰሪያ ፡ ማስፈለጉንና ፡ ተለዋጭነቱን ፡ ያሳያል ። ከባለቤትም ፡ በይርቅ ፡ ተሳቢ ፡ ካለው ፡ ማሰሪያ ፡ ማስፈለግ ፡ አይቀርም ፤ ኄር ፡ እግዚ ፡ ለእለ ፡ ይትዔገሥዎ ፡ እንዲል ። ውስጠ ፡ ዘና ፡ መስም ፡ ሲስቡ ፡ ባለቤታቸውን ፡ መምሰል ፡ አይተዉም ፤ ይህም ፡ አምላክ ፡ ክቡር ፡ በህላዌሁ ÷ አምላከ ፡ ክቡረ ፡ በህላዌሁ ። ማርያም ፡ መስተምሕርት ፡ ኀበ ፡ ወልዳ ÷ ማርያምሃ ፡ መስተምሕርተ ፡ ኀበ ፡ ወልዳ ፡ ማለቱን ፡ ያሳያል ።

፴፪፤ ላንድ ፡ ባለቤት ፡ ፪ ፡ ውስጠ ፡ ዘ ÷ ወይም ፡ ፪ ፡ ግልጠ ፡ ዘ ፡ ባንድ ፡ ወገን ፡ ሲቀጸል ፡ መንታ ፡ ይባላል ፤ ይህም ፡ ማርያም ፡ ኅሪተ ፡ አምላክ ፡ ወፍቅርተ ፡ መላእክት ፡ ዐርገት ፡ ሰማየ ። ተሰብሐ ፡ እግዚአብሔር ፡ ክቡረ ፡ ስም ፡ ወልዑለ ፡ ምኵናን ። (፪ ፡ ግልጠ ፡ ዘ) ፡ ተዐውቀ ፡ እግዚ ፡ ዘገብረ ፡ ሰማየ ፡ ወምድረ ፡ ወዘለብሰ ፡ ሥጋ ፡ በይሁዳ ፡ እንደ ፡ ማለት ፡ ነው ። ፪ኛም ፡ ላንድ ፡ ባለቤት ፡ ውስጠ ፡ ዘ ፡ ግልጠ ፡ ዘ ፡ እንዲህ ፡ እንዳኹኑ ፡ ተጫፍረው ፡ ባንድ ፡ ወገን ፡ አይቀጸሉም ፤ በግራና ፡ በቀኝ ፡ ሲቀጸሉ ፡ ግን ፡ ስማቸው ፡ መከዳ ፡ ይባላል ፤ ይህም ፡ አስተርአየ ፡ ልዑል ፡ አምላክ ፡ ዘኢያስተርኢ ፡ በሥጋ ፡ እንደ ፡ ማለት ፡ ነው ። በመከዳነት ፡ ግን ፡ መንታ ፡ እየኾኑ ፡ ቢቀጸሉ ፡ ጸያፍ ፡ አይባሉም ፤ ይህም ፡ ብዙኅ ፡ መልእክት ፡ ወነዊኀ ፡ ስብከት ፡ ጳውሎስ ፡ ዘተጸውዐ ፡ ወተፈልጠ ፡ እምአርድእት ፡ ተሰብሐ ፡ ጥቀ ፡ እምኵሎሙ ፡ ሐዋርያት ፡ እንደ ፡ ማለት ፡ ነው ።

፴፫፤ ፫ኛም ፡ የቅጽል ፡ ባለቤት ፡ ከአንቀጽ ፡ ባለቤት ፡ ቀድሞ ፡ የባለቤት ፡ አንቀጽ ፡ ሲወድቅበት ፡ አታላይ ፡ ቅጽል ፡ ይባላል ። ይህም ፡ ተመትረ ፡ ሥላሴ ፡ ዘፈጠሩ ፡

ጊዮርጊስ ፡ በሰይፊ ፡ ኀጺን ። ተሰቅለ ፡ ማርያም ፡ ዘወለደት ፡ አምላከ ፡ ዲበ ፡ ዕፅ ፡ ምኑን ። ተንሥአ ፡ ፈሪሳውያን ፡ ወሰዱቃን ፡ ዘሰቀሉ ፡ ክርስቶስ ፡ እሙታን ። በጥሬ ፡ ቅጽልም ÷ እሞሙ ፡ ለሰማዕት ፡ ብዙኃን ፡ ማርያም ፡ እያለ ፡ አታላይነቱን ፡ ያሳያል ። በባለቤት ፡ ላይ ፡ የሚወድቅ ፡ ነገር ፡ በዘርፍና ፡ በቅጽል ፤ በሳቢም ፡ የሚወድቅ ፡ በተሳቢ ፡ ይጠበቃል ። በዘርፍ ፡ ሲጠበቅ ÷ አክበርዎ ፡ መላእክት ፡ ለዘሰማይ ፡ አምላክ ፡ ይላል ። በቅጽልም ፡ ሲጠበቅ ÷ አዕበይዎ ፡ እስራኤል ፡ ለዘነግሥ ፡ ዳዊት ፡ ይላል ። በባለቤትም ፡ ሲጠበቅ ÷ ወተኀፍሩ ÷ እስመ ፡ እግዚአብሔር ፡ አኅሰሮሙ ፡ ይላል ። በቅጽል ፡ ተሳቢም ፡ ሲጠበቅ ÷ ረስዕዎ ፡ እስራኤል ፡ ለእግዚ ፡ ዘየዐቢ ፡ ኀይለ ፡ ወብዙኀ ፡ መንክረ ፡ ገብረ ፡ ሎሙ ፡ ይላል ።

፴፬ ፤ ፬ኛም ፡ መልክአ ፡ ፊደሉ ፡ ሳይለወጥ ፡ ወንድና ፡ ሴት ፡ እያስተባበረ ፡ ለ፪ቱም ፡ ወገን ፡ የሚቀጸል ÷ ፀዋግ ፡ ጸጓር ፡ አዳም ፡ ድንግል ÷ ሐለይት ፡ ሰንቀውት ፡ ቀነይት ፡ ዐበይት ÷ ይህን ፡ የመሰለ ፡ ፈናፍንት ፡ ቅጽል ፡ ስሙ ፡ መድበል ፡ ይባላል ። ሐዋሪ ፡ ከያኒ ፡ ከማለት ፡ የወጡ ፡ ሐዋርያና ፡ ኬንያም ፡ መሳይ ፡ ተከታይ ፡ የሌላቸው ፡ በሕታውያን ፡ ስለ ፡ ኹኑ ÷ የሣልስ ፡ ዲቃሎች ፡ ወይም ፡ ሕግ ፡ አፍራሾች ፡ ይባላሉ ። ሐዋርያትና ፡ ነቢያትም ፡ የሴቶች ፡ ብቻ ፡ እንጂ ፡ የወንዶች ፡ አይዶሉም ፤ ሐወርት ፡ ነበይት ፡ ካላለ ፡ መድበል ፡ ኹኖ ፡ አያስተባብርም ። ይኸውም ፡ በከኼዳቸው ፡ ይታወቃል ፤ ሐዋሪ ፡ ሪት ፤ ሐዋርያን ፡ ያት ፤ ሐወርት ። ነቢይ ፡ ይት ፤ ነቢያን ፡ ያት ፤ ነበይት ። ነበየ ፡ ተነበየ ፡ ማለት ÷ ነቢብ ፡ ነበ ፡ ተነበ ፡ ካለው ፡ የወጣ ፡ ዲቃላና ፡ ተቀጥላ ፡ ነው ። የብዙውንም ፡ ላንድ ፡ ሲቀጽል ÷ ሰማዕት ፡ መፃምርት ፡ ይላል ፤ ኹሉም ፡ የስሕተት ፡ ልማድ ፡ ነው ። ሌላም ፡ ይህን ፡ የመሰለ ፡ ብዙ ፡ ይገኛል ።

## ሐተታ ።

፴፭ ፤ የቅጽሎች ፡ ጠባይ ፡ ውስጠ ፡ ዘና ፡ ግልጠ ፡ ዘ ፡ በማለት ፡ ተወስኗል ፤ ከነዚህ ፡ ከ፪ቱ ፡ አይወጣም ። ዐይነታቸው ፡ ግን ፡ ብዙ ፡ ነው ፤ ከግልጠ ፡ ዘም ፡ ይልቅ ፡ የውስጠ ፡ ዘ ፡ ዐይነት ፡ ይበዛል ። ውስጠ ፡ ዘ ፡ ደግሞ ፡ ከመድረሻው ፡ ፊደል ፡ ስም ፡ ነሥቶ ፡ ሣልስና ፡ ሳድስ ፡ ይባላል ፤ የንባቡም ፡ ዐይነት ፡ ስድስት ፡ ነው ። ፩ኛው ፡ መከከሉን ፡ ራብዕ ፡ አድርጎ ፡ ቀታሊ ፡ ተቀታሊ ፡ አቅታሊ ፡ ተቃታሊ ፡ አስተቃታሊ ፡ እያሰኘ ፡ ከ፭ቱ ፡ አዕማድ ፡ ከኀላፊና ፡ ከትንቢት ፡ ወጥቶ ፡ በ፪ ፡ ይፈታል ። ፪ኛው ፡ መከከሉን ፡ ሣልስ ፡ አድርጎ ፡ ዐቢይ ፡ ነቢይ ፡ ዐዚዝ ፡ ገዚፍ ፡ ቀጢን ፡ ጻሊም ፡ ቄሪር ፡ እያለ ፡ በሳድስ ፡ ፊደል ፡ ይጨርሳል ። ፫ኛው ፡ መከከሉን ፡ በሣልስ ፡ ፈንታ ፡ ራብዕ ፡ ያደርጋል ፤ ነዳይ ፡ ሠናይ ፡ ጠዋይ ፡ ቀላይ ፡ መከሕ ፡ ከዋው ፡ ለዋው ፡ ጸያፍ ፤ የመሰለው ፡ ኹሉ ። ፬ኛው ፡ መነሻውን ፡ ራብዕ ፡ አድርጎ ፡ ኹሉን ፡ በሳድስ ፡ ይጨርሳል ፤ ጻድቅ ፡ ኃጥእ ፡ ራትዕ ፡ ባዕል ፡ ባዕድ ፡ ቃውም ፡ ላእክ ፡ ካህን ፤ የመሰለው ፡ ኹሉ ። ፭ኛው ፡ ዐመል ፡ ስላለበት ፡ (ኄረ ፡ ኀየረ ፡ ኄረወ) ፡ ኄር ፡ ኄራዊ ፤ ዬጋን ፡ ዬጋኒ ፡ ሤራዪ ፡ እያለ ፡ በኃምስ ፡ ይነሣል ፤ እስከ ኹን ፡ የተነገሩቱ ፡ ሳድሶች ፡ ኹሉም ፡ ካንደኛው ፡ ዐምድ ፡ የወጡ ፡ ናቸው ።

፴፮ ፤ ፮ኛው፡ግን፡ከተገብሮና፡ከሐውልት፡ይወጣል ፤ አካኼዱም፡ከነዚህ፡ልዩ፡ነው ። በሳድስ፡ተነሥቶ፡መካከሉን፡ካዕብ፡ያደርጋል ። ይህም፡ተቀትለ፡ቅቱል፥ተቀደሰ፡ቅዱስ፥ተሰብሐ፡ስቡሕ፥ነበረ፡ንቡር፥ደክመ፡ድኩም፥ጸንዐ፡ጽኑዕ፡ማለቱን፡ያሳያል ። በባረከ፡ቤት፡ግን፡መነሻውንም፡ቡሩክ፡ሱቱፍ፡ጉቡእ፡ሡሩር፡እያለ፡ካዕብ፡ያደርጋል ። በዴገነም፡ቤት፡ዲጉን፡ሢሩይ፡ሊሉይ፡ቂቁይ፡ጊጉይ፡እያለ፡በሣልስ፡ይነሣል ። መድረሻው፡ወ፡ሲኾን፡ህልው፡ሕስው፡እያለ፡ኹሉን፡ሳድስ፡ያደርጋል ፤ ያፈታቱም፡ምስጢር፡ሥራው፡ያለቀለት፡ያለፈና፡ያኹን፡ቢያሳይ፡እንጂ ፤ ገና፡ወደ፡ፊት፡የሚመጣ፡ትንቢት፡አያሳይም ። በዕብራይስጥም፡ሆዌ፡ይባላል ፤ ክውን፡የኾነ፡የተደረገ፡ማለት፡ነው ።

፴፯ ፤ የግልጠ፡ዘም፡ጠባይ፡፪፡ነው ፤ በአንቀጽ፡ላይ፡ሲወድቅ፡ቅጽል ፤ በጥሬ፡ላይ፡ሲወድቅ፡ዘርፍ፡አያያዥ፡ይባላል ። ጸጋ፡ዘአብ፡ኂሩት፡ዘወልድ፡ሱታፌ፡ዘመንፈስ፡ቅዱስ፡እንደ፡ማለት ፤ ምስጢሩ፡ግን፡ከቅጽልነት፡አይወጣም ። ወገን፡ቅጽልም፡ከዘርፍ፡አያያዥ፡ዘ፡የወጣ፡ነው ፤ አወጣጡም፡በዘርፍ፡አካኼድ፡ተነግሯል ። መስም፡ቅጽልም፡የሣልስና፡የሳድስ፡ውስጠ፡ዘ፡ድርብ፡ነው ፤ ከተገብሮ፡በቀር፡ካራቱ፡አዕማድ፡ከ፪፡ከ፪ቱ፡፩፡፩፡መስም፡ይወጣል ። ይህም፡ቀታሊ፡አቅታሊ፡ብሎ፡መቅተሊ፡መቅትል ፤ ተቃታሊ፡አስተቃታሊ፡ብሎ፡መስተቃትል፡ማለቱን፡ያሳያል ። አፈታቱም፡እንዳወጣጡ፡ዕጥፍ፡ድርብ፡ነው ፤ በቀታሊ፡እንደ፡ቀታሊ፥በአቅታሊም፡እንደ፡አቅታሊ፥በቀሩትም፡እንዲሁ፡ይፈታል ፤ በኹሉም፡ኀላፊና፡ትንቢት፡አለበት ።

፴፰ ፤ የዘርና፡የነባር፡ጥሬም፡ዘርፍ፡ሳይገዝ፡አለመቀጸሉ፥ውስጠ፡ዘነት፡ስለሌለው፡ነው ፤ ቤተ፡ልሔም፡ሀገረ፡ዳዊት፥ማርያም፡እመ፡አምላክ፥መላእክት፡ሐራ፡ሰማይ፥ያዕቆብ፡እኁወ፡እግዚእነ፡እያለ፡ዘርፍ፡ሲይዝ፡ግን፡ውስጠ፡ዘነትና፡የውስጠ፡ዘ፡አፈታት፡ያገኛል ። የግብርና፡የተቀብዖም፡ስም፡ዘርፍ፡ሳይዝ፡ለተጸውዖ፡ስም፡መቀጸሉ፡ውስጠ፡ዘ፡ስለ፡ኾነ፡ነው ፤ ይህም፡ኢየሱስ፡ክርስቶስ፡(ቅቡዕ) ፤ ስምዖን፡ጴጥሮስ፡(ኰኵሓዊ)፡ባለው፡ይታወቃል ፤ ግእዙማ፡ምን፡ተጠርጥሮ ። በስልኤል፡ነሃቢ፥ዮሴፍ፡ጸራቢ፥ገብርኤል፡መልአክ፥ዘካርያስ፡ካህን፡ወነቢይ፡ወሰማዕት ፤ የመሰለው፡ኹሉ ።

፴፱ ፤ ንኡስ፡ቅጽል፥በጥያቄ፡ቃል፡የሚነገር፡የተጠያቂና፡የተመርማሪ፡ቅጽል፡ነው ፤ አንድና፡ብዙ፥ወንድና፡ሴት፡ያስተባብራል፡(ቍ፪፲፯) ። ይህም፥አየ፡ገቦ፡ረገዙ ፤ አያተ፡ሥሕጻታተ፡ነበቡ ፤ በአይኒ፡ታሕጻጽ፡እያሰኘ ። ሲበቃም፥ምንት፡ውእቱ፡ሰብእ ፤ መኑ፡ዝንቱ ፤ መኑ፡ይእቲ፡ዛቲ ። መኑ፡አንተ ፤ ወምንት፡ንሕነ ፤ ምንት፡እማንቱ፡ማለቱን፡ያሳያል ። ለጊዜም፡ሲቀጸል ፤ በአይ፡መዋዕል፡ወበአይ፡አዝማን ፤ ለአይ፡ዓመታት፡ወለማእዜ፡መዋዕል ፤ አየ፡ጊዜ፡ሐይወ ። ለበታም፡ሲቀጸል፥እምአይ፡ብሔር፡አንተ፡ያሰኛል ። አይቴ፡ሲል፡ግን፡በቂ፡እየኾነ፡ባለቤት፡አልቦ፥አይቴኑ፡አሐውር ፤ አይቴ፡ብሔራ፡ወአይቴ፡ማኅደራ፡ያሰኛል ። ለሌላውም፡ጥሬ፡ሲቀጸል፥በአይ፡ሥልጣን ፤ ታሕተ፡አይ፡ዕፅ ። በከፊልም፥

አይ ፡ ዕፅ ፡ ይኄይስ ፡ እምዕፀው ፡ ያሰኛል ፡፡ ስፍን ፡ እስፍንቱም ፡ እንዲሁ ፡ ናቸው ፤ ስፍን ፡ ኀፍረት ፡ ዘይረክበኒ ፡ በይእቲ ፡ ዕለት ፤ እስፍንቱ ፡ መዋዕሊከ ፡፡ አንክሮም ፡ ሲኾኑ ፥ እስፍንተ ፡ ተአምራተ ፡ ረብሐ ፤ እስፍንተ ፡ እዜኑ ፡ እከያቲሃ ፡ ለልሳን ፡ ያሰኛሉ ፡፡

፵ ፤ ደቂቅ ፡ ቅጽል ፤ ከውእቱ ፡ እስከ ፡ ንሕነ ፡ ያሉ ፡ ፲ሩ ፡ የኪያሁ ፡ ተወራራሾች ፥ ወይም ፡ ተቃዋሚዎቹ ፡ ስለ ፡ ኾኑ ፥ በማድረግ ፡ አድራጊ ፥ በማስደረግ ፡ አስደራጊ ፡ በማደራረግ ፡ አደራራጊ ፡ እየኾኑ ፡ ይነገራሉ ፡ እንጂ ፤ እንደ ፡ ኪያሁ ፡ በማድረግ ፡ ተደ ራጊ ፥ በማስደረግ ፡ አድራጊ ፡ ተደራጊ ፥ በማደራረግ ፡ ተደራራጊ ፡ ኹነው ፡ አይነገ ሩም ፡ (ቍ፪፲፰) ፡፡ ኪያም ፡ በገቢር ፡ ጊዜ ፥ ወራሻቸውና ፡ ተውላጣቸው ፡ ዐጸፋቸውና ፡ በቂያቸው ፡ ኹኖ ፡ ሲዘረዘርና ፡ ሲቀጸል ፥ ኪያሁ ፡ መንፈሰ ፤ ኪያሃ ፡ ፍኖተ ፤ ኪያከ ፡ አውልዐ ፡ ገዳም ፡ ያሰኛል ፤ በበቂነትም ፡ ሲነገር ፥ ዘኪያክሙ ፡ ሰምዐ ፡ ኪያየ ፡ ሰምዐ ፡ ይላል ፡፡ እነዚህም ፡ ጥቅሶች ፡ ውእቱ ፡ ይእቲ ፡ አንተ ፡ አንትሙ ፡ አነ ፡ በማለት ፡ ፈንታ ፡ የገቡ ፡ ናቸው ፡፡ ካሥሩ ፡ ሰራዊት ፡ ፪ቱ ፡ ውእቱና ፡ ይእቲ ፡ ብቻ ፡ ውእተ ፡ ይእተ ፡ እያ ሰኙ ፡ ራሳቸውን ፡ ይችላሉ ፡፡ ስምንቱ ፡ ግን ፡ እግረ ፡ ቀለማቸው ፡ የማይፈልስ ፡ ጕልት ፡ ስለ ፡ ኾነ ፡ አለኪያሁ ፡ በራሳቸው ፡ ቁመው ፡ አይነገሩም ፡፡ ኪያሁ ፡ በተደራጊነት ፡ የውእቱ ፡ ወራሽ ፡ ስለ ፡ ኾነ ፡ አገባብ ፡ ተጫኖት ፡ በይእቲና ፡ በውእቶን ፡ ፈንታ ፥ ለኪ ያሃ ፡ ሰዓት ፥ በኪያሆን ፡ መዋዕል ፡ እያለ ፡ አለርስቱ ፡ ገብቶ ፡ ይገኛል ፤ ኹሉም ፡ የመ ላሽ ፡ ስሕተት ፡ ነው ፡፡

፵፩ ፤ ለሊሁም ፡ እንደ ፡ ውእቱ ፡ ባለቤት ፡ ይኾናል ፡ እንጂ ፤ እንደ ፡ ኪያሁ ፡ ተደራጊ ፡ ተሳቢ ፡ አይኾንም ፡፡ ሲቀጸልም ፡ ለሊሁ ፡ እግዚ ፡ ጸብአ ፡ ሎሙ ፤ ለሊሁ ፡ አምላክ ፡ ይመጽእ ፡ ወያድኅነነ ፤ ዘለሊሁ ፡ ዳዊት ፡ እግዚእየ ፡ ይቤሎ ፡ ያሰኛል ፡፡ ለነ ውእቱም ፥ ውእቱ ፡ ለሊሁ ፥ ይእቲ ፡ ለሊሃ ፥ አንተ ፡ ለሊከ ፡ እየተባለ ፡ ይቀጸላል ፤ በዐ ጸፋነትም ፡ በቂ ፡ ይኾናል ፤ አካኼዱ ፡ ኹሉ ፡ እንደ ፡ ውእቱ ፡ ነው ፡፡ ኵሉ ፡ ከተጸውዖ ፡ ስም ፡ በቀር ፥ ኵሉ ፡ ብእሲ ፡ ኵላ ፡ እከይ ፡ እያሰኘ ፡ ለብትኖች ፡ ኹሉ ፡ ይቀጸላል ፡፡ ፩ኛ ፡ ደግሞ ፡ ባሕቲቱና ፡ ዕራቁ ፥ እግዚአብሔር ፡ ባሕቲቱ ፡ ቅዱስ ፤ ማርያም ፡ ባሕ ቲታ ፡ ልዕልተ ፡ ኵሉ ፡ ፍጥረት ፤ ወመልአ ፡ ለነፍስ ፡ ዕራቃ ፡ በረከተ ፡ እያሰኙ ፡ ይቀ ጸላሉ ፤ የቀረውም ፡ ኋላ ፡ በጸፋ ፡ ይነገራል ፡፡ በይን ፡ ደግሞ ፡ በይናት ፡ በበይናት ፡ ቲሁ ፡ እያሰኘ ፡ በዝቶና ፡ አገባብ ፡ ወድቆበት ፡ ሲነገር ፥ ዐጸፋ ፡ እንጂ ፡ ቅጽል ፡ አይኾ ንም ፤ ማሰሪያውም ፡ ፪ ፡ ብቻ ፡ ነው ፤ ተደራራጊና ፡ አደራራጊ ፡ አንቀጽ ፡፡

## አኀዝ ፡ ቅጽል ፡፡

፵፪ ፤ የጅምላ ፡ አኃዝ ፡ ለጥሬ ፡ ኹሉ ፡ ሲቀጸል ፡ ከ፩ ፡ እስከ ፡ ፲ ፡ በገቢርና ፡ በተ ገብሮ ፥ ከ፩ ፡ እስከ ፡ ምእልፊት ፡ በወንድና ፡ በሴት ፡ ይተባበራል ፡፡ ሲቀጸልም ፡ በክት ፡ በከፊል ፡ በደጊመ ፡ ቃል ፡ ይነገራል ፤ በክት ፡ ሲነገር ፥ መጽኡ ፡ ዐሠርቱ ፡ ዕደው ፤ ወኀ ረየ ፡ ካልአነ ፡ ሰብዓ ፡፡ በከፊል ፥ አሐዱ ፡ አካል ፡ እምነ ፡ ሠለስቱ ፡ አካላት ፡ ኮነ ፡ ሰብአ ፡፡ በደጊመ ፡ ቃል ፥ ንዑ ፡ ንረድ ፡ ወንንሣእ ፡ ለነ ፡ አሐተ ፡ አሐተ ፡ ብእሲተ ፥ ወንለድ ፡

እምኔሆን ፡ አሐደ ፡ አሐደ ፡ ውሉደ ፡ ይላል ። ርስ ፡ በርሱም ፤ ተጋብኡ ፡ አሐዱ ፡ ዐሠርቱ ፡ ሰብአ ፥ ወይም ፡ አሐዱ ፡ ምእት ፥ ክልኤቱ ፡ ምእት ፥ ሠለስቱ ፡ ምእት ፡ እያለ ፡ ይቀጸጻላል ። በብትን ፡ ሰዋስው ፡ የሚገቡ ፡ ደቂቅ ፡ አገባቦች ፡ ለአሐዱ ፡ በአሐዱ ፡ ምስለ ፡ አሐዱ ፡ እያሰኙ ፡ ይሰማሙታል ፤ ደጊም ፡ እየኾኑም ፡ ሲገቡበት ፡ በደጊመ ፡ ቃል ፡ ይፈታል ። ይህም ፥ ለለ ፡ አሐዱ ፤ ላንዱም ፡ ላንዱም ፡ ለያንዳንዱ ። በበ ፡ አሐዱ ፤ በያንዳንዱ ፥ እያንዳንዱ ፥ አንዱንም ፡ አንዱንም ። ወአርፍቅዎሙ ፡ በበ ፡ ኀምሳ ፡ ወበበ ፡ ምእት ፥ ፶ ፡ ፶ውን ፡ ፲ ፡ ፲ውን ፡ እያሰኘ ፡ ሌላውን ፡ ኹሉ ፡ ያሳያል ።

፯፻፫ ፤ አኀዝ ፡ ጥንትና ፡ መሠረት ፡ እየኾነ ፡ በታሪክ ፡ ልማድ ፡ ይነገራል ፤ ታሪኩም ፡ የዘመን ፡ ቍጥር ፡ ነው ፤ በዐሠርቱ ፡ ወተስዐቱ ፡ ምእት ፡ ወአርብዓ ፡ ዓመተ ፡ ሥጋዌ ፡ ተንሥኡ ፡ ጎግ ፡ ወማጎግ ፡ ፍሉጣነ ፡ ሕግ ፡ ከመ ፡ ይትቃተሉ ፡ በበይናቲሆሙ ፡ እንደ ፡ ማለት ። የተርታም ፡ አኀዝ ፡ ከቀዳምና ፡ ከአሐድ ፡ እስከ ፡ ዓሥር ፡ ወታስዕ ፡ በወንድና ፡ በሴት ፡ እየተለየ ፥ ከዕሥራ ፡ እስከ ፡ ምእልፌት ፡ እየተባበረ ፡ ለጥሬ ፡ ኹሉ ፡ ይቀጸላል ። የዕለትም ፡ አኀዝ ፡ ዐሡር ፡ ወሰኑይ ፥ ዐሡር ፡ ወረቡዕ ፡ መዋዕል ፡ እያለ ፡ ሲቀጸል ፡ አፈታቱ ፡ እንደ ፡ ጅምላ ፡ ነው ፤ ፲፪ ፡ ፲፬ ፡ ቀን ፡ ያሰኛል ፤ የቀረውን ፡ በ፲፱ ፡ ቀኑ ፡ ተመልከት ። የጊዜም ፡ አኀዝ ፡ ምዕር ፡ ሲቀር ፡ ለጊዜያት ፡ ኹሉ ፡ ይቀጸላል ፤ አፈታቱም ፡ እንደዚሁ ፡ ነው ፤ ሥልሰ ፡ ጊዜያተ ፡ ብሎ ፡ ፫ ፡ ጊዜ ፡ ያሰኛል ። ርብዕ ፡ በእመት ፤ ዕሥራ ፡ ወከዕበ ፡ በመስፈርት ፡ እያለም ፡ ከልክና ፡ ከመስፈሪያ ፡ ጋራ ፡ ሲነገር ፡ እንዲሁ ፡ ይፈታል ።

፯፻፬ ፤ ምዕር ፡ ፩ ፡ ጊዜ ፤ ምዕራት ፡ ፪ ፡ ጊዜ ፥ ወይም ፡ ብዙ ፡ ጊዜ ፡ ይኾናሉ ፤ ከጅምላና ፡ ከተራ ፡ አኀዝ ፡ ጋራ ፡ አሐተ ፡ ምዕረ ፡ ወምዕረ ፡ ከዕበ ፥ ምዕራተ ፡ ብዙኃተ ፡ እያለ ፡ ሲነገር ፥ ምዕር ፡ ባለቤት ፡ አኃዙ ፡ ቅጽል ፡ ይኾናል ። ደቂቅ ፡ ቅጽልም ፥ ዛተ ፡ ምዕረ ፥ ይእተ ፡ ምዕረ ፡ እያለ ፡ ይሰማማዋል ፤ ሲዘረዝርም ፡ ምዕሬሁ ፡ ሃ ፤ ምዕሬሃ ፡ ለይእቲ ፡ መስፈርት ፡ ያሰኛል ። ኀድጊ ፡ ምዕረ ፡ ይጽገቡ ፡ ውሉድ ። ብላዕ ፡ ወስተይ ፡ ምዕረ ፡ ወተፈሣሕ ፡ ሲል ፥ ጥቂት ፡ አኹን ፡ ፊት ፡ ተብሎ ፡ ይፈታል ። የዕጽፍም ፡ አኀዝ ፡ አፈድዮሙ ፡ ከዕበተ ፡ ዐመፃሆሙ ። ምክዕቢተ ፡ ክብር ፡ ይደልዎሙ ፡ እያሰኘ ፡ ከጥሬው ፡ ተናበ ፡ ይነገራል ። የክፍልም ፡ አኀዝ ፡ ተስዐቱ ፡ እድ ፥ ዐሠርቱ ፡ እድ ፥ ሰብዐተ ፡ እደ ፡ እያሰኘ ፥ የእድ ፡ ቅጽል ፡ ኹኖ ፡ በጅምላ ፡ ቍጥር ፡ ይነገራል ፤ እድ ፡ የተባለም ፡ ክፍል ፡ ነው ። በተራ ፡ ቍጥር ፡ ግን ፡ ሲነገር ፡ ከእድ ፡ ተናቦ ፡ የቅጽል ፡ አፈታት ፡ ይፈታል ፤ ይህም ፡ ሣልስተ ፡ እዴሃ ፡ ለሀገር ፤ ራብዕተ ፡ እዴሃ ፡ ለምድር ፤ ሳድስተ ፡ እዴሃ ፡ ለኢንዝኩ ፡ ሳብዕተ ፡ እድ ፥ ሰባተኛ ፡ እጅ ፡ እያሰኘ ፡ ሌላውን ፡ ኹሉ ፡ ያሳያል ። የዘመድ ፡ ቅጽል ፡ ጓዝ ፡ እስከዚህ ፡ ነው ።

## በዕድ ፡ ቅጽል ።

፯፻፭ ፤ ቅጽልን ፡ ባዕድ ፡ የሚያሰኘው ፥ አገባቡ ፡ የባለቤት ፥ አንቀጹ ፡ የተሳቢ ፡ ኹኖ ፡ ሲነገር ፡ ነው ። ባዕድ ፡ ቅጽል ፡ በፈታት ፡ ሲለይ ፡ ተሳቢውን ፥ ሲነበብ ፡ ባለቤቱን ፡ መስሎ ፡ ይነገራል ፤ ዘመድ ፡ ቅጽል ፡ ግን ፡ ሲነበብም ፡ ሲለይም ፡ ባለቤቱን ፡ ብቻ ፡

ይመስላል ። ይህም ፡ ዳዊት ፡ ዘነግሠ ፡ ለእስራኤል ፡ ሲል ፥ ለእስራኤል ፡ የነገሠ ፡ ማለቱን ፡ ያሳያል ። ዳግመኛም ፡ ባዕድ ፡ ቅጽል ፡ አንድና ፡ ብዙ ፡ ወንድና ፡ ሴት ፡ ቅርብና ፡ ሩቅ ፡ ሳያናግር ፡ ያናገረ ፡ ይመስላል ። ባዕድ ፡ ቅጽልም ፡ የሚኾኑ ፡ ፫ ፡ ናቸው ፤ ግልጠ ፡ ዘ ፡ ውስጠ ፡ ዘ ፥ የቦታ ፡ የጊዜ ፡ የልክ ፡ ቅጽሎች ። ባዕድ ፡ ግልጠ ፡ ዘ ፡ በ፫ቱ ፡ አዕማድ ፡ ሲገባ ፡ አንቀጹን ፡ ቢዘረዝርም ፡ ባይዘረዝርም ፡ በዝርዝርነት ፡ ይፈታል ።

፵፮ ፤ በድራጊ ፡ ሲገባ ፥ ወይን ፡ እንተ ፡ ተከ(ሉ)ልዋ ፡ ገበእት ፡ ፈረየት ፡ አስካለ ። በተደራጊ ፥ መስቀል ፡ ዘተሰቅ(ለ)ሎ ፡ ክርስቶስ ፡ ዕፀ ፡ ሎጥ ፡ ውእቱ ። በስደራጊ ፥ መቅደስ ፡ እንተ ፡ አሕነ(ጸ)ጻ ፡ ሰሎሞን ፡ ኪራምሀ ፡ መንክርት ፡ ጥቀ ። በተደራራጊ ፥ ዳዊት ፡ ዘተጻብ(አ ፡ ምስለ)አ ፡ አቤሴሎም ፡ መፍቀሬ ፡ ወልድ ፡ ጥቀ ። በደራራጊ ፥ ሰሎሞን ፡ ዘአስተጻብ(አ)አ ፡ ዳዊት ፡ ምስለ ፡ ኢዮአብ ፡ ኢፈርሀ ፡ እምኔሁ ። ተሳቢውንም ፡ ሲዘረዝር ፥ በሐውልት ፡ ግስ ፡ ዐብየ ፡ ሰሎሞን ፡ ዘጸንዐት ፡ መንግሥቱ ። በተገብሮ ፥ ጸድቀ ፡ ኢዮብ ፡ ዘይትነከር ፡ ትዕግሥቱ ። በማድረግ ፥ ተሞቅሐ ፡ ጳውሎስ ፡ ዘሰበኩ ፡ አርዳኢሁ ፡ ወንጌለ ። በስደራጊ ፥ ጽሙእ ፡ ጥቀ ፡ ዳዊት ፡ ዘአምጽ(እዎ)ኡ ፡ ሥዩማኒሁ ፡ ማየ ፡ ቤተ ፡ ልሔም ፡ ሐራ ። በተደራራጊ ፥ ሞተ ፡ ዒሊ ፡ ዘተቃተሉ ፡ ደቂቁ ፡ ምስለ ፡ ኢሎፍላውያን ። በደራራጊ ፥ ሞአ ፡ ለዓለም ፡ ክርስቶስ ፡ ዘአስተቃተለት ፡ ወንጌሉ ፡ ሰማዕተ ፡ ምስለ ፡ ዐላውያን ፡ ይላል ። የተሳቢውን ፡ ዘርፍና ፡ የዘርፉንም ፡ ዘርፍ ፡ ሲዘረዝር ፥ ዳዊት ፡ ዘየዐቅብዎ ፡ ደቀ ፡ ጽርሑ ፤ ብእሲ ፡ ዘኑልቈ ፡ ስመ ፡ ፊደሉ ፡ ሠላስ ፡ ይላል ።

፵፯ ፤ በባዕድ ፡ ግልጠ ፡ ዘ ፡ የሚዘረዘሩ ፡ ደቂቅ ፡ አገባቦች ፡ ፱ ፡ ናቸው ። ለ ፡ በቊም ፡ ቀሪ ፤ በእንተ ፡ በይነ ፡ እንበይነ ፡ ስለ ፤ ምስለ ፡ ከ—ጋራ ፤ ኀበ ፡ መንገለ ፡ እንተ ፡ ውስተ ፡ ለ ፡ ወደ ፤ እስከ ፡ በቊሙ ፡ ድረስ ፤ እም ፡ ከ ፤ ከመ ፡ እንደ ፤ መጠነ ፡ ያኽል ። እንበለም ፡ ለኒህ ፡ ለዘጠኙ ፡ አሉታና ፡ አፍራሽ ፡ እየኾነ ፡ ከኢ ፡ ተደርቦ ፡ ይገባል ። ያገባቦችም ፡ ዝርዝር ፡ ይህ ፡ ነው ፤ ሔዋን ፡ ዘነግሠ ፡ ላቲ ፡ አምላክ ። አዳም ፡ ዘሞተ ፡ በእንቲአሁ ፡ እግዚእ ። መስቀል ፡ ዘተሰቅለ ፡ ቦቱ ፡ አምላክ ። ክርስቶስ ፡ ዘሞቱ ፡ ምስሌሁ ፡ ፈያት ። ማርያም ፡ እንተ ፡ ተፈነወ ፡ ኀቤሃ ፥ አው ፡ እስከኔሃ ፡ ገብርኤል ። ምጡቅ ፡ ውእቱ ፡ ሰማይ ፡ ዘመጽአ ፡ እምኔሁ ፡ ገብርኤል ። አርብዓ ፡ ዓመተ ፡ ነግሠ ፡ ዳዊት ፤ ዘነግሠ ፡ ከማሁ ፥ አው ፡ መጠኖ ፡ ሰሎሞን ። በቀሩትም ፡ አዕማድ ፡ እንዲህ ፡ ተዘርዝረው ፡ ይገባሉ ። ዳግመኛም ፡ ደቂቅ ፡ አገባቦች ፡ ሳይገቡና ፡ ሳይዘረዘሩ ፥ አናቅጽ ፡ ብቻ ፡ ተዘርዝረው ፥ ድኅነ ፡ አዳም ፡ ዘሞቶ ፡ እግዚእ ፤ ከብረ ፡ መስቀል ፡ ዘተሰቅሎ ፡ አምላክ ፡ እያሰኙ ፡ አገባቦችን ፡ ያሰማሉ ። እንበለም ፡ አሉታና ፡ አፍራሽ ፡ ሲኾን ፥ አዳም ፡ ዘኢተሰቅለ ፡ አምላክ ፡ እንበሌሁ ፥ አበ ፡ ሥጋነ ፤ አምላክ ፡ አ(ያ)ለርሱ ፡ ያልተሰቀለ ፡ አዳም ፡ የሥጋ ፡ አባታችን ፡ ነው ፡ ያሰኛል ። ይህ ፡ የበእንተ ፡ አፍራሽ ፡ ነው ፤ የቀሩትንም ፡ እንደዚሁ ፡ እያሰማማኽ ፡ አግባ ። የግልጠ ፡ ዘ ፡ ዐዋጅ ፡ ይህ ፡ ነው ።

፵፰ ፤ ባዕድ ፡ ውስጠ ፡ ዘ ፡ ደግሞ ፡ እንደ ፡ ግልጠ ፡ ዘ ፡ ነው ፤ በንባብ ፡ ባለቤቱን ፡ በፈታት ፡ ተሳቢውን ፡ መስሎ ፡ ሲነገር ፥ ተሳቢና ፡ አንቀጽ ፡ አገባብ ፡ ይዘረዝራል ፤ አንቀጹን ፡ ዘርዝሮ ፡ ከተሳቢው ፡ እየተናበበ ፡ ሲነገር ፥ ዐይነቱ ፡ ወይም ፡ አርእስቱ ፡ ፫ ፡ ነው ። ፩ኛው ፡ ተገብሮና ፡ ሐውልት ፡ ውስጠ ፡ ዘ ፡ ካድራጊ ፡ ተሳቢ ፡ ተናቦ ፡ በገቢር ፡

አንቀጽ ፤ ከስደራጊ ፡ ተሳቢ ፡ ተናበ ፡ በስደራጊ ፡ አንቀጽ ፡ ይፈታል ። ፪ኛው ፡ ገቢር ፡ ውስጠ ፡ ዘ ፡ ከድራጊ ፡ ተሳቢ ፡ ተናበ ፡ በድራጊ ፡ አንቀጽ ፤ ከስደራጊ ፡ ተሳቢ ፡ ተናበ ፡ በስደራጊ ፡ አንቀጽ ፡ ይፈታል ። ፫ኛው ፡ ተደራራጊ ፡ ሣልስ ፡ ቅጽል ፡ ከተደራራጊ ፡ ተሳቢ ፡ ተናበ ፡ በተደራራጊ ፡ አንቀጽ ፤ ከደራራጊ ፡ ተሳቢ ፡ ተናበ ፡ በደራራጊ ፡ አን ቀጽ ፡ ይፈታል ።

፵፱ ፤ (፩ኛ) ፤ ወይን ፡ ትክልተ ፡ ገባእት ፡ ፈረየት ፡ አስካለ÷ገበራርት ፡ የተከሏት ፡ ወይን ፡ ዘለላን ፡ አፈራች ። ትክልት ፡ በንባቡ ፡ ወይንን ፡ ይመስላል ፤ ሲፈታ ፡ ግን ፡ አ ገባቡና ፡ ዝርዝሩ ፡ የርሷ ፤ አንቀጹ ፡ የገባእት ፡ ነው ። ገባእት ፡ አድራጊ÷ወይን ፡ ተደ ራጊ ፡ ተሳቢ ፡ ናቸውና ፤ የተገብሮ ፡ ውስጠ ፡ ዘ ፡ ከድራጊ ፡ ተሳቢ ፡ ተናበ ፡ በገቢር ፡ አ ንቀጽ ፡ ይፈታል ፡ ያልነው ፡ ይህ ፡ ነው ። ሐውልት ፡ ውስጠ ፡ ዘ ፡ ከድራጊ ፡ ተናበ ፡ በገ ቢር ፡ አንቀጽ ፡ ሲፈታ÷ዳዊት ፡ ንጉሥ ፡ (አው)፡ነጋሢ ፡ እግዚአብሔር ፤ እግዜር ፡ ያነገ ሠው ፡ ዳዊት ። ተገብሮ ፡ ውስጠ ፡ ዘ ፡ ከስደራጊ ፡ ተናበ ፡ በስደራጊ፡አንቀጽ ፡ ሲፈታ ፤ መቅደስ ፡ ሕንጽተ ፡ ሰሎሞን ፡ ኪራምሀ ፤ ሰሎሞን ፡ ኪራምን ፡ ያሠራት ፡ መቅደስ ፡ ያሰኛል ። (፪ኛ) ፤ ገቢር ፡ ውስጠ ፡ ዘ ፡ ከድራጊ ፡ ተናበ ፡ በድራጊው ፡ አንቀጽ ፡ ሲፈታ ፡ ኅብስት ፡ በላዔ ፡ ነዳይ ፤ ድኻ ፡ የሚበላው ፡ እንጀራ ። ከስደራጊውም ፡ ተናበ ፡ በስደ ራጊ ፡ አንቀጽ ፡ ሲፈታ ፤ ኪራም ፡ ሐናጼ ፡ ሰሎሞን ፡ መቅደሰ ፤ ሰሎሞን ፡ መቅደስን ፡ ያሠራው ፡ ኪራም ፡ ያሰኛል ። (፫ኛ) ፤ የተደራራጊ ፡ ሣልስ ፡ ቅጽል÷ከተደራራጊ ፡ ተናበ ፡ በተደራራጊ ፡ አንቀጽ ፡ ሲፈታ ፤ ዳዊት ፡ ተጻባኤ ፡ አቤሴሎም ፡ ወልዱ ፤ ልጁ ፡ አቤሴሎም ፡ የተጣላው ፡ ዳዊት ። ከደራራጊም ፡ ተናበ ፡ በደራራጊ ፡ አንቀጽ ፡ ሲፈታ ፤ ሰሎሞን ፡ ተጻባኤ ፡ ዳዊት ፡ ምስለ ፡ ኢዮአብ ፤ ዳዊት ፡ ከኢዮአብ ፡ ጋራ ፡ ያጣላው ፡ ሰሎሞን ፡ ያሰኛል ።

፶ ፤ ተሳቢውንም ፡ ሲዘረዝር÷ያ፰ቱ ፡ አዕማድ ፡ ውስጠ ፡ ዘ ፡ ከተሳቢው ፡ ጋራ ፡ ተናበ ፡ እንዳንቀጹ ፡ ስልት ፡ ይፈታል ። የተገብሮ ፡ ሣልስ÷አብ ፡ ተሰባሒ ፡ ወልድ ፡ በደብረ ፡ ታቦር ፤ ልጁ ፡ በደብረ ፡ ታቦር ፡ የተገለጠ ፡ አብ ። የሐውልት ፡ ሳድስ÷ሰሎ ሞን ፡ ጽኑዐ ፡ መንግሥት ፤ መንግሥቱ ፡ የጠና ፡ ሰሎሞን ። የገቢር ፡ ሣልስ ፤ ጳውሎስ ፡ ሰባኬ ፡ አርድእት ፡ ወንጌለ ፤ አርድእቱ ፡ ወንጌልን ፡ ያስተማሩ(ለት) ፡ ጳውሎስ ። ያስ ደራጊ ፡ ሣልስ÷ዳዊት ፡ አምጻኤ ፡ ሥዩማን ፡ ማየ ፡ ሐራ ፡ ኢሰትየ ፡ እምኔሁ ፤ ሹማምቱ ፡ ወታደሮችን ፡ ውሃ ፡ ያስመጡለት ፡ ዳዊት ፡ ከርሱ ፡ አልጠጣም ። የተደራራጊ ፡ ሣልስ÷ ዔሊ ፡ ተቃታሌ ፡ ደቂቅ ፡ ምስለ ፡ ኢሎፍላውያን ፤ ልጆቹ ፡ ከኢሎፍላውያን ፡ ጋራ ፡ የተዋጉ ፡ ዔሊ ። ያደራራጊ ፡ ሣልስ÷ክርስቶስ ፡ አስተቃታሌ ፡ ወንጌል ፡ ሰማዕተ ፡ ምስለ ፡ ዐላውያን ፤ ወንጌሉ ፡ ሰማዕታትን ፡ ከዐላውያን ፡ ጋራ ፡ ያጋደለች(ለት) ፡ ክርስ ቶስ ። የተጸውዖ ፡ ስም ፡ ጊዮርጊስ ፡ ሚካኤሉ ፡ እያሰኘ ፡ የማይዘረዝር ፡ ስለ ፡ ኾነ ፡ እንደ ፡ ሌላው ፡ ስም ፡ በተሳቢነት ፡ አይገባም ።

፶፩ ፤ አገባቦቹንም ፡ ሲዘረዝር ፡ ከተሳቢው ፡ ጋራ ፡ ተናበ ፡ ነው ፤ ለን ፡ ሲዘረዝር÷ ሔዋን ፡ ንግሥተ ፡ አምላክ ፤ አምላክ ፡ ለርሷ ፡ የነገሠ ፤ ወይም ፡ የነገሠላት ፡ ሔዋን ። በእንተን ፡ ሲዘረዝር÷አዳም ፡ ምዉተ ፡ እግዚእ ፤ ጌታ ፡ ስለ ፡ ርሱ ፡ የሞተ ፡ አዳም ። በን ፡

ሲዘረዝር ፥ መስቀል ፡ ስቁለ ፡ አምላክ ፤ አምላክ ፡ በርሱ ፡ የተሰቀለ ፥ ወይም ፡ የተሰቀለ በት ። ምስለን ፡ ሲዘረዝር ፥ አምላክ ፡ ምዉተ ፥ አው ፡ መዋቴ ፡ ፈያት ፤ ወንበዶች ፡ ከርሱ ፡ ጋራ ፥ ወይም ፡ ዐብረውት ፡ የሞቱ ፡ አምላክ ። ኀበን ፡ እስከን ፡ ሲዘረዝር ፥ ማር ያም ፡ ፍኖተ ፡ ገብርኤል ፡ እምሰማይ ፤ ገብርኤል ፡ ከሰማይ ፡ ወደ ፡ ርሷ ፥ እስከ ፡ ርሷ ፡ የተ ላከ ፡ ማርያም ። እምን ፡ ሲዘረዝር ፥ ሰማይ ፡ ምጹእ ፥ አው ፡ መጻኤ ፡ ገብርኤል ፡ ኀበ ፡ ማርያም ፤ ገብርኤል ፡ ወደ ፡ ማርያም ፡ ከርሱ ፡ የመጣ ፡ ሰማይ ። ከመን ፡ ሲዘረዝር ፤ አልቦ ፡ ሰራቂ ፡ ቅሡፈ ፡ ክርስቶስ ፤ ክርስቶስ ፡ እንደ ፡ ርሱ ፡ የተገረፈ ፡ ሌባ ፡ የለም ። መጠነን ፡ ሲዘረዝር ፥ ብዙኃት ፡ ዓመታተ ፡ ዳዊት ፡ ነጋሥያተ ፥ አው ፡ ንጉሣተ ፡ ሰሎ ሞን ፤ ሰሎሞን ፡ ርሳቸውን ፡ ያኽል ፡ የነገሡ ፡ የዳዊት ፡ ዘመኖች ፡ ብዙዎች ፡ ናቸው ፡ በል ። እንበለን ፡ ለኒሀ ፡ ለዘጠኙ ፡ አፍራሽና ፡ አሉታ ፡ ስታደርግ ፡ እስካኹን ፡ በተነገሩቱ ፡ ቅጽሎች ፡ ኢን ፡ ጨምር ። ይህም ፡ አበ ፡ ሥጋነ ፡ አዳም ፡ ኢስቁለ ፡ አምላክ ፤ አምላክ ፡ ያለርሱ ፡ ያልተሰቀለ ፡ አዳም ፡ ማለቱን ፡ ያሳያል ፤ በቀሩትም ፡ ኢን ፡ እየጨመርኽ ፡ እንዲህ ፡ አግባ ። ከዚህ ፡ የቀረውን ፡ የውስጠ ፡ ዘ ፡ ጠባይ ፡ በሳቢና ፡ በተሳቢ ፡ በሙሻ ዘር ፡ ክፍል ፡ ተመልከት ።

፶፱ ፤ የቦታ ፡ የጊዜ ፡ የልክ ፡ አገባቦች ፥ የነዚህ ፡ የሦስቱ ፡ ባዕድ ፡ ቅጽልነት ፤ አገባቦች ፡ እንደ ፡ ግልጠ ፡ ዘ ፡ ባለቤትን ፥ አናቅጽ ፡ ተሳቢን ፡ ያሳያሉና ፤ ስለዚህ ፡ ነው ። የቦታ ፡ አገባቦች ፤ ወንሰግድ ፡ ውስተ ፡ መከን ፡ ኀበ ፡ ቆመ ፡ እግረ ፡ እግዚእነ ። መከን ፡ ኀበ ፡ ይትገበር ፡ መንገለ ፡ ይትገበር ፡ ውእደ ፡ ይትገበር ፡ መሢዕተ ፡ ቅዳሴ ፡ ቅዱስ ፡ ውእቱ ። በምድረ ፡ በድው ፡ ኀበ ፡ አልቦ ፡ ዕፅ ፡ ወማይ ። የጊዜ ፡ አገባቦች ፤ ተዘርዉ ፡ ሐዋርያት ፡ በዕለት ፡ አመ ፡ ተእኀዘ ፡ እግዚእነ ። ይመጽእ ፡ መዋዕል ፡ አመ ፡ ይብሉ ፡ ብፁዓት ፡ መከናት ። የልክ ፡ አገባቦች ፡ ሲቀጸሉ ፡ ከአኃዝ ፡ ጥሬ ፡ ተቈጥረው ፡ እንደ ፡ ተነገሩት ፡ ነው ፡ እንጂ ፤ ሌላ ፡ አነጋገር ፡ የላቸውም ። የቦታና ፡ የጊዜ ፡ አገባቦች ፡ ባለ ቤታቸውን ፡ የሚመስሉ ፡ በዝርዝር ፡ (ቦቱ ፡ ባቲ) ፡ ብቻ ፡ እንደ ፡ ኾነ ፡ አስተውል ፤ ይህም ፡ እስካኹን ፡ በተነገሩቱ ፡ ይታወቃል ። በባለቤትና ፡ በቅጽል ፡ መከከል ፡ ከባለ ቤቱ ፡ ዘርፍና ፡ ከዘርፉ ፡ ቅጽል ፡ በቀር ፡ ባዕድ ፡ ቃል ፡ አይገባም ፤ ይህም ፡ አምላከ ፡ ሰማይ ፡ ምጡቅ ፡ ሕያው ፡ ማለቱን ፤ አምላክ ፡ ሕያው ፡ ዘሰማይ ፤ ወይም ፡ ተወሰኑት ፡ ሃይማኖት ፡ በጉባኤ ፡ ርትዕት ፡ አለማለቱን ፡ ያሳያል ። ካንቀጽ ፡ ወዲያም ፡ ቅጽል ፡ እን ደዚሁ ፡ ይፈረቅቃል ፤ ይኸውም ፡ ዮሐንስ ፡ ሰበከ ፡ ወንጌላዊ ፡ እንደ ፡ ማለት ፡ ነው ።

፷ ፤ የበቂና ፡ ያጸፋም ፡ ነገር ፡ እንደዚህ ፡ ነው ፤ ቅጽል ፡ ኹሉ ፡ ባለቤት ፡ ሲቀር ፡ በባለቤት ፡ ፈንታ ፡ በቂ ፡ ተጠያቂ ፥ ወይም ፡ ወኪል ፡ ባለቤት ፡ አከል ፡ መኾኑ ፡ ካኹን ፡ ቀደም ፡ በጭር ፡ ቃል ፡ ተነግሯል ፡ (ቍ፴፩) ። በበቂነቱም ፡ ተሳቢና ፡ ዘርፍ ፡ ይኾናል ፤ ቅጽልም ፡ ይቀጸልለታል ። ተሳቢ ፥ ምንተ ፡ ይመስል ፡ ዘአጥመቀ ፡ በማይ ፤ ዜንውዎ ፡ ለዮሐንስ ፡ ዘትሬእዩ ፡ ወዘትሰምዑ ። ዘርፍ ፥ ወአንተኒ ፡ ሕፃን ፡ ነቢየ ፡ ልዑል ፡ ትሰ መይ ፤ ተጠምቀ ፡ ሰማያዊ ፡ በእደ ፡ ምድራዊ ። ቅጽል ፥ ቅዱስ ፡ ኀያል ፤ ናዝራዊ ፡ ቅዱስ ። ዐጸፋ ፡ የሚኾኑ ፡ ግን ፡ ፪ ፡ ብቻ ፡ ናቸው ፤ ደቂቅ ፡ ቅጽልና ፡ ዝርዝር ።

፻፬ ፤ ከ፲ሩ ፡ መደብ ፡ ፬ቱ ፡ ሩቆች ፡ እነውእቱ ፡ ቅጽልና ፡ ዐጸፋ ፡ መኾናቸው ፡ ባልታየ ፡ ነገር ፡ ነው ፤ ሲቀጸሉና ፡ ሲታጸፉም ፡ በማድረግ ፡ ተደራጊ ፥ በማስደረግ ፡ አስደራጊ ፥ ተደራጊ ፥ በማደራረግ ፡ ተደራራጊ ፡ እየኾኑ ፡ ይነገራሉ ። ይህም ፡ ተፈ ነወ ፡ ኢዮአብ ፡ ኀበ ፡ ሰብአ ፡ ኤዶምያስ ፥ ወውእቱ ፡ ቀተሎሙ ፡ አቅተሎሙ ፡ አስተቃ ተሎሙ ፡ ማለቱን ፡ ያሳያል ። አንቀጽና ፡ ዘርፍም ፡ ሲታጠፍ ፥ ሰበከ ፡ ጴጥሮስ ፡ ሃይማ ኖተ ፡ ክርስቶስ ፡ ብሎ ፥ አንቀጹን ፡ ወበውእቱ ፡ (ስብከት) ፡ ወይም ፡ ወቦቱ ፡ ተሰብሐ ፤ ዘርፉንም ፡ ውእቱኒ ፡ (ክርስቶስ) ፡ ገብረ ፡ ሎቱ ፡ መንክራተ ፡ ይላል ። ተሳቢም ፡ ኹኖ ፡ በተደራጊነት ፡ ሲነገር ፥ ውእተ ፡ ይእተ ፥ ወይም ፡ በወራሹ ፡ ኪያሁ ፡ ኪያሃ ፡ ያሰኛል ። ቅጽልም ፡ ቢኾን ፡ ዐጸፋነት ፡ አይቀርበትም ፤ ወትቤሎ ፡ ይእቲ ፡ ብእሲት ፡ ሀበኒ ፡ እም ውእቱ ፡ ማይ ። ብቻውን ፡ ሲነገር ፡ በቅጽልነቱ ፡ በቂ ፥ በደቂቅነቱ ፡ ዐጸፋ ፤ ከባለቤት ፡ ጋራም ፡ ሲነገር ፡ ጭብጥ ፡ ወይም ፡ ጨበጣ ፡ ቅጽል ፡ ይባላል ። አንተኑ ፡ ስምዖን ፡ ወልደ ፡ ዮና ፤ አንተኬ ፡ ትሰመይ ፡ ኬፋ ። አንቲኒ ፡ ዓዲ ፡ እምሰአልኪዮ ። አንትሙ ፡ ዕደው ፡ አክብሩ ፡ አንስቲያክሙ ፡ እስመ ፡ እማንቱሂ ፡ ይወርሳ ፡ ክብረ ። ወከማሁ ፡ አንትንሂ ፡ አንስት ። አነ ፡ ዮሐንስ ፡ እኁክሙ ። ንሕነ ፡ አግብርቲከ ፡ ንሴብሐከ ።

፻፭ ፤ የዘ ፡ እንተ ፡ እለም ፡ ደቂቆች ፡ እነዝኩ ፡ ዝክቱ ፡ ቅጽልና ፡ ዐጸፋ ፡ መኾና ቸው ፡ እንዳራቱ ፡ ቅርቦች ፡ በታየ ፡ ነገር ፡ ሲገቡ ፡ ነው ፤ ምስጢራቸው ፡ እማሬ ፡ ነውና ። ሞተኑ ፡ ዝኩ ፡ ሕፃን ፤ ዳኅንኑ ፡ ዝስኩ ፡ አቡክሙ ፤ እስመ ፡ ዝንቱ ፡ ዝክቱ ፤ ወዝክቱ ፡ ዝንቱ ። ዝ ፡ ዝንቱ ፡ የቅርብ ፡ ቅርብ ፤ ዝኩ ፡ ዝክቱ ፡ የቅርብ ፡ ሩቅ ፡ ነው ። መጽሐፍ ፡ ግን ፡ ዝኩ ፡ ዝንቱ ፡ ዝኰ ፡ ዘንተ ፡ በማለት ፡ ፈንታ ፥ ውእቱ ፡ ደብር ፤ ርኢ ፡ ውእተ ፡ ደብረ ፡ ይላል ፤ የመላሽ ፡ ስሕተት ፡ ነው ። ውእቱ ፡ የሚቀጸለው ፡ ወይም ፡ የሚያጽ ፈው ፡ ባለቤት ፡ ባይን ፡ የማይታይ ፡ የሩቅ ፡ ሩቅ ፡ ስውርና ፡ ድብቅ ፡ ነው ፡ እንጂ ፤ ባይን ፡ ቀምሎ ፡ በጣት ፡ ጠንቍሎ ፡ የሚያዩትና ፡ የሚያሳዩት ፡ ነገር ፡ አይዶለም ።

፻፮ ፤ ውእቱ ፡ ኪያሁ ፡ ለሊሁ ፤ እነዚህ ፡ ፫ቱ ፡ ሲቀጸሉ ፡ ነገር ፡ ለማጽናት ፡ ይደ ጋግማሉ ፤ ውእቱ ፡ ሰማያዊ ፡ ወውእቱ ፡ ምድራዊ ፤ አንተ ፡ ሐማሚ ፡ ወመዋቲ ፡ ዘከመ ፡ ዕሬናከ ፡ ምስሌነ ፤ ወአንተ ፡ ኢሐማሚ ፡ ወኢመዋቲ ፡ ዘከመ ፡ ዕሬናከ ፡ ምስለ ፡ አብ ። ኪያከ ፡ አበ ፡ ኪያከ ፡ መጋቤ ፡ ወኪያከ ፡ ረዳኤ ። ለሊሁ ፡ ካህን ፡ ወለሊሁ ፡ በግዕ ፡ ወለ ሊሁ ፡ ምሗዕ ። ሲያጽፉም ፡ መልኀ ፡ ጴጥሮስ ፡ መጥባሕተ ፡ ኀጺን ፤ ወይእቲ ፡ ከነቶ ፡ ለእዝን ። ዘእንተ ፡ ርእሱ ፡ በግዕት ፡ ዕድሜ ፡ አኅጸረ ፤ ወኪያሃ ፡ በገነት ፡ ሰወረ ። ሰበኬ ፡ ብርሃን ፡ ዮሐንስ ፡ ስምዐ ፡ ኮነ ፤ ወለሊሁ ፡ ኢኮነ ፡ ብርሃነ ። መሀረ ፡ ክርስቶስ ፡ መጥ ምቀ ፡ ርእስ ፡ እንዘ ፡ ለሊሁ ፡ ይሜጡ ፡ ርእሶ ፡ ያሰኛሉ ። ለሊሁ ፡ ደግሞ ፡ እንደ ፡ ውእቱ ፡ በባለቤት ፡ በዘርፍ ፡ በተሳቢ ፡ ዐጸፋ ፡ ይነገራል ፤ በባለቤት ፥ አብ ፡ ፈነወ ፡ ወልዶ ፡ ለከ ዊነ ፡ ሰብእ ፤ ወለሊሁ ፡ ኢተፈነወ ። ተፈነወ ፡ ወልዱ ፡ ለአብ ፡ ለከዊነ ፡ ሰብእ ፡ እንዘ ፡ ኢሐዱ ፡ ምስሌሁ ፤ ወለሊሁሰ ፡ ኢኮነ ፡ ሰብአ ። በተሳቢ ፥ አብ ፡ ፈነዎ ፡ ለወልዱ ፤ ወለ ሊሁ ፡ ሰምዐ ፡ ወተአዘዘ ።

፻፯ ፤ ኵሉ ፡ ደምላይና ፡ ጠቅላይ ፡ የአኃዝ ፡ ጥሬ ፡ ስለ ፡ ኾነ ፡ ለብዙም ፡ ለጥቂ ትም ፡ በጠቅላይነት ፡ ይቀጸላል ፤ ካንድ ፡ የወጣ ፡ ፪ም ፡ ፲ም ፡ ኵሉ ፡ ይባላል ። ኵሉ ፡

ፍጥረት፥ኵሉ ፡ ዓለም፥ኵሉ ፡ ትውልድ ፤ ወተሀውከት ፡ ኵላ ፡ ሀገር ፤ አንተ ፡ ወኵሉ ፡ ቤትከ ። ሲበቃም ፡ ኵሉ ፡ ዐረየ ፤ ኵሉ ፡ ይኄሊ ፡ ትካዘ ፡ ርእሱ ፤ ወኵሉ ፡ ከመ ፡ ልብስ ፡ ይበሊ ። ሲያጥፍም ፡ በሩቅ፥እመኒ ፡ ኵሎሙ ፡ ዐለዉከ ። በቅርብም ፡ ተሰባሕክሙ ፡ አ ፡ ሐዋርያት ፡ በሰቢከ ፡ ወንጌል ፤ ወኵልክሙ ፡ ሰማዕተ ፡ ኮንክሙ ፡ ይላል ። በሕቲቱና ፡ ዕራቁ ፡ ለባለቤት ፡ ሲቀርቡ ፡ ቅጽል፥ከባለቤት ፡ ሲርቁ ፡ ተሳቢ ፡ ይኾናሉ ፤ ዐጸፋነት ፡ ግን ፡ የላቸውም ፤ ከባለቤትም ፡ በይርቁ ፡ አፈታታቸው ፡ ከተለየ ፡ ተሳቢ ፡ እንጂ ፡ ቅጽል ፡ አይኾኑም ። ቅጽል፥አከ ፡ በእንተ ፡ እሉ ፡ ባሕቲቶሙ ፡ ዘእስእል ፤ ኢይከውን ፡ ሥጋ ፡ ባሕቲቱ ፡ መድኀኒተ ። ተጠምቀ ፡ በማይ ፡ ዕራቁ ፤ ኢትስተይ ፡ ማየ ፡ ዕራቆ ። ተሳቢ፥ኢይከውን ፡ ሥጋ ፡ መድኀኒተ ፡ ባሕቲቶ ፤ ወአሥጡ ፡ ቀሣውቲሆሙ ፡ ዕራቆ ፤ ኢትቁም ፡ ዕራቀከ ።

፺፰ ፤ ከንቱ ፡ ቅጽልና ፡ በቂ ፡ ይኾናል ፤ ቅጽል፥ከንቱ ፡ ንዋይ ፡ ይከውን ፡ ከመ ፡ ኢምንት ፤ ለአጽድቆ ፡ ሕልም ፡ ነገሮሙ ፡ ከንቱ ። በቂ፥እመ ፡ ኢጻመውከ ፡ በርትዕ ፡ ትረከብ ፡ ከንቶ ፤ እመ ፡ ኢኀደጉ ፡ ከንቶሆሙ ፡ (ጣዖታቸውን) ። ተሳቢም ፡ ሲኾን፥ትነብር ፡ ምድር ፡ ከንቱታ ፤ ከንቱ ፡ ኹና ፡ ያሰኛል ። ርእስ ፡ (ርእሱ ፡ ሳ ፡ ሶሙ ፡ ሶን ፡ ስከ ፡ ኪ ፡ ክሙ ፡ ክን ፡ የ ፡ ነ) ፡ ርስ ፡ ራስ ፡ ባለቤት፥መክብበ ፡ ሕዋሳት ። ሲዘረዘርም ፡ ፍችው ፡ እንደ ፡ ውእቱና ፡ እንደ ፡ ለሊሁ ፡ ነው ፤ ለሊሁ ፡ ለነውእቱ ፡ እንዲቀጸል፥ይህም፥ውእቱ ፡ ርእሱ ፡ ይእቲ ፡ ርእሳ ፡ አንተ ፡ ርእስከ ፤ ሲፈታም ፡ ርሱ ፡ ራሱ ፡ ባለቤቱ፥አንተ ፡ ራስኽ ፡ ባለቤትኽ ፡ እያሰኘ ፡ እስከ ፡ ንሕነ ፡ ላሉት ፡ ይቀጸላል ። ለሌላ ፡ ስም ፡ ግን ፡ ዘርፍ ፡ ሳይዝ ፡ አይቀጸልም ፤ ይህም፥እብን ፡ ርእሰ ፡ ማእዘንት ፤ ኤጲስቆጶስ ፡ ርእሰ ፡ ካህናት ፡ እንደ ፡ ማለት ፡ ነው ። ዳግመኛም ፡ የተደራጊ ፡ ተሳቢና ፡ ዐጸፋ ፡ ዘርፍ ፡ ይኾናል ፡ እንጂ፥ባለቤት ፡ አይኾንም ። ለሊከኑ ፡ ትንእድ ፡ ርእሰከ ፤ ክርስቶስኒ ፡ አከ ፡ ርእሶ ፡ ዘንእደ ። ዘርፍ ፡ ሲኾን፥ትካዘ ፡ ርእሱ ፤ ምስማከ ፡ ርእሱ ። ደቂቅ ፡ አገባብም ፡ ሲጨምር፥አድለወ ፡ ለርእሱ ፤ ዘመከረ ፡ ብኪ ፡ መከረ ፡ በርእሱ ፤ ይቤ ፡ በእንተ ፡ ርእሱ ፡ ይላል ።

## ዝርዝር ።

፺፱ ፤ የዝርዝር ፡ ጠባይ ፡ ከአናቅጽ ፡ ጋራ ፡ ባ፩ኛ ፡ ምዕራፍ ፡ በ፯ኛና ፡ በ፱ኛ ፡ ዕርከን ፡ ተነግሯል ። ጥሬ ፡ ኹኖ ፡ ነባር ፡ ኹኖ ፡ አገባብም ፡ ኹኖ ፡ ባ፲ ፡ ባ፲ ፡ መደብ ፡ በዘመድ ፡ በባዕድ ፡ የሚዘረዘር ፡ ቃል ፡ ኹሉም ፡ ደቂቅ ፡ ርባታ ፡ ተብሏል ። ስለ ፡ ንኡሳንም ፡ አናቅጽ ፡ ንኡስ ፡ ርባታ ፡ ይባላል ። ዘመድና ፡ ባዕድ ፡ ዝርዝሮች ፡ ብእሲታ ፡ ብእሲሁ፥ዛቲ ፡ ብእሲት ፡ ዝኩ ፡ ብእሲ ፡ በማለት ፡ ፈንታ ፡ እየገቡ ፡ ቅጽልና ፡ ዐጸፋ ፡ ይኾናሉ ፤ ሲፈቱም ፡ ይች ፡ ሴት ፡ ያ ፡ ሰው፥ወይም ፡ ሴትዮዋ ፡ ሰውዮው ፡ ያሰኛሉ ። ጥሬ ፡ ከግእዝ ፡ በቀር ፡ በ፮ቱ ፡ ኹሉ ፡ ይጨርሳል ፤ በካዕብ ፡ የሚጨርስ ፡ ጥሬ ፡ ዝርዝሩ ፡ እንደ ፡ ከንቱ ፡ ነው ፡ (ከንቶሁ ፡ ሃ ፡ ሆሙ ፡ ን ፤ ከንቱከ ፡ ኪ ፡ ክሙ ፡ ን ፡ የ ፡ ነ) ። በሣልስ ፡ በራብዕ ፡ በኃምስ ፡ በሳብዕ ፡ የሚጨርስም ፡ እንደዚሁ ፡ በባዕድ ፡ ይዘረዝራል ፤ ብእሲ ፡ ብእሲሁ፥ደብተራ ፡ ደብተራሁ፥ቀዳሴ ፡ ቀዳሴሁ፥መሰንቆ ፡ መሰንቆሁ ። በሳ

ድስ ፡ የሚጨርስ ፡ ግን ፡ በዘመድ ፡ በባዕድ ፡ ይዘረዝራል ፤ ብእሲት ፡ ቱ ፥ እም ፡ ሙ ፥ ውሉድ ፡ ዱ ፥ ደቅ ፡ ቁ ፥ አዕይንት ፡ ቱ ፡ ቲሁ ፥ አርድእት ፡ ቱ ፡ ቲሁ ፥ አርዳእ ፡ እ ፡ ኢሁ ። አብ ፡ አቡ ፡ አቡሁ ። እድ ፡ እዱ ፡ እዴሁ ። ምግባር ፡ ሩ ፡ ሪሁ ። አገባቦችም ፡ ዘርና ፡ ነባር ፡ ስለ ፡ ኾኑ ፡ በዘመድ ፡ በባዕድ ፡ ይዘረዘራሉ ፤ ተውላጥ ፡ ጡ ፡ ጣ ፤ ኀበ ፡ ኀቤሁ ፡ ሃ ። በጭራሽም ፡ ዝርዝር ፡ የማያስገቡ ፡ አሉ ፡ (ዕር፲፫ ፡ ቍ ፡ ፺፱) ።

፳ ፤ ዝርዝር ፡ ዐጥፎና ፡ ጠቅሶ ፡ የሚያሳየው ፡ ፬ ፡ ነገር ፡ ነው ፤ ባለቤትና ፡ ተሳቢ ፡ ዘርፍና ፡ ደቂቅ ፡ አገባብ ። ያንቀጽና ፡ የደቂቅ ፡ አገባብ ፡ ዝርዝር ፡ ባለቤትን ፡ ሲያሳይ ፤ ቀተለ ፡ ቀቲለከ ፡ በእንቲአሃ ፡ ምስሌሆሙ ፡ ብሎ ፥ ውእቱ ፡ አንተ ፡ ይእቲ ፡ እሙንቱ ፡ ማለትን ፡ ያሰማል ። የዐበይትና ፡ የንኡሳት ፡ አናቅጽ ፡ ዝርዝር ፡ በተደራጊና ፡ ባድራጊ ፡ በተደራጊ ፡ ተሳቢ ፡ ፈንታ ፡ ይነገራል ። ፈጠሮ ፡ እግዚአብሔር ፡ ለአዳም ፡ ወረሰዮ ፡ እግዚአ ፡ ፍጥረት ። አምጽአ ፡ ሰሎሞን ፡ ለኪራም ፡ ወአሕነጸ ፡ መቅደሰ ። እመ ፡ ብዝኀ ስቴ ፡ ኮነ ፡ መስሐቴ ፡ ኢንኅሥሥ ፡ አብዝኖቶ ። እምከመ ፡ ኮነ ፡ እክል ፡ ዘያጸንዕ ፡ ሰብአ ፡ ርቱዕ ፡ ብልዐቱ ። የቀረውም ፡ የገቢር ፡ አንቀጽ ፡ ዝርዝር ፡ እንዲህ ፡ እየኾነ ፡ በተሳቢ ፡ ፈንታ ፡ ይነገራል ። የሐውልትና ፡ የተገብሮ ፡ የተጋብሮ ፡ አንቀጽ ፡ ዝርዝር ፡ ባገባቦች ፡ ፈንታ ፡ ይነገራል ፤ ይህም ፡ ለእመ ፡ መጽአ ፡ ዘይከብረከ ፡ ሲል ፥ እምኔከ ፤ ተአምሩ ፡ ከመ ፡ መጽሐፈ ፡ ክርስቶስ ፡ ትትለአከክሙ ፡ ሲል ፥ ለክሙ ፡ በኀቤክሙ ፤ ወተፈኒዎ ፡ ኢየሱስ ፡ ኀበ ፡ ሄሮድስ ፡ ተቃጸበ ፡ ሲል ፥ ቦቱ ፡ በላዕሌሁ ፡ እያሰኘ ፡ ሌላውን ፡ ኹሉ ፡ ያሳያል ። ያርእስትና ፡ የውስጠ ፡ ዘ ፡ የሳቢ ፡ ዘርም ፡ ዝርዝር ፡ እንዲሁ ፡ በገባብ ፡ ፈንታ ፡ ይነገራል ።

፳፩ ፤ የተደራጊም ፡ ዝርዝር ፡ በምስለ ፡ ፈንታ ፡ ሲነገር ፥ መኑ ፡ የአምር ፡ ኅሊናሁ ፡ ለእግዚ ፡ ወመኑ ፡ ተማከሮ ። በአርእስትም ፥ ዐርከ ፡ ዘእንበይነ ፡ ከርሡ ፥ ለእመ ፡ አልብከ ፡ ውእቱ ፡ ይቀድም ፡ ተቃትሎተከ ፤ በውስጠ ፡ ዘም ፡ ይከውን ፡ ተቃታሊከ ፡ ያሰኛል ። ዳግመኛም ፡ ሣልስና ፡ ሳድስ ፡ ቅጽሎች ፡ ሲዘረዘሩ ፡ ተሳቢ ፡ እየኾኑ ፡ በበዝና ፡ በእንዘ ፡ ዐማርኛ ፡ ይፈታሉ ። ይህም ፥ ማእዜ ፡ ርኢናከ ፡ ርኁበከ ፡ ወጽሙአከ ፡ ወዕሩቀከ ፡ ሲል ፤ ተርበኽ ፡ ተጠምተኽ ፡ ታርዘኽ ። ነቋረከ ፡ ትባእ ፡ ውስተ ፡ ሕይወት ፡ ሲል ፥ ፩ ፡ ዐይና ፡ ኹነኽ ። ኀደግዋ ፡ ለሀገር ፡ ርኅታ ፤ ከፍተው ፥ ወይም ፡ ክፍቷን ። አኀዝዎ ፡ ሕያዎ ፤ በሕይወቱ ፡ ሳለ ፥ ደኅንኛውን ፥ ወይም ፡ ሳይሞት ፡ ያሰኛል ። ዝርዝሩ ፡ ካዕብ ፡ ሲኾን ፡ ግን ፡ ተሳቢና ፡ ባለቤት ፡ ያሳያል ፤ ይህም ፥ ሕያዉ ፡ ተንሥአ ፡ ባለው ፡ ይታወቃል ፤ ሕያው ፡ ኹኖ ፡ ሲሉት ፡ ተሳቢ ፥ ደገኛው ፡ ሲሉት ፡ ባለቤት ፡ ይኾናል ።

፳፪ ፤ ያ፰ቱ ፡ አዕማድ ፡ አርእስትና ፡ የውስጠ ፡ ዘ ፥ የሳቢ ፡ ዘርና ፡ የጥሬ ፡ ዝርዝር ፡ በዘርፍ ፡ ፈንታ ፡ ይነገራል ። ተዐቅፉ ፡ ፈሪሳውያን ፡ በረፊቀ ፡ ክርስቶስ ፡ ምስለ ፡ ኃጥኣን ፡ ወበበሊዖቱ ፡ ምስሌሆሙ ። ስንክሳር ፡ ያየድዐነ ፡ ዕለተ ፡ ሞቶሙ ፡ ለሰማዕት ፡ ወዘከመ ፡ እፎ ፡ ተቀትሎቶሙ ። እሙን ፡ ይኩን ፡ ዐርኩ ፡ ለንጉሥ ፡ ወጸሓፊሁኒ ፡ መልእክታተ ። ልዑላን ፡ ፍጥረታተ ፡ እግዚእ ፡ እሙንቱ ፡ መላእክት ፡ ወጥቀ ፡ ፍቁራኒሁ ። ዕጹብ ፡ ውእቱ ፡ ንብረተ ፡ ባሕታውን ፡ ገዳመ ፡ ወብልዐቶሙ ፡ አቍጽለ ። ወልደቱ ፡ ተዐውቀ ፡ እመንፈስ ፡ ቅዱስ ። ዕጹብ ፡ ጥበበ ፡ ሰሎሞን ፡ ወመንክር ፡ ግብሩ ። ባለቤት ፡ ለገን

ዘቡ ፡ ኹሉ ፡ ዘርፍ ፡ ስለ ፡ ኾነ ፥ በዘርፍ ፡ ፈንታ ፡ የገባ ፡ ዝርዝር ፡ የባለቤትም ፡ ዐጸፋ ፡ ይኾናል ። ዐቢይ ፡ እግዚአብሔር ፡ ወብዙኅ ፡ አኰቴቱ ፡ ሲል ፥ አኰቴተ ፡ ርእሱ ፡ ወይም ዚአሁ ፡ ይሰማበታል ። አርቆ ፡ ያዕቆብ ፡ ወዮሐንስ ፡ ኀደጉ ፡ አባሆሙ ፡ ወመሣግሪሆሙ ፡ ቢል ፤ አቅርቦም ፡ አክብር ፡ አባከ ፡ ወእመከ ፡ ቢል ፥ ዘርፉ ፡ ዘመድ ፡ ይኹን ፡ እንጂ ፡ ዐጸፋነቱ ፡ ከዘርፍ ፡ አይወጣም ።

፹፫ ፤ የገቢር ፡ አንቀጽ ፡ አርእስትና ፡ ውስጠ ፡ ዘ ፡ ሳቢ ፡ ዘር ፡ ከተሳቢ ፡ ጋራ ፡ ሲና በቡ ፡ ዘርፋቸው ፡ በዘ ፡ እንተ ፡ እለ ፡ ይያያዛል ፤ አፍቅሮተ ፡ ሰብእ ፡ ዘእግዚአብሔር ። ከዘርፍም ፡ ጋራ ፡ ሲያያዙና ፡ ሲናበቡ ፡ ተሳቢያቸው ፡ ግእዝና ፡ ኃምስ ፡ ሳብዕም ፡ ኹኖ ፡ ይነገራል ። ሲያያዝ ፥ በሊዖቱ ፡ ለብእሲ ፡ ኅብስተ ፤ ሲናበብ ፥ በሊዖተ ፡ ብእሲ ፡ ኅብስተ ፡ ይላል ፤ የቀሩትም ፡ እንደዚህ ፡ ናቸው ። በባለቤትና ፡ በተሳቢ ፡ በዘርፍ ፡ ፈንታ ፡ የገባ ፡ ዝርዝር ፡ በውእቱና ፡ በኪያሁ ፡ ይቀናል ፤ ውእቱንና ፡ ኪያሁን ፡ እስካኹን ፡ በገባው ፡ አስተውል ። በሎ ፡ በሎቱ ፡ የሚቀኑም ፡ ወሀበንና ፡ መጠወን ፡ የመሰሉ ፡ አናቅጽ ፡ አሉ ፤ የገቢር ፡ አናቅጽ ፡ አርእስትና ፡ ውስጠ ፡ ዘ ፡ ሳቢ ፡ ዘር ፡ ተዘርዝረውና ፡ ዐርፈው ፡ ሲስቡ ፡ በኪያሁ ፥ ሲናበቡ ፡ ግን ፡ በዚኣሁ ፡ ይቀናሉ ። የቀሩትም ፡ አዕማድ ፡ ዝርዝሮች ፡ በሚሰማሟቸው ፡ ደቂቅ ፡ አገባቦች ፡ ይቀናሉ ። በዘርፍ ፡ ፈንታም ፡ የሚነገር ፡ ከነዚኣሁ ፡ ተናበ ፡ በርሳቸው ፡ ይቀናል ።

፹፬ ፤ ካ፩ኛው ፡ ዐምድ ፡ ከቦዝ ፡ ስለ ፡ ባለቤትም ፡ ዐጸፋ ፡ ከሚነገሩ ፡ ዝርዝሮች ፡ በቀር ፡ የቀሩቱ ፡ በለ ፡ ይገጥማሉ ። የተጋጠሙቱ ፡ አናቅጽና ፡ ተሳቢ ፡ ቢኾኑ ፡ ሳቢና ፡ ተሳቢ ፤ ዘርፍና ፡ ባለቤት ፡ ቢኾኑ ፡ ግን ፡ ጠቃሽ ፡ ተጠቃሽ ፡ ይባላሉ ። ደቂቅ ፡ አገባብም ፡ በለ ፡ ሲጋጠም ፡ እንደዚሁ ፡ ጠቃሽ ፡ ተጠቃሽ ፡ ነው ። በአንቀጽ ፡ ዝርዝር ፡ የሚሳብ ፡ ለ ፡ ሳቢው ፡ ገቢር ፡ አንቀጽ ፡ ቢኾን ፡ በልማዳዊ ፡ ዐማርኛ ፡ ይፈታል ፤ ተገብሮ ፡ ቢኾን ፡ ግን ፡ በሚሰማሙቱ ፡ ደቂቅ ፡ አገባቦች ፡ ይፈታል ። ተገሐሣ ፡ ለመዐት ፤ ከቍጣ ፡ ራቅ ። አፍጥን ፡ ተግሕሦታ ፡ ለእከይ ፤ ከክፉት ፡ ፈጥነኽ ፥ ወይም ፡ ቶሎ ፡ ብለኽ ፡ ራቅ ። ዮ ፡ ያ ፡ ዮሙ ፡ ዮን ፤ እኒህ ፡ ዝርዝሮች ፡ በለ ፡ በሎቱ ፡ በሚቀኑ ፡ አናቅጽ ፡ ዝርዝር ፡ ላይ ፡ እየተጨመሩ ፡ በኪያሁ ፡ ሃ ፡ ሆሙ ፡ ሆን ፡ ፈንታ ፡ ይነገራሉ ፤ ስማቸውም ፡ ድርብ ፡ ዝርዝር ፡ ይባላል ። ሀበኒዮ ፥ ሀቦሙያ ፥ ጸግዉኒያ ፤ ሀበኒዮሙ ፥ ዘወሀበኒዮን ።

፹፭ ፤ የአኃዝ ፡ ዝርዝር ፥ የድምላው ፡ በቦታው ፡ ተነግሯል ፡ (ቍ፩፻፪) ፤ የተራ ውም ፡ ይህ ፡ ነው ። ቀዳሚሁ ፡ ሃ ፡ ሆሙ ፡ ሆን ፤ ቀዳሚከ ፡ ኪ ፡ ክሙ ፡ ክን ፡ የ ፡ ነ ። ቀዳ ሚቱ ፡ ታ ፡ ቶሙ ፡ ቶን ፤ ቀዳሚትከ ፡ ኪ ። ዳግሙ ፡ ዳግምቱ ፤ ሣልሱ ፡ ሣልስቱ ፡ እያ ሰኘ ፡ እስከ ፡ ዓሥር ፡ ዓሥርት ፡ ይዘረዘራል ። ዝርዝሩም ፡ ለአካል ፡ ለነገር ፡ ለጊዜ ፡ ለክ ፍል ፡ ይኾናል ፤ ለአካል ፡ ሲኾን ፥ ወፅአ ፡ ካልኡኒ ። ለነገር ፥ ሣልስከ ፡ ዝንቱ ። ለጊዜ ፥ ሣልሰሙ ፡ ዮም ። ለክፍል ፥ ሣልስትኪ ፡ በብድብድ ፡ ወበረኃብ ፥ ወሣልስትኪ ፡ በኲ ናት ። የኹሉም ፡ ዝርዝር ፡ በቦታው ፡ ተነግሯል ፡ (ቍ፩፻፫) ።

## ፮ኛ ፡ ክፍል ፡፡

ጸዋትወ ፡ አገባብ፥የዘርና ፡ የነባር ፡ ሕንባብ፥ወይም ፡ ያገባቦች ፡ አገባብና ፡ ፍች፥ ፫ኛውን ፡ ክፍል ፡ መልሶ ፡ እየዘረዘረ ፡ የሚተች ፡፡ አገባብ ፡ ሲባል ፡ ኹሉም ፡ የዝ ርዋን ፡ ቃላት ፡ ሰብሳቢ ፡ ነው ፤ በተለየ ፡ ግን ፡ ዐቢይ ፡ አገባብ ፡ በአናቅጽ ፡ ብቻ፥ንኡስ ፡ አገባብ ፡ በአናቅጽና ፡ በቅጽል ፥ ደቂቅ ፡ አገባብ ፡ በጥሬ ፡ ወይም ፡ በብትን ፡ ይገባል ፤ ብትንና ፡ ጥሬ ፡ ፩ ፡ ወገን ፡ ነው ፡፡

### ፲፱ኛ ፡ ዕርከን ፡፡

### ዐበይት ፡ አገባቦች ፡፡

፰፮ ፤ እስመ ፤ ና ፡ ስለ ፡ እንደ ፡ ይኾናል ፡፡ ና ፡ ሲኾን ፡ በኀላፊና ፡ በትንቢት ፡ በዘ ንድና ፡ በነባር ፡ አንቀጽ ፡ በጽድቅ ፡ በሉታ ፡ ይገባል ፤ በኋላ ፡ ኹኖ ፡ የፊቱን፥በፊትም ፡ ኹኖ ፡ የኋላውን ፡ ያስረዳል ፡፡ በኀላፊ፥ኢያምሠጠ ፡ አዳም ፡ እምኵነኔሁ ፡ ለእግዚአብ ሔር፥እስመ ፡ በልዐ ፡ እምዕፀ ፡ ዘኢአዘዞ ፡ ይብልዖ ፡፡ ወይም፥እስመ ፡ ኢዐቀበ ፡ ትእዛዞ ፡ ለእግዚአብሔር ፤ ተወከፈ ፡ አዳም ፡ በድልወት ፡ ፍትሐ ፡ሞተ ፡ ሥጋ ፡ ወነፍስ ፡ እም እግዚኡ ፡፡ በትንቢት ፡ ሲገባ፥ሰማዕት ፡ ኢይፈርሁ ፡ ሞተ ፡ ሥጋ ፤ እስመ ፡ ይሬእይዋ ፡ ለመንግሥተ ፡ ሰማይ ፡ በዐይነ ፡ ተስፋ ፡፡ በዘንድ ፡ ሲገባ ፡ በነባር ፡ ይፈታል ፤ ይህም ፡ ጻድቃን ፡ ይብልዎ ፡ ለክርስቶስ ፡ እንዘ ፡ ያመጽእ ፡ ላዕሌሆሙ ፡ መከራ ፡ ሥጋ ፡ ኄር ፡ ውእቱ ፤ እስመ ፡ ከመ ፡ ይኩን ፡ ዝ ፡ መከራ ፡ ሕይወተ ፡ ነፍሳቲሆሙ ፡ ሲል ፥ ይህ ፡ መ ከራ ፡ የነፍሳቸው ፡ ሕይወት ፡ ይኾን ፡ ዘንድ ፡ (እንዲኾን ፡ ሊኾን) ፡ ነውና ፡ ያሰኛል ፡፡ በነባር ፡ ሲገባ፥ውሉደ ፡ እግዚአብሔር ፡ በእንተ ፡ ክርስቶስ ፡ ይትዔገሡ ፡ መከራ ፤ እ ስመ ፡ ውእቱ ፡ አርአያሆሙ ፡፡ ወይም ፡ እስመ ፡ አኮ ፡ ዛቲ ፡ ዓለም ፡ ዘትነብር ፡ ለዓለም ፤ ይሬእይዋ ፡ ጻድቃን ፡ ከመ ፡ እዳው ፡፡ እስመ ፡ ና ፡ በተባለበት ፡ ኹሉ ፡ ስለ ፡ ይሰማማ ዋል ፤ በተለየ ፡ ግን ፡ ስለና ፡ እንደ ፡ ሲኾን ፡ በኀላፊና ፡ በነባር ፡ ይገባል ፡፡ ይህም ፡ ተሠ ገወ ፡ቃል ፥ እስመ ፡ ተዋረደ ፡ አዳም ፡፡ አዳም ፡ ስለ ፡ ተዋረደ ፡፡ እሙን ፡ ነገር ፡ እስመ ፡ ክርስቶስ ፡ መጽአ ፡ ውስተ ፡ ዓለም ፤ እንደ ፡ መጣ ፡ ማለቱን ፡ ያሳያል ፡፡ አምጽኡ ፡ ሎቱ ፡ ወርቀ ፡ እስመ ፡ ንጉሥ ፡ ውእቱ ፡ ሲል ፥ ንጉሥ ፡ ነውና ፥ ንጉሥ ፡ ስለ ፡ ኾነ ፥ ንጉሥ ፡ እንደ ፡ መኾኑ ፡ ተብሎ ፡ በሦስቱም ፡ ይፈታል ፡፡ አንዳንድ ፡ መምህራን ፡ ፬ኛ ፡ ብሎ ፡ ይኾናል ፡ ይላሉ ፤ በስለና ፡ በና ፡ በ፪ቱ ፡ ፈንታ ፡ የገባ ፡ ትርፍ ፡ ዐማርኛ ፡ ነው ፡ እንጂ፥ መደበኛ ፡ አይዶለም ፡፡ በሦስቱ ፡ ግን ፥ ምእተ ፡ ምክዕቢተ ፡ የዐስዮሙ ፡ ክርስቶስ ፡ ለጻ ድቃኒሁ ፡ እስመ ፡ በእንቲአሁ ፡ ተወከፉ ፡ መከራ ፤ ተመንደቡሂ ፡ ወሐሙ ፤ ዓዲ ፡ ሰ ቀሉ ፡ ሥጋሆሙ ፡ ምስለ ፡ ፍትወት ፡ እያሰኘ ፡ በዋዌ ፡ እስከ ፡ ፫ ፡ አንቀጽ ፡ ይወርዳል ፤ እስከ ፡ ፫ም ፡ ማለት ፡ የሰዋስው ፡ እንጂ ፡ የመጽሐፍ ፡ አይዶለም ፡፡ እስመ ፡ እንደ ፡ ተ ብሎ ፡ መፈታቱ ፡ በከመ ፡ ቦታ ፡ እየገባ ፡ ስለ ፡ ተገኘ ፡ ነው ፡፡ ዳእሙ ፡ በባሕቱ ፡ ቦታ ፡ ስለ ፡ ገባ ፡ ብቻ ፡ ተብሎ ፡ እንዲፈታ ፡፡ ንኡስ ፡ አገባብም ፡ ሲኾን ፡ በኀላፊና ፡ በትን ቢት ፡ በነባር ፡ አንቀጽ ፡ እየገባ ፡ እኮ ፡ ቢያ ፡ ይኾናል ፤ ምስጢሩም ፡ ደስታና ፡ ሐዘን ፡

አንክሮ ፡ ነው ። እስመ ፡ ሖረ ፤ ኼደ ፡ እኮ ÷ ኼደ ፡ ቢያ ። እስመ ፡ የሐውር ፤ ዝኒ ፡ ከማሁ ። እስመ ፡ ርኢከኒሁ ፡ አመንከኒ ፤ አይተኸ ፡ እኮ ÷ አይተኸ ፡ ቢያ ። በነባርም ፡ እስመ ፡ ብዙኃን ፡ እለ ፡ አኀዙ ፡ ሠሪዐ ፡ ዜና ፡ ሲል ፡ እንዲሁ ፡ ይፈታል ።

፰፯ ፤ አኮኑ ፤ ዐቢይ ፡ አገባብ ። አኮኑ ፡ በገባብነቱ ፡ አስረጅ ፡ ነውና ÷ እንደ ፡ እስመ ፡ በኀላፊ ፡ በትንቢት ፡ በነባር ፡ አንቀጽ ፡ እየገባ ፡ ና ፡ ተብሎ ፡ ይፈታል ። ፪ኛም ፡ እስመ ፡ ና ፡ በተባለበት ፡ ስለን ፡ እንዲደርብ ÷ አኮኑም ፡ በገባብነቱ ፡ ና ፡ ሲባል ÷ ባንቀጽነቱ ፡ የጥያቄ ፡ አገባብ ፡ ኑ ፡ ሁ ፡ ስላለበት ፡ ነውና ፡ አይዶለምን ፡ ተብሎ ፡ በ፪ ፡ ይፈታል ። ይህም ፡ ገደፎሙኑ ፡ እግዚ ፡ ለሕዝቡ ÷ ሐሰ ፤ አኮኑ ፡ አነ ፡ እስራኤላዊ ። አኮኑ ፡ በፋሲካነ ፡ ተሰቅለ ፡ ክርስቶስ ። አኮሁ ፡ ነፍስ ፡ ተዐቢ ፡ እምሲሲት ፡ በለው ፡ ይታወቃል ፤ አኮኑ ፡ አገባብ ፡ መባሉ ÷ የኋሊትም ፡ ተሰቅለ ፡ አኮኑ ፡ እያለ ፡ ማሰሪያ ፡ ማስጣሉ ፡ በሰዋስው ፡ እንጂ ÷ በመጽሐፍ ፡ አይዶለም ፤ በመጽሐፍስ ፡ ከኑ ፡ በቀር ፡ አኮ ፡ አገባብ ፡ ተብሎ ፡ አይጠራም ። ያንቀጽነቱንም ፡ አሉታና ፡ አፈታት ፡ በደቂቅ ፡ ርባታ ፡ ተመልከት ፡ (ቍ፺፰) ። አምጣነ ፡ ደግሞ ፡ ቅጽል ፡ ሲኾን ፡ ባገባብነቱ ፡ ና ፡ ይኾናል ፤ ይኸውም ፡ በሰዋስውና ፡ በቅኔ ፡ ነው ፡ እንጂ ÷ በመጽሐፍ ፡ እንደ ፡ አኮኑ ፡ ነው ። እስመ ፡ አኮኑ ፡ አምጣነ ፡ እነዚህ ፡ ፫ቱ ፡ ና ፡ ለመኾን ፡ በኀላፊና ፡ በነባር ፡ ሲገቡ ፡ በጽንዕ ፡ ይፈታሉ ፤ ይህም ፡ ቀንአ ፡ ሰይጣን ፡ ላዕለ ፡ አዳም ፤ እስመ ፡ አኮኑ ፡ አምጣነ ፡ እመ ፡ ዐቀበ ፡ ትእዛዘ ፡ ፈጣሪሁ ፡ ኢይመውት ፡ ለዓለም ፤ አይሞትም ፡ ነበርና ። ኢአምንዎ ፡ አይሁድ ፡ ለዘዕዉሩ ፡ ተወልደ ፡ ከመ ፡ ተፈወሰ ፤ እስመ ፡ አኮኑ ፡ አምጣነ ፡ ዕዉር ፡ ውእቱ ፤ ዕውር ፡ ነበረና ፡ ማለቱን ፡ ያሳያል ።

፰፰ ፤ በእንተ ፤ በይነ ፤ እንበይነ ። እነዚህ ፡ ፫ቱ ፡ ዐበይት ፡ አገባቦች ፡ ሲኾኑ ፡ ዘን ፡ በር ፡ ከፋች ፡ አድርገው ፡ በኀላፊ ፡ አንቀጽ ፡ እየገቡ ፡ ስለ ፡ ይኾናሉ ። ንወድሳ ፡ ለማርያም ፡ በእንተ ፡ ዘተወልደ ፡ እምኔሃ ፡ እግዚእነ ፤ ሞተ ፡ ክርስቶስ ፡ በይነ ፡ ዘሞተ ፡ እንበይነ ፡ ዘሞተ ፡ አዳም ። ምስጢራቸውም ፡ እንደ ፡ ከመ ፡ አንጻርነት ፡ ነው ። ደቂቅ ፡ አገባብም ፡ ሲኾኑ ÷ በእንተ ፡ ስለ ፡ በ ፡ ይኾናል ፤ ስለ ፡ የበጎ ÷ በ ፡ የክፉ ፡ ነው ፤ ይኸውም ፡ ነገር ፡ በእንተ ፡ ይሁዳ ፡ ወበእንተ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ በለው ፡ ይታወቃል ፤ ስለ ፡ ይሁዳና ፡ ስለየሩሳሌም ÷ በይሁዳና ፡ በየሩሳሌም ፡ ላይ ፡ ማለት ፡ ነውና ። ን ፡ ሲኾን ፡ ደግሞ ÷ ደስ ፡ ይበለው ፡ ብሎ ÷ ደስ ፡ ይበለው ፡ ሲል ፤ ደስ ፡ አይበለው ፡ ብሎ ÷ ደስ ፡ አይበለው ፡ ሲል ፡ ይኾናል ፤ ቃል ፡ ሥጋ ፡ ኮነ ፡ በእንተ ፡ አዳም ፤ አዳምን ፡ ደስ ፡ ይበለው ፡ ብሎ ፤ እምአፈ ፡ ደቂቅ ፡ ወሕፃናት ፡ አስተዳሎከ ፡ ስብሐተ ፡ በእንተ ፡ ጸላኢ ፤ ዲያብሎስን ፡ ደስ ፡ አይበለው ፡ ብሎ ። ሲዘረዘርም ÷ በእንቲአሁ ፡ ሃ ፡ ብሎ ፡ ስለ ፡ ርሱ ፡ የርሱን ፡ ነገር ÷ በርሱ ፡ ላይ ፡ በርሱ ፡ ምክንያት ፡ እያሰኘ ፡ እንዳርእስቱ ፡ ይፈታል ። በይነ ፡ በ ፡ እያጋነነው ፡ ሳያጋንነውም ÷ እንበይነ ፡ ብቻውን ፡ ኹኖ ፡ ፪ቱም ፡ ስለ ፡ ይኾናሉ ። በበይነ ፡ ዝንቱ ÷ በይነ ፡ ምንት ÷ እንበይነ ፡ ምዲት ።

፰፱ ፤ ህየንተ ፤ ተውላጠ ፤ ፍዳ ፤ በቀለ ። እነዚህ ፡ ፬ቱ ፡ ዐበይት ፡ አገባቦች ፡ ሲኾኑ ÷ ከበቀለ ፡ በቀር ፡ ፫ቱ ፡ ዘን ፡ በር ፡ ከፋች ፡ አድርገው ፡ ህየንተና ፡ ፍዳ ፡ በኀላፊ ÷ ተውላጠ ፡ በኀላፊና ፡ በትንቢት ፡ እየገቡ ፡ ኹሉም ፡ ስለ ፡ ይኾናሉ ። ህየንተ ፡ ዘገብሩ ፡

ግንፋለ። ተውላጠ፡ ዘይሴሰይ። ተወክፈ፡ አዳም፡ ፍትሐ፡ ሞት፡ ፍዳ፡ ዘአበሰ። በቀለ፡ ደግሞ፡ በቁም፡ ቀሪነቱን፡ ሳይለቅ፡ ስለ፥እንደ፡ ይኾናል፤ ብፁዕ፡ ዘይትቤቀለከ፡ በቀለ፡ ተበቀልክነ፤ ስለ፡ ተበቀልሽን፥እንደ፡ ተበቀልሽን። ደቂቅ፡ አገባብም፡ ሲኾኑ፡ ህየንተ፡ ስለ፥ፈንታ፥እንደ፡ ይኾናል፤ በዋጋ፡ በለውጥ፡ በካሳ፡ ይገባል። ስለ፡ሲኾን፥ይሙት፡ ህየንተ፡ ሕዝብ። ፈንታ፥ፈደዩኒ፡ እኪተ፡ ህየንተ፡ ሠናይት። ተቀንየ፡ያዕቆብ፡ ህየንተ፡ ራሔል። እንደ፡ሲኾን፥አ፡እግዚኦ፡ አሕመልምል፡ሊተ፡ ነፍስየ፡ ህየንተ፡ ዕፅ፡ ትክልት፡ ማእከለ፡ ገነት። ሲዘረዘርም፡ ህየንቴሁ፡ ሃ፤ በርሱ፡ ፈንታ፡ ስለ፡ ርሱ፡ ያሰኛል። ተውላጠም፡ ለውጥነት፡ በለው፡ በብትን፡ እየገባ፡ ስለ፡ ይኾናል፤ ተውላጠ፡ዝ፥ስለዚህ። ሲዘረዘርም፡ እንደ፡ ጥሬነቱ፡ ተውላጡ፡ ጣ፡ ብሎ፡ ለውጡ፡ ልዋጩ፡ ያሰኛል። ፍዳም፡ በብትን፡ ሲገባ፡ ስለ፡ ይኾናል፤ ፍዳ፡ ወይን፡ ይስተይ፡ ማየ፡ ዝናም፤ ስለ፡ ወይን፥በወይን፡ ብድር፥ወይም፡ ፈንታ።

፸፤ ኀበ፤መንገለ፤ውእደ። እነዚህ፡፫ቱ፡ ዐበይት፡ አገባቦች፡ ሲኾኑ፡ ዘንድ፡ የ፡ ይኾናሉ። ዘንድ፡ ሲኾኑ፡ በዘማች፡ በነባር፡ ያሳስራሉ፤ ይህም፡ ተመዊአቱ፡ ለንጉሥ፡ ይከውን፥ ወይም፡ ውእቱ፡ ኀበ፡ መንገለ፡ ውእደ፡ ኢፈድፈደ፡ ሰራዊቱ፤ ካልበዛ፡ ዘንድ፡ ይኾናል፥ወይም፡ ነው፡ ማለቱን፡ ያሳያል። የ፡ ሲኾኑ፡ ግን፡ የቦታ፡ ቅጽሎች፡ ናቸውና፤ በ፬ኛ፡ ክፍል፡ ተነግሯል፡(ቍ፱፲፮)። የቦታም፡ ቅጽሎች፡ ስለ፡ ኹ፡ ፮፡ የቦታ፡ አገባቦች፡ ይሰማሟቸዋል። ፩ኛ፤ ኀበ፡ መንገለ፡ እንተ፡ ውስተ፡ ለ፡ ወደ፡ ሲኾኑ፥ውእደ፥ወደ፡ ለመባል፡ መደበኛ፡ አገባብ፡ ነውና። ፪ኛ፤ እንተ፡ በ፡ ሲኾን። ፫ኛ፤ በ፡ በቁም፡ ቀሪ፡ ሲኾን። ፬ኛ፤ እም፡ መነሻ፡ ሲኾን። ፭ኛ፤ እስከ፡ መድረሻ፡ ሲኾን፤ የ፡ ለሚኾን፡ አገባብ፡ እነዚህ፡ ፮ቱ፡ እየተሰማሙት፡ ሲነገር፡ ፍችው፡ ይበዘበዛል። ይህም፥የሐውሩ፡ አግብርት፡ እምኀበ፡ ሀለዉ፡ መንገለ፡ ኀበ፡ ሀሎ፥ ውእደ፡ ኀበ፡ ሀሎ፥እንተ፡ ኀበ፡ ሀሎ፥ውስተ፡ ኀበ፡ ሀሎ፥ለኀበ፡ ሀሎ፥እስከ፡ ኀበ፡ ሀሎ፡ እግዚኦሙ፤ ባሮች፡ ካሉበት፡ ጌታቸው፡ ወዳ፥እስከለበት፡ ይኼዳሉ። ይሄልዉ፡ አግብርት፡ እንተ፡ ኀበ፡ ሀሎ፥በኀበ፡ ሀሎ፡ እግዚኦሙ፤ ባሮች፡ ጌታቸው፡ ባለበት፡ ይኖራሉ፡ ማለቱን፡ ያሳያል። ዳግመኛም፡ በ፡ እም፡ እንተ፡ በየምስጢራቸው፡ ሲሰማሙት፥አልቦ፡ በኀበ፡ ኢይከብር፡ ነቢይ፤ የማይከብርበት። በ፡ ብሔር፡ እምኀበ፡ ይወፅእ፡ ብሩር፤ የሚወጣበት። ኢየአምር፡ እንተ፡ ኀበ፡ ይመጽእ፡ ኀጢአት፤ የሚመጣበትን፡ ያሰኛል። የቦን፡ ዝርዝር፡ በን፡ ከን፡ ወደን፡ ማምጣታቸው፡ የቦታ፡ ቅጽሎች፡ ሲኾኑ፡ ነው፤ ኀበ፡ ሀሎ፡ ቀደላ። ኀበ፡ ተለይቶ፡ በትንቢትና፡ በደጊም፡ ሲገባ፥ሲ፡ ሲ፡ ሳ፡ ሳ፡ ስ፡ ስ፡ እየ፡ እየ፡ እያሰኘ፡ በእንዘ፡ ዐማርኛ፡ ይፈታል፤ ሰሎሞን፡ ኀበ፡ ኀበ፡ ይነውም፡ ይከሥት፡ ዐይኖ፡ ሲ፡ ሲ፤ ኀበ፡ ኀበ፡ ይነቅህሰ፡ ይከድኖ። ማየ፡ አይኅ፡ እስከነ፡ አርብዓ፡ መዋዕል፡ ኀበ፡ ኀበ፡ ይመልእ፡ ሖረ፡ እየ፡ እየ፤ ወእምድኅሬሁሰ፡ ኀበ፡ ኀበ፡ ይነትግ። ደቂቅ፡ አገባብም፡ ሲኾኑ፡ ፫ቱ፡ ዅሉ፡ ወደ፥ አጠገብ፡ ይኾናሉ። አሐውር፡ ኀበ፡ አብ፤ ነበረ፡ ኀበ፡ ዐዘቅት። ሖሩ፡ መንገለ፡ መስዕ፤ ኢታቅሞ፡ መንገሌከ። እቱ፡ ውእደ፡ ሕዝብከ፤ በውእደ፡ ማየ፡ ባሕር፥አጠገብ። በተለየ፡ ግን፡ ኀበ፡ በአካል፡ ሲገባ፡ ዘንድ፤ መንገለ፡ ወገን፡ ይኾናል፤ እንተ፡

ሀለወት፡ኀበ፡አብ። ኢኮነ፡አምላከ፡እመንገለ፡እሙ፤ አላ፡እመንገለ፡አቡሁ። ሲዘ ረዘሩም፡ኀቤሁ፡ሃ፥ መንገሌሁ፡ሃ፥ ውእዴሁ፡ሃ፥ ወይም፡ውእዱ፡ዳ፡ ያሰኛሉ፤ ከኀበና፡ከመንገለ፡በቀር፡የውእደ፡ዝርዝር፡አልተለመደም።

፸፩፤ እንዘ፤ ዐቢይ፡አገባብ። ሲ፡ሳ፡ስ፡እየ፡ቸልታ፡ይኾናል። ሲ፡ሳ፡ስ፡ ሲኾን፡በነባር፡በዘማች፡ከዚያውም፡በትንቢት፡በጽድቅ፡ባሉታ፡ይገባል፤ ከሀሎና፡ ከሀለወ፡በቀር፡በትንቢት፡ብቻ፡እንጂ፡በኀላፊ፡አይገባም። ይህም፥ እንዘ፡ይበ ልዑ፡ኢትበልዑ፡ንበልዕ፤ ሲበሉ፡ሳትበሉ፡ስንበላ። እንዘ፡ውእቱ፤ ሲኾን፡ሲኖር፡ ሳለ። እንዘ፡ሀሎ፡በ፡አልበ፡አኮ፤ ሳለ፡ ሳይኖር፡ሳይኾን። ዖደ፡አድያመ፡ዮርዳኖስ፡ እንዘ፡ይጸርሕ፤ እየጮኸ፡ማለቱን፡ያሳያል። ቸልታም፡ ሲኾን፥ ሞተ፡እንዘ፡የሐ ምም፥ ታሞ፤ ተቀብረ፡እንዘ፡ይመውት፥ ሙቶ፡ያሰኛል። ሲ፡ስ፡እየ፡በሚኾንበት፡ ቸልታነትን፡ይደርባል፤ ይህም፡እንዘ፡ይበልዕ፥ ሲበላ፡በልቶ፤ እንዘ፡ትበልዕ፥ ስት በላ፡በልተኽ፤ ጸርሐ፡እንዘ፡ይብል፥ ሲል፡እያለ፡ብሎ፡ማሰኘቱን፡ያሳያል።

፸፪፤ መጠነ፤ አምጣነ፤ ዐቅመ፤ ዐበይት፡አገባቦች። ቅጽልነታቸው፡ በንደ ኛው፡ምዕራፍ፡መጨረሻ፡በ፯፻፱፡ተነግሯል። አገባብም፡ኹነው፡በኀላፊና፡በትን ቢት፡ሲገቡ፥ ያኽል፡ስለ፡እንደ፡ይኾናሉ። ፫ቱ፡ኹሉ፡ጥሬ፡ዘሮች፡ናቸው፤ አም ጣነም፡የመጠነ፡ብዥ፡ነው፤ ዘይቤያቸው፡ልክ፡መጠን፥ ፍቻቸው፡ያኽልና፡ስለ፡ እንደ፤ ምስጢራቸው፡ስፍርና፡ቍጥር፡ግምት፡ስለ፡ኾነ፥ ልኩና፡መጠኑ፡ስፍሩና፡ ቍጥሩ፡በታወቀና፡ባልተወቀ፡በውስጠ፡ብዙነት፡ይገባሉ። በኀላፊ፥ መጠነ፡ጸለ ይኩ፡በሕይወትየ። በትንቢት፥ አምጣነ፡ትበልዕዎ፡ለዝንቱ፡ኅብዝት፤ ይህን፡ኅብ ዝት፡የምትበሉት፡ያኽል፥ ወይም፡በምትበሉት፡ልክ፤ ስለምትበሉት፥ እንደምትበ ሉት፡መጠን፡እያሰኘ፡ሌላውን፡ኹሉ፡ያሳያል። ዐቅመ፡ውስተ፡ልቡ፡ኀደረ፡ ፍቅረ፡ቃል፡ወሕይወቱ፤ ያደረበት፡ያኽል፥ ባደረበት፡ልክ፤ ስላደረበት፡እንዳደ ረበት፡መጠን። በአንጻራቸውም፡ከማሁ፡ፈድፋደ፡ሲከተሉ፤ በአምጣነ፡ይነፍኀ፡ ነፋስ፡ላዕሌሆሙ፡ከማሁ፡ይፈደፍድ፡ጽንዖሙ። አምጣነ፡ይከልአሙ፡ውእቱ፡ፈድ ፋደ፡ይነግሩ፡ሎቱ፡እያለ፡እንዲሁ፡ይፈታል። አምጣነ፡ተለይቶ፡በእንዘ፡ቦታ፡ እየገባ፡ሳ፡ይኾናል፤ ይህም፥ ወበሐቱ፡እብል፡አምጣነሰ፡ሕፃን፡ውእቱ፥ ሕፃን፡ኹኖ፡ ሳለ። አምጣነ፡ሀሎ፡መርዓዊ፡ምስሌሆሙ፥ ሳለ። ኢይክል፡ሰብእ፡ሐይወ፡አም ጣነ፡ኢይበልዕ፡ወኢይሰቲ፤ ሳይበላ፡ሳይጠጣ፡ማለቱን፡ያሳያል። ና፡ሲኾን፡እስመ፡ በገባበት፡ይገባል፤ አገባቡም፡ከእስመና፡ከአኮ፡ጋራ፡ቀድሞ፡ተነግሯል። መጠነ፡ ደግሞ፡ተለይቶ፡የሩቁን፡በቅርብ፡የቅርቡን፡በሩቅ፥ ያንዱን፡በብዙ፡የብዙ ውን፡ባንድ፥ ዘርዝሮም፡ሳይዘረዝርም፡ውጥን፡ይጨርሳል። የሩቁን፡በቅርብ፡ሲወ ጥን፥ አ፡ዳዊት፡ንጉሠ፡ሰሎሞን፡መጠነ፡አንተ፡ላዕለ፡እስራኤል፤ አንተ፡የንጉሥ ከውን፡ያኽል። የቅርቡን፡በሩቅ፡ሲወጥን፥ ሰሎሞን፡ንጉሥከ፡መጠነ፡አቡከ፡ላዕለ፡ እስራኤል። በቀረውም፡ሰበከ፡ጴጥሮስ፡ወንጌለ፡መጠነ፡ሙሴ፡አሪተ። ኢትሬኢኑ፡ መጠነ፡ይበልዕ፡ወይሰቲ፤ እንዲበላና፡እንዲጠጣ፡እያሰኘ፡ከመ፡በገባበት፡ይገ

ባል ። ደቂቅ፡ አገባብም፡ ሲኾኑ፡ ከመ፡ በገባበት፡ እየገቡ፡ እንደ፡ ይኾናሉ፤ በፊታ ታቸውም፡ ምስጢራቸውን፡ አይለቁም ።

፸፫፤ ከመ፤ ዐቢይ፡ አገባብ። እንደ፡ ዳ፡ ዲ፡ ድ፡ ይኾናል ። በ፡ ዘ፡ እያጋነ ኑት፡ ሳያጋንኑትም፥ ከማሁ፡ እንጻር፡ እየኾነው፡ ሳይኾነውም፡ በኀላፊና፡ በትን ቢት፡ ይገባል፤ በንጻር፡ ባብነት፡ ይነገራል ። በንጻር፥በከመ፡ ይምሕር፡ አብ፡ ውሉዶ፡ ከማሁ፡ ይምሕሮሙ፤ ወበከመ፡ ይርሕቅ፡ ሠርቅ፡ እምዐረብ፡ አርሐቀ፡ እምኔነ ። ባብ ነት፥ ተሰቅሉ፡ ጴጥሮስ፡ ወእንድርያስ፥በከመ፡ ተሰቅለ፡ ክርስቶስ፡ ይላል ። ውጥን፡ ጨራሽም፡ ሲኾን፡ እንደ፡ መጠን፡ ነው፤ ርሱ፡ በገባበት፡ ይገባል ። ፪ኛም፡ ከመ፡ ዘ፡ እንተ፡ እለ፡ በገቡበት፡ አንቀጽና፡ ጥሬ፡ ሲገባ፡ መሰለ፡ ይኾናል፤ ለምንት፡ ትኄልዩ፡ ከመ፡ ዘኢመጻእኩ፤ ያልመጣኹ፡ ይመስል፥ እንዳልመጣኹ፡ ኹሉ፤ ከመ፡ ዘሰራቂኑ፥ ሌባ፡ ይመስል፥ እንደ፡ ሌባ፡ ኹሉ ። በግእዝም፡ በታ፡ እየገባ፡ መሰለን፡ ሲያስከትል፡ ን፡ ይኾናል፤ ይህም፡ ከመ፡ ሰዶም፡ እምኮነ፥ ወከመ፡ ገሞራ፡ እመሰልነ፡ (ገሞራን፡ በመሰልን) ፡ በለው፡ ይታወቃል ። ሲዘረዝርም፡ አልቦ፡ ዘከማሁ፡ ሃ፤ ርሱን፡ የሚመ ስል፥ወይም፡ የመሰለ፥እንደ፡ ርሱ፡ ያለ፡ ሰኛል ። ፫ኛም፤ ከመ፥ መሐለ፡ ነበበ፡ ዖቀ፡ ጠየቀ፡ ርእየ፡ ሰምዐ፡ ኀለየ፡ በሚሉና፡ ይህን፡ በመሰሉ፡ አናቅጽ፡ ሲሳብ፡ ነገር፡ ኹኖ፡ ማድረግ፡ መደረግን፡ ያሳያል፡ እንጂ፤ እንጻር፡ አይኾንም ። ይህም፥ኢ ሰማዕኩኑ፡ ከመ፡ ነግሠ፡ አዶንያስ ። ይትፈጸም፡ ዘተብህለ፡ በነቢይ፡ ከመ፡ ናዝራዊ፡ ይሰመይ፡ ወልድየ ። በነባርም፡ ወሰምዐ፡ ያዕቆብ፡ ከመ፡ ቦ፡ እክል፡ በብሔረ፡ ግብጽ ። ተዘከር፡ እግዚኦ፡ ከመ፡ መሬት፡ ንሕነ፡ እያሰኘ፡ ተሳቢነቱን፡ ያሳያል ። ተሰፈወና፡ ተነበየ፡ እነዚህ፡ ፪ቱ፡ ሲስቡት፡ ግን፡ በትንቢት፡ ብቻ፡ ይገባል፤ ተፈሥሐት፡ ሳራ፡ በልደተ፡ ይሥሐቅ፥ወተሰፈወት፡ ከመ፡ ይልህቅ ። ተነበዩ፡ ነቢያት፡ ከመ፡ ይትወ ለድ፡ ክርስቶስ፥ወከመ፡ ይትቀተል፡ ወይትነሣእ፤ እንዲወለድ፥እንዲሞትና፡ እንዲ ነሣ ። አንዳንድ፡ ጊዜም፡ ርኢ፡ ዘከመ፡ ይጽሕፍ፥ወለቡ፡ ዘከመ፡ ይነብብ፥ወስማዕ፡ ዘከመ፡ ያወሥእ፡ እያለ፡ ሲገባ፥አጣጣፉን፡ አነጋገሩን፡ አመላለሱን፡ ተብሎ፡ መፈ ታት፡ ያምርለታል ። ፬ኛም፤ ሲነባበርና፡ሲደረደር፡በኀላፊና፡በትንቢት፡ይገባል፤ ሲነባበር፡ ከመ፡ ከመ፡ ቀርበ፥ወከመ፡ ከመ፡ ይበጽሕ፡ ጊዜሁ፡ እያለ፡ ፈጽሞ፡ ያሰ ኛል ። ሲደረደርም፥ነአምን፡ ከመ፡ ሐመ፡ ወከመ፡ ሞተ፥ከመሂ፡ ተንሥአ፡ ወከመ፡ ዐርገ፡ እያሰኘ፡ በተሳቢነት፡ ይነገራል ። በቅርብ፡ ዐጸፋም፡ ሲገባ፥ከመ፡ ዝ፡ ወከመ፡ ዝ፡ መከርኩ፡ አነ፤ እንዲህና፡ እንዲህ ። ከመ፡ ከመ፡ ዝ፡ ግዒሮ፡ ሞተ፤ እንዲህ፡ እን ዲህ፡ ብሎ፥ወይም፡ ተናግሮ፡ እያሰኘ፡ ተሳቢነቱን፡ ያሳያል ። ሠረዝም፡ ሲኾን፥ሰሎ ሞን፡ ለመንግሥት፡ ከመ፡ ዳዊት፥ወመንግሥት፡ ለዳዊት፡ ከመ፡ መንበር፡ እያለ፡ በነ ባር፡ ይገባል ። ከመ፡ በዘንድ፡ አንቀጽ፡ ሲወድቅ፡ አዳማቂ፡ ኹኖ፡ ይቀራል፤ ከመ፡ ይብጻሕ፡ ዘተብህለ፤ ይህም፡ ይደርስ፡ ዘንድ፥እንዲደርስ፡ ሊደርስ፡ ተብሎ፡ ሲፈታ፡ እንዲ፡ ያሰኘው፡ ጠባዩ፡ ነው፡ እንጂ፤ ከመ፡ እንዳይዶለ፡ አስተውል ። ደቂቅ፡ አገ ባብም፡ ሲኾን፡ በጥሬ፡ በቅጽል፡ በብትን፡ ቃል፡ ኹሉ፡ እየገባ፡ እንደ፡ ይኾናል፤ ምስ ጢሩም፡ እንጻርነት፡ ነው ። ተቀሥፈ፡ ከመ፡ ገብር፥ወተስቅለ፡ ከመ፡ እቡስ፤ ከመ፡

**ዘልገሰ** ፤ (ተቀ፡ ግ) ፤ ታመመ፡ ተደወየ፤ ቈሰለ፡ ዐበጠ፡ ተላጠ፤ የገላ ። ዘልገሰ፡ ሥለንታሁ፡ ወፀፀየ፡ ልሳኑ፡ (መጽ፡ ምስ) ።

**ዝልጕስ**፤ (ሳን፡ ሳት፡ ግስት) ፤ የታመመ፡ የቈሰለ፤ ድጡይ፡ ቍማጣ ። እመርዔተ፡ አባግዕ፡ ቦ፡ ዘይከውን፡ ጥዑየ፡ ወቦ፡ ዝልጉስ ። ኖላዌ፡ አባግዕ፡ ሶበ፡ ይሬኢ፡ አሐቲ፡ ዝልግስት፡ አፉሃ፡ ወለእመ፡ ኢክልአ፡ ፍጡነ፡ ይከውና፡ ሥሎን፡ ዝልጕሳተ ። ዝልጕሳን፡ (ኢይበአ፡ ውስተ፡ ምሥዋዕ) ። በአርብዓሁ፡ ለአውላጋ፡ ወበሣልሱ፡ ለዝልጉስ፡ (አፈ፡ ተ፲፯ ። ቀሌ ። ቀሌ ። ፊልክ፡ ፲፰) ። ገዳፍ፤ ያልታረመ፡ መጽሐፍ፤ አላዋቂና፡ ዘባራቂ፡ ሰካር፡ የጣፈው፡ (ዐማርኛ) ።

**ዝልጋሴ**፤ ቍስል፡ ዕከክ፤ ደዌ፡ ሥጋ፡ ቍምጥና፤ ኮብሽ ። ዝልጋሴ፡ እኩይ ። ዝልጋሴ፡ ወለምጽ ። እምቍስለ፡ ዝልጋሴ፡ ንጣውእ፡ (ኢዮ፪፡ ፰ ። ፍ፡ ነ፡ ፶ ። ፳፶ ። አርጋ፡ ፮) ።

(ጥ) **ዘልሐ** ፤ (ዕብ፡ ዳላሀ፤ ዛሌሕ) ፤ ቀዳ፡ ጠለቀ፡ ደነበቀ፤ ጨለፈ ። ማይ፡ ዕሙቅ፡ ውስተ፡ ልበ፡ ብእሲ፡ መምክር፤ ወብእሲ፡ ጠቢብ፡ ይዜልሖ፡ (ምሳ፳፡ ፭) ። ዘለለ፡ ጠመቀ፡ በጠበጠ፤ በተን፡ ረጨ፡ ፈነጠቀ፤ ኹሉም፡ የውሃ፡ ነው ። ደለወን፡ እይ ።

**ዘሊል** ፤ ሎት ፤ (ዘለ፡ ይዘልል፡ ይዝልል ። ዕብ፡ ዛላል ። ዐረ፡ ዘልዘለ) ፤ መንዘልዘል፡ መንጠልጠል፤ መንቃንቅ፡ መወዛወዝ፤ የዛፍ፡ የፍሬ ። መዝለል፡ ማለፍ፤ መዘለል፡ መታለፍ፤ የተራ ። ዘለላ፡ ዝልዝል፡ ዝልል፡ ዝላይ፡ ማለት፡ ከዚህ፡ የወጣ፡ ነው ።

**መዝለል** ፤ **ምዝላል** ፤ መሎጊያ፤ ደጓሳ፡ ዕንጨት፡ የሳንሳ፡ የሚይዙበት ። ድንባዝን፡ እይ፡ ከዚህ፡ ጋራ፡ አንድ፡ ነው፤ ባለብሎዮች፡ ግን፡ ቀፎ፡ ባጥይ፡ ይሉታል ። ወጸርዎ፡ ክልኤቱ፡ በምዝላል፡ (ዘኍ፲፫፡ ፳፬) ።

**ዘሊፍ** ፤ ፎት ፤ (ዘለፈ፡ ይዘልፍ፡ ይዝልፍ ። ዕብ፡ ዛላፍ ፤ ረጨ) ፤ መመንጨት ፤ ሳያቋርጡ፡ መፍሰስ፡ መውረድ፤ መጕረፍ፡ መኼድ፤ የወንዝ ። ዘለፍ፡ ማለት፡ መዝለፍለፍ ። በቁሙ፡ መዝለፍ፤ መስደብ፡ መንቀፍ፤ መምከር፡ መገሠጽ፡ መመስከር፡ መፍረድ ። ኢትዝልፎሙ፡ ለእኩያን፤ ዝልፎ፡ ለጠቢብ ። ፈያታዊ፡ ዘየማን፡ ዘለፈ፡ ርእሶ፡ በጊዜ፡ ሞቱ ። ይዘልፈከ፡ ቃለ፡ አፉከ ። ምግባራቲከ፡ ይዘልፋከ ። ይዝልፉ፡ ማእከሌነ፡ (ምሳ፱፡ ፰ ። ፊልክ፡ ፶፱ ። ኢዮ፲፭፡ ፮ ። ተረ፡ ቈር ። ዘፍ፴፮፡ ፴፯) ። መዘለፍ፤ መቀረጥ፤ መቈጥቈጥ፡ (ዐማርኛ) ። የመጥረቢያ፡ ልጅ፡ መዘለፊያ፡ እንዲሉ ።

**ዘላፊ** ፤ በቁሙ፤ የሚነቅፍ፡ የሚዘልፍ፤ የሚያጸይፍ ። ሔልያስ፡ ዘላፌ፡ ሕጋ፡ ለቤተ፡ አክአብ ። ተክለ፡ ሃይማኖት፡ ዘላፌ፡ ረሲዓን፡ (ስንክ፡ የካ፳፰ ። ደራሲ) ።

**አዝለፈ** ፤ አዘወተረ፤ አራደፈ፡ አከታተለ፤ አበዛ፤ መላለስ ። ወተረን፡ እይ ። ዘአዝለፈ፡ ትዕግሥቶ ። ሶበ፡ አዝለፈ፡ ጸሎተ ። ከመ፡ ያዝልፍ፡ ገቢረ፡ ትሩፋት፡ (ማቴ፲፡ ፳፪ ። ፊልክ፡ ፶፮ ። ፈ፡ መ፡ ፪፡ ፪) ። አ(ሰ)ዘለፈ፡ አሰደበ፤ አስነቀፈ ።

**አዝላፊ**፤ የሚያዘወትር፤ አዘውታሪ ። ለእመ፡ ኮነ፡ አዝላፌ፡ ለገቢር ። ይኩኑ፡ አዝላፍያነ፡ ጾም፡ ወጸሎት፡ (ፊልክ፡ ፪፻፳፯ ። ፍ፡ ነ፡ ፲፡ ፯) ። አሰዳቢ፤ አስነቃፊ ።

**መዝለፌ** ፤ ዝኒ፡ ከማሁ፤ አዘውታሪ ። መዝለፌ፡ ስካር፡ ወእከይ ። መዝለፊተ፡ ተፀምዶ ። ኩኑ፡ ለጸሎት፡ መዝለፍያነ፡ (ፍ፡ ነ፡ ፭ ። ፲፡ ፰ ። ፲፱) ። የሚዘልፍ፡ የሚነቅፍ፤ ዘላፊ፤ አዘላፊ ። ኮነነ፡ መዝለፌ፡ ኅሊናነ፡ (ጥበ፪፡ ፲፬) ።

**ተዘልፈ**፤ ተዘወተረ፤ ተለመደ ። በቁሙ፤ ተዘለፈ፡ ተሰደበ፡ በገዛ፡ አፉ፤ ተጸጸተ፡ ተወቀሠ፡ በኅሊናው ። እመ፡ ተዘከርኩ፡ ተዘለፍኩ ። ወባሕቱ፡ በዘተዘለፍኩ፡ ተመሰውኩ ። ቦ፡ እለ፡ ይዘለፉ፡ ወይትመውኡ፡ (ኢዮ፳፩፡ ፯ ። ጓ፪፡ ፯ ። ቄር) ።

**ዝሉፍ** ፤ (ፋን፡ ፋት፡ ልፍት) ፤ የተዘወተረ፤ ዝውትር ። ዘልፈ፡ ለዝላፉ፡ ለዓለም፡ በማለት፡ ፈንታ፡ ዝሉፈ፡ ለዝሉፉ፡ ይላል፤ የተሳሳተ፡ ነው ። ይትቀነይ፡ ሎቱ፡ ዝሉፈ ። ኢትግድፈነ፡ ለዝሉፉ ። እስከ፡ ለዝሉፉ፡ (ዘፀ፳፩፡ ፮ ። መዝ፡ ፸፫ ። ኢዮ፳፫፡ ፫) ። ዳግመኛም፡ መረግድ፤ አፈው፡ በማለት፡ ፈንታ፡ ዝሉፍ፡ ይላል፤ ይህ፡ ደግሞ፡ የተሳሳተ፡ ነው ። ዝሉፍ፡ ወእንቡዝ፡ ኢይዜከርዋ ። ወያመጽኡ፡ ለኪ፡ ዝሉፈ፡ (ኢዮ፳፰፡ ፲፰ ። ሕዝ፳፯፡ ፲፯) ።

—፤ በቁሙ፤ የተዘለፈ፡ የተነቀፈ፤ አውታታ፡ ደፋር፤ ይሎኝ፡ አይል ። ኢትኩን፡ ዝሉፈ፡ በልሳንከ ። ዝሉፍ፡ ለይትገሠጽ ። ዝሉፋን፡ እለ፡ ኢይትኤዘዙ ። ነፍስ፡ ዝልፍት፡ ኢትዜወር፡ (ሢራ፭፡ ፲፬ ። ኪዳ ። ቲቶ፩፡ ፮ ። ሢራ፲፱፡ ፫) ። ጕጕኣን፡ ዘላፍያን፡ በማለት፡ ፈንታ፡ ዝሉፋን፡ ይላል፤ ስሕተት፡ ነው፡ (፪ጢሞ፡ ፫፡ ፬ ። ሮሜ፩፡ ፴) ።

**ዝልፈት** ፤ ማዘውተር፤ መዘውተር፤ ዝውተራ፡ አለማቋረጥ ። በዝልፈቱ፡ ወዕጽበቱ፡ (ፊልክ) ። መዝለፍ፡ መዘለፍ፤ አዘላለፍ፡ ዘለፋ፤ ተግሣጽ፡ ትምርት ። በእንተ፡ ዝልፈት፡ ትዝኅርቶሙ ። ለዝልፈት፡ አበሳሆሙ ። እለ፡ ይጸልኡ፡ ዝልፈተ፡ (ፊልክ፡ ፻፺፱ ። ጥበ፩፡ ፱ ። ምሳ፲፭፡ ፲) ።

**ዚልፋ** ፤ ዜልፋ፡ (ዕብራ) ፤ የሴት፡ ስም፤ አመተ፡ ልያ፡ ብእሲተ፡ ያዕቆብ፡ (ዘፍ፳፱፡ ፳፬) ። ግእዝ፡ ግን፡ ዘለፋ፡ ይላል፤ ስሕተት፡ ነው ።

**ዘለፋ** ፤ በቁሙ፤ ስድብ፡ ነቀፋ፡ ምክር፡ ተግሣጽ ። ዘለፋ፡ ክሡት ። ዘለፋ፡ ካህናት ። ንጽሕፍ፡ እንከ፡ ዘለፋሁ፡ ለንስጥሮስ፡ (ምሳ፳፯፡ ፭ ። መዝ፡ ፵፱ ። መጽ፡ ምስ) ።

**ዘልፍ** ፤ **ዘልፈ** ፤ ብዙ፡ ጊዜ፡ ኹልጊዜ፤ ወትሮ፡ ዘወትር፤ በየቀኑ፤ ዕለት፡ ዕለት፤ ጧት፡ ማታ፤

ሠርክ ፡ ዘላለም ፤ ዘሬም ፡ ነገም ። በእንተ ፡ ደዌከ ፡ ዘዘልፍ ። ወከመ ፡ ዝ ፡ ይከውን ፡ ለዘልፍ ። መሥዋዕት ፡ ዘልፍ ፡ (፩ጢሞ ፡ ፭ ፡ ፳፫ ። ዘኍ ፡ ፳፰ ፡ ፲፮ ። ዕዝ፫ ፡ ፭) ። ዘልፈ ፡ ለለ ፡ ዕለቱ ። እዜከረክሙ ፡ ዘልፈ ። ይእዜኒ ፡ ወዘልፈኒ ። ዘልፈ ፡ እሬእዮ ፡ ለእግዚ ። ወዘልፈ ፡ ስብሐቲሁ ፡ ውስተ ፡ አፉየ ፡ (ዘፀ፲፮ ፡ ፭ ። ሮሜ፩ ፡ ፱ ። ቅዳ ። መዝ ፡ ፲፭ ። ፴፫) ።

**ዘልፋዊ** ፤ ዘዘልፍ ፤ የዘወትር ፡ የዘላለም ፤ የማይቀር ፡ የማይታጐል ።

**ዝላፍ** ፤ ወትሮ ፤ ዘላለም ። ዝላፍና ፡ ዘልፍ ፡ ፩ ፡ ናቸው ። እስመ ፡ ምስሌሆሙ ፡ ለዝላፉ ፡ ሀሎ ። እምይእቲ ፡ ዕለት ፡ ወለዝላፉ ። ወከነ ፡ ለዝላፉ ፡ ቀትል ፡ (ኪዳ ። ዳን፭ ፡ ፳፱ ። ፪ነገ ፡ ፫ ፡ ፩) ።

**ተዛለፈ** ፤ ተዘዋተረ ፤ ተዘወታተረ ። በቁሙ ፤ ተሳደበ ፡ ተሰዳደበ ፤ ተሟገተ ፡ ተከራከረ ። መደቡ ፡ መደራረግ ፡ ሲኾን ፡ ማድረግም ፡ አለበት ። ኢትዛለፍ ፡ በማእከለ ፡ ሊቃውንት ። ለማርያም ፡ እኅተ ፡ ሙሴ ፡ ሶበ ፡ ተዛለፈቶ ፡ አውፅእዋ ፡ እምትዕይንት ። እምድኅረ ፡ ተዛለፉ ፡ በስምዕ ፡ ከመ ፡ ቀታሌ ፡ ነፍስ ፡ ውእቱ ። ይዛለፎሙ ፡ ለብዙኃን ፡ አሕዛብ ፡ (ሢራ፯ ፡ ፲፱ ። ዲድ ፡ ፴፭ ። ቀሌ ። ኢሳ፪ ፡ ፬) ።

**ትዝልፍት** ፤ ዝውተራ ፡ አዘውታሪነት ፤ ተሳዳቢነት ። ክርክር ፡ ስድብ ፤ ንዝንዝ ፡ ውዝግብ ፤ ችክታ ። በእንተ ፡ ትዝልፍቱ ። አኮ ፡ በሀከክ ፡ ወበትዝልፍት ። ትዝልፍተ ፡ ኅሊና ፡ ስሑን ፡ (ቀኖና ። ግብ፲፱ ፡ ፴፮ ። ቄር ፡ ጸላ) ።

**ዘሊቅ** ፤ (ዘለቀ ፡ ይዘልቅ ፡ ይዝልቅ) ፤ በቁሙ ፤ መዝለቅ ፤ መዘልቀቅ ፡ (ዐማርኛ) ።

**ዘሊስ** ፤ (ዘለሰ ፡ ይዘልስ ፡ ይዝልስ) ፤ በቁሙ ፤ መዘለስ ፡ ዘለሳ ፡ መጣል ፡ (ዐማርኛ) ።

**ዘም** ፤ ዞም ፤ (ጽር ፡ ዞሞስ) ፤ ደም ፡ እዝኅ ፤ መረቅ ፡ እሙክ ፡ (ሕዝ፳፬ ፡ ፲ ። መሳ፮ ፡ ፲፱ ፡ ፳) ።

**ዜመ** ፤—**አዜመ** ፤—ዘዪም ፡ ዜመ ።

**ዘሚድ** ፤ ዶት ፤ (ዘመደ ፡ ይዘምድ ፡ ይዝምድ ። ፀመደ) ፤ ማዛመድ ፡ ማዋደድ ፡ ማስማማት ፤ ማጣመር ፡ ማራክብ ፡ ማገናዘብ ፤ መጥመድ ፡ ማዛወግ ፡ ኹለቱን ፡ ነገር ፡ አንድ ፡ ማድረግ ። ፀመደን ፡ እይ ፤ የዚህ ፡ መንቲያ ፡ ነው ።

**አዝመደ** ፤ አዘመደ ፤ አስጠመደ ።

**ተዘምደ** ፤ ተዘመደ ፤ ዘመድ ፡ ኾነ ፡ ተስማማ ። እሉ ፡ እለ ፡ ይዘመዱ ፡ ወይሰናሰሉ ፤ እስመ ፡ ተወልዱ ፡ እምአበው ፡ ወእምሔዋን ። ለእመ ፡ ዘመወ ፡ ምስለ ፡ ካልእት ፡ ዘትዘመድ ፡ (ፍ ፡ ነ ፡ ፳፱ ፡ ፪ ። ፈ ፡ መ ፡ ፩ ፡ ፫) ።

**ተዛመደ** ፤ በቁሙ ፤ ተዘማመደ ፤ ተስማማ ። መዛመድ ፡ በ፪ ፡ ወገን ፡ ነው ፤ በሥጋ ፡ በነፍስ ፤ ለኹለቱም ፡ ብዙ ፡ ስልት ፡ አለው ።

**ዝሙድ** ፤ (ዳን ፡ ዳት ፡ ምድ) ፤ የተዘመደ ፡ የተዛመደ ፤ የተዘማመደ ፤ ዝምድ ።

**ዝምደት** ፤ መዘመድ ፡ መዘማመድ ፤ አዘማመድ ፡ ህመድነት ፡ ዝምድና ። ዝምደት ፡ ዘኢትትፌጸም ። ዝምደተ ፡ እምሔዋን ። ዝምደተ ፡ ሕብና ፡ (ፍ ፡ ነ ፡ ፵፪ ፡ ፮) ።

**ትዝምድ** ፤ (ዳት) ፤ መዘመድ ፤ ዝምድና ። ዘመድ ፤ ወገን ፡ ነገድ ፤ ልጅ ፡ ቤተ ፡ ሰብ ፤ ትውልድ ። እምድርከ ፡ ወእምትዝምድከ ፤ ወገን ። እሉ ፡ ትዝምደ ፡ ያዕቆብ ። ኅሩተ ፡ ትዝምድ ። ኵሉ ፡ በበ ፡ ትዝምዱ ፡ ኵሎ ፡ መዋዕለ ። በኵሉ ፡ ትዝምዶሙ ፡ (ኩፋ ፡ ፲፪ ። ፴፱ ። ጥበ፵ ፡ ፫ ። ኩፋ ፡ ፭ ። ፮) ።

**ትዝምድና** ፤ ዝምድና ፡ ዘመድነት ፤ ተወላጅነት ። ትዝምድና ፡ ዘውሉድ ፡ (ፍ ፡ ነ ፡ ፵፪ ፡ ፮) ።

**አስተዛመደ** ፤ (ዘመደ) ፤ አዛመደ ፡ አዘማመደ ፤ አስማማ ። አድራጊና ፡ አደራራጊ ፡ ብዙ ፡ ጊዜ ፡ በፍች ፡ ይተባበራል ። ተሰምዮት ፡ በመንፈስ ፡ ዘያስተዛምድ ፡ ምስለ ፡ መንፈስ ፡ ቅዱስ ፤ ከመ ፡ ተዘምዶት ፡ ሥጋዊ ፡ ያስተሳትፍ ፡ ምስለ ፡ ሥጋ ፡ (ፍ ፡ ነ ፡ ፶፩) ።

**ዘመድ** ፤ (ብ ፡ አዝማድ) ፤ በቁሙ ፤ ወላጅ ፡ አባት ፡ እናት ፤ ተወላጅ ፡ ወንድም ፡ እኅት ፤ አንት ፡ አክሥት ፤ ወገን ፡ ነገድ ፤ ሥን ፡ ፍጥረት ፤ ዐይነቱና ፡ ስሙ ፡ ትውልዱና ፡ ዘሩ ፡ አንድ ፡ የኾነ ። ወገን ፡ ነገድ ፡ የሩቅ ፤ ዘመድ ፡ አዝማድ ፡ የቅርብ ። ወልድ ፡ ዘይስሕት ፡ ያስተኃፍር ፡ ዘመዶ ። አክብሪ ፡ ታሕማኪ ፡ እስመ ፡ እምይእዜ ፡ ዘመድኪ ። ወአዝማዲሃኒ ፡ ጻድቃን ፡ እሙንቱ ፤ አባት ፡ እናት ፡ (ምሳ፳፱ ፡ ፲፭ ። ጦቢ፭ ፡ ፲፪ ። ዳን፭ ፡ ፫) ። አነ ፡ ዐዘርያ ፡ ዘመደ ፡ አናንያ ። እስመ ፡ ዘመድከ ፡ ይእቲ ፤ ወንድም ፡ እኅት ፡ (ጦቢ፭ ፡ ፲፪ ። ዘሌ፲፰ ፡ ፲፬) ። ኵሉ ፡ እንስሳ ፡ ያፈቅር ፡ ዘመዶ ። እምኵሉ ፡ ዘመደ ፡ ዓሣ ። ኵሉ ፡ ዘመደ ፡ መብልዕ ፤ ወገን ፡ ነገድ ፡ ዐይነት ፡ (ሢራ፲፫ ፡ ፲፭ ። ማቴ፲፫ ፡ ፵፯ ። ዘፍ፵ ፡ ፲፯) ። ወገብረ ፡ ዘንተ ፡ አርባዕተ ፡ ዘመደ ፡ በዕለት ፡ ሳድስት ፡ ወኮነ ፡ ኵሉ ፡ ዕሥራ ፡ ወክልኤተ ፡ ዘመደ ፤ ሥን ፡ ፍጥረት ፡ (ኩፋ ፡ ፪) ።

—፤ ጥሬ ፡ ዘር ፤ ሌላ ፡ ፊደል ፡ ባዕድና ፡ ምእላድ ፡ ሳይጨምር ፡ አንቀጹን ፡ መስሎ ፡ የሚገኝ ፡ ቃል ። ቀተለ ፡ ቀትል ፤ ገብረ ፡ ግብር ፤ ቀደሰ ፡ ቅዳሴ ፤ ነደ ፡ ነድ ፤ ቈረ ፡ ቍር ፤ ጸመ ፡ ጾም ፤ እንደዚህ ፡ ያለ ፡ ይህን ፡ የመሰለ ፡ ኹሉ ፡ ዘመድ ፡ ዘር ፡ ይባላል ፤ መሰል ፡ ማለት ፡ ነው ።

**አዝሙድ** ፤ (ዳት) ፤ የቅመም ፡ ስም ፤ አበሱዳ ፤ አቡሱዳን ፡ ነጭና ፡ ጥቍር ፡ ዐይነት ፡ (ዐማርኛ) ።

(ጥ) **ዘምዎ** ፤ ዎት ፤ (ዘመወ ፡ ይዜሙ ፡ ይዘሙ ። ዘነየ) ፤ መዝመት ፤ ሰውን ፡ የሰውን ፡ ገንዘብ ፡ ሴትን ፡ መማረክ ፡ መዝረፍ ፤ መስረቅ ፡ መቀማት ። መዘሞት ፡ መሴሰን ፤ ጣዖት ፡ ማምለክ ፤ ከሕግ ፡ መውጣት ፡ ማለፍ ፡ መትረፍ ። ዘምዎተ ፡ ብእሲ ፡ ምስለ ፡ ብእሲ ። ዘዘመወ ፡ በእንስሳ ። እለ ፡ ይዜምዉ ፡ ተባዕት ፡ ም

ስለ፡ ተባዕት፤ ወአንስት፡ ምስለ፡ አንስት። ብእሲ፡ ዘይዜሙ፡ በነፍስተ፡ ሥጋሁ፡(፩፡ መ፡ ፯፡ ፭፡ ፪፡ ፱። ሚራ፳፫፡ ፲፯)። እስመ፡ ዘምዎ፡ ትዜሙ፡ ምድር። ዘመወት፡ በዕፀ፡ ወበእብን። ከመ፡ ይብልዑ፡ ዝቡሐ፡ ለአማልክት፡ ወይዘምዉ፡ (ኤር፫፡ ፱። ሆሴ፭፡ ፪። ራእ፪፡ ፲፬)።

**ዘማዊ፤ (ዊት፡ ውያን፡ ያት)፤** በቁሙ፤ የሚሴስን፡ ሴሰኛ፤ አመንዝራ። ብእሲ፡ ዘማዊ። አረጋዊ፡ ዘማዊ። ኢትደመሩ፡ ምስለ፡ ዘማውያን። ትውልድ፡ ዐማፂት፡ ወዘማዊት፡ (ሚራ፳፫፡ ፲፯። ፳፭፡ ፪። ፩ቆሮ፡ ፭፡ ፱። ማቴ፲፪። ፴፱)።

**ዝማዌ፤** መሴስን፡ መገልሞት፤ ግልሙትና፡ ዘማዊነት።

**ዝሙት፤** በቁሙ፤ ሴሰን፡ ቅንዝር፡ ምንዝር፤ ከልክ፡ ያለፈ፡ የተረፈ። ዝሙተ፡ ብእሲት፡ ምስለ፡ ብእሲት፤ ዝሙተ፡ ብእሲ፡ ምስለ፡ ብእሲ፡ ወበእንስሳ። ቤተ፡ ዝሙት። ትርሲተ፡ ዝሙት፡ (፩፡ መ፡ ፯፡ ፭። ሕዝ፲፯፡ ፴፱። ምሳ፯፡ ፲)።

**ዘማ፤ (ብ፡ ዘማት)፤** በቁሙ፤ ጋለሞታ፡ አመንዝራ፡ ሴት፤ ኹሉን፡ የምቶድ፡ የማትለች፤ ባንድ፡ ወንድ፡ ያልቆመች። ብእሲት፡ ዘማ። ዘቲ፡ ትውልድ፡ ዘማ፡ ወኃጥእት። ዘርዐ፡ ዘማውያን፡ ወዘማት። ሑር፡ አውስብ፡ ብእሲተ፡ ዘማ፡ ወአዋልደ፡ ዘማ። በከመ፡ ይገብራ፡ አንስት፡ ዘማት፡ (ምሳ፳፡ ፫። ማር፰፡ ፴፰። ኢሳ፶፯፡ ፫። ሆሴ፩፡ ፪። ዲድ፡ ፫)።

**አዘመወ፤** አሴሰነ፤ ዘማዊ፡ አደረገ፤ አገለሞተ፤ አስገለሞተ። አዘመውካ፡ ለብእሲተ፡ ካልእከ። ወያዜምወኒ፡ ዘእንበለ፡ ፈቃድየ፡ (ዲድ፡ ፭። ገድ፡ ተክ)።

**መዘምው፤** የሚያሴስን፤ ዝሙት፡ የሚያስተምር፤ የሚያገብር።

**ዘሚም፤ ሞት፤ (ዘመ፤ ዘመመ፡ ይዘምም፡ ይዝምም። ዐረ፡ ዘመ። ሱር፡ ዛም)፤** መሸበብ፡ መለበብ፤ መለጐም፡ መመንገግ፤ እንዳይበላና፡ እንዳይጠባ፡ ማድረግ። ዝም፡ ማለት፤ ዝም፡ ማሰኘት፡ አፍን፡ መዝጋት፤ መያዝ፡ ማሲያዝ። ረመመን፡ እይ። መዝመም፡ ማጋደል፤ መወዛወዝ፡ መነዋወጥ፤ ዜማን፡ በቃል፡ በበትር፡ ማቅለጥ።

**ዝማሜ፤ (ምያት)፤** በቁሙ፡ የዜማ፡ ሕግ፡ አዘማመም፤ ከዜማው፡ ጋራ፡ የዘንግ፡ የመቋሚያ፡ አንሣሥ፡ አጣጣል። ዝማሜ፡ አምሳለ፡ ኪደተ፡ አንበሳ፡ ውእቱ፡ (ገድ፡ አብርሀ)።

**ዝማም፤ (ማት)፤** ዝምታ፡ አርምሞ። ታናሽ፡ ቅርጫት፡ እንደ፡ ከረጢት፡ ኹኖ፡ የእንስሳን፡ አፍ፡ የሚከት፤ መንግግ፡ በመያዝና፡ በማሰር፡ ፈንታ፡ የሚደረግ። ትግሣጽ፡ ወትምህርት፡ ልጓም፡ ወዝማም፡ (ፈላስ)።

—፤ ንሮ፡ መንደልት፤ ያፍንጫ፡ ቀለበት፡ የአራዊትና፡ የእንስሳት፡ ስናግ፤ ገመድ፡ እያበቱ፡ የሚስቡበት። ትወዲ፡ ሎቱ፡ ዝማማተ፡ ውስተ፡ አንፉ። እወዲ፡ ለከ፡ ዝማማተ፡ ውስተ፡ አንፍከ፡ (ኢዮ፵፡ ፳። ኢሳ፴፯፡ ፳፱)። ወጸበን፡ እይ።



ዝማም፡

**ዘመመን፤ ዘመሚት፤ (ዐማርኛ)፤** ዘመመን፡ የነደ፡ ድርድር፤ ዘመሚት፡ ቀይ፡ ጕንዳን።

**ዝማሞ፤** ስመ፡ ሀገር፤ የመንዝ፡ ክፍል፡ በሞፈር፡ ውሃ፡ ዳር፡ ያለ።

**ዘመን፤ (ናት፤ አዝማን፡ ናት። ዕብ፡ ወሱር፡ ዝማን። ዐረ፡ ዘመን፤ ዘማን)፤** በቁሙ፤ ዓመት፡ ጊዜ፡ ወራት፤ በየስሙና፡ በየክፍሉ። ዘመን፡ ወአዝማን፡ ወመንፈቀ፡ ዘመን። ኵሉ፡ በበ፡ ዘመኑ። ዘመናት። እምቅድመ፡ መዋዕል፡ ወአዝማናት፡ (ራእ፲፪፡ ፲፬። ሔኖ፪፡ ፭። አቡሻ፡ ፩። ቅዳ፡ አፈ)። ዘመነ፡ መፀው፡ ወሐጋይ፤ ወራት። ዓምንና፡ ጊዜን፡ ተመልከት።

**ዘመነ፤ (ይዜምን፡ ይዘምን)፤** ዘመናይ፡ ኾነ፤ ዘመን፡ ወሰነ፡ ቀጠረ። ዐደመን፡ እይ።

**ዘመናዊ፤** ዘመናይ፤ ባለጊዜ፡ ባለወራት፤ ሹም፡ ባለጠጋ፤ ኀላፊ፡ ነገር፡ ለጊዜው፡ ብቻ፡ የሚፈለግ። መብልዕ፡ ማሳኒ፡ ወዘመናዊ። ትፍግዕት፡ ዘመናዊት፡ ወኀላፊት። ሕይወት፡ ዘመናዊት፡ (ፍ፡ ነ፡ ፱። አፈ፡ ድ፳፯። አቡሻ፡ ፴፰)።

**ዘምሮ፤ ሮት፤ (ዘመረ፡ ይዜምር፡ ይዘምር። ዕብ፡ ዛማር፤ ዛሜር)፤** ማዝመር፤ አዝመራን፡ ማጨድ፡ መቍረጥ፤ መሰብሰብ፡ መከተት፤ መዝራትም፡ ይኾናል። አዝማሪ፡ መኾን፤ ሌሌ፡ ማለት፡ መዝፈን። ሐሊያሁ፡ ወዘመራሁ፡ በበረከተ፡ እግዚ፡ (ሚራ፵፯፡ ፮)።

—፤ መዠመር፡ መወጠን፤ የሥራ። መምራት፡ መቀኘት፤ መዘመር፡ ማመስገን፤ በልዑል፡ ዜማ፡ በዐቢይ፡ ቃል፤ በከበሮና፡ በጸናጽል፡ በሌላውም፡ ኹሉ። ይዘምሩ፡ በጊዜ፡ ተመጥዎ፡ ቍርባን፡ ኵሎሙ፡ ምእመናን። ቦ፡ እመላእክት፡ ዘይዜምር፡ ወቦ፡ ዘይቄድስ። ውእቱ፡ ዝማሬ፡ ዘኮኑ፡ ይዜምሩ፡ ቦቱ። ይዜምሩ፡ በአቅርንት። ይዜምሩ፡ በመሰንቆ። ወበመዝሙር፡ ዘዐሠርቱ፡ አውታሪሁ፡ ዘምሩ፡ ሎቱ፡ (ፍ፡ ነ፡ ፲፫። ቀሌ። ስንክ፡ ኅዳ፯። ፩ዜና፡ ፲፭፡ ፳፱። ፩ነገ፡ ፲፮፡ ፲፯። መዝ፡ ፴፪)።

—፤ ማማጠን፤ ይግባኝ፡ ማለት። መጥቀስ፤ ምስክር፡ መጥራት፤ ኹሉም፡ የሙግት፡ ነው። መጽሐፍ፡ ግን፡ በዘመረ፡ ፈንታ፡ ተዘመረ፡ ይላል፤ ስሕተት፡ ነው። ተዘ

መረ ፡ በቈሳር ፤ ወኀበ ፡ ቈሳር ፡ የሐውር ። ተዘመር ፡ በስመ ፡ ዚኣሁ ፤ አማጠነ ፡ (ግብ፳፭ ፡ ፳፭ ። ሲኖዶ) ። ያቀውሙ ፡ ቃላቲሆሙ ፡ ተዘሚሮሙ ፡ እምቅዱሳት ፡ መጻሕፍት ። እላ ፡ ክልኤ ፡ ቃላተ ፡ ተዘመርነ ፡ እንዘ ፡ ትእልፊት ፡ ዘከመ ፡ ዝ ፤ ጠቀሰ ፡ (ቄር ፡ ጸላ ። ተረ ፡ ኤጲ.) ። መመስከር ፡ ማወጅ ፡ መናገር ፤ መስበክ ፡ ማስተማር ። በአርእዮ ፡ መኑ ፡ ዘይዜምር ፤ ከመ ፡ ያስተርኢ ፡ እንዘ ፡ ይዜምር ፡ እምአብ ፤ ወመንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ይዜምር ፡ ከመ ፡ ይሠምር ፡ አብ ፡ (ቄር ፡ ተረ ፡ ኤጲ.) ። ዳግመኛም ፡ በዘመረ ፡ ፈንታ ፡ አዝመረ ፡ ይላል ፤ አያስኝም ። ሃይማኖተ ፡ መስቀል ፡ በዐውድ ፡ አዝመረ ። እንዘ ፡ ታዘምር ፡ ሃይማኖተከ ፡ በዐውድ ። አዝመረ ፡ ወልደ ፡ እግዚ ፡ በአቡሁ ፡ ሰማያዊ ፡ ወይቤ ፤ ኢያእመርክሙኑ ፡ ከመ ፡ ዘውስተ ፡ ቤተ ፡ አቡየ ፡ ሀሎኩ ፡ (ስንክ ፡ ጥቅ፳ ። ጥር፲፰ ። መጽ ፡ ምስ) ።

**ዘማሪ** ፤ **(ሪት ፡ ርያን ፡ ያት)** ፤ በቁሙ ፤ የሚዘምር ፡ ዜመኛ ፡ አመስጋኝ ፤ መሪ ፡ ዝማሪ ፡ ቀንቃኝ ። በአፈ ፡ ዘማሪ ፡ ዳዊት ፡ (ቄር ፡ ጸላ) ።

**መዘምር** ፤ **(ርት ፡ ራን ፡ ራት)** ፤ ዝኒ ፡ ከማሁ ፤ ዘማሪ ፡ አዝማሪ ፤ ባለበገና ። በከመ ፡ ይቤ ፡ መዘምር ። መዘምራን ፡ ወመዘምራት ፡ (መጽ ፡ ምስ ። ዕዝ፪ ፡ ፳፩) ።



መዘምር ፡

**መዝሙር** ፤ **(ራት ፤ መዛሙርት ። ዕብ ፡ ሚዝሞር ። ሱር ፡ ማዝሙራ ። ዐረ ፡ መዝሙር)** ፤ በቁሙ ፤ ምስጋና ፡ ውዳሴ ፡ ጸሎት ፤ መጽሐፈ ፡ ዳዊት ፤ ከ፻፶ው ፡ ክፍላት ፡ አንዱም ፡ አንዱም ፡ ክፍል ። መዝሙረ ፡ ዳዊት ፡ ትመስል ፡ ገነተ ፤ መዝሙረ ፡ ድንግል ፤ መዝሙረ ፡ ክርስቶስ ። በከመ ፡ ይቤ ፡ በውስተ ፡ መዝሙር ፡ ዘክልኤቱ ፡ (ደራሲ ። ግብ፲፫ ፡ ፴፫) ። ማመስገኛ ፡ ንዋየ ፡ ማሕሌት ፡ በገና ፡ ክራር ፡ ክበሮ ፡ ጸናጽል ፤ የመሰለው ፡ ኹሉ ። ንሥኡ ፡ መዝሙረ ፡ ወሀቡ ፡ ክበሮ ፤ መዝሙር ፡ ሐዋዝ ፡ ዘምስለ ፡ መሰንቆ ። በከበሮ ፡ ወበመዝሙር ፡ ይዜምሩ ፡ ሎቱ ፡ (መዝ ፡ ፹ ። ፻፵፰) ። ዜማ ፡ ድምፅ ፡ ከሰው ፡ ከበገና ፡ የሚወጣ ። ደረሰ ፡ ያሬድ ፡ መጽሐፈ ፡ መዝሙር ። ትረክብ ፡ መዝሙረ ፡ ነቢያት ። ወኢያጸምዕ ፡ መዝሙረ ፡ መሰንቆክሙ ፡ (ታሪ ፡ ነገ ። ፩ነገ ፡ ፲ ፡ ፭ ፡ ፲ ። ዓሞ፭ ፡ ፳፫) ።



መዝሙር ፡

**አዝመረ** ፤ **አዘመረ** ፤ አስቈረጠ ፤ አሳጨደ ። አ(ስ)ዝመረ ፤ አስመሰገነ ።

**አዝመራ** ፤ **(ዐማርኛ)** ፤ በቁሙ ፤ ዐጨዳ ፡ ስብሰባ ፤ ወይም ፡ ዝሪት ።

**አዝመር** ፤ **(ዐረ ፡ አስመር)** ፤ ያይነት ፡ ስም ፤ ደባባ ፡ ደባሳ ፤ የበሰለ ፡ የሻከከ ፡ ፍሬ ፡ የሚመስል ፤ ፍጹም ፡ ቀይ ፡ ወይም ፡ ፍጹም ፡ ጥቍር ፡ ያይደለ ፡ ማእከላዊ ፡ ሕብር ፡ (ራእ፲፰ ፡ ፲፪ ፡ ፲፮) ።

**አዛምር** ፤ የዳቦ ፡ ቅጠል ፤ ዐይነቱ ፡ አረንጓዴ ፡ ብጫቴ ፡ (ዐማርኛ) ።

**ተዘመረ** ፤ በቁሙ ፤ ተዘራ ፡ ታጨደ ። ምስክር ፡ ተጠራ ፤ ተጠቀሰ ። ተመሰገነ ፡ ተወደሰ ። ተዜመ ፡ ተቃኘ ፡ ተደረደረ ። ልማዱ ፡ ግን ፡ አድራጊ ፡ ነው ።

**ዝሙር** ፤ **(ራን ፡ ራት ፡ ምርት)** ፤ የታመነ ፡ የተመሰገነ ፤ እሙን ፡ ምስጉን ፤ የማይጠረጠር ፡ ምስክር ። ዝሙረ ፡ ቃላትየ ፡ ነቢይ ፡ ኤርምያስ ። ለዝንቱ ፡ ዝሙር ፡ ጳውሎስ ። ወዝሙር ፡ ጳውሎስ ፡ እንዘ ፡ ይብል ፡ (ቄር ፡ እስት ። ጸላ) ።

**ዝማሬ** ፤ **(ርያት)** ፤ መዘመር ፡ አዘማመር ፡ ዝመራ ፤ ዥመራ ፡ ቅንቀና ፤ ዜማ ፡ የዜማ ፡ ምስጋና ። ዝማሬ ፡ መላእክት ፡ ቅዱሳን ። ዘምሩ ፡ በአልባቢክሙ ፡ ዝማርያተ ፡ ወስባሕያተ ፡ (ፊልክ ፡ ፻፺፭ ። ፊመ ፡ ፴፪ ፡ ፯) ። በቁሙ ፤ የዜማ ፡ መጽሐፍ ፡ ስም ፡ ከ፭ቱ ፡ ጸዋትወ ፡ ዜማ ፡ አንዱ ፡ የቅዳሴ ፡ ወንድም ፡ ከድርገት ፡ በኋላ ፡ የሚቃኝ ፡ የሚዜም ፡ የሚዘመም ።

**ምዝማር** ፤ **(ራት)** ፤ ጥቅስ ፤ የመጽሐፍ ፡ ቃል ፡ ምስክር ፡ የሚኾን ። ብዙኃ ፡ ምዝማር ፡ ብየ ። ዘእምቅዱሳት ፡ መጻሕፍት ፡ ምዝማር ፡ (መጽ ፡ ምስ ። ቄር) ።

**ዛሚር** ፤ **(ዕብራ)** ፤ ዜማዊ ፡ ያፍ ፤ እጅግ ፡ ድምፀ ፡ መልካም ፤ ያሮድዮን ፡ ወንድም ፡ ወይም ፡ ርሱ ፡ ራሱ ፡ ያፈ ፡ ያሬድ ። ተመልሰኽ ፡ አሮድዮንን ፡ እይ ።

**ዘመረግድ** ፤—**ዕንቍ** ፤—**መረግድ** ፡ ረገደ ።



ዛሚር፡

**ዘኒብ፤በት፤(ዘነበ፡ይዘንብ፡ይዝንብ)፤** ማወዛወዝ፤መቍላት፡መሽጕብ፡መንስነስ።

**ዘነብ፤(ብ፡ አዝናብ። ዕብ፡ ዛናብ። ሱር፡ ዙንባ። ዐረ፡ ደነብ)፤** ኅራት፤ የእንስሳትና፡ የአራዊት፡ ቅጥይ፡ በስተኋላቸው፡ የሚበቅል፤ ጫፍ፡ ውልብልቢት፡ ጭራ። ዘነበ፡ከልብ። ዘነበ፡አፍራስ። ምቱረ፡ዘነብ። ርእስ፡ወዘነብ። ወቦሙ፡ዘነብ፡ከመ፡ዘነበ፡ዐቅራብ።ወአዝናቢሆሙ፡ከመ፡አራዊተ፡ምድር፡(ምሳ፳፯፡ ፲፯። ስንክ፡ መስ፳፪። ዘሌ፳፪፡ ፳፫። ኢሳ፲፬፡ ፲፱። ራእ፱፡፲፡ ፲፱)። ዘነበለ፡ አዘነበለ፤ ዝንበ፡ መዘንቢያ፡ ማለት፡ ከዘኒብ፡ ወጥቷል፡ (ዐማርኛ)።



ዘነብ፡

**ዝንብ፤(ዕብ፡ ዝቡብ)፤** በቁሙ፡ ኹሉን፡ የሚቀምም፡ የሚልስ፡ የንብ፡ ጕማ፤ ምናምንቴ፡ እንስሳ። ከገጠር፡ ንብ፡ የከተማ፡ ዝንብ፤ ዝንብ፡ ቢሰበሰብ፡ መግላሊት፡ አይከፍት፡ እንዲሉ፡ (ዐማርኛ)።



ዝንብ፡

**ዘንቢር፤(ብ፡ዘናቢር። ዐረ፡ዙንቡር፤ ዚንባር)፤** ተርብ፤ የውሻ፡ ዝንብ፡ የሚነድፍ፡ የሚነክስ፡ተቈናጣጭ። ወሰበ፡መጽአ፡ንጉሠ፡ፋርስ፡ኀበ፡ሀገረ፡ንጽቢን፡ወዐገታ፡አምጽአ፡ቅዱስ፡ባዕለ፡



ዘንቢር፡

ሰራዊቱ፡ደመና፡ዘናቢር፡ወትንንያ፤ወነደፍዎሙ፡ለአፍራሲሆሙ፡(ስንክ፡ ጥር፲፰)።

**ዘንበሪ፤(ዕብ፡ ዛምሪ)፤** የሰው፡ ስም፤ ከነገደ፡ስምዖን፡ወገን፡የስሉ፡ ልጅ፤ ያባቱ፡ ቤት፡ አለቃ፤ ከመንዝራይቱ፡ ክክስቢ፡ ጋራ፡ ባንድነት፡ ተጣምሮ፡ ተኝቶ፡ ሳለ፤ ካህኑ፡ ፊንሐስ፡ ያልዓዛር፡ ልጅ፡ በዘገሩ፡ ባበታ፡ ጦሩ፡ አጣምሮ፡ ወግቶ፡ የገደለው፤ የደብተራ፡ ኦሪት፡ ዕልው፡ (ዘኍ፳፭፡ ፲፬)።

**ዝንጊብል፤(ዕብ፡ ዛንግቢል)፤** በቁሙ፤ የተክል፡ ወገን፤ ሥሩ፡ ከቅመም፡ የሚገባ፤ ሽታው፡ የሚጣፍጥ፡ ጣዕሙ፡ የሚሰነፍጥ።

**ዘንጐጎ፤ ጎት፤(ዘንጎጎ፡ ይዘነጕጕ፡ ይዘንጕጕ)፤** ማሽሟጠጥ፤ በነገር፡ መንካት፡ መንካት፤ መስደብ፡ መዝለፍ፤ ማነወር፡ መንቀፍ፤ ማፌዝ፡ ማላገጥ። ይዘነጕግዎሙ፡ በእንተ፡ ዘጕዩ። ይዘነጕጉነ፡ በኀጢአ፡ ሕግ። ይጼዕሉክሙ፡ ወይዘነጕጉክሙ። ወከማሁ፡ ፈያትኒ፡ ይዘነጕግዎ፡ (ዮሴፍ። ጥበ፪፡ ፲፪። ማቴ፭፡ ፲፩። ፳፯፡ ፵፬)። ዘንግ፡ ማለት፡ ከዚህ፡ ወጥቷል፤ መንኪያ፡ መጕነጫ፡ ማለት፡ ነው፡ (አስቴ፬፡ ፲፭። ፭፡ ፪)።

**ዘንጓጕ፤(ጒት፡ ጕያን፡ ያት)፤** የሚያሽሟጥጥ፤ አሽሟጣጭ፡ ዘላፊ፡ ነቃፊ፤ ምላሱ፡ እንደ፡ ዘንግ፡ በሩቅ፡ የሚጠቅስ፡ የሚነካ። ይክውን፡ ዘንጓጔ፡ (ምሳ፲፫፡ ፩)።

**አዘንጎጎ፤** አሰደበ፤ አስነቀፈ። አዘንጐግሙ፡ ነፍሳቲክሙ። ቦ፡ እለ፡ ይክሕዱ፡ ወያዘነጕጉ፡ ህሉተ፡ ሥርዐተ፡ (ዮሴፍ። መጽ፡ ምስ)።

**ተዘንጎጎ፤** ተሽሟጠጠ፤ ተሰደበ፡ ተነቀፈ፤ ማላገጫ፡ ኾነ። ወተዘንጕጉ፡ በኀበ፡ ሀሰዉ፡ (ዘዳ፴፪፡ ፴፯)።

**ዝንጉግ፤ ጕ፤** የተሰደበ፡ ንቁፍ፤ ምኑን፡ ጎሱር። ከመ፡ ዝንጉጕ፡ ኢትኩኑ፡ (ምሳ፳፭፡ ፲)።

**ዝንጓጌ፤** ስድብ፡ ሽሙጥ፤ ተግዳሮት፡ ለግጥ፡ (ዘፍ፴፡ ፳፫። ሉቃ፩፡ ፳፭)። በባእስ፡ ወበዝንጓጌ፡ ይፌንዎሙ። ነገረ፡ ዝንጓጌ። ኢይረክቦ፡ ዝንጓጌ፡ (ኢሳ፳፯፡ ፰። ጥበ፭፡ ፫። ፩ዜና፡ ፲፯፡ ፱)።

**ዘንግዐ፤(ዘግዐ፤ ስሯ፡ ግ)፤** ዘነጋ፡ ረሳ፡ አጠፋ፡ ቀድሞ፡ ያውቀው፡ የነበረውን፤ ልቡ፡ ደንግጦ፡ አእምሮው፡ ተናውጦ፤ ወይም፡ በቀን፡ ብዛት፡ አርጅቶ፡ ገርኝቶ፤ ራሱ፡ ጠፍቶ፡ ተበላሽቶ። ዘግዐን፡ እይ፤ የዚህ፡ ሥር፡ ነው። ዘንግዐኒ፡ ልብየ። ሶበ፡ አኮ፡ ከመ፡ ዝ፡ እምእቤ፡ ዘንጋዕከ። ከመ፡ አብድ፡ እዘነግዕ፡ (ሉቱ፡ ዕዝ፲፡ ፶፩። ራእ፡ ባሮ። ፪ቆሮ፡ ፲፩፡ ፲፯፡ ፳፫)።

—፤ ለፈለፈ፡ ቀባጠረ፤ነገር፡ አበዛ፤ ምስጢሩ፡ ከዚያው፡ ይገባል። ወሶበ፡ ትጼልዩ፡ ኢትዘንግዑ፡ ከመ፡ አሕዛብ፡ (ማቴ፯፡ ፯)።

**አዘንግዐ፤** አዘነጋ፤ ዝንጉ፡ አደረገ፤ አስረሳ፡ ልብ፡ አጠፋ። አብዝኆ፡ መጻሕፍት፡ ያዘነግዕ፡ ልበ። ናሁ፡ አነ፡ ኣንጕግዎ፡ ወኣዘነግዓ፡ ልባ፡ (ግብ፡ ፳፮፡ ፳፬። ሆሴ፪፡ ፲፬)።

**ተዘንግዐ**፤ ተዘነጋ፡ ተረሳ፤ ጠፋ፡ ቀረ።

**ዝንጉዕ፤(ጓን፡ ጓት፡ ግዕት)**፤ የተዘነጋ፡ ዝንግ፤ ውዳቂ። የዘነጋ፡ ዝንጉ፤ ልበ፡ ቢስ፤ ተለል፡ ተለል፡ የሚል፡ (ቋንቋውን፡ የሚያውቅለት፡ ሳይኖር፡ አላስተርጓሚ፡ የሚናገር፡ (፩ቆሮ፡ ፲፬፡ ፲፩)። ዝንጉዕ፡ አይሁዳዊ። ኢይኩን፡ ዕዉረ፡ ወኢጽሙመ፡ ወኢ ዝንጉዐ። ዝንጉዓን፡ እለ፡ አልቦሙ፡ ልብ፡ (ቄር፡ እስት። ፍ፡ ነ፡ ፩። ፳፬፡ ፫)።

**ዝንጋዔ፤(ዕያት)**፤ በቊሙ፤ መዘንጋት፡ አዘ ነጋግ፤ ዝንጋታ፡ ርሳታ፤ ተረት፡ ተርታ፤ ከንቱ፡ ነገር። መንፈስ፡ ዝንጋዔ። አ፡ ለዝ፡ ዝንጋዔ። ወከነ፡ ዝንቱ፡ ነገር፡ በቅድሜሆሙ፡ ከመ፡ ዝንጋዔ፡ ወኢአምን ዎን፡ (ሆሴ፬፡ ፲። ቄር፡ እስት። ሉቃ፳፬፡ ፲፩)።

**ዝንድ፤(ዐረ)**፤ የብረት፡ ዘንግ፤ የመዝጊያ፡ ስናግ፡ ረዥም፡ ሸንገል። የዋዌን፡ ፍች፡ እይ፤ ዘንድ፡ ዘንደ፡ ማለት፡ ዐማርኛው፡ ከዚህ፡ የወጣ፡ ነው።

**ዜነወ፤—ነገረ፤—ዘየነ፤ዘይነወ።**

**ዘንይ፤ ዮት፤ (ዘነየ፡ ይዘኒ፡ ይዝኒ። ዕብ፡ ዛናህ። ሱር፡ ዝናእ። ዐረ፡ ዘነይ፤ ዘመወ)**፤ መዘናት፤ መዳራት፤ መቈላመም፡ የዝሙት፡ ዋዜማ፡ መቆም። መሴሰን፡ መቀንዘር፤ ባልን፡ ወይም፡ ሚስትን፡ ትቶ፡ ወደ፡ ሌላ፡ መኼድ፤ በዝሙት፡ ሥራ፡ ማደፍ፡ መርከስ፤ ዘር፡ መዝራት፡ ማውጣት፡ ማፍሰስ፤ ዘመወን፡ እይ፤ የዚህ፡ መንቲያ፡ ነው።

**ዝንየት፤ዝኔት**፤ መዘሞት፤ ዝሙት፡ ዝና፤ የዝሙት፡ ሥራ። ዘር፡ እድፍ፡ ርስሐት። እመ፡ ቦ፡ ዘወድቀ፡ በዝንየት፡ ወበሕልም፡ ይትከላእ፡ እም ቍርባን፡ ኪያሃ፡ ዕለተ። እመ፡ ቦ፡ ዘወፅአ፡ ዝንየት፡ ወውእቱ፡ እንዘ፡ ንቁህ፡ ይትገሐሥ፡ እምቍርባን፡ ስድስተ፡ ዕለተ። ዝኔት፡ በኀሊና፡ ርኩስ። እመ፡ ቦ፡ ዘይትከዐዎ፡ ዝንየት፡ ለዝሉፉ፡ (ቄድር፡ ገ፸፡ ፸፯)። ወከዐዉ፡ ዝንየቶሙ፡ ዲቤሃ፡ (ሕዝ፳፫፡ ፰)።

**ዘኒም፤ ሞት፤ (ዘን(ነ)መ፡ ይዘንም፡ ይዝንም። ዕብ፡ ዛራም፤ ዜሬም)**፤ መዝነም፤ ከላይ፡ ከአየር፡ ከሰማይ፡ መውረድ፡ መፍሰስ፤ በኀይል፡ መረጨት፤ የውሃ፡ የእሳት፡ የበረድ፡ የመቅሠፍት። ዘ ነመ፡ በይእቲ፡ ሌሊት፡ ፀቢይ፡ ዝናም። ዘነመ፡ እሳት። ይዘንም፡ መዓግር፡ ላዕለ፡ ኃጥኣን። በረድ፡ ይዘንም፡ (ዮሴፍ። ሉቃ፲፯፡ ፳፱። መዝ፡ ፲። ፳፯)።

**አዝነመ**፤ አዘነመ፡ አወረደ፤ ረጨ፡ አፈሰሰ። አስደራጊነትም፡ አለበት። እኤዝዝ፡ ደመናተ፡ ከመ፡ ኢያዝንሙ፡ ላዕሌሃ። አዘዘ፡ ደመና፡ ወአዝነመ፡ መና። ኣዘንም፡ በረደ። ወአዝነመ፡ እግዚ፡ እሳተ፡ ወተየ፡ እምሰማይ፡ (ኢሳ፭፡ ፮። መዝ፡ ፸፯። ዘፀ፱፡ ፲፰። ዘፍ፲፱፡ ፳፬)።

**ዝናም፤ (ማት)**፤ በቊሙ፤ የውቅያኖስ፡ ውሃ፡ በደመና፡ ዐይበት፡ ተቋጥሮ፡ በነፋስ፡ ወደልጋዝ፡ ተጭኖ፡ ወደ፡ ላይ፡ ወዳየር፤ እየወጣ፡ ተመልሶ፡ ወደ፡ ባሕር፡ ወደ፡ የብስ፡ የሚረጭ፡ የሚፈስ፡ የሚነሰነስ። የዐቍር፡ ማየ፡ በከርሠ፡ ደመና፡ ወያወርድ፡ ዝ ናመ፡ እምከርሠ፡ ማሕፀና። በእንተ፡ ዝናማት፡ ከመ፡ ዝናም፡ ይፈኑ። ተዘከር፡ እግዚኦ፡ ርደተ፡ ዝናማት፡ (ቅዳ፡ ጎር። ጸዋት)።

**ዘናና፤ (ዘነ፡ ዘነነ፤ ዘንዘነ፤ ዘኒን፤ መውገጥ)**፤ ብስ፡ ክብ፡ እንክብል፡ ደንጊያ፤ በወይፈን፡ ግንባር፡ ላይ፡ የሚታሰር፡ መቅጫ። በደንጕራ፡ ዕንጨት፡ ላይ፡ የሚሰካ። በቊሙ፡ ዘነዘና፡ ራሳም፡ የሙገጫ፡ ግልገል። ለመርከብና፡ ላትሮንስም፡ መልሕቅ፡ ይነገ ራል፡ (አዋል)። ጐንደሮች፡ ግን፡ ውኻሞውን፡ ዘነ ዘና፡ ይሉታል። ኹሉም፡ ዐማርኛ፡ ነው።

**ዘኒፍ፤ (ዘነፈ፡ ይዘንፍ፡ ይዝንፍ)**፤ ማዘንፍ፤ የልብስ፡ የቃል፡ (ዐማርኛ)።

**ተዛነፈ**፤ በቊሙ፡ ተዛነፈ። (ግጥም፤ ስለ፡ ሳውልና፡ ስለ፡ ኬፋ፡ ሞት)፤ ጳውሎስ፡ ታርደ፡ በኔሮን፡ ሰይፍ፤ ኹለቱ፡ ዓመት፡ ፈርጅ፡ ሳይዛነፍ፤ ሰቅሎ፡ ለመ ግደል፡ በመጨረሻ፤ ወሰዱት፡ እንጂ፡ ከምሥራቅ፡ ዋሻ፤ ጴጥሮስን፡ ማርከ፡ ከባቢሎን፤ ሮም፡ እንድትከብር፡ እንድትገን።

**ዘኒቅ፤ (ዘነቀ፡ ይዘንቅ፡ ይዝንቅ። ዕብ፡ ዛኖቅ፤ ቀዲም፡ ቀኒጽ)**፤ መዘንቅ፡ ማዛ ነቅ፤ መቀየጥ። መገርንቅ፡ አብዝቶ፡ መጨመር፤ የግብር፡ የነገር። ዘንቅ፡ ማለት፡ ከዚህ፡ ወጥቷል። ግእዝ፡ ካማ ርኛ።

**ዝናር፤(ራት። ዐረ፡ ዙናር። ሱር፡ ዙ ናራ። ጽር፡ ዘናሪዎን)**፤ በቊሙ፤ መታጠቂያ፡ ዐጭር፡ የወገብ፡ ማሰሪያ፤ ወይም፡ ድግ። ሞጣሕት፤ ወርደ፡ ጠባብ፡ ቁመተ፡ ረዥም፡ እንደ፡ ድግ፡ ያለ፤ ዲያቆናት፡ የሚያጣፉት፡ የሚያወነዝፉት፡ በትከሻቸው፡ ላይ፡ የሚያደርጉት። ቀኒተ፡ ሐቌ፡ በዝናር፡ በከመ፡ ይቤ፡ እግዚእነ፤ ለይኩን፡ ሐቌክሙ፡ ቅኑተ። ኢይ ቅንቱ፡ ሐቌሆሙ፡ ዲያቆናት፡ በዝናር፡ በጊዜ፡ ጸ ሎት፤ እስመ፡ ግዑዛን፡ እሙንቱ። ከመ፡ ያዑድ፡ ዝናረ፡ ላዕለ፡ ክሣዱ፤ ወኢይግበር፡ ዝናረ፡ ላዕለ፡ አሐዱ፡ መትከፍቱ። ዝናራት፡ ዘውእቶሙ፡ ፊቃር፡ (ፍ፡ ነ፡ ፲፬። ፯፡ ፬። ፈ፡ መ፡ ፴፩፡ ፫፡ ፭)።

**ዝንቱ፤(ዝ፡ ንቱ)**፤ የቅርብ፡ ዐጸፋና፡ ቅ ጽል፤ ይህ፡ ይኸው፤ ይኸኛው። ን፡ በር፡ ከፋች፤ ቱ፡ አርቲክል፡ ነው፤ ዝን፡ ዙ፡ በማለት፡ ፈንታ፡ ዝንቱ፡ ይላል፡ እንጂ፡ ዐጭሩ፡ መልካሙ፡ ዙ፡ ነበረ፤ ዝኩ ንና፡ ዝክቱን፡ እይ፤ የዚህ፡ አንጻር፡ ነው። ዝንቱስ፡ ይፀርፍ፤ ዝንቱ፡ ምስለ፡ ዝንቱ፤ በእንተ፡ ዝንቱ፤ ዐ ጸፋ። ዝንቱ፡ ሕዝብ፤ ዝንቱ፡ ነዳይ፤ ዝንቱ፡ ይስማ ኤል፤ ቅጽል። ዘንተ፡ (ዘ)፡ ይህን፤ ይህነን፤ ይኸውን፡ ይኸኛውን። ዘንተ፡ አሕሠምከ፡ ወዘንተ፡ አሠነይከ፡ (ሳታት)።

**ዝዕላ፤(ዐረ፡ ዚር። ዕብ፡ ዜር)**፤ ዘርፍ፡ ጌጥ፡ ጐፍላ፤ አበባ፡ ዐጽቅ፡ ዛላ፤ በቆብ፡ በባርኔጣ፡ ላይ፡

ሠራ ፤ ዙሮ ፡ ተጠምጥሞ ፡ የሚገጥም ። ወሔቅ ፡ እ
መት ፤ ወእመት ፡ ርሕቡ ፡ እምሔቀ ፡ ምድር ፡
(ሕዝ፵፫ ፡ ፲፫ ፡ ፲፬) ።

**ሐይቅ ፤ (ቃት) ፤** ዙሪያ ፡ ዳርቻ ፡ ወደብ ፡
ጽንፍ ፤ የባሕር ፡ ጠረፍ ። ታናሽ ፡ መጠነኛ ፡ ባሕር ፡
ዙሪያው ፡ ዳርቻው ፡ የሚታይ ፤ በተራራ ፡ በየብስ ፡ የተከ
በበ ፤ እንደ ፡ ዚይ ፡ እንደ ፡ ሐይቅ ፡ እንደ ፡ ጣና ፡ ያለ ።
ሐይቀ ፡ ባሕር ። ኀበ ፡ ሐይቀ ፡ ባሕር ። መንገለ ፡
ሐይቀ ፡ ጌንሴሬጥ ። ድንጋግ ፡ ዘሐይቅ ፡ (መሳ፭ ፡
፲፯ ። ማቴ፲፭ ፡ ፳፱ ። ሉቃ፭ ፡ ፩ ። አርጋ ፡ ፪) ።

**ሔር ፤—ቸር ፡—ኄዩር ፡ ኄረ ፡ ኄር ።**

**ሐየሰ ፤—ተሻለ ፤—ኄዩስ ፡ ኄሰ ፡ ኀየሰ ።**

**ሐዩስ ፤ ሶት ፤ (ሔሰ ፤ ሐየሰ ፡ የሐይስ ፡
ይሒስ) ፤** መንቀፍ ፡ ማጸየፍ ፤ ማነወር ፡ መክሰስ ፤
መስደብ ፡ መቈጣት ። ኢትሒስ ፡ ዘእንበለ ፡ ትሕትት ።
ሶቤሃ ፡ የሐይስ ፡ ርእሶ ። ኢትሒሰኒ ፤ እስመ ፡ ኀሠ
ሥኩ ፡ ኣእምር ። ይሒስከ ፡ እግዚ ፡ (ሢራ፲፩ ፡ ፯ ።
ኢዮ፴፫ ፡ ፳፯ ። ጦቢ፭ ፡ ፲፬ ። ይሁ ፡ ፱) ።

**ሐያሲ ፤ (ሲት ፡ ስያን ፡ ያት ፤ የስት) ፤**
የሚነቅፍ ፡ ነቃፊ ፤ ከሳሽ ፡ ወቃሽ ።

**አሔሰ ፤ አሕየሰ ፤** አስነቀፈ ፤ አስነወረ ። ኢ
ታሒስ ፡ ርእሰከ ። ያሐይስ ፡ ርእሶ ፡ (ሢራ፴ ፡ ፴፩ ።
ምሳ፱ ፡ ፯) ።

**ተሐይሰ ፤** ተነቀፈ ፤ ተሰደበ ፡ ተነወረ ። ከመ ፡
ኢትትሐየስ ፡ አንተ ፡ በእበደ ፡ ዚኣሁ ። ከመ ፡ ኢት
ርፍቁ ፡ ለሖነኒ ፡ ወኢትትሐየሱ ፡ (ሢራ፳፪ ፡ ፲፫ ።
፩ቆሮ ፡ ፲፭ ፡ ፴፬) ።

**ተሓየሰ ፤** ተነቃቀፈ ፤ ተጣላ ፡ ተካሰሰ ። ኅ
ድጉ ፡ ለቢጽክሙ ፡ ዘተሓየስክምዎ ፡ እመ ፡ ቦ ፡
ዘተሓየሰ ፡ ምስለ ፡ ቢጹ ፡ ይኅድግ ፡ ሎቱ ፡ (ማር
፲፩ ፡ ፳፭ ። ቅዳ ። ቆላ፫ ፡ ፲፫) ።

**ሕዩስ ፤ (ሳን ፡ ሳት ፡ ይስት) ፤** የተነቀፈ ፡
የተነቃቀፈ ፤ ንቁፍ ፤ ስዱብ ፡ ነውረኛ ።

**ሒሰት ፤** መንቀፍ ፤ መነቀፍ ፡ አንቃቀፍ ፤ ነ
ቀፋ ፡ ነቀፌታ ፡ ስድብ ።

**ሒስ ፤** ነውር ፡ ገመና ፤ ኀጢአት ፡ በደል ፡ የሚ
ያስነቅፍ ፡ ነገር ፤ ነቀፋ ። ንጹሕ ፡ አንተ ፡ እምዝ ፡
ሒስ ፡ ዘኀቡኣት ። እንተ ፡ እንበለ ፡ ሒስ ። ዘአልቦ ፡
ነውር ፡ ወሒስ ። ሒስ ፡ ንስቲት ፡ (ሔኖ፳፭ ፡ ፲፭ ።
አስቴ፰ ፡ ፲፫ ። ጥበ፲ ፡ ፲፭ ። ፲፫ ፡ ፯) ።

**ሔት ፤ (ዕብራ) ፤** ስመ ፡ ፊደል ፡ ሳምን ፤
ሐውቾ ፡ ሐ ፤ ዘሩ ፡ ሐዬው ፤ ፍችው ፡ ሕይወት ። ሐው
ትና ፡ ሔት ፡ አንድ ፡ ስም ፡ ናቸው ። ሔት ፤ ክፍልየ ፡
እግዚ ፡ (መዝ ፡ ፻፲፰ ፡ ፶፯—፷፬ ። ሰቈ፩ ፡ ፰ ። ፪ ፡ ፰ ።
፫ ፡ ፳፱ ። ፬ ፡ ፰) ።

**ሐከየ ፤—ሰነፈ ፤—ሀክይ ፡ ሀከየ ።**

**ሐከከ ፤—ክርክር ፤—ሀኪክ ፡ ሀከከ ።**

**ሐኪክ ፤ ኮት ፤ (ሐከ ፤ ሐከከ ፡ የሐክክ ፡
ይሕክክ ። ዐረ ፡ ሐከ ። ዕብ ፡ ሐካኽ) ፤** ማከክ ፡
መፎከት ፡ ማቍሰል ፤ መላጥ ፡ መቅረፍ ፤ መፋቅ ፡ መ
ላግ ፤ መሞረድ ፡ መፈግፈግ ፤ የገላ ፡ የቈርበት ፡ የንጨት ፡
የብረት ። ነሥአ ፡ ገልዐ ፡ ወአኀዘ ፡ ይሕክክ ፡ ቍስሎ ።
ኀለቈ ፡ እንዘ ፡ አሐክክ ፡ ጸውበ ። (ኢዮ፪ ፡ ፰ ። ፯ ፡
፭) ። ዕከካም ፡ መኾን ፤ ዕከክ ፡ መልበስ ፤ በዕከክ ፡ ደዌ ፡
መያዝ ። ዘሐከከ ፡ አባሉ ፡ (መ ፡ ፈ) ።

**ሐካኪ ፤ (ኪት ፡ ክያን ፡ ያት ፤ ከክት) ፤**
የሚያክ ፡ የሚያቈስል ፤ ጥፍራም ፤ ዕከካም ። ራስን ፡
ባንበሳና ፡ በነምር ፡ መስሎ ፡ ዐካኪ ፡ ዘራፍ ፡ ማለት ፡
ከዚህ ፡ የወጣ ፡ ነው ፡ ይባላል ።

**ተሐከ ፤ ተሐከከ ፤** ታከከ ፡ ተፈገፈገ ፤ ተላገ ፡
ተሞረደ ።

**ሕኩክ ፤ (ካን ፡ ካት ፡ ክክት) ፤** የታከከ ።
ያከክ ፤ ዕከክ ፡ የወረሰው ።

**ሕከክ ፤** በቊሙ ፤ ዕከክ ፡ የገላ ፡ የቈበርት ፡
ደዌ ። በአበቅ ፡ እኩይ ፡ ወበሕከክ ፡ ዘአልቦ ፡ ፈውስ ፡
(ዘዳ፳፰ ፡ ፳፯) ።

**ሐኪም ፤ ሞት ፤ (ሐከመ ፡ የሐክም ፡
ይሕክም ። ዐረብ ። ዕብ ፡ ወሱር ፡ ሐካም) ፤**
ብልኅ ፡ መኾን ፡ መፈልሰፍ ፤ በውቀት ፡ ማደግ ፤ ጥበ
ብን ፡ ዕውቀትን ፡ ገንዘብ ፡ ማድረግ ። ዝም ፡ ዕክም ፡
ጸጥ ፡ ማለት ፤ አለመቀባጠር ። መጽሐፍ ፡ ግን ፡ በሐከመ ፡
ፈንታ ፡ ተሐከመ ፡ ይላል ፤ ስሕተት ፡ ነው ። በአርምሞ ፡
ወበተሐክሞ ፡ ይመስል ፡ ጠቢበ ፡ (ምሳ፲፯ ፡ ፳፰) ።
በቊሙ ፤ ማከም ፡ መፈወስ ፤ ድውይን ፡ መዳሰስ ፡ መዳበስ ፤
ማገም ፡ መብጣት ፡ መድኀኒት ፡ መስጠት ። ኬንን ፡ እይ ፤
የዚህ ፡ መንቲያ ፡ ነው ። ግስንቱ ፡ ዐጕልና ፡ ገቢር ፡ እንደ ፡
ኾነ ፡ ባፈታቱ ፡ አስተውል ።

**ሐኪም ፤ (ማን ፡ ማት ፡ ሐካም) ፤** ብልኅ ፡
ዐዋቂ ፡ ፈላስፋ ፤ ኬንያ ፡ ጥልቅ ፡ ረቂቅ ፡ ዕውቀት ፡ ያለው ።
ወስመ ፡ መምህሩ ፡ ዘመሀሮ ፡ ጥዐበ ፡ አርስጣጣሊስ ፡
ሐኪም ። ወሰመየት ፡ ስሞ ፡ እብነ ፡ ሐኪም ፡ (ዮሴፍ ።
ክብ ፡ ነገ) ። በቊሙ ፤ ፈዋሽ ፡ የሰውን ፡ ደዌ ፡ ከነስሙ ፡
ከነመድኀኒቱ ፡ በየስልቱ ፡ የሚያውቅ ፤ በሽተኞች ፡ እንደ ፡
ቄስ ፡ የሚሹት ።

**ሖል ፤-መከከለኛ ፤-ሐዊል ፡ ሐወለ ።**

**ሐላ ፤ ሐሊባ ፤—ድንኳን ፤—አሆላ ፡ አ
ሆሊባ ።**

**ሐሊብ ፤ ቦት ፤ (ሐለበ ፡ የሐልብ ፡ ይሕ
ልብ ። ዐረብ ። ዕብ ፡ ሐላብ) ፤** ማለብ ፤ ከእንስሳት ፡
ጡት ፡ ወተት ፡ ማውጣት ። ከመ ፡ ሐሊብ ፡ ሐለብከኒ ።
ሕልብ ፡ ሐሊበ ። የሐልቦሙ ፡ ለእንስሳ ፡ (ኢዮ፲ ፡ ፲ ።
ምሳ፳፱ ፡ ፳፰ ። ስንክ ፡ መስ፲፰) ። መስረቅ ፡ የሰውን ፡ ገ
ንዘብ ፡ እንደ ፡ ጡትና ፡ እንደ ፡ ወተት ፡ መሳብ ፤ ሳይታዩ ፡
መውሰድ ። ሌባ ፡ ማለት ፡ ከዚህ ፡ ወጥቷል ።

**ሐላቢ፤(ቢት፡ ብያን፡ ያት፤ ለብት)፤** የሚያልብ፡ ዐላቢ፤ ባለጥገት።

**ተሐልበ፤**ታለበ፤ ወተቱን፡ ሰጠ።

**ሕሉብ፤(ባን፡ ባት፡ ልብት)፤**የታለበ፡ ዕልብ፡ ወተት፤ ወይም፡ ጥገት፤ ጡት።

**ሐሊብ፤** ወተት፤ ነጭ፡ ፈሳሽ፡ ሴትንት፡ ካላቸው፡ ከሕያዋን፡ ፍጥረት፡ ከወላጆች፡ ጡት፡ የሚወጣ፡ የሕፃናት፡ የገላግልት፡ ምግብ። እስመ፡ ሥሉ፡ ዘይት ወጋዐ፡ ሐሊበ፡ ሕፃን፡ ውእቱ። ወኵኑ፡ ከመ፡ ሕፃናት፡ ወአፍቅሩ፡ ሐሊበ፡ ነባቤ። ሐሊበ፡ አልሕምት፡ ወአባግዐ፤(ዕብ፭፡ ፲፫። ፩ጴጥ፡ ፪፡ ፪። ገድ፡ ዘሚ)። በቤት፡ አንቀጽ፡ ከምትጠራ፡ ከምድር፡ የሚወጣም፡ ፍሬና፡ ማዕደን፡ ጥሩ፡ ነገር፡ ኹሉ፡ ሐሊብ፡ ይባላል፤ የምድር፡ ፀላባ፡ እንዲሉ። ወቦኡ፡ ምድረ፡ እንተ፡ ትውሕዝ፡ ሐሊበ፡ ወመዓረ፡(ሚራ፵፯፡ ፰)። ለዕፀዋትም፡ ይነገራል። ወያንጸፈጽፍ፡ ሐሊቦሙ፡ (ራእ፡ ባሮ)። ሐሊብ፡ ነባቢ፤ ያለውም፡ የወጣኒ፡ የሕፃናት፡ ትምርት፡ ምስጢረ፡ ሥላሴ፡ ይባላል። የሐሊብ፡ መሠረት፡ ምግብነት፡ ሲኾን፡ ፫፡ ግብር፡ አለው፤ ሕይወተ፡ ሕፃናት፡ ነው፤ ያሳድጋቸዋል፤ ኀይል፡ ይሰጣቸዋል፤ ትምርትም፡ ለነፍስ፡ ምግብነቱ፡ እንደ፡ ሐሊብ፡ ነው።

**ሕልበት፤** ማለብ፤ መታለብ፡ አስተላለብ። አፍንጫ፤ ያፍንጫ፡ ጕንጭ፡ ግራና፡ ቀኙ፤ ወይም፡ መክከሉ፡ ሹሉ፡ የሚሰነገው። ተአሰርኑ፡ ሎቱ፡ ሕልቀተ፡ ውስተ፡ ሕልበቱ፡ (ኢዮ፵፡ ፳፬)። በቁሙ፤ ዕልበት፡ አብሽ፤ ካብሽ፡ የሚሠራ፡ የጦም፡ ወጥ፡ (ዐማርኛ)።

**ማሕለብ፤(ብ፡ መሐልብ)፤**ማለቢያ፡ ቂጀ፤ የወተት፡ ዕቃ፡ መሣሪያ።

ማሕለብ፡

**ሐለደ፤—ጨረሰ፤—ኀልዶ፡ ኀለደ፡ ኀላዲ።**

(ጥ) **ሐለወ፤—ኖረ፤—ሀልዎ፡ ሀለወ።**

(ባ) **ሐለወ፤—ጠበቀ፤—ኀሊው፡ ኀለወ፡ ኀላዊ።**

**ሐለዚዝ፤(ዐረ፡ ሐለዞን)፤**ዛጕል፡ ልብሱ፤ ቀንዳም፡ ልጋጋም፡ ትል፤ እንደ፡ ሔለይ፡ ከዛጕሉ፡ ውስጥ፡ የሚከተት፤ ክረምት፡ ሲገባ፡ ደመና፡ ሲዞር፡ ባንድ፡ ቀን፡ ዝናም፡ የሚፈጠር፤ ነጮችና፡ ዐረቦች፡ ቀቅለው፡ አብስለው፡ እንዳሹቅና፡ እንደ፡ በቈልት፡ እንደ፡ ሽንብራ፡ እሸት፡ እየጠረጠሩ፡ የሚበሉት። ቀርነናእን፡ እይ፤ ከዚህ፡ ጋራ፡ አንድ፡ ነው። ባለቅኔዎች፡ ግን፡ ለውዝ፡ ይሉታል፤ ዘሩ፡ ለዚዝ፡ ነውና፡ ለዘን፡ እይ።

**ሐልዘዘ፤** አፈራ፤ ሐለዞን፡ ወለደ፤ ዝናቡ፡ ምድሩ።

(ጥ) **ሐለየ፤—ዐሰበ፤—ኀልዮ፡ ኀለየ፡ ኀሊና።**

**ሐልይ፤ዮት፤(ሐለየ፡ የሐሊ፡ ይሕሊ። ዐረ፡ ሐሊየ)፤** መለዘብ፡ መለስለስ፤ መላም፡ መጣም፡ መጣፈጥ፤ የግብር፡ የነገር። መዝፈን፡ ማመስገን፤ መቀኘት፡ መግጠም፤ መወረብ፡ ማለዘብ፤ኢያዚሙ፡ ምስጋና፡ ማቅረብ። ለዘብ፡ ማለት፡ ከዚሁ፡ የወጣ፡ ነው፤ የዜማውን፡ ጣዕም፡ ማማሩን፡ መቃብፎሩን፡ ያሳያል። አሐሊ፡ ማሕሌተ። ንሕሊ፡ ማሕሌተ፡ መንፈሳዊተ። ሕልዩ፡ ለእግዚ፡ በጸናጽል። ምሕረተ፡ ወፍትሐ፡ አሐሊ፡ ለከ። ሐሰያሁ፡ ወዘመራሁ። ኪያየ፡ የሐልዩ፡ እለ፡ ይሰትዩ፡ ወይነ፡ (ኢሳ፭፡ ፩። ፈ፡ መ፡ ፴፪፡ ፯። ዮዲ፲፮፡ ፩። መዝ፡ ፻። ሚራ፵፯፡ ፯። መዝ፡ ፷፰)።

—፤ መጕባት፤ ጕብ፡ መማለጃ፡ መስጠት። ምስጢሩ፡ ማለዘብ፡ ካለው፡ ይገባል፤ ያልበላ፡ ዳኛ፡ እውነት፡ ለመፍረድ፡ የማይፈራ፡ ክክራ፡ ሽካራ፡ ነውና። ወሐሰይኪዮሙ፡ ይምጽኡ፡ ኀቤኪ። ወመበሎ፡ ለፊልክስ፡ ዘይሁቦ፡ ጳውሎስ፡ ወየሐልዮ፡ ንዋየ፡ (ሕዝ፲፮፡ ፴፫። ግብ፳፬፡ ፳፮)።

**ሐላዪ፤(ዪት፡ ይያን፡ ያት፤ ለይት)፤** የሚዘፍን፡ ዘፋኝ፤ አመስጋኝ፡ ገጣሚ፤ ባለቅኔ፡ ባለዜማ። ወፀአ፡ ሐላይያት፡ ወተቀበላሁ። ሐሰይት፡ ወሐላይያን፡(፩ነገ፡ ፲፰፡ ፮። መክ፪፡ ፰)።

**መሕልይ፤መሕለዪ፤መሐልይ፤** ገኒ፡ ከማሁ፤ ዘፋኝ። መዝፈኛ፤ ጊዜ፡ መሣሪያ፡ ቦታ።

**ምሕላይ፤** መዝፈኛ፡ ቦታ፤ ቅኔ፡ ማሕሌት፡ የሰርግ፡ ቤት፤ የመሰለው፡ ኹሉ።

**ማሕሌት፤(ታት። አው፡ ማሕልይ፤ ብ፡ መሐልይ)፤** ዘፈን፡ ምስጋና፤ ወረብ፡ ለዘብ፤ ቅዳሴ፡ ውዳሴ፤ ቅኔ፡ ግጥም፤ ጕማ፡ ታመማ፡ የብዙ፡ ሰው፡ ዜማ። ማሕሌተ፡ አብድ። አዋልደ፡ ማሕሌት። አልቦ፡ ዘይክል፡ አእምሮታ፡ ለይእቲ፡ ማሕሌት፡ ዘእንበለ፡ እልክቱ። ያስምዕክሙ፡ ቃለ፡ መሰናቁት፡ ዘሕፃናት፡ ወማሕሌተ፡ ዘመላእክት። ተስእሉነ፡ ነገረ፡ ማሕሌት፡ ወይቤሉነ፡ ሕልዩ፡ ለነ፡ እማሕልዩሃ፡ ለጽዮን፤ እፎ፡ ነሐሊ፡ ማሕሌተ፡ እግዚ፡ በምድር፡ ነኪር። ማሕልየ፡ መሓልይ፡ ዘሰሎሞን፡ (መክ፯፡ ፭። ፲፪፡ ፬። ራእ፲፬፡ ፫። ቅዳ፡ ሕር። መዝ፡ ፻፴፮። ማሕ፡ ፩)።

**ማሕሌታዊ፤(ታይ)፤** የማሕሌት፡ ሰው፤ ደብተራ፡ አወዳሽ፤ መርቶ፡ የሚቀኝ፡ ራሱን፡ የቻለ። ድምጣም፡ ድምጠ፡ መልካም፤ ማሕሌት፡ የሚያሞቅ፡ የሚያደምቅ፤ መዝፈን፡ መቀንቀን፡ መወረብ፡ ማስረ

ገጥ ፡ ክበሮ ፡ መዝበጥ ፡ የሚያውቅ ። ማሕሌታይ ፡ ሚካኤል ፡ መዐርዒረ ፡ ዜማ ። ደሬድ ፡ ማሕሌታይ ፡ (ደራሲ ። ስንክ ፡ ግንቦ ። አፈ ፡ ተ፳፱) ።

**ተሐልየ ፤ ተሐለየ ፤** ተጉባ ፡ ተማለደ ፤ ጉብ ፡ ተቀበለ ። ወመኩንንኒ ፡ ይትሐለይ ፡ ሕልያነ ። ወብዙኅ ፡ ተሐልዮሙ ፡ እምኀበ ፡ ኢያሶን ፡ ወእምኀበ ፡ ቢጹ ፡ ኀደግዎሙ ፡ (ሰንክ ፡ ፫ ። ግብ፲፯ ፡ ፱) ።

**ሕልያን ፤ (ዐረ ፡ ሑልዋን ፤ በርጢል ። ዕብ ፡ ሾሐድ ። ሱር ፡ ሾሒዳ) ፤** መማለኛ ፡ ጉቦ ፤ ክፉ ፡ ስጦታ ፤ ለመጥፎ ፡ ዳኛና ፡ ላባይ ፡ ምስክር ፡ የሚሰጥ ። ያፈቅሩ ፡ ሕልያነ ። ይነሥኡ ፡ ሕልያነ ። እምኃ ፡ ወሕልያን ፡ ያዐውሮሙ ፡ ለጠቢባን ፡ (ኢሳ፩ ፡ ፳፫ ። ፩ ፡ ፳፫ ። ሢራ፳ ፡ ፳፱) ።

**ሔለይ ፤** በቁሙ ፤ ዔሊ ፡ ደንጊያ ፡ ልብሱ ። ልዝብ ፡ ልሙጽ ፤ ወይም ፡ ጨኺ ፡ ድምጠ ፡ ቀጭን ።



ሔለይ ፡

**ሔልዩ ፤ (ጽር ፡ ሒሊዉ) ፤** ፀሓይ ፤ ሥዕለ ፡ ፀሓይ ። ሀገረ ፡ ሔልዩ ፡ (ዘፍ፵፩ ፡ ፵፭ ። ሕዝ፴ ፡ ፲፯) ።

**ሐለከ ፤ (ትግሬ) ፤** ወደረ ፡ ሰንከለ ፤ ቀየደ ፡ ሸንከፈ ፤ የከብት ። በቁሙ ፤ ተላላክ ፡ ሕልከኛ ፡ ኹነ ፡ (ዐማርኛ) ።

**ሐለለ ፤ (ሐረረ) ፤** ዐረረ ፡ ከሰለ ፤ ተቃጠለ ። ዘሩ ፡ ሐሪር ፡ ነው ፤ ረ ፡ ሲሉ ፡ ለ ፡ የሚሉ ፡ ሰዎች ፡ የረ ፡ ጸያፎች ፡ ያገቡት ፡ ነው ። ትግሬ ፡ ግን ፡ ሐለለ ፡ ብሎ ፤ ደከመ ፡ ዛለ ፡ ጠወለገ ፡ ይላል ።

**አሕለለ ፤ (አሕረረ) ፤** አሳረረ ፤ አቃጠለ ። ፈነወ ፡ እሳተ ፡ ወአሕለሎን ፡ ለአዕፅምትየ ። ሶበ ፡ ለልብየ ፡ እሳተ ፡ ሐዘን ፡ አሕለሎ ። እትነ ፡ እሳት ፡ ኢያሕለላ ፡ (ሰቈ፩ ፡ ፲፫ ። ደራሲ ። ስንክ ፡ ሐምሌ፳) ።

**መሐልል ፤ ማሕልል ፤** የሚያሳርር ፡ የሚያቃጥል ። ሽቱ ፡ የሚያበጅ ፡ የሚያወጣ ፤ ቀማሚ ፡ አንጣሪ ፤ የሚያቀልጥ ፡ የሚያጣፍጥ ። ውእቱ ፡ ዘገብረ ፡ አፈዋተ ፡ ዕጣን ፡ በንጹሕ ፡ ግብረ ፡ መሐልል ፡ (ዘፀ፴፰ ፡ ፳፱) ። ሐረረን ፡ እይ ።

**ሕላል ፤—ሠርቀ ፡ ወርኅ ፤—ሀላል ።**

**ሐሊም ፤ ሞት ፤ (ሐለመ ፡ የሐልም ፡ ይሕልም ። ዕብ ፡ ወሱር ፡ ሐላም ። ዐረ ፡ ሐሉመ) ፤** ማለም ፤ በንቅልፍ ፡ ልብ ፡ ሕልም ፡ ራእይ ፡ ማየት ። ወደገመ ፡ ሐሊመ ። ሐለምኩ ፡ ሕልመ ፡ ወደንገፀት ፡ ነፍስየ ። ወሊቃውንቲክሙ ፡ ሕልመ ፡ የሐልሙ ። ለእመ ፡ ሐለመ ፡ ኢጲስቆጶስ ፡ አንስተ ፡ ኢይቅረብ ፡ (ዘፍ፴፯ ፡ ፭ ። ዳን፪ ፡ ፫ ። ዮኤ፪ ፡ ፳፰ ። ኪዳ) ። በሐለመ ፡ ፈንታ ፡ ተሐለመ ፡ ይባላል ፤ ስሕተት ፡ ነው ። ሐላምያን ፡ እለ ፡ ይትሔለሙ ፡ ለክሙ ፡ (ኤር ፴፱ ፡ ፯ ። ፴፯ ፡ ፰) ። መወፈር ፡ መግዘፍ ፡ ታላቅ ፡ መኾን ፤ መጽናት ፡ መበርታት ። ሕልመልሜሌክን ፡ ተመልከት ።

**ሐላሚ ፤ (ሚት ፡ ምያን ፡ ያት ፤ ለምት) ፤** በቁሙ ፤ የሚያልም ፤ ሕልም ፡ ራእይ ፡ የሚያይ ፤ ሕልማም ፡ ባለሕልም ። ነቢይ ፡ አው ፡ ሐላሚ ፡ ሕልም ። ይትኄፈሩ ፡ ሐላምያነ ፡ ሕልም ፡ (ዘዳ፲፫ ፡ ፩ ። ሚክ፫ ፡ ፯) ።

**አሕለመ ፤** አሳለመ ፤ ሕልም ፡ አሳየ ።

**ተሐልመ ፤** ታለመ ፤ በሕልም ፡ ታየ ።

**ሕልም ፤ (ማት ። ብ ፡ ሕለም ፡ አሕላም ፤ ማት) ፤** በቁሙ ፤ በንቅልፍ ፡ ውስጥ ፡ የሚታይ ፡ ነገር ፤ እንደ ፡ ትንቢት ፡ ያለ ። ሕልም ፡ ፪ ፡ ወገን ፡ ነው ፡ የነፍስ ፡ የሥጋ ፤ የነፍስ ፡ ሕልም ፡ ፍሬ ፡ ያለው ፡ ነው ፤ ትንቢት ፡ ራእይ ፡ ይባላል ፡ (ዘፍ፴፯ ፡ ፯ ። ሢ፩ ፡ ፩ ። ዳን፪ ፡ ፩) ። የሥጋ ፡ ሕልም ፡ ግን ፡ እንደ ፡ ምትሀት ፡ ኹኖ ፡ ቅዠት ፡ ይባላል ፤ ከንቱ ፡ ማለት ፡ ነው ፤ ለኹሉም ፡ ክፉና ፡ በጎ ፡ አለው ፤ ሳሕስሐን ፡ እይ ። ወሕልምኒ ፡ ከንቱ ፡ ያደነግፆ ፡ ለአብድ ። እስመ ፡ ለብዙኃን ፡ አስሐቶሙ ፡ ሕልም ። ሕልም ፡ ዘዘሙት ። አሕላም ፡ እኩያት ። አሕላማት ፡ ሕሡማት ፡ (ሢራ፴፩ ፡ ፩ ፡ ፯ ። ፈ ፡ መ ፡ ፲፬ ፡ ፰ ። አፈ ፡ ድ፳፱ ። ፊልክ ፡ ፻፰) ።

**ሕልመልሜሌክ ፤** ስመ ፡ ኮከብ ፡ ዐቢይ ፡ መጋቤ ፡ ሐጋይ ፤ ካራቱ ፡ ዐበይት ፡ ከዋክብት ፡ አንዱ ። ዘይቤው ፡ ሕልመ ፡ ንጉሥ ፡ ማለት ፡ ይመስላል ፤ ምስጢሩ ፡ ግን ፡ ታላቅንት ፡ ነው ። ፪ኛ ፡ ስሙ ፡ ፀሓይ ፡ ይባላል ፤ ምግብናውም ፡ ፺፩ ፡ ቀን ፡ ነው ፡ (ሔኖ ፡ ፹፱) ።

**ሐለፈ ፤—ዐለፈ ፤—ኀሊፍ ፡ ኀለፈ ።**

**ሐለፈ ፤ (ዐረብ) ፤** ማለ ፡ ተረገመ ፤ ተገዘተ ።

**ተሓለፈ ፤** ተማማለ ፤ ተካየደ ።

**ትሕላፍ ፤** መሓላ ፤ ቃል ፡ ኪዳን ። አልቦሙ ፡ ትሕላፍ ፡ ምስለ ፡ ሶርያ ፡ (መሳ፲፰ ፡ ፯) ።

**ሐለጸ ፤ (ዕብ ፡ ሐላጽ) ፤** መዘዘ ፡ አወጣ ፡ ከወገቡ ፤ የሰይፍ ፡ የዘር ፡ የአባለ ፡ ዘር ። ዐለጠ ፤ ዐልጫ ፡ ኾነ ።

**ሕልጽ ፤** ወገብ ፤ የትጥቅ ፡ ሙያ ፤ ከጭን ፡ ማውድና ፡ ከባላው ፡ በላይ ፡ ከጐድንና ፡ ከሕንብርት ፡ በታች ፡ መካከሉ ። ሐቋን ፡ እይ ፤ ከዚህ ፡ ጋራ ፡ አንድ ፡ ነው ፤ ባለቅኔዎች ፡ ግን ፡ ለይተው ፡ ኅምስ ፡ ኃምሳይ ፡ ሕዋስ ፡ ኅፍረተ ፡ ብእሲት ፡ ይሉታል ። እመኒ ፡ ተኀብአ ፡ ማእከለ ፡ አቍያጽ ፤ እምተረግዘ ፡ ኢያምሠጠ ፡ ሕልጽ ፡ (ቅኔ) ።

**ሐልቀ ፤—ዐለቀ ፤—ኀሊቅ ፡ ኀልቀ ።**

**ሐሊቅ ፤ ቆት ፤ (ሐለቀ ፡ የሐልቅ ፡ ይሕልቅ ። ዐረ ፡ ሐለቀ) ፤** መዞር ፡ መከበብ ፤ ዙሪያ ፡

ክብ ፡ ማድረግ ። ወይም ፡ መከበብ ፤ ክቡብ ፡ ክበባም ፡ መኾን ፤ የሥራ ።

**ሕልቅ**፤(ብ ፡ አሕላቅ)፤ ጕንጭ፤መንጋጋ፡ ከንመላሱ ፡ ወይም ፡ ከንራሱ ፤ ከናናቱ ፡ ከንጭንቅላቱ ። ዘይሁብዎ ፡ ለካህን ፡ መዝራዕተ ፡ ወሕልቀ ፡ (ዘዳ፲፰ ፡ ፫) ። ጕረሮ ፤ ክበብ ፡ ክርክር ፡ ያለው ፡ ውስጠ ፡ ክፍት ፤ መዋጫውና ፡ መስልቀጫው ።

**ሕልቀት**፤(ቃት)፤ ቀለበት ፤ የጣት ፡ ጌጥ ፤ ሌጣ ፡ ሰንኬቶ ፡ ወይም ፡ ፈርጥና ፡ ማኅተም ፡ ያለው ። ሕልቀትየ ፡ ዘአጽባዕትየ ። ሕልቀተ ፡ ወርቅ ፡ ውስተ ፡ አዒብዒሃ ። አውፅአ ፡ ንጉሥ ፡ ሕልቀት ። ሕልቀተ ፡ ማዕተብ ፡ (ኩፋ ፡ ፵፩ ። ገድ ፡ ተክ ። አስቴ፫ ፡ ፪ ። ሚራ ፵፱ ፡ ፲፩) ። ያፍጫ ፡ ስናግ ፡ የብረት ፡ ቀለበት ፤ እንደ ፡ ሰዓት ፡ ፍንጅ ፡ የሚከፈትና ፡ የሚዘጋ ። ሕልበትን ፡ እይ ።



ሕልቀት ፡

**ሕላቅ**፤(ቃት)፤ምዕማድ፤የዐምድ ፡ እግር፤ ዐምድ ፡ የሚቆምበት ፡ ስክትት ፡ መሠረት ፤ የዐምዱን ፡ ሥር ፡ ለመንከስ ፡ ለመጕረሥ ፡ አፉ ፡ እንደ ፡ ቀለበት ፡ ክብ ፡ የኾነ ። ዲበ ፡ ምንት ፡ ስቁል ፡ ሕላቃቲሃ ፡ (ኢዮ ፴፰ ፡ ፯ ። ቅዳ ፡ ኤጲ) ።

**መሐልቅ**፤ ክብ ፡ ሥራ ፤ ምእዙን ፡ ምላላ ፡ ያይደለ፤እንደ ፡ ሰፌድ ፡ እንደ ፡ ምጣድ ፡ ያለ ። ሀሎ ፡ በአዘስም ፡ ሥዕለ ፡ ምትረተ ፡ ርእሱ ፡ ለዮሐንስ ፡ መጥምቅ ፡ ሥዑለ ፡ በመሐልቀ ፡ ብርት ፡ (ታሪ ፡ አዙ) ። በቁሙ ፤ ግርሽ ፡ የብር ፡ ገንዘብ ፡ ክብነት ፡ ያላት ፤ ዐይነቷ ፡ የብር ፡ መጠኗ ፡ የዝሩር ። በጎርም ፡ ኀ ፡ ሲጣፍ ፡ ግን ፤ መኀልቅ ፡ ማለት ፡ ታናሽ ፡ ክፍል ፡ የብር ፡ ካያኛ ፡ ማለት ፡ ነው ፤ ማነሷንና ፡ መከፈሏን ፡ እንኳ ፡ ክብነቷን ፡ አይሻም ።

**ሕልቅ**፤(ጽር ፡ ፆልኪ ። ዕብ ፡ ቤቃዕ) ። ድሪም ፤ የዲድርክም ፡ አላድ ፡ ወይም ፡ የሰቅል ፡ እኩሌታ ። ዲናርን ፡ ድርህምን ፡ ድርክሜን ፡ እይ ፤ ከዚህ ፡ ጋራ ፡ አንድ ፡ ነው ፤ ባለብሉዮች ፡ ግን ፡ ወቂት ፡ ይሉታል ። ነሥአ ፡ አዕኑገ ፡ ዘወርቅ ፡ ዘዘ ፡ ሕልቅ ፡ ድልወቱ ፤ ወአውቃፈ ፡ ዘዘ ፡ ዐሥሩ ፡ ሕልቅ ፡ ድልወቱ ፡ (ዘፍ፳፬ ፡ ፳፪) ።

**ሐለቅ**፤(ትግሬ)፤ የደም ፡ ሥር ፡ በሽታ ፤ እንደ ፡ ጨብጥና ፡ እንደ ፡ ቂጥኝ ፡ ደም ፡ የሚያበላሽ ።

**ሐለስ**፤—ዐጻ፤—ዐለስ ።

**ሐለስት**፤ ሐለስትዮ፤(ታት ። ዕብ ፡ ሐላሹት ። ዐረ ፡ ኀሊስ)፤ ክልስ፤ቅልቅል ፡ ድብልቅ፤ ነጭና ፡ ጥቍር ፡ ዝንጕርጕር ፤ ንጣቱን ፡ ጥቍረት ፡ ጥቍረቱን ፡ ንጣት ፡ የተቀላቀለው ፤ ዘሩና ፡ ጠጕሩ ፡ ነጭ ፡ ብቻ ፡ ወይም ፡ ጥቍር ፡ ብቻ ፡ ያይደለ ፤ ዲቃላ ፤ ጠጣ ፡ ነጩ ፡ ዝንጀር ፤ የበዳ ፡ አህያ ። ቦኑ ፡ ለከንቱ ፡ ይነቀ ፡ ሐለስትዮ ፡ (ኢዮ፮ ፡ ፩ ። ዳንኤ ፡ ፳፩ ። መዝ ፡ ፻፫) ።



ሐለስትዮ ፡

**ሕለት**፤—ዘንግ፤—ኀሊል ፡ ኀለለ ።

**ሐሙኢዳ**፤—ቀጠሮ፤—ሀሙኢዳ ።

**ሐሚግ**፤(ሐመገ ፡ የሐምግ ፡ ይሕምግ ። ሐመቀ)፤ ማመግ፤ ማጥፋት ፡ ማበላሸት ፡ የምግብ ። ማደፍረስ ፡ መበጥበጥ ፤ የውሃ ፡ የመጠጥ ። ማይ ፡ ዘሐመግሙ ፡ በእገሪክሙ ። ፈለገ ፡ ዘሐመግሙ ፡ በደመ ፡ ቅቱላን ። እንዘ ፡ የሐምጉ ፡ ማያተ ፡ ብዙኀ ፡ (ሕዝ፴፪ ፡ ፲፱ ። ጥበ፲፩ ፡ ፯ ። ዕንባ ፡ ፲፭) ። ማፍዘዝ ፡ ማደንገዝ ፤ ማቦዝ ፡ ማብለዝ ፤ ማድከም ፤ የዐይን ። ምስጢሩ ፡ ጽርየት ፡ ማሳጣት ፡ ነውና ፤ ማደፍረስ ፡ ካለው ፡ ይገባል ።

**አሕመገ**፤ አሳመገ ፤ አስደፈረሰ ፡ አስፈዘዘ ።

**ተሐምገ**፤ ታመገ ፤ ተበላሸ ፤ ደፈረሰ ፡ ፈዘዘ ። አልቦ ፡ ተሐምገ ፡ ውስተ ፡ ጽርየታ ። ተሐምጉ ፡ ማያቲሆሙ ። ረሥአ ፡ ወተሐምጋ ፡ አዕይንቲሁ ፡ ወኢይሬኢ ፡ (አፈ ፡ ተ፳፫ ። መዝ ፡ ፵፩ ። ዘፍ፳፯ ፡ ፩ ። ፩ነገ ፡ ፬ ፡ ፲፭) ።

**ሕሙግ**፤(ጋን ፡ ጋት ፡ ምግት)፤ የታመገ ፡ ዕምግ፤ ክፉ ፡ ጥፉ ፡ ብልሹ ፤ ድፍርስ ። ማይ ፡ ሕሙግ ። ወይን ፡ ሕሙግ ፤ መብልዐ ፡ ሕሙግ ፡ የሐምግ ፡ ልብ ፡ (ኤር፪ ፡ ፲፰ ። ፈላስ ፡ ገ፲፫) ።

**ሕምገት**፤ማመግ ፡ መታመግ ፤ መደፍረስ ፡ አደፈራረስ ፤ ድፍረሳ ፡ ድፍርስነት ፡ (ሄርማ ፡ ገ፶፩) ።

**ሕመግ**፤ እድፍ ፤ ጭቅቅት ፡ ንጢአት ፤ የአእምሮ ፡ ዝገት ፤ ድንቍርና ። ንጹሕ ፡ ውእቱ ፡ ወአልቦ ፡ ውስቴቱ ፡ ሕመግ ፡ (አፈ ፡ ድ፴፬) ።

**ሐሚድ**፤ዶት፤(ሐመደ ፡ የሐምድ ፡ ይሕምድ ። ዐረ ፡ ወትግ ፡ ሐምደ፤ገነየ)፤ ማመድ ፡ መብላት ፤ ማቃጠል ፡ ማመት ፤ ሐመድ ፡ ሕመት ፡ ማድረግ ፤ የእሳት ፡ የመብራት ፡ የኖራ ፡ የንጨት ። መቍረጥ ፡ መጕመድ ፡ መጕማመድ ፤ የስለት ። ገመደን ፡ እይ ፤ የዚህ ፡ ጎር ፡ ነው ። ይውዒ ፡ ይትሐመድ ፡ በማለት ፡ ፈንታ ፡ የሐምድ ፡ ይላል ፡ ስሕተት ፡ ነው ፡ (ሕዝ፲፭ ፡ ፬) ።

**አሕመደ**፤አሳመደ ፤ አስበላ ፡ አስጠፋ ።

**ተሐምደ** ፤ ታመደ ፤ ተበላ ፡ ጠፋ ፤ ሐመድ ፡ ኾነ ። በማያት ፡ ይጠበለሉ ፡ ወምድር ፡ ትትሐመድ ፡ (ኪዳ) ።

**ሕሙድ** ፤ (ዳን ፡ ዳት ፡ ምድ) ፤ የታመደ ፤ የተበላ ፡ የተቃጠለ ፤ ሐመድ ፡ የኾነ ፡ (መጽ ፡ ምስ) ።

—፤ ዐሜዳ ፡ አፍንጫ ፡ ጐራዳ ፤ ዝንጀሮ ፡ ፊት ፤ ቍርፋድ ።

**ሐመድ** ፤ በቁሙ ፤ ዐመድ ፡ የእሳት ፡ ብላቶ ፡ ንጭ ፡ ትቢያ ። የሣር ፡ የገለባ ፡ ሲኾን ፡ ስለ ፡ ጥቍረቱ ፡ ጠለስ ፡ ይባላል ። አውዐየ ፡ ለሀገር ፡ ወኮነት ፡ ሐመደ ። ጠፍኡ ፡ ከመ ፡ ሐመደ ፡ ሠዐ ። መሬት ፡ ወሐመድ ፡ (ኢያ፷ ፡ ፳፫ ። ኢሳ፵፫ ፡ ፲፯ ። ዘፍ፲፰ ፡ ፳፯) ።

—፤ ደቃቅ ፡ ክሰል ፤ ጥላት ፡ ጥቀርሻ ። ሐመደ ፡ እቶን ፡ (ዘፀ፱ ፡ ፰) ።

—፤ ዐቧራ ፡ ትቢያ ፤ ደቃቅ ፡ ዐፈር ። ወደዩ ፡ ሐመደ ፡ ዲበ ፡ ርእሶሙ ። ሐመደ ፡ ይቀምሑ ፡ (ኢዮ፪ ፡ ፲፪ ። መዝ ፡ ፻፩) ። ማናቸውም ፡ ደቃቅ ፡ ነገር ፡ ኹሉ ፡ ሐመድ ፡ ይባላል ፤ ደቂቅ ፡ ማለት ፡ ነው ። ሐመደ ፡ እብን ፤ ኖራ ፡ በረቅ ፡ ጠመኔ ።

**ሐመዳዊ** ፤ (ዊት ፡ ውያን ፡ ያት) ፤ ዐመዳም ፤ ዐመድማ ፡ ቡላ ፡ ዐፈርቻ ፤ ዐይነቱ ፡ ሕብሩ ፡ ሐመድ ፡ የሚመስል ። አፍራስ ፡ ሐመዳውያን ፡ (ዘካ፮ ፡ ፫) ።

**ሐመዳ** ፤ ዐመዳይ ፤ ብትን ፡ ውርጭ ፤ ዐመድማ ፡ ንጭ ፤ ከውሃ ፡ ላይ ፡ ሲያርፍ ፡ የሚረጋ ፤ ዋግ ፡ እየኾነ ፡ እኽል ፡ የሚያበላሽ ። የስሙ ፡ ምስጢር ፡ ፪ ፡ ነው ፤ ንጣትና ፡ አጥፊነት ። አስሐትያን ፡ እይ ፤ ከዚህ ፡ ጋራ ፡ አንድ ፡ ነው ። ቍር ፡ ወበረድ ፡ ወአስሐትያ ፡ ወሐመዳ ። እምአይቴ ፡ ይወፅእ ፡ ሐመዳ ፤ ወመኑ ፡ ይወልዶ ፡ ለሐመዳ ፡ ሰማይ ፡ (ሔኖ፴፱ ፡ ፪ ። ኢዮ፴፰ ፡ ፳፱ ፡ ፳፱) ። ለብትን ፡ በረዶም ፡ ይነገራል ፡ (፩ዜና ፡ ፲፩ ፡ ፳፪) ።

**ሐመድማድ** ፤ ዐመደ ፤ ዐመድማደ ፤ ዐመድማ ፡ ቅጠል ፡ ዐመድ ፡ የነፋበት ፡ የሚመስል ።

**ሐሚው** ፤ ዎት ፤ (ሐመወ ፡ የሐሙ ፡ ይሕሙ) ፤ ማመት ፡ ማመኽ ፤ መታመት ፡ መታመኽ ፡ ዐማት ፡ ዐማች ፡ ማድረግ ፤ ወይም ፡ መኾን ። መምረር ፡ መጐፍነን ፤ ሐሞት ፡ መኾን ፡ ወደ ፡ ሐሞት ፡ ጠባይ ፡ መለወጥ ፤ የምግብ ። ክፉ ፡ ጋብቻንም ፡ ያሳያል ።

**ተሓመወ** ፤ ተማመቸ ፤ ዐማችና ፡ ዐማት ፡ ተኳኳነ ፤ ተጋባ ፡ ተዛመደ ። ምንት ፡ አነ ፡ ከመ ፡ እትሓመዎ ፡ ለንጉሥ ። እስመ ፡ ተሓመውነ ፡ ምስለ ፡ አሕዛብ ። ኢትትሓመውዎሙ ። እምእለ ፡ ይትሓመዉነ ፡ ውእቱ ፡ (፩ነገ ፡ ፲፰ ፡ ፲፰ ። ዕዝ፱ ፡ ፲፬ ። ዘዳ፯ ፡ ፫ ። ሩት፪ ፡ ፳) ።

**አስተሓመወ** ፤ አስተማመቸ ፤ አስተማጨ ፤ አዛመደ ።

**መስተሓምው** ፤ (ውት ፡ ዋን ፡ ዋት) ፤ አማጭ ፤ አስተማጭ ። (ተረት) ፡ አማጭን ፡ መጦር ፤ አማጭን ፡ በጦር ። የባል ፡ ወንድም ፤ ዘመዱ ፡ ጐማው ፤ ርሱ ፡ ሲሞት ፡ ሚስቱን ፡ የሚወርስ ፤ የሚያገባ ። ክድነኒ ፡ ዐጽፊከ ፤ እስመ ፡ መስተሓምው ፡ አንተ ፡ (ሩት፫ ፡ ፱ ። ፲፩ ፡ ፲፪ ። ፬ ፡ ፩—፰) ። መስተሓምው ፡ ከማለት ፡ ይልቅ ፤ ወራሲ ፡ መውርስ ፡ ቢል ፡ በቀና ።

**ታሕማ** ፤ (ማት) ፤ ዐምቻ ፡ ጋብቻ ፤ ዐማችነት ። ገብረ ፡ ታሕማ ፡ ምስለ ፡ ነገሥተ ፡ አሕዛብ ፡ (አርጋ ፡ ፩) ። ዐማች ፤ የቤት ፡ ልጅ ፡ ባል ። ወይቤልዎ ፡ ለሎጥ ፡ ብከኑ ፡ ታሕማ ፡ በዝየ ። ወወፅአ ፡ ኀበ ፡ ታሕማቲሁ ፡ (ዘፍ፲፱ ፡ ፲፪ ፡ ፲፬) ።

—፤ ዐማት ፤ የባል ፡ ወይም ፡ የሚስት ፡ አባት ፡ እናት ። አክብሪ ፡ ታሕማኪ ። ወቀበሮሙ ፡ በክብር ፡ ለታሕማቲሁ ፡ (ጦቢ፲ ፡ ፲፪ ። ፲፬ ፡ ፲፫) ።

**ሐም** ፤ **ሐማ** ፤ **ሐምው** ፤ (ብ ፡ ሐማን ፤ አሕማው) ፤ ወንድ ፡ ዐማት ። ሐመ ፡ ሙሴ ። እስመ ፡ ሐሙሁ ፡ ለቀያፋ ። አዝማዲሁ ፡ ወእምዝ ፡ ሐማን ፡ (ዘፀ፲፰ ፡ ፲፪ ። ዮሐ፲፰ ፡ ፲፫ ። ፍ ፡ ነ ፡ ፳፯) ።

—፤ ዐማች ። እመሰ ፡ ጸባእክሙነ ፡ ትጸብኡ ፡ ውሉደክሙ ፡ ወአሕማወክሙ ፡ (ዮሴፍ ።

**ሐማት** ፤ (ብ ፡ አሕማት) ፤ ሴት ፡ ዐማት ። ረከባ ፡ ለሐማተ ፡ ጴጥሮስ ፡ (ማቴ፰ ፡ ፲፬) ። መርዓት ፡ በማለት ፡ ፈንታ ፡ ሐማት ፡ ይላል ፤ ስሕተት ፡ ነው ። ዘይገብር ፡ ከመ ፡ ዝ ፡ ወይሰክብ ፡ ምስለ ፡ ሐማቱ ፡ ያውዕይዎ ፡ በእሳት ፡ (ኩፋ ፡ ፵፩) ።

**ሐሞት** ፤ (ብ ፡ ሐማውት) ፤ በቁሙ ፤ መራራ ፡ ፈሳሽ ፡ በፍጥረት ፡ ኹሉ ፡ ሆድ ፡ ከጕበት ፡ ጋራ ፡ እንደ ፡ ሽንት ፡ ውሃ ፡ በታናሽ ፡ ፊኛ ፡ ታቍሮ ፡ የሚገኝ ፤ ዐይነቱ ፡ የዘይት ፤ ምሬቱ ፡ የሬት ፤ ሲበዛ ፡ ደዌ ፡ የሚኾን ፤ የሚያሰክር ፡ ራስ ፡ የሚያዞር ። የምረርን ፡ ፍች ፡ እይ ፤ ከዚህ ፡ ጋራ ፡ አንድ ፡ ነው ። ተክዕወት ፡ ውስተ ፡ ምድር ፡ ሐሞትየ ። ምንት ፡ ውእቱ ፡ ልቡ ፡ ወከብዱ ፡ ወሐሞቱ ፡ ለዝ ፡ ዓሣ ። ወሀብዎ ፡ ይስተይ ፡ ወይነ ፡ ወሐሞተ ፡ ድሙረ ፡ (ኢዮ፲፮ ፡ ፲፫ ። ጦቢ፮ ፡ ፯ ። ማቴ፳፯ ፡ ፴፬) ። ሬትና ፡ ከርቤ ፡ ሌላውም ፡ ኹሉ ፡ ከዚህ ፡ ስም ፡ ንሥቶ ፡ ሐሞት ፡ ይባላል ፤ መራራ ፡ ማለት ፡ ነው ። ወደዩ ፡ ሐሞተ ፡ ውስተ ፡ መብልዕየ ፡ (መራራ ፡ ቅጠል) ። ምንት ፡ ይመርር ፡ እምሐሞት ፡ (ሬት ፤ የሬት ፡ ወገን) ። (መዝ ፡ ፷፰ ። ምሳ፭ ፡ ፬) ።

**ሐሚዝ** ፤ ዘት ፤ (ሐመዘ ፡ የሐምዝ ፡ ይሕምዝ ። ዐረ ፡ ሐሚፀ ። ሱር ፡ ሕማጽ ። ዕብ ፡ ሐማጽ) ፤ መሖምጠጥ ፤ መስንፈጥ ፤ መቡካት ፡ መበላሸት ። መምረር ፡ መጐምዘዝ ፤ መጐፍነን ። መርዘኛ ፡ መርዛም ፡ መኾን ፡ በመርዝ ፡ መግደል ። መጥላት ፡ መመረዝ ፤ ቂም ፡ በቀል ፡ መያዝ ። መቈጣት ፡ መወገሸት ፤ እንደ ፡ መርዝ ፡ ኹኖ ፡ ሰው ፡ እስከ ፡ መግደል ፡ እስከ ፡ ማጥፋት ። ሐመወና ፡ መፀ ፡ የዚህ ፡ ጎር ፡ ናቸው ፤ ባንዳንድ ፡ ወገን ፡ ይመሳሰላሉ ።

**ሕምዝ** ፤ (ዛት) ፤ መርዝ ፤ የተቀመመ ፡ መድኀኒት ፡ የሚገድል ፡ የሚያድን ። ከእንስሳትና ፡ ከአራዊት ፡

ከተሐዋስያን ፤ ከዕፀው ፡ ከአሥራው ፡ ከማር ፡ ከቅጠል ፤ ከቋያና ፡ ከቡቃያ ፡ ወገን ፡ ከማግሰኛ ፡ ፍጥረት ፡ የሚገኝ ፤ መራራ ፡ ሖምጣጣ ፡ ጐምዛዛ ። ዘከመ ፡ እንስሳት ፡ እለ ፡ ቦሙ ፡ ሕምዝ ፤ ወዘከመ ፡ አራዊት ፡ መሣጥያን ፡ እለ ፡ ይሴሰዩ ፡ ሕምዛተ ። ወበቍላትኒ ፡ ቀታልያን ፡ እለ ፡ ያማስንዎ ፡ ለልብ ፡ ወለሥሉ ፡ ዘሥጋ ፡ በበሊያቱ ። ወላዕለ ፡ ዝንቱ ፡ ፍትሕ ፤ እመ ፡ ተረክበ ፡ እምነ ፡ ዝንቱ ፡ ክፍል ፡ አሐዱ ፡ ጾታ ፡ ዘያማስን ፡ ጥዑየ ፡ ወዘይፈውስ ፡ ድዉየ ፤ ይትገሐሥ ፡ ጥዑይ ፡ እምበሊያቱ ፤ ወለድዉይሰ ፡ ብዉሕ ፡ ከመ ፡ ይብላዕ ፡ እመንገለ ፡ ጾታ ፡ መድኃኒት ፡ (ፍ ፡ ነ ፡ ፳፫) ።

—፤ ቍጣ ፡ መዐት ፤ ክሕደት ፡ ኀጢአት ። ዐቢይ ፡ ሕምዙ ። መሠረታተ ፡ ሕምዝ ፡ (ራእ፲፪ ፡ ፲፪ ። ቅዳ ፡ ዲዮ) ።

—፤ መራራ ፡ ሸካራ ፡ ክፉ ፡ ነገር ፤ ሰው ፡ የሚጐዳ ፡ ቃል ። ሕምዘ ፡ አርዌ ፡ ምድር ፡ ታሕተ ፡ ከናፍሪሆሙ ፡ (መዝ ፡ ፻፴፱) ። መሪር ፤ ሐሞት ፤ ዕጕሥታር ፡ በማለት ፡ ፈንታ ፡ ሕምዝ ፡ ይላል ፤ መራራ ፡ ክፉ ፡ ማለት ፡ ነው ። እግዚ ፡ አስተየኒ ፡ ማየ ፡ ሕምዝ ። አጽገበኒ ፡ ሕምዘ ። ምረተ ፡ ሕምዝየ ፡ (ኤር፰ ፡ ፲፬ ። ሰቈ፫ ፡ ፲፭ ፡ ፲፱ ። ዘዳ፴፪ ፡ ፲፯) ። ባወራረድና ፡ ባንጻር ፡ አፈታት ፡ ባለብሉዮች ፡ ስራዊት ፤ ባለቅዳሴዎች ፡ ምድር ፡ ይሉታል ።

ሐምሐም ፤—ቅል ፤—ሐመመ ።

(ጥ) ሐመየ ፤—አሰረ ፤—ኀምዮ ፡ ኀመየ ።

ሐምይ ፤ ዮት ፤ (ሐመየ ፡ የሐሚ ፡ ይሕሚ ። ሱር ፡ ሐነየ) ፤ ማማት ፡ መበዝበዝ ፤ መንቀፍ ፡ መስደብ ፤ ሰውን ፡ በኋላው ፡ በክፉ ፡ ማንሣት ፤ በላዩ ፡ ክፉ ፡ ቃል ፡ መናገር ። ሐመይዎ ፡ ለሙሴ ። ሐመዩኒ ፡ በሐሰት ። ዘየሐሚ ፡ ቢጾ ፡ በጽሚት ። ዘየሐሚ ፡ አባሁ ። ሐመይክሙ ፡ ዐቢያተ ፡ ወድፉካተ ፡ ቃላተ ፡ ላዕለ ፡ ዕበዩ ። (ዘኍ፲፪ ፡ ፩ ። ሆሴ፯ ፡ ፲፫ ። መዝ ፡ ፻ ። ምሳ፳ ፡ ፳ ። ሔኖ፭ ፡ ፬) ። ሐመወ ፡ ሐመዘ ፡ ሐመመ ፡ ሐመየ ፡ እሊህ ፡ ፬ቱ ፡ ዘመዳሞች ፡ ናቸው ።

ሐማዪ ፤ (ዪት ፡ ይያን ፡ ያት ፤ መይት) ፤ የሚያማ ፡ (ዐሚ) ፡ ሐሜተኛ ፡ ሐሚና ፤ ሰዳቢ ፡ ነቃፊ ፤ ለፋፊ ፡ ለፍላፊ ። ሰብእሰ ፡ ሐማዩ ፡ በላዒ ፡ ሥጋ ፡ ወሰታዩ ፡ ደም ። ኢትኩን ፡ ሐማዩ ። ኢይኩና ፡ ሐማይያተ ። ወይከውኑ ፡ ሐመይት ፡ ወሐማይያን ፡ ብዙኀ ፡ (ድጓ ። ሚራ፭ ፡ ፲፬ ። ፍ ፡ ነ ፡ ፲ ፡ ፰ ። ፀር ፡ ኢሳ፫ ፡ ፳፯ ። ሮሜ፩ ፡ ፴) ።

አሕመየ ፤ አሳማ ፡ አስነቀፈ ፤ አሰደበ ።

ተሐምየ ፤ ታማ ፡ ተነቀፈ ፤ ተሰደበ ። ለሊክ ፡ ዘትትሔመይ ፡ ወአከ ፡ ውእቱ ፡ (አፈ ፡ ተ፲፩) ።

ተሓመየ ፤ ተማማ ፤ ተነቃቀፈ ፤ ተቀናና ፡ ተመቀኛኘ ። ኢትትሓመዩ ፡ በበይናቲክሙ ። ተሓምዮ ፡ (ያዕ፬ ፡ ፲፩ ። ገላ፭ ፡ ፳፮ ። ፩ጴጥ ፡ ፪ ፡ ፩) ።

ሕሙይ ፤ (ያን ፡ ያት ፡ ሚት) ፤ የታማ ፡ የተነቀፈ ፤ ስዱብ ፡ ንቁፍ ። ግብረ ፡ ሕሙይ ፤ ፍትወት ፡ ሕሙይ ። ሕሙየ ፡ ግብር ፡ (ዮሴፍ ። ፊልክ ፡ ፻፳፩) ። የተማማ ፡ የተነቃቀፈ ፤ ንቅፍቅፍ ፤ ፍርቅርቅ ።

ሕሜት ፤ ሕምየት ፤ ማማት ፡ መንቀፍ ፤ መታማት ፡ መነቀፍ ።

ሐሜት ፤ (ሱር ፡ ሐኔት) ፤ በቁሙ ፤ ዐሚታ ፡ ነቀፋ ፡ ስድብ ፤ ክፉ ፡ ነገር ፡ ገመና ፡ ነውር ፤ ስም ፡ የሚያጠፋ ፡ የሚሰብር ፤ በውነት ፡ ወይም ፡ በሐሰት ፡ የሚነገር ። ዝንጓጔ ፡ ወሐሜት ፡ ወዝክር ፡ ሕሡም ። ዘአልቦ ፡ ሐሜት ። ቀሲስ ፡ ንጹሐ ፡ ይኩን ፡ እምሐሜት ፡ (ዮሴፍ ። ቲቶ፩ ፡ ፯ ። ቀኖ ፡ ኒቅ) ። አንዳንድ ፡ መጣፍ ፡ በሐሜት ፡ ፈንታ ፡ እንደ ፡ ሱርስቱ ፡ ሐኔት ፡ ይላል ፤ ፍችው ፡ አንድ ፡ ነው ። ቃሕው ፡ ወሐኔት ፡ (ሚራ፵ ፡ ፳) ። ባለብሉዮች ፡ ግን ፡ ኀዝንኀዝ ፡ ዝብዝብ ፡ ይሉታል ።

ሐሚል ፤ ሎት ፤ (ሐመለ ፡ የሐምል ፡ ይሕምል ። ዐረ ፡ ሐመለ ፤ ጸረ ። ዕብ ፡ ሐማል ፤ ራራ) ፤ መፅነስ ፡ ማበብ ፤ ማፍራት ፡ መሸከም ። መማረር ፡ መልቀም ፤ መዘንጠፍ ፡ መመልመል ፤ የፍሬ ፡ የቅጠል ። ወፈረ ፡ ገዳመ ፡ ይሕምል ፡ ሐምለ ፡ ምድር ። ወበዕለተ ፡ ዐርብ ፡ የሐምል ፡ ሐምለ ፡ ገዳም ፡ ዘእንበለ ፡ ይኅሪ ፡ መሪረ ፡ ወጥዑመ ፡ (፬ነገ ፡ ፬ ፡ ፴፱ ። ገድ ፡ ተክ) ።

ሐማሊ ፤ (ሊት ፡ ልያን ፡ ያት ፤ መልት ። አው ፡ ሐማል ፤ ላን ፡ ላት) ፤ የሚሸከም ፡ ተሸካሚ ፤ ማራሪ ፡ ለቃሚ ። ሐማል ፡ ወንድና ፡ ሴት ፡ ያስተባብራል ።

ሐምል ፤ (ብ ፡ አሕማል ፡ ላት) ፤ ቅጠል ፡ ቅጠላቅጠል ፤ ማር ፡ ቋያ ፡ ቡቃያ ፡ ተክል ፤ ሥንቆ ፡ ጐመን ፤ ስላሖ ፡ ቅመም ፤ በየስሙና ፡ በያይነቱ ፤ የሚበላ ፡ የማይበላ ፡ ማናቸውም ፡ ኹሉ ። ዐጺደ ፡ ሐምል ። ሐምለ ፡ ገዳም ። ሐምለ ፡ ሁስጱ ፡ ዘይወፅእ ፡ ዲበ ፡ አረፍት ፡ (ዮሐ፲፰ ፡ ፩ ። ሉቃ ፡ ዕዝ፲፪ ፡ ፶፰ ። ፫ነገ ፡ ፬ ፡ ፴፫) ።

ሐምለ ፡ ብሒእ ፤ መራራ ፡ ስንፋጣ ፤ ሐዞ ፡ ስናፍጭ ፤ አውጥ ፡ ፀሞጭ ፤ የመሰለው ፡ ኹሉ ፡ (ዘፀ፲፪ ፡ ፰ ። ዘኍ፱ ፡ ፲፩) ።

ሐምለ ፡ ሣዕር ፤ ፍሬ ፡ እክል ፤ እሸት ፡ ምርት ፡ (ኩፋ ፡ ፯) ።

ሐምለ ፡ ቅብዕ ፤ መሎኬ ፤ ቅባታም ፡ ማላጋ ፡ ጠውላጋ ፤ እንዳንጣሪያና ፡ እንደ ፡ ሳማ ፡ ያለ ፤ የመሎኩን ፡ ፍች ፡ እይ ፤ ከዚህ ፡ ጋራ ፡ አንድ ፡ ነው ። (ኢሳ፶፩ ፡ ፳) ። ዕብራይስጡ ፡ ግን ፡ ከወጥመድ ፡ የገባ ፡ በኸር ፡ አጋዘን ፡ ይላል ፡ እንጂ ፡ ሐምለ ፡ ቅብዕ ፡ አይልም ።

አሕመለ ፤ አስረገዘ ፤ ጫነ ፡ አሸከመ ፤ አስለቀመ ።

**አሕመልመለ** ፤ (ተቀ ፡ ግ) ፤ ለመለመ ፡ ረጠበ ፤ ወጣ ፡ በቀለ ፤ ተገኘ ፡ ተፈጠረ ፤ ቅጠል ፡ መሰለ ። ያሕመለምል ፡ አውግር ። ወእምአሐቲ ፡ መዝገብ ፡ ዘእምእስትንፋስ ፡ አፉሁ ፡ ይሠርጻ ፡ ወያሕመለምላ ፡ ነፍሳት ። ሕብር ፡ እንተ ፡ ታሕመለምል ። ወርቀ ፡ ዐረብ ፡ ዘያሕመለምል ፡ (ዓሞ፬ ፡ ፲፫ ። ቅዳ ፡ ግሩ ። ዘሌ፲፫ ፡ ፵፬ ። አርጋ) ።

—፤ አለመለመ ፤ አረጠበ ፤ አበቀለ ፡ አስገኘ ። አሕመልምል ፡ ሊተ ፡ ሣዕረ ፡ ዘየብስ ። አሕመልምል ፡ ሊተ ፡ ነፍስየ ። ያሕመለምል ፡ ሣዕረ ፡ ለእንስሳ ፡ (ሱቱ ፡ ዕዝ፫ ፡ ፵፰ ። ፊልክ ። ቅዳ ፡ ኤጲ) ። አመለመለ ፤ ጠቀለለ ፤ የጥጥ ፡ የፀምር ፡ ለመፍተል ።

**ሐመልሚል** ፤ (ላን ፡ ላት ፡ ማል) ፤ የለመለመ ፤ ርጥብ ፡ ቅጠላም ፤ ቅጠልማ ፡ ቅጠልያ ፤ ቅጥልጣል ፤ ዐይነት ፡ ቅጠል ፡ አረንጓዴ ፡ የሚመስል ። ወይም ፡ ብጫ ፤ የወራ ፡ ቅጠል ፡ የበሰለ ፡ ፍሬ ፡ ሊወድቅና ፡ ሊደርቅ ፡ የቀረበ ፤ ወይባ ፡ ዐደይ ፡ አበባ ፡ የሚመስል ፡ የሎሚ ፡ የብርትኳን ፡ ዐይነት ። የሚያብረ ፡ የሚበርቅ ፡ የሚያብረቀርቅ ፡ የወርቅና ፡ የንሐስ ፡ ዐይነት ። ነሥአ ፡ በትረ ፡ ልብን ፡ ሐመልሚለ ፤ ርጥብ ። ዕንቍ ፡ ሐመልሚል ። ፈረስ ፡ ሐመልሚል ፡ (ዘፍ፴ ፡ ፴፯ ። ፪ ፡ ፲፪ ። ራእ፮ ፡ ፰) ። በሐመልሚል ፡ ፈንታ ፡ ሐመልማል ፡ ይላል ፤ አያሰኝም ፡ (ራእ፰ ፡ ፯) ።

**ሐመልማል** ፤ (ላት) ፤ ለምለም ፤ ቈያ ፡ ቡቃያ ፡ ሣር ፡ ቅጠል ፤ እኽል ፡ ተክል ፤ ዛፍ ፡ ቋጥቋጦ ፤ ለጋ ፡ ቀንበጥ ፡ ሙሽራ ፤ ለባልብ ፡ ውልብልቢት ፤ መላው ፡ የማግስኛ ፡ ፍጥረት ። ለታብቍል ፡ ምድር ፡ ሐመልማለ ፡ ሣዕር ። ኵሉ ፡ ሐመልማለ ፡ ሐቅል ፡ ወኵሉ ፡ ሐመልማለ ፡ ምድር ። እምቅድመ ፡ ያስተርኢ ፡ ገጸ ፡ የብስ ፡ ወእምቅድመ ፡ ይብቊሉ ፡ ሐመልማላት ፡ (ዘፍ፩ ፡ ፲፩ ። ፪ ፡ ፭ ። ቅዳ) ። አመልማሎ ፡ የጥጥ ፡ ነደ ፤ የንድፍ ፡ ጥቅል ፡ (ዐማርኛ) ።

**ሐመልማለ ፡ አቍጽል** ፤ ርጥበት ፡ ልምላሜ ፤ ልብስነት ፡ (ሔኖ፭ ፡ ፩) ።

**ሐመልማለ ፡ ወርቅ** ፤ የወርቅ ፡ ሽበ ፤ ወይም ፡ ቅጠል ፡ ሥሥ ፡ ረቂቅ ፡ (መዝ ፡ ፷፯) ።

**ሐመልማለ ፡ ዘርዕ** ፤ ቡቃያ ፤ ተክል ፤ ተዘርቶ ፡ የሚበቅል ፡ ኹሉ ፡ (ሢራ፵ ፡ ፳፪) ።

**ሐመልማለ ፡ ሐምል** ፤ የበሰለ ፡ የገረጣ ፡ ቅጠል ፤ ወይም ፡ የጕመን ፡ (መዝ ፡ ፴፯) ።

**ሐመልማለ ፡ ሣዕር** ፤ መስክ ፡ ጨፌ ፡ ለቆ ፤ ርጥብ ፡ ሣር ፡ (ማርሻ ፡ ፴፱) ።

**ሐምሌ** ፤ በቁሙ ፤ የወር ፡ ስም ፡ የመስከረም ፡ ፲፩ኛ ፤ ቅጠላም ።

**ሕምል** ፤ (ላት ። ዐረ ፡ ሒ.ምል) ፤ ሸክም ፤ ጭነት ። ዕሥራ ፡ እልፍ ፡ ሕምለ ፡ ሥርናይ ፡ (ዮሴፍ) ።

**ሐመል** ፤ (ዐረ ፡ አልሐመል) ፤ ኮከብ ፤ የኮከብ ፡ ስም ፤ አውራ ፡ በግ ። ከፀሐይ ፡ ጋራ ፡ በመጋቢት ፡ ፴ ፡ ዕለት ፡ ፵፫ ፡ ኬክሮስ ፡ ይመግባል ፡ (አቡሻ ፡ ፬) ። የስሙ ፡ ምስጢር ፡ ማስረገዝና ፡ ማሸከም ፡ ነው ፤ መጋቢት ፡ በወዲያ ፡ እንደ ፡ መስከረም ፡ ነውና ፤ ቅጠሉና ፡ ልምላሜው ፡ ሳይቀር ፡ መዋዕለ ፡ ፅንስ ፡ መኾኑን ፡ ያሳያል ።

**ሐሜለት** ፤ (ጽር ፡ ሒ.ሚሎቲ ። ሱር ፡ ሚልታ) ፤ የላይ ፡ ልብስ ፤ ካባ ፡ በርኖስ ፤ መጐናጠፊያ ፡ ደበሎ ፡ ዐጥፍ ። ሐ ፡ አርቲክል ፡ ነው ፤ ሚለት ፡ ከሜላት ፡ ጋራ ፡ ይስማማል ፤ የሚላትን ፡ ፍች ፡ እይ ፤ ባለብሉዮች ፡ ግን ፡ ኀባኔ ፡ ጥምጥም ፡ ይሉታል ፡ (፫ነገ ፡ ፲፱ ፡ ፲፫ ። ፬ነገ ፡ ፪ ፡ ፰ ፡ ፲፫ ፡ ፲፬) ። በሠቀ ፡ ወበ ሐሜለት ፡ (ዕብ፲፩ ፡ ፴፯) ።

**ሐሚም** ፤ ሞት ፤ (ሐመ ፤ ሐመመ ፡ የሐምም ፡ ይሕምም ። ዐረ ፡ ሐመ ። ዕብ ፡ ወሱር ፡ ሐም) ፤ መሞቅ ፡ መተኰስ ፡ መፋጀት ፤ በንዳድ ፡ በትኵሳት ፡ መያዝ ። መታመም ፡ መከራ ፡ መቀበል ፤ ማማጥ ፡ መጨነቅ ፡ ማዘን ፡ ማልቀስ ፡ መናደድ ። ተሐምም ፡ ዐቢየ ፡ ፈፀንት ። ዘእንበለ ፡ ትሕምም ፡ ተፈወስ ። በእንቲኣነ ፡ ሐመ ። ተሐምም ፡ ለወሊድ ። ሐመምኩ ፡ ላዕሌከ ፡ (ሉቃ፬ ፡ ፴፰ ። ሢራ፲፰ ፡ ፲፱ ። ኢሳ፶፫ ፡ ፬ ። ራእ፲፪ ፡ ፪ ። ፪ነገ ፡ ፩ ፡ ፳፮) ።

—፤ መመቅኘት ፤ መጎፈግ ፡ መቤስ ፡ መሠሠት ። የሐምም ፡ አቅርቦ ፡ እዴሁ ፡ ውስተ ፡ አፉሁ ፡ (ምሳ፳፮ ፡ ፲፭) ።

**ሐማሚ** ፤ (ሚት ፡ ምያን ፡ ያት ፤ መምት) ፤ የሚታመም ፡ ታማሚ ፤ ሕማም ፡ የሚስማማው ፤ ሐዘንተኛ ፡ መከረኛ ። አንተ ፡ ሐማሚ ፡ ዘከመ ፡ ዕፁናከ ፡ ምስሌነ ፤ ወአንተ ፡ ኢሐማሚ ፡ ዘከመ ፡ ዕፁናከ ፡ ምስለ ፡ አብ ። ነአምን ፡ ከመ ፡ ቃለ ፡ እግዚ ፡ ኢሐማሚ ። ሐማሚት ፡ አርኣያ ፡ ገብር ፡ (ሃይ ፡ አበ ። ተረ ፡ ቄር) ።

—፤ የሚመቀኝ ፡ ምቀኛ ፤ ሥሡ ፡ ንፉግ ። ዐይንከኑ ፡ ሐማሚ ፡ ውእቱ ። ዐይኑ ፡ ለሐማሚ ፡ ይጠውዕ ፡ እክለ ። ብእሲ ፡ ሐማሚ ። ቅንአተ ፡ ሐማሚ ። ሐማምያን ፡ (ማቴ፳ ፡ ፲፭ ። ሢራ፲፬ ፡ ፲ ። ምሳ፳፰ ፡ ፳፪ ። ጥበ፰ ፡ ፳፩ ። ሮሜ፩ ፡ ፳፱) ።

(ጥ) **ሐማም** ፤ (ዐረ) ፤ ፍል ፡ ውሃ ፤ ማወት ፡ ቤት ፡ ብስኔ ።

**ሕሙም** ፤ (ማን ፡ ማት ፡ ምምት) ፤ የሞቀ ፡ ሙቅ ፤ የታመመ ፡ ድዉይ ፤ ሕዙን ። ማይ ፡ ሕሙም ፤ (ሙቅ ፡ ግም ፡ ድፍርስ) ። ብእሲሁ ፡ ቅሡፍ ፡ ወሕሙም ። ሕሙማን ፡ ይፈቅድዎ ፡ ለዐቃቤ ፡ ሥራይ ። ኵሉ ፡ ዓለም ፡ ሕሙም ፡ ወትኩዝ ። ተንሣእኩ ፡ ሕሙምየ ፡ (ዐዝ፯) ። ሕምምት ፡ ነፍስየ ፡ (ስንክ ፡ ጥቅ፳ ። ኢሳ፶፫ ፡ ፫ ። ማቴ፱ ፡ ፲፪ ። ሮሜ፰ ፡ ፳፫ ። ዕዝ፱ ፡ ፭ ። ሱቱ ፡ ዕዝ፱ ፡ ፵፭) ።

**ሕማም** ፤ (ማት) ፤ ትኵሳት ፡ ንዳድ ፤ በቁሙ ፡ በሽታ ፤ ሐዘን ፡ ጭንቅ ፡ መከራ ፤ ወይሌ ፡ ዋይታ ፡ ወዮታ ። ክቡድ ፡ ሕማም ። ኀበ ፡ አልቦ ፡ ደዌ ፡ ወአልቦ ፡ ሕ

ማም ። ከመ ፡ ይፈጽም ፡ በሕማማት ። ሕማሙ ፡ ለዝ ፡ ዓለም ። አሐቲ ፡ ሕማም ፤ ካልእት ፡ ሕማም ፡ (ሚራ፴፱ ፡ ፱ ። ቀሌ ። ዕብ፪ ፡ ፲ ። ሮሜ፰ ፡ ፲፰ ። ራእ፱ ፡ ፲፱ ። ፲፭ ፡ ፲፱) ።

**ሕማምት ፤ (ትግሬ) ፤** ያውሬ ፡ ስም ፡ ግስላ ፤ ቀጡ ፡ ብስጩ ፡ ተናዳጅ ።

**ሕመሜ ፤** መመቅኘት ፤ ምቀኝነት ፤ ተንኰል ፡ ሽንገላ ፡ የሚያናድድ ፡ ነገር ። እምሕመሜ ፡ እኩይ ። ወሕመሜ ፡ ይትናገር ፡ አፉሆሙ ፡ (ቅዳ ። ምሳ፳፱ ፡ ፱) ።

(ጥ) **ሕመት ፤ (ሳቢና ፡ ጥሬ ፡ ዘር) ፤** መሞቅ ፤ አሻሻቅ ። ሙቀት ፡ ትኩሳት ። ጥቀርሻ ፡ ጥላት ፤ ከሰል ፡ የእሳት ፡ ትራፊ ፡ መልሶ ፡ እሳት ፡ የሚበላው ፤ ከንጨት ፡ ከደንጊያ ፡ የሚወጣ ፡ ፍጹም ፡ ጥቍር ። ጸሊም ፡ እምነ ፡ ሕመት ፡ ራእየሙ ። ጸሊም ፡ ከመ ፡ ሕመት ። ማየ ፡ ሕመት ፡ (ሰቈ፬ ፡ ፰ ። ሄርማ ፡ ገ፳፱ ። ፪ቆሮ ፡ ፫ ፡ ፫) ።

**ሐመተ ፤ (ተቀ ፡ ግ) ፤** በቁሙ ፤ ዐመተ ፡ በላ ፡ አቃጠለ ፤ አከሰለ ፤ አጠቈረ ፡ ከሰል ፡ አስመሰለ ። ሐመደን ፡ እይ ፤ ከዚህ ፡ ጋራ ፡ አንድ ፡ ነው ።

**አሕመመ ፤** ዐመመ ፤ አሳመመ ፤ አሞቀ ፡ አተኰሰ ፤ አሳዘነ ፡ አስጨነቀ ። አሕመሞ ፡ ፀሓይ ፡ ርእሶ ። ኢያሕመምሙ ፡ ላህበ ፡ ፀሓይ ። ሀሎ ፡ ዘያሐምም ፡ ወያስተፌሥሕ ። ኢያሕመሞ ፡ ይሁዳ ፡ ለኤፍሬም ፡ (ዮና፬ ፡ ፰ ። ኢሳ፵፱ ፡ ፲ ። ሚራ፯ ፡ ፲፭ ። ኢሳ፲፩ ፡ ፲፫) ።

**አሕማሚ ፤ መሕምም ፤** የሚያሳምም ፤ አሳዛኝ ፡ አስጨናቂ ። ደዌ ፡ ወሕማሕም ፡ አማምያን ፡ (ፍ ፡ ነ ፡ ፵፫ ፡ ፱) ።

**ማሕመሚ ፤** ዝኒ ፡ ከማሁ ። ዝብጠት ፡ ማሕመሚ ፡ (ፊ ፡ መ ፡ ፰ ፡ ፫) ።

**ማሕምም ፤ ማሕመም ፤** (ጥሬና ፡ ቅጽል) ፤ ምጥ ፡ ጭንቅ ። አኅዘሙ ፡ ማሕምም ፡ (ዘፀ፲፭ ፡ ፲፬) ። የሚያሳምም ፡ የሚጐዳ ፤ የሚያስጨንቅ ። ዘበጥዎ ፡ ዝብጠተ ፡ ዐቢየ ፡ ወማሕምመ ፡ (ስንክ ፡ መጋ፳፯) ።

**አስተሐመመ ፤ (አስተሕመመ) ፤** የሐመመና ፡ የአሕመመ ፡ ድርብ ፤ ገቢርና ፡ ዐጕል ። አሳመመ ፤ ለሕማም ፡ ሰጠ ። እግዚ ፡ ፈተወ ፡ ያስተሐምሞ ፡ (ተረ ፡ ቄር፩) ።

—፤ አስታመመ ፡ ረዳ ፤ ጠበቀ ፤ ሰበሰበ ። እሰ ፡ አስተሐምምዎ ፡ ለአትናቴዎስ ። ዘኢክህለ ፡ ሠሪዐ ፡ ቤቱ ፡ እፎ ፡ ያስተሐምም ፡ ቤተ ፡ እግዚ ። አስተሐምም ፡ ዘውስተ ፡ ገዳም ፡ ሐመልማለ ፡ (አዋል ። ፩ጢሞ ፡ ፫ ፡ ፭ ። ምሳ፳፯ ፡ ፳፱) ።

—፤ ዐሰበ ፡ አስተነተነ ፤ ተጋ ፡ እንቅልፍ ፡ ዐጣ ። ምስጢሩ ፡ ከዚያው ፡ ከማስታመም ፡ ይገባል ። ያስተሐምሙ ፡ ኅበ ፡ ዘይትሌዐል ። ሙት ፡ እምፍትወታቲሁ ፡ ለዝ ፡ ዓለም ፡ ወአስተሐምሞቱ ። ተኀሥሥ ፡ አስተሐሚማ ፡ እስከ ፡ ትረክብ ፡ (አፈ ፡ ድ፳፯ ። ፊልክ ፡ ፫ ። ሉቃ፲፭ ፡ ፰) ።

**መስተሐምም ፤ (ምት ፡ ማን ፡ ማት) ፤** የሚያስታምም ፡ አስታማሚ ፤ ትጉህ ፡ ንቁህ ፤ ዐሳቢ ፡ አስተንታኝ ። መስተሐምማን ፡ ለግብረ ፡ ቅድስና ፡ (ቀሌ) ።

**ተሐመመ ፤** ተቃና ፡ ተመቀኘ ። ተሓምሞ ፡ ወተቃንኦ ። አከ ፡ በተሓምሞ ፡ (፩ጢሞ ፡ ፮ ፡ ፬ ። ሮሜ ፲፫ ፡ ፲፫) ።

**አስተሓመመ ፤** አስተማመመ ፤ አመቀኘ ። ነገር ፡ ሠርቶ ፤ መድኅኒት ፡ ሰጥቶ ።

**መስተሓምም ፤** ክፉ ፡ መድኀኒት ፤ የሚያም ፡ የሚገድል ፡ ሥራይ ፡ የሚኾን ። ወይም ፡ ሰውየው ፡ ባለ መድኀኒቱ ። ብእሲ ፡ መስተሓምም ፤ አው ፡ ተጠያፊ ፡ (ቄስጠ) ።

**ሐምሐም ፤ (ዕብ ፡ ወሱር ፡ ቂቃዮን ። ዐረ ፡ የቅጢንት) ፤** ቅልዕ ፤ ቅል ፡ የቅል ፡ ዐይነት ፡ ኹሉ ፤ በቈላ ፡ በእንቅልቅል ፡ በሙቀት ፡ አገር ፡ የሚበቅል ፤ ሐረጋም ፡ ሰፋሐ ፡ አቍጽል ፤ ፍሬው ፡ ገንቦ ፡ ማድጋ ፡ የሚያክል ፤ የሚበላ ፡ የሚያገለግል ። ወአዘዘ ፡ እግዚ ፡ ሐምሐመ ፡ ወበቈለ ። ዘመደ ፡ ሐምሐም ፡ (ዮና፬ ፡ ፮—፲ ። ቄስጠ) ።



ሐምሐም ፡

**ሐመጸ ፤ (ትግ ፡ ሐምጸ ። ዕብ ፡ ሐማጽ) ፤** በካ ፡ ሖመጠ ፡ ሖመጠጠ ፤ ሸመጠረ ፤ ሖምጣጣ ፡ ኾነ ።

**ሐሚቅ ፤ ቆት ፤ (ሐመቀ ። ዐረ ፡ ሐሚቀ) ፤** ማበድ ፡ መከንፍ ፤ ክፉ ፡ መጥፎ ፡ መኾን ።

**ሕሙቅ ፤ (ቃን ፡ ቃት ፡ ምቅት) ፤** ያበደ ፡ አብድ ፤ መጥፎ ፡ ምናምን ፡ ከንቱ ፡ ብልሹ ። እፎ ፡ ትት መየጡ ፡ ዳግመ ፡ ውስተ ፡ ኅሳር ፡ ወሕሙቅ ፡ ነገር ፡ (ቄር ፡ ስም ። ገላ፬ ፡ ፱) ።

**ሕመቅ ፤** እብደት ፤ እብድነት ፤ ክፋት ፡ ቅለት ።

**አሕመቀ ፤ አስተ(ሕ)ሐመቀ) ፤** አሳበደ ፤ እብድ ፡ አደረገ ፤ አስመሰለ ። ናቀ ፡ ነቀፈ ፤ አቃለለ ። ፍኖተ ፡ እንተ ፡ ትደሉ ፡ ለትሩፋት ፡ ኢያስተሐሚቅ ፡ ልደተ ፡ ተወልደ ፡ (ቄር ፡ ጸላ) ።

**ሕምር ፤—ቀይ ፡ ዐይነት ፤—ኅምር ።**

**ሐመረ ፤ (ሐመለ ፤ ጸረ ፤ ሰከመ) ፤** ተጫነ ፡ ተሸከመ ፤ ተሸከሞ ፡ ኼደ ፡ ተነዳ ።

**ሐመር ፤ (ብ ፡ አሕማር ፡ ራት ። ዐረ ፡ ሒማር ። ዕብ ፡ ሐሞር ፤ አህያ) ፤** መርከብ ፡ የባሕር ፡ አህያ ፤ የሚጫን ፡ የሚሸከም ፤ ተጭኖ ፡ የሚኼድ ፡ የሚነጕድ ፡ በጢስ ፡ በነፋስ ፡ የሚነዳ ፤ ከብረት ፡ ከንጨት ፡ የተሠራ ፡ የተሰናዳ ። ረከበ ፡ ሐመረ ፡ ዘይነግድ ፤ ወ ተዐሰበ ፡ ሐመረ ፡ ወዐርገ ፡ ውስቴቱ ። አሕማረ ፡ ተርሴስ ። ነገሥተ ፡ አሕማር ፡ (ዮና፩ ፡ ፫ ። መዝ ፡ ፵፯ ።

ሔኖ ፡ ፲፩) ። ሐመረ ፡ የብስ፤ የምድር ፡ ባቡር ፤ ሌላ ውም ፡ በእሳት ፡ ኀይል ፡ የሚኼድ ፡ ኹሉ ። ረከበንና ፡ መርከብን ፡ እይ ።



ሐመር ፡

**ሐሜር ፤ (ዕብራ) ፤** የመስፈሪያ ፡ ስም ፤ የእኽል ፡ መስፈሪያ ፤ ዐሥር ፡ ኢፍ ፡ የሚይዝ ፤ ታላቅ ፡ ዐሥረ ፡ ፈጅ ፡ (ሕዝ፵፭ ፡ ፲፫ ፡ ፲፬ ። ሆሴ፫ ፡ ፪) ።

**ሐመር ፤ (ዐረ ፡ ሑመር) ፤** የዛፍ ፡ ስም ፤ ፍሬው ፡ ጥቍር ፡ ጣፋጣ ፡ ሖምጣጣ ። ወይም ፡ የባሕር ፡ ቱል ፤ ታላላቅ ፡ ባቄላ ፤ ጠንቋዮች ፡ እንደ ፡ ጠጠር ፡ እየበተኑ ፡ የሚያሟርቱበት ። ተጠይሮ ፡ በአንጽፎ ፡ ሐመድ ፡ ወፍሬ ፡ ዕፀው ፡ ወሖመር ፡ ወበቀልት ፡ ወኅጠታተ ፡ ዘጕል ፡ (ፍ ፡ ነ ፡ ፵፯) ። ፋወለን ፡ እይ ።

**ሐመር ፤** እንቡጥ ፡ ከነፍሬው ። ሖምረ ፡ ጽራእ ፤ የጽራእ ፡ እንቡጥ ፡ የብርብራ ፡ ዐይነት ፤ ወፍራም ፡ ረዣዥም ፡ ጥፍጥ ፤ ሰውም ፡ እንስሳም ፡ የሚበላው ፤ ፍሬው ፡ እጅግ ፡ ታናናሽ ፡ ከራራ ፡ ደረቅ ። ባለሐዲሶች ፡ ግን ፡ ቃሞ ፡ ተረር ፡ ይሉታል ። የጽራእን ፡ ፍች ፡ ተመልከት ፡ (ሉቃ፲፭ ፡ ፲፯) ።



ሖመር ፡

(ጥ) **ሐምሰ ፤ ሰት ፤ (ሐመሰ ፡ ይሔምስ ፡ የሐምስ ። ዐረ) ፤** ማመስ ፡ ማገላበጥ ፤ ለማሞቅ ፡ ለማድረቅ ። መዋኘት ፤ ባሕርን ፡ ማማሰል ። መብላት ፡ መቀለብ ፤ ለመሥባት ፡ ለመድለብ ፤ የእንስሳ ። ቦሙ ፡ ልማድ ፡ ሶአባግዕ ፡ ይብልዑ ፡ ኀቡረ ፤ ወሶበሂ ፡ ይወርዱ ፡ ይስተዩ ፡ ማየ ፤ አው ፡ የሐምሱ ፡ ኢይትፈለጡ ፡ ዘዘ ፡ ዚኣሆሙ ፤ አላ ፡ ኅቡራን ፡ በሡሉ ፡ ግዕዘሙ ፡ (ሥር ፡ ጳኵ) ። ሐመሰ ፡ ብሎ ፡ ዋኘ ፡ ማለት ፡ የትግሬ ፡ ነው ፤ ሙሴና ፡ ሐማሴን ፡ ከዚህ ፡ ወጥቷል ። የባሕር ፡ ዳር ፡ ቅርብ ፡ አጠገብ ፤ ጠረፍ ፡ ወደብ ፡ ማለት ፡ ነው ።

**ሐማስ ፤ (ትግሬ) ፤** ጠይም ፡ ዳለቻ ፡ ድፍርስ ፤ የጠጠር ፡ ውሃ ፡ መሳይ ።

**ሕሙስ ፤ (ዐረብ) ፤** ሽንብራ ፤ የቀይ ፡ ዳማ ። የታመሰ ፡ ዕምስ ።

**ሐምስ ፤—ዐምስት ፤—ኀመሰ ።**

**ሐሞት ፤—ዐሞት ፤—ሐመወ ፤**

**ሕመት ፤—ክሰል ፤—ሐመመ ።**

**ሐንበበ ፤ (ስሯ ፡ ግ ። ሐበበ) ፤** አፈራ ፤ ፍሬ ፡ ያዘ ፡ ተሸከመ ። ሐንበበት ፡ ፍሬ ፡ (አርጋ ፡ ፪) ።

**ሕንቡብ ፤** ያፈራ ፡ ፍሬያም ፡ ፍሬያማ ። ያበጠ ፤ ያፈረጠመ ፡ (ሲኖዶ) ።

**ሕንባብ ፤ (ባት ። ዐረ ፡ ሐብ ፤ ጌናብ) ፤** የንጩት ፡ ፍሬ ፡ ሥጋማ ፤ እንደ ፡ ወይን ፡ እንደ ፡ ዘይት ፡ እንደ ፡ ተምር ፡ ያለ ፤ አጋምን ፡ እንኮሬን ፡ ቀጋን ፡ የመሰለ ፡ ከብ ፡ እንከብል ፤ ለፈሳሽም ፡ ቅንጣት ፡ ይነገራል ። ሕንባበ ፡ ፍሬሃ ። ኢትትቀረም ፡ ሕንባባተ ፡ ወይንከ ፡ ዘወድቀ ። ሕንባባት ፡ እምውስተ ፡ አስካል ። ሕንባባተ ፡ ዘይት ፡ ክልኤቲ ። ሕንባባተ ፡ ሮማን ። ሕንባበ ፡ ማይ ። ሕንባባተ ፡ ነጠብጣብ ። ሕንባባተ ፡ በረድ ፡ (አርጋ ። ዘሌ፲፱ ፡ ፲ ። ሱቱ ፡ ዕዝ፱ ፡ ፳፬ ። ኢሳ፲፯ ፡ ፮ ። ስንክ ፡ ጥር፲፫ ። ቅዳ ፡ ግሩ ። ኢዮ፴፰ ፡ ፳፰ ። ሄርማ) ።

**ሐንበለ ፤ (ስሯ ፡ ግ ። ሐበለ) ፤** ኮረቸ ፤ ጫነ ፡ አመቻቸ ፤ ደበደበ ፡ ደለደለ ።

**ሕንባል ፤ (ላት ። ዐረ ፡ ሐንበል) ፤** ኮርቻ ፡ ምቹ ፡ ድብዳብ ፤ መደላድል ። የዳባ ፡ ቀሚስ ፡ የንት ፡ በርኖስ ፤ የቄርበት ፡ ልብስ ፤ ዐጥፍ ፡ ግላስ ። ሕንባላተ ፡ ገመል ። ሡሉ ፡ ሕንባላት ፡ ዘላዕሌሁ ፡ ነበረ ፡ (ዘፍ፴፩ ፡ ፴፬ ። ዘሌ፲፭ ፡ ፱) ።



ሕንባል ፡

**ሕንብርብሬ ፤ (ሕበር ፤ ሓበረ ። ዕብ ፡ ሐባርቡሮት) ፤** ለምጥ ፡ ቋቍቻ ፤ ድል ፤ ቡሬነት ፡ ዝንጕርጕርነት ። ብርሀት ፡ ወጸዐድዒድ ፡ ሕንብራ ፡ ይእቲ ። ወዘሕንብርብሬኒ ። የሣድግኑ ፡ ነምር ፡ ሕንብርብሬሁ ፡ (ዘሌ፲፫ ፡ ፴፱ ። ፲፬ ፡ ፶፯ ። ኤር፲፫ ፡ ፳፫) ። በነቢር ፡ ዘይቤ ፡ ሲፈቱት ፡ ግን ፤ ብጕር ፡ ዕትራት ፡ ኪንታሮት ፡ ጢ ፡ ያሰኛል ።

**ሕንብርት ፤ (ነበረ ፤ ንብርት) ፤** በቁሙ ፡ ዕንብርት ፡ የሆድ ፡ መካከል ፡ የዕትብት ፡ ሥር ፡ መብቀያው ። በላም ፡ ለሕንብርትከ ፡ ማእከለ ፡ ጠባይዕ ፡ ዘተመልአከ ። ማእከለ ፡ ከርሥ ፡ ሀላዊ ። ሕንብርተ ፡ ከርሡ ፡ (ደራሲ ። ኢዮ፵ ፡ ፲፭) ።

—፤ አንዠት፤ የሆድ፡ ውስጥ፤ ማሕፀን። ኅቡረ፡ ወፃእነ፡ እምሕንብርትኪ፡ (ኩፋ፡ ፴፭)።

—፤ የምድር፡ ጕብር፤ ተራራ፡ ኰረብታ፡ ገመገም። ደብረ፡ ጽዮን፡ ማእከለ፡ ሕንብርታ፡ ለምድር። ናሁ፡ ሕዝብ፡ ይወርድ፡ እምነበ፡ ሕንብርተ፡ ምድር። እለ፡ ይነብሩ፡ ውስተ፡ ሕንብርተ፡ ምድር፡ (ኩፋ፡ ፰። መሳ፱፡ ፴፯። ሕዝ፴፰፡ ፲፪)።

**ሕናግ፤ (ትግሬ)፤** ትናግ፤ ትናጋ፡ ላንቃ። ሐኪን፡ እይ።

**ሐንገዝ፤ (ሐገዘ፤ ሐገዝ። ዐረ፡ ሐጂብ)፤** ሽፋል፤ ቅንድብ፤ ጠጕሩ፡ የማያድግ፡ የማይረዝም፤ ሐገዝን፡ እይ። ይትላጸይ፡ ሥዕርተ፡ ርእሱ፡ ወጽሕሞ፡ ወሐንገዞ፡ (ዘሌ፲፬፡ ፱)። ብብት፡ ብልት፡ ኅፍረት፤ ያገጭ፡ ሥር፡ ሽለቆው። ጸጕር፡ ሠርጸ፡ ድማሕ፡ ወሐንገዝ። ሕንጋዙ፡ (ጕርዒሁ)፡ (መጽ፡ ምስ። ገድ፡ ላሊ)።

**ሐነወ፤ (ዕብ፡ ሐናሕ። ዐረ፡ ሐና)፤** ሰፈረ፤ ሰፍራ፡ ያዘ፤ ጐገዮ፡ ሠራ፡ ድንኳን፡ ተከለ።

**ሐኖት፤ (ዕብ፡ ወዐረ፡ ሐኑት። ሱር፡ ሓኑታ)፤** መደብር፤ የንግድ፡ የገበያ፡ ቤት፤ መብል፡ መጠጥ፡ ጨዎታ፡ መሸታ፡ ያለበት፤ ዓለማዊ፡ እንግዳ፡ የሚያርፍበት። ሥጋ፡ ሐኖት። ኢይብልዑ፡ ውስተ፡ ቤት፡ ሐኖት፤ እመ፡ ቦ፡ ካህን፡ ዘበልዐ፡ ውስተ፡ ሐኖት። ወኢትባእ፡ ሐኖተ፡ ለግሙራ፡ (ምሳ፳፫፡ ፳። ፊ፡ መ፡ ፴፪፡ ፩። ሃይ፡ አበ)።

**ሐንዋት፤ (ዐረ፡ ሐዋኒት። ዕብ፡ ሐኑዮት)፤** መደብሮች። አንዳንድ፡ መጽሐፍ፡ በሐንዋት፡ ፈንታ፡ እንዳረቡ፡ ሐ(ከ)ዋኒት፡ ይላል፡ (ግብ፳፰፡ ፲፭)።

**ሐንዘር፤ (ዐረ፡ ኺንዚር። ዕብ፡ ሐዚር። ሱር፡ ሕዚራ)፤** ሐማማ፡ ሕሪያ፤ ርኩስ፡ የቤት፡ እንስሳ፤ እስራኤል፡ የሚጸየፉት፡ አሕዛብ፡ የሚነፈንፉት። ባለብሉዮች፡ ግን፡ አነር፡ ይሉታል፤ ሐሠመንና፡ ሐረወን፡ እይ፡ (ሔኖ፺፰፡ ፲)።

**ሐንሓን፤ (ትግ)፤** ስርን፡ ኰሸኰሽ፤ ያፍንጫ፡ ዐጥንት፤ ማእከለ፡ አዕይንት።

**ሐነጠ፤ (ዐረብ። ዕብ፡ ሐናጥ። ሱር፡ ሕናጥ)፤** ሽቱ፡ ቀባ፡ ለቀለቀ፤ በሽቱ፡ ለወሰ፡ ዐጀለ፤ የሬሳ፡ አቀባብ፤ እንዳይፈርስ፡ እንዳይበሰብስ፡ በሚያደርግ፡ በታወቀ፡ ሽቱ። ጸዐጠን፡ እይ፤ ከዚህ፡ ጋራ፡ አንድ፡ ነው። ወሐነጠ፡ ዮሳ፡ ሥጋሁ፡ በከርቤ፡ ወበለሊኖት፡ ወአስቀጠኒን፡ (አቡሻ፡ ፵፰)።

**ሐኔት፤—ሐሜት፤—ሐመየ፤ ሐነየ።**

**ሐኒክ፤ ኮት፤ (ሐነከ፡ የሐንክ፡ ይሕንክ። ዐረ፡ ሐነከ። ዕብ፡ ሐናኽ)፤** ጠልቆ፡ ማወቅ፤ ማስተዋል። ማፈር፤ መሰቅጠጥ። ዘየአምር፡ ሐኒክ። የሐንክዎ፡ ወይፈርህዎ። ሰላም፡ ለከ፡ ገብረ፡ ዮሐንስ፡ ቡሩክ፤ በምግባርከ፡ ሐኒክ፡ (ምሳ፫፡ ፲፫። ሉቃ፱፡ ፵፭። ስንክ፡ ኅዳ፳፯)።

—፤ መባረክ፡ መቀደስ፤ የቤት፡ የንዋየ፡ ቅድሳት። ማኘክ፡ ማላመጥ፤ መበጠስ፡ መቍረጥ፤ የጥርስ፡ የመኪና። ዕንክ፡ ማለት፤ እጅ፡ በጅ፡ መስጠት። መጣፍ፡ ግን፡ በሐንከ፡ ፈንታ፡ አንከየ፤ ይላል፤ የተሳሳተ፡ ነው፤ ነከየን፡ እይ።

**ሕንከት፤** ማፈር፤ መቍረጥ፡ ቁረጣ። ዝንቱ፡ ፍና፡ ፈውስ፡ ውእቱ፡ ወአኮ፡ ሕንከት፡ (ተረ፡ ቄር፩)።

**ሕንካ፤ (ዕብ፡ ሐኑካ)፤** ቅዳሴ፡ ቡራኬ፡ ያዲስ፡ ቤት፡ ምረቃ፤ የታቦት፡ የመቅደስ፡ የቤተ፡ ክሲያን፡ ዕቃ፡ መሾምና፡ መክበር፡ የግዜር፡ ገንዘብ፡ መኾን። በዓለ፡ ሕንካ፡ (ዮሴፍ)።

**ሔኖክ፤ (ዕብ፡ ሐኖኽ)፤** የሰው፡ ስም፤ ሐዲስ፡ ቅዱስ፡ ማለት፡ ነው፡ (ዘፍ፬፡ ፲፯። ፭፡ ፲፰። ፳፭፡ ፬)።

**ሕንክ፤ (ነበርና፡ ትእዛዝ፡ አንቀጽ)፤** ዕንክ፡ ውሰድ፡ ተቀበል። ሕንክሙ፡ ብልዑ፡ (ማቴ፳፮፡ ፳፮)።

—፤ ስጥ፡ ዐድል፤ ዕንካችኹ፡ በል። ሀብን፡ እይ፤ የዚህ፡ ጎር፡ ነው።

**ሐኑክ፤ (ትግ)፤** ምግብ፤ የሚጐረሥ፡ የሚታኘክ።

**ማሕነክ፤ (ብ፡ መሓንክ)፤** ማኘኪያ፡ መንጋጋ፤ የመኪና፡ ጥርስ፤ የሥጋ፡ መምትሪያ፤ የሰው፡ ወጥመድ፤ ሥጋን፡ ከናጥንቱ፡ የሚፈጭ፡ የሚያልም፡ የሚደቍስ፡ የሚቈርጥ፡ የሚበጣጥስ። መንበክ፡ ወማሕነክ። ወአንተሰ፡ እስክንድር፡ ንጉሥ፡ ተዐቀብ፤ እስመ፡ አልቦ፡ ዘይወፅእ፡ እምድኅረ፡ ቦአ፡ ውስተ፡ ዛቲ፡ ሀገር፡ እምነጋድያን፡ ከመ፡ ይንግር፡ ዜና፡ ለእለ፡ ይመጽኡ፤ ወአዝዘዘሙ፡ ለሰራዊትከ፡ ይትዐቀቡ፤ እስመ፡ ኀበ፡ ኆኅትሂ፡ ወማእከለ፡ ቤትሂ፡ ወማዕገትሂ፡ ሀሎ፡ ማሕነክ፡ ወሠርም፡ ወማዕምቅ፤ ወእምድኅረ፡ ወድቀ፡ አልቦ፡ ዘይትነሣእ፤ አላ፡ ይትከዐው፡ አማዑቱ፡ ወይትቀጠቀጥ፡ አዕፅምቱ፡ (አዋል። ዜና፡ እስ)።

**ሐንከሰ፤ (ዲቃ፡ ግ። ሐነከ፤ ነከሰ)፤** ዐነከሰ፤ ዐጭር፡ ኾነ፤ ዐፈረ፡ ተሰቀጠጠ፤ ተሰብሮ፡ ተቈርጦ፡ ተሸምቅቆ፡ ወይም፡ ስሎ፡ ደርቆ፤ የእግር። ተጠራጠረ፤ አወላወለ፡ አመነታ፤ የልቡና። ሐንከሱ፡ በፍኖቶሙ። እስከ፡ ማእዜኑ፡ ተሐነክሱ፡ በክልኤ፡ ልብክሙ። እስመ፡ ሀካይ፡ የሐነክስ፡ በፍኖት፡ (መዝ፡ ፲፯። ፫ነገ፡ ፲፰፡ ፳፩። አፈ፡ ድ፴)።

**ሐንካስ፤ (ሳን፡ ሳት)፤** ዐንካሳ፡ ሽምድምድ፤ እግሩ፡ ተካክሎ፡ የማይቆም፡ የማይኼድ። ዕዉር፡ ወኢሐንካስ። ዕዉራን፡ ይሬእዩ፡ ወሐንካሳን፡ የሐውሩ። ሐንካሳን፡ ወይቡሳን፡ (ዘሌ፳፩፡ ፲፰። ማቴ፲፩፡ ፭። ዮሐ፭፡ ፫)። ተጠራጣሪ፡ ወላዋይ።

**ሕንካሴ፤** ማንከስ፤ መጠራጠር። ጥርጥር፤ ጥርጠራ። ከመ፡ ይሕየው፡ ሕንካሴክሙ፡ (ዕብ፲፪፡ ፲፫)።

**ሕንክስና ፤** ዐንካስነት ፤ ተጠራጣሪነት ። ሕንክ ስናሆሙ ፤ (፪ነገ ፡ ፳፪ ፡ ፵፮) ።

ሕንካስ ፡

**ሐንክሶ ፤** ማንከስ ፤ መጠራጠር ፤ ዐንካሳ ፡ መ ኾን ።

**ሐንክሶ ፤ (ዐረ ፡ ሐንከስ) ፤** ቖቁ ፤ የቖቁ ፡ ዕንጨት ፡ ቅጠል ፤ መዐዛው ፡ ከሩቅ ፡ የሚሸት ። ማር ያም ፡ ድንግል ፡ ምዕዝት ፡ ዘእምሐንክሶ ፡ (ደራሲ)።

**ሐንፈጠ ፤ (ዲ ቃ ፡ ግ ። ነፈጠ) ፤** ጫረ ፡ ጐ ፈጨረ ፤ ላጠ ፡ መለጠ ፤ ፊቱን ፡ ነጨ ። እመ ፡ ቦ ፡ ዘሞተ ፡ ኢተሐንፍጡ ፡ ገጸክሙ ። በአምሳለ ፡ አንስርት ፡ ወ ቋዓት ፡ እንዘ ፡ የሐነፍጡ ፡ ገጾሙ ፡ በአጽፋሪሆሙ ፤ (ፍ ፡ ነ ፡ ፵፭ ። ስንክ ፡ መስ፲፭) ። ነፈጠን ፡ እይ ።

**ሐንፈጠ ፤—ቀረጠ ፤—ኀንፈጠ ፡ ኀንፈጠ ።**

**ሐንፈጸ ፤ (ዲ ቃ ፡ ግ ። ነፍጸ) ፤** አንፈሰ ፡ አ ንዘረዘረ ፤ አዘራ ፡ አበጠረ ፤ አጐለበ ፡ አንጓለለ ። በአሰ ፡ የሐንፍጽክሙ ፡ ከመ ፡ ዐለስ ። ዘየሐነፍጸከ ፡ ሰይጣን ፤ (ሉቃ፳፪ ፡ ፴፩ ። አፈ ፡ ተ፴፩ ። ፊልክ ፡ ፻፹፱ ። አርጋ ፡ ፩)። ነፍጸንና ፡ ኀንጸጸን ፡ እይ ።

**ተሐንፈጸ ፤** ተነፈሰ ፡ ተበጠረ ፤ ተለየ ፡ ተንጓ ለለ ። ዘርዐ ፡ ሐሰስ ፡ አመ ፡ ተሐንፈጸ ፡ ይበውእ ፡ ኀበ ፡ ዘርዑ ፡ ሶበ ፡ ዘርዕዎ ፤ (አዋል) ።

**ሕንፉጽ ፤** የተነፈሰ ፤ የተንዘረዘረ ። ዕንፉጭ ፡ ግርድ ፡ ኀፋሽ ፤ ብጣሪ ።

**ሐንፈጽ ፤ (ትግሪኛ) ፤** ቅይጥ ፤ ቅልቅል ፡ ገብስና ፡ ስንዴ ፡ ዐብሮ ፡ የሚዘራ ። ሐለስትን ፡ እይ ፤ ከ ዚህ ፡ ጋራ ፡ አንድ ፡ ነው ።

**ሐኒጽ ፤ ጾት ፤ (ሐነጸ ፡ የሐንጽ ፡ ይሕ ንጽ ። ነደቀ) ፤** ማነጥ ፡ መቅረጥ ፤ መጥረብ ፤ የዋሻ ፡ የንጨት ። መሥራት ፡ መመሥረት ፡ መንደቅ ፤ የቅጥር ፡ የቤት ። ሐኒጸ ፡ ሀገር ። ንሕንጽ ፡ በእብን ። ሕንጹ ፡ አ ብያተ ፤ (ኩፋ ፡ ፲ ። ኢሳ፱ ፡ ፲ ። ፴፮ ፡ ፩) ። መፍጠር ፡ ማ ደስ ፤ ማጽናት ፡ ማበርታት ፤ እንዳይፈርስ ፡ ማድረግ ። ከመ ፡ ይሕንጽ ፡ ለከ ፡ ዘርዐ ፡ እምኔሃ ። ከመ ፡ ይሕ ንጹ ፡ መዝበራ ፡ ለጽዮን ። ለዓለም ፡ አሐንጽ ፡ ምሕ ረተ ። ሕነጸ ፡ ሥርዐተ ፡ ማኅበር ፤ (ኩፋ ፡ ፲፱ ። ዕዝ፱ ፡ ፱ ። መዝ ፡ ፹፰ ። ስንክ ፡ መስ፳፱) ።

**ሐናጺ ፤ (ጺት ፡ ጽያን ፡ ያት ፤ ነጽት) ፤** የሚያንጥ ፡ የሚቀርጥ ፡ ጠራቢ ፤ ዐናጺ ፡ ገንቢ ። ሐናጽ ያንኒ ፡ ፈጸሙ ፡ ሥነኒ ። አብጽሐ ፡ እልፈ ፡ ሐናጽያነ ፤ (ሕዝ፳፯ ፡ ፬ ። ዮሴፍ) ።

**አሕነጸ ፤** አሳነጠ ፡ አሠራ ። ምሥራብ ፡ ጣዖት ፡ ዘአሕነጸ ፡ አንጥያኮስ ፤ (ዮሴፍ) ።

**ተሐንጸ ፤** ታነጠ ፡ ተሠራ ፤ ተዘጋጀ ። አመ ፡ ትትሐነጽ ፡ ኢየሩሳሌም ። ተሐነጽክሙ ፡ ዲበ ፡ መሠ ረተ ፡ ሐዋርያት ። ለክሙ ፡ ተሠርዐ ፡ ወተሐንጸ ፡ ትፍ ሥሕት ፤ (ድጓ ። ኤፌ፪ ፡ ፳ ። ሱቱ ፡ ዕዝ፳ ፡ ፳፪) ።

**ሕኑጽ ፤ (ጻን ፡ ጻት ፡ ንጽት) ፤** የታነጠ ፡ የ ተሠራ ፤ ጥርብ ፡ ዝግጁ ። አህጉር ፡ እለ ፡ ሕኑጻት ፡ አረ ፋቲሆን ። ጥቅም ፡ ዘሕንጽት ፡ በእብነ ፡ በረድ ፤ (፪ ዜና ፡ ፳፩ ፡ ፫ ። ሔኖ፲፬ ፡ ፱) ።

**ሕንጸት ፤** ማነጥ ፡ መታነጥ ፤ አስተናነጥ ፤ ሕ ንጻ ። ዕንጨት ፡ ማለት ፡ ከዚህ ፡ የወጣ ፡ ነው ። ቀዳሚት ፡ ሕንጸታ ፡ ለኢየሩሳሌም ። ሥዩማን ፡ ላዕለ ፡ ግብረ ፡ ሕንጸት ። በመዋዕሊሁ ፡ ተፈጸመ ፡ ሕንጸታ ፡ ለቤት ። እምጊዜ ፡ ሕንጸተ ፡ ቤት ፡ ዳግማይ ፤ (ቀሌ ። ስንክ ፡ መስ፲፮ ። ጥቅ፲፮ ። ዮሴፍ) ።

**ሕንጻ ፤ (ጻት) ፤** የቤት ፡ የዋሻ ፡ ሥራ ፡ መል ክና ፡ ቅርጥ ፡ ያለው ፤ ቤት ፡ ግንብ ፡ ዋሻ ። ውሉድ ፡ ወሕንጻ ፡ ሀገር ፡ ያዐብዩ ፡ ስመ ። ሕንጻሁ ፡ ለምሥ ራብ ። አኮ ፡ ለሰብእ ፡ ዛቲ ፡ ሕንጻ ፡ ዘእንበለ ፡ ለእግዚ። አንትሙ ፡ ሕንጻ ፡ እግዚ ። አዳም ፡ ሕንጻ ፡ ላሊበላ ፡ ኢይብላዕ ፡ እምዕፀ ፤ (ሢራ፵ ፡ ፲፱ ። ማቴ፳፬ ፡ ፩ ። ፩ ዜና ፡ ፳፱ ፡ ፩ ። ፩ቆሮ ፡ ፫ ፡ ፱ ። ቅኔ) ። ድሕንጻን ፡ እይ ፤ የዚህ ፡ ዘር ፡ ነው ።

ሕንጻ ፡

**ሕንጼ ፤** ዝኒ ፡ ከማሁ ፤ ሕንጻ ፡ ሕንጸት ። ሕ ንጼሃ ፡ ወሡራሬሃ ፡ አዳም ። አመ ፡ ሕንጼሃ ፡ ለኢየሩ ሳሌም ፤ (ድጓ ። ስንክ ፡ ኅዳ፳፮) ።

**ሕንጽዋል ፤** ጌንፄ ፡ ገረማ ፡ ሲናር ፤ ዐረማሞ ፤ ክፉ ፡ ዐረም ። ህየንተ ፡ ሥርናይ ፡ ክርዳድ ፤ ወህየንተ ፡ ሰገም ፡ ሕንጽዋል ፤ (ኢዮ፴፩ ፡ ፵) ።

ሕንጽዋል ፡

**ሐንጸጸ ፤—ጠረጠረ ፤—ኀንጽጸ ፡ ኅን ጸጸ ።**

**ሐነቀ ፤ — ዐነቀ ፤ — ኀኒቅ ፡ ኀነቀ ።**

**ሐንቅቆ ፤ ቆት ፤ (ሐንቀቀ ፡ የሐነቅቅ ፡ የሐንቅቅ) ፤** መኰራት ፡ መንጠራራት ፤ ያልተሰጠውን ፡ መሻት ፤ አምጡ ፡ ውለዱ ፡ ማለት ፤ መደላደል ፡ መቀማጠል ፤ መብሰክሰክ ፡ መንቀባረር ፤ የወይዛዝርና ፡ የመኳንንት ፡ የባለጠጎች ፡ የሕፃናት ፤ ለበሽተኞችም ፡ ይኾናል ። ምስጢሩ ፡ ደሮ ፡ ዕለቡ ፡ ፀሓይ ፡ በንቅብ ፡ አግቡ ፡ እንደ ፡ ማለት ፡ ነው ። በሐንቀቀ ፡ ፈንታ ፡ ተሐንቀቀ ፡ ይላል ፤ ስሕተት ፡ ነው ። እምከመ ፡ አጽገብካ ፡ ለነፍስከ ፡ ኢትትሐንቀቅ ። ነፍስ ፡ እንተ ፡ ተሐንቀቀት ፡ ታስተጋብእ ፡ ኀቤሃ ፡ ሕማመ ፡ ኀጢአት ፡ (ማር ፡ ይሥ፲ ፡ ፱ ። ፳፰ ፡ ፫) ።

**ሕንቁቅ ፤ (ቃን ፡ ቃት ፡ ቅቅት) ፤** ኵሩ ፤ ድልድል ፡ ቅምጥል ፤ ብስክስክ ፡ እንቅብር ። (ተረት ፤ ትግራይ) ፤ ሕንቅቅት ፡ መርዓቲ ፡ እንተ ፡ ሰዐምዋ ፡ ትበኪ ።

**ሕንቃቄ ፤ (ቅያት) ፤** ክፉ ፡ ዐመል ፤ ኵራት ፤ መደላደል ፡ መቀማጠል ፤ መቅለጥ ፡ መቅበጥ ፡ መቅበጥበጥ ፤ ተድላ ፡ ሥጋንና ፡ ምግበ ፡ ሥጋን ፡ ብቻ ፡ መውደድ ። አየንን ፡ እይ ፤ የዚህ ፡ ጎር ፡ ነው ። ኢይኩን ፡ ላዕሌክሙ ፡ ነውር ፡ እኩይ ፡ ወሕንቃቄ ፤ አፍቅሮተ ፡ ተድላ ፡ ወመባልዕት ፡ ከመ ፡ ይስሐብክሙ ፡ ውስተ ፡ ፍትወተ ፡ ከንቱ ። ንኅድግ ፡ ሥላቀ ፡ ወሕንቃቄ ። ማዕርገ ፡ ሕንቃቄ ። ወይኅድግ ፡ ሕንቃቅያተ ፡ (መቃ ፡ ገ፳፱ ። አፈ ፡ ተ፳፱ ። ማር ፡ ይሥ፲ ፡ ፲፩) ።

**ሕንቅርት ፤ (ጽር ፡ ኽኔፍቲሪዮን) ፤** ከውር ፤ ያንጥረኛ ፡ አጕደ ፤ ታናሽ ፡ ጕድጓድ ፡ የከሰል ፡ ምድጃ ። ሕ ፡ ባዕድ ፡ ኹኖ ፡ ኢለበታው ፡ ገብቷል ፤ ነቄረን ፡ እይ ። ደዮ ፡ ውስተ ፡ ሕንቅርት ፡ (ዘካ፲፩ ፡ ፲፫) ። ዕብራይስጡ ፡ ግን ፡ (ሀሽሊኬሁ ፡ ኤል ፡ ሀዮጼር) ፡ ግድፎ ፡ ኀበ ፡ ለሓኵ ፡ ይላል ፤ የፈጣሪን ፡ ቦታ ፡ መቅደስንና ፡ ዐጸደ ፡ ለብሓዊን ፡ ባንድነት ፡ ያሳያል ። ፪ኛ ፡ ደግሞ ፡ በለሓኵ ፡ ፈንታ ፡ (ሀኦጻር ፡ ብሎ) ፡ መዝገብ ፤ ቤተ ፡ መዛግብት ፤ ግምጃ ፡ ቤት ፡ ሙዳየ ፡ ምጽዋት ፡ ይላል ፡ እንጂ ፡ እንጥረኛንና ፡ ከውርን ፡ አያሳይም ፡ (ማቴ፳፯ ፡ ፫—፯) ። ሀዮጼር ፡ ያለውን ፡ ሀኦጻር ፡ ማለት ፡ ዮድና ፡ አሌፍ ፡ ይዋረሳሉና ፤ ስለዚህ ፡ ነው ።

**ሐኔት ፤ — ሐሜት ፤ — ሐመ(ነ)የ ።**

**ሐኖት ፤ — የመሸታ ፡ ቤት ፤ — ሐነወ ።**

**ሐንጸን ፤ (ዐረ ፡ ሐንፋእ) ፤** ገበሎ ፡ ጕበና ፤ የዕሥሥትና ፡ የንሽላሊት ፡ ዐይነት ፡ ፬ ፡ እግር ፡ ያለው ፡ ኅራታም ፤ በግሩና ፡ በልቡ ፡ የሚኼድ ። ባለብሎዮች ፡ ግን ፡ አርጃኖ ፡ እንዝዝ ፡ ይሉታል ። ላጽቂት ፡ ወሐንጸን ፡ (ዘሌ፲፩ ፡ ፴) ።



ሐንጸን ፡

**ሐሥአ ፤ — በረደ ፤ — ኀሢዕ ፡ ኀሥዐ ።**

(፩) **ሐሠየ ፤ — ዐሸ ፤ — ሐሰይ ፡ ሐሰየ ።**

(፪) **ሐሠይ ፤ ዮት ፤ (ሐሠየ ፡ የሐሢ ፡ ይሕሢ) ፤** ማስደሰት ፤ ማሳሠይ ፤ ዕሠይ ፡ ማሰኘት ። መሠየት ፤ መኵምኰት ። ኢትሠሥዕ ፡ ለሖሉ ፡ መብልዕ ፡ ወኢተሐሢ ፡ ለሖሉ ፡ ዘርኢከ ፡ (ሢራ፴፯ ፡ ፳፱) ።

**ተሐሠየ ፤ ተሐሥየ ፤** ተደሰተ ፤ ዕሠይ ፡ አለ ። ይትፌሣሕ ፡ ሰማይ ፡ ወትትሐሠይ ፡ ምድር ። ይትሐሠዩ ፡ ብከ ። እንዘ ፡ ትትሐሠይ ፡ (ድጓ ። ኩፉ ፡ ፳፩ ። ሢራ፴፱ ፡ ፲፭) ።

**ሐሤት ፤** ዕሠይታ ፤ ፍጹም ፡ ደስታ ፤ የልብ ፡ ተድላ ፡ የሚያዘልል ፡ የሚያስፈነጭ ፤ እልል ፡ ዕሦ ፡ ዕሦ ፡ የሚያሰኝ ፤ ዕሦ ፡ ቅሉ ፡ ዕሠይ ፡ ማለት ፡ ነው ፡ (መዝ ፲፭ ። ፳ ። ፶) ።

**ሐሠከ ፤ — ዘነበ ፤ — ሐሲክ ፡ ሐሰከ ።**

**ሐሢም ፤ ሞት ፤ (ሐሠመ ፡ የሐሥም ፡ ይሕሥም ። ዐረ ፡ አሺመ ። ዕብ ፡ አሼም ፤ አበሰ) ፤** መክፋት ፡ መባስ ፤ ማደፍ ፡ መርከስ ፤ በግብር ፡ ዐሣማን ፡ መምሰል ፡ እንዳሣማ ፡ መኾን ፤ ለመልክም ፡ ይኾናል ። እስከ ፡ ሐሠመ ፡ ጺአቱ ፡ ሎቱ ። ሐሠምሙ ፡ ለሕያዋን ፡ ጼና ፡ አብድንት ። ወሶበ ፡ ሰምዐ ፡ ሐሠሞ ፡ ዝንቱ ፡ (ዮሴፍ) ። ቦ ፡ እለ ፡ የሐሥማ ፡ ውስተ ፡ ሕንጻ ። መልክ ፡ ክፉ ፡ ኹነው ፡ የሚፈጠሩ ፡ (ሄርማ ፡ ገ፹) ።

**ሕሡም ፤ (ማን ፡ ማት ፡ ሥምት) ፤** የከፋ ፡ ክፉ ፤ ጥፉ ፡ መጥፎ ፡ ቢስ ። ሕሡም ፡ ራእዮሙ ። እለ ፡ ይትሐወሱ ፡ ሕሡማን ። ምግባራት ፡ ሕሡማት ። ኢታውሥእ ፡ ሕሡመ ፡ በአፉከ ። ተአመን ፡ ከመ ፡ ሕሡም ፡ አልቦ ፡ ዘይረክበከ ። ኢይረክባ ፡ ምንትኒ ፡ ሕሡም ፡ (ዘፍ፵፩ ፡ ፲፱ ። ጥበ፲፯ ፡ ፩ ። ዮሴፍ ። ኢሳ፶፰ ፡ ፲፫ ። ሢራ፲፱ ፡ ፲ ። ፍ ፡ ነ ፡ ፳፱ ፡ ፯) ።

**ሕሠም ፤ (ማት) ፤** ክፋት ፤ ክፉነት ፡ መጥፎነት ፤ የመልክ ። ኢታስተአክዮ ፡ ለሰብእ ፡ እንበይነ ፡ ሕሠሚሁ ። ኢይክሉ ፡ ይክድኑ ፡ ሕሠሚሆሙ ፡ በተሰርግዎ ። ሕሠመ ፡ ራእየ ፡ ብእሲቱ ፡ (ሢራ፲፩ ፡ ፪ ። አፈ ፡ ተ፲፩ ። ፍ ፡ ነ ፡ ፳፱ ፡ ፩) ። ለጠባይና ፡ ለግብርም ፡ ይኾናል ። በእንተ ፡ ሕሠመ ፡ ግዕዙ ። አህ ፡ እምዘቲ ፡ ሕሠም ። ገቢረ ፡ ሕሠማት ፡ (ፍ ፡ ነ ፡ ፳፱ ። አፈ ፡ ተ፲፩ ። ፊላስ) ።

— ፤ ጥፋት ፤ ጕዳት ። ዘኢይረክቦ ፡ ሕሠም ። ኵሉ ፡ ዘይረክባ ፡ እምሕሠማት ። ኵሉ ፡ ግብረ ፡ ሕሠም ፡ (አርጋ ። ፍ ፡ ነ ፡ ፳፰ ። ዮሴፍ) ።

**ሕሥመት ፤** መክፋት ፡ ማስከፋት ፤ ክፉነት ፡ መጥፎነት ።

**አሕሠመ ፤** አከፋ ፤ አስከፋ ፤ ክፉ ፡ አደረገ ፤ ኢ ስደረገ ። አሠንዩ ፡ ወአሕሥሙ ። ኢትቅናእ ፡ ከመ ፡ ታሕሥም ። ለምንት ፡ አሕሠምከ ፡ በዝ ፡ ሕዝብ ። ኢታሕሥም ፡ ዲበ ፡ ነባሪከ ። ኢታሕሥሙ ፡ ላዕለ ፡

እሉ ። ሀኬት ፡ ወድካም ፡ አሕማምያን ፡ (ኢሳ፴፩ ፡ ፳፫ ፡ መዝ ፡ ፴፮ ፡ ዘፀ፳ ፡ ፳፱ ፡ ፳፫ ፡ ሚሬ፯ ፡ ፳ ፡ ዘፍ ፲፱ ፡ ፯ ፡ ፍ ፡ ነ ፡ ፵፫ ፡ ፱) ።

**ሐማማ፤(ማት)፤** በቁሙ ፡ ሕሪያ፤ ሕሡመ ፡ መልክእ ፡ ወመብልዕ ፡ (ዐማርኛ) ።

ሐማማ፡

**ሐሦዐ፤—በረደ፤—ኀሦዐ ።**

**ሐሠፈ፤—ሸከረ፤—ኀሠፈ ።**

**ሐሦረ፤—ጐሰቈለ፤—ኀሦረ ።**

**ሐሢር፤ ሮት፤ (ሐሠረ ፡ የሐሦር ፡ ይሕሦር ። ቀሲስ)፤** መሰብሰብ ፡ ማጓለብ ፡ ማጋበስ፤ የማር ፡ የገለባ ። መላጥ ፡ መምለጥ ፡ መቅረፍ ፡ መሸልቀቅ ፡ መፈልፈል ፡ መጠርጠር፤ የፍሬና ፡ የንቡጥ ። ማሸት ፡ መጥመቅ፤ የቈሎ ፡ የሽት ፡ የወይን ፡ የዘይት ፡ የድፍድፍ ።

**ሐሣሬ፤(ሬት ፡ ርያን ፡ ያት፤ ሠርት)፤** ገለባ ፡ አውሜ ፡ ጨ፤ ጕድፍ ፡ ጠራጊ ።

**ሐሠር፤** በቁሙ፤ ዐሠር ፡ ገለባ ፡ እብቅ ፡ ንፋሽ፤ ፍሬው ፡ የወጣለት ። ማር ፡ ድርቆሽ ፡ ቈሻሻ ፡ ጥራጊ ፡ ጕድፍ ። ክምረ ፡ ሐሠር ። ወሐሠሮሰ ፡ ያውዒ ፡ በእሳት ። ሐሠር ፡ ለገቢረ ፡ ግንፋል ። ከመ ፡ ሐሠር ፡ ዘቅድመ ፡ ገጸ ፡ ነፋስ ፡ (ሚራ፳፩ ፡ ፱ ፡ ማቴ፫ ፡ ፲፪ ፡ ዘፀ፭ ፡ ፯ ፡ ኢዮ፳፩ ፡ ፲፰) ።

**ሐፈጠ፤—መቃ ፡ ደሰቀ፤—ኀፈጥ ፡ ኀፈጠ ።**

**ሐፈን፤ ኖት፤ (ሐፈነ ፡ የሐፍን ፡ ይሕፍን ። ዐረብ ። ዕብ ፡ ሐፋን)፤** ማፈን ፡ መሸፈን፤ መዝጋት ፡ መድፈን፤ ማፈሥ ፡ መዝገን፤ መጨበጥ ፡ መጀበን፤ ባንድ ፡ ወይም ፡ በ፪ ፡ እጅ ፡ መታፈን ።

**ሕፍን፤** ዕፍኝ ፡ ጥርኝ፤ ውስጥ ፡ እጅ ፡ ዝርጉ ፡ ጠፍጣፋው ፡ ጣቶች ፡ የሚያፍኑት ፡ የሚዝጉት፤ ላንድም ፡ ለኹለትም ፡ ይኾናል ። መኑ ፡ ዘሰፈሮ ፡ ለማይ ፡ በሕፍኑ ። ሠናይ ፡ ምልአ ፡ እድ ፡ በዕረፍት ፡ እምነ ፡ ክልኤ ፡ ሕፍን ፡ በዐመፃ ። ምልአ ፡ ሕፍኑ ። ይንሣእ ፡ መጠነ ፡ ሠለስቱ ፡ ሕፍን ፡ እምነ ፡ ማይ ፡ ወይኅፅብ ፡ ርእሶ ፡ በስመ ፡ ሥላሴ ፡ (ኢሳ፵ ፡ ፲፪ ፡ መክ፬ ፡ ፮ ፡ ዘሌ፪ ፡ ፪ ፡ ፍ ፡ ነ ፡ ፫) ።

— ፤ የገንዘብ ፡ ስም ፤ ፪ ፡ ድሪም ፤ ስጢጥሬን ፡ እይ ። ቀርቡ ፡ እለ ፡ ክልኤ ፡ ሕፍነ ፡ ይነሥኡ ፡ ወይቤሉ ፡ ኢይሁብኑ ፡ ክልኤ ፡ ሕፍነ ፡ (ቄር ። ማቴ፲፯ ፡ ፳፬) ።

**ሐፈሠ፤(ሐፈነ)፤** ዐፈሠ ፡ ተረፈሰ ፤ አብዝቶ ፡ ዘገነ ፡ ዛቀ ። አነሣ ፡ ወሰደ ፤ ጠረገ ፡ አሶገደ ።

ወሐፈሦዎ ፡ በድኖ ፡ ለሳኦል ። ዐውሎ ፡ ዘየሐፍሦ ። ይነሥአሙ ፡ ዐውሎ ፡ ወየሐፍሦሙ ፡ ነፋስ ፡ (፩ዜና ፡ ፲ ፡ ፲፪ ፡ ኢሳ፲፯ ፡ ፲፫ ፡ ፶፯ ፡ ፲፫) ።

**ሐፍሦ፤(ሕፍን)፤** ዝግኝ ፡ ጥርኝ ፡ ጭብጥ ። ጥቂት ፡ ታናሽ ፡ ገንዘብ ፡ በረከት ፡ እጅ ፡ መንሻ ፡ ግብር፤ ለጣዖት ፡ ለጠንቋይ ፡ የሚሰጥ ። ይሁቡ ፡ ሐፍሠ ፡ በእንቲኣሁ ። እምዘትነሥእ ፡ ሐፍሦ ፡ (ኢሳ፰ ፡ ፳ ፡ ግብ፲፯ ፡ ፲፯) ። ኰባያ፤ ጽዋ ። ሐፍሠ ፡ ወይነ ፡ ዘቢብ ፡ (ሆሴ፫ ፡ ፩) ።

**ሐፍሦት፤ (ዕብ ፡ ሐፍሺት)፤** ነጻነት ፡ ሐራነት፤ ብቸኝነት ፡ ከሰው ፡ መለየት ። ቤተ ፡ ሐፍሦት ። የድውያን ፡ ቤት፤ ለምጻሞችና ፡ ኮብሻሞች ፡ ደዌያቸው ፡ ከሰው ፡ እንዳይናኝ ፡ ለብቻቸው ፡ የሚኖሩበት ፡ (፪ዜና ፡ ፳፮ ፡ ፳፩) ።

**ሐጽ፤—ፍላጻ፤—ሐጺጽ ፡ ሐጺ ።**

**ሐጸበ፤—ዐጠበ፤—ኀፂብ ፡ ኀፀበ ።**

**ሐጸወ፤—ሰለበ፤—ኀጺው ፡ ኀጻወ ።**

**ሐጸየ፤—ዐጨ፤—ሐፅይ ፡ ሐፀየ ።**

**ሐጺን፤—ብረት፤—ኀጺን ።**

**ሐጺጽ፤ ጾት፤ (ሐጸ፤ ሐጸጸ ፡ የሐጽጽ ፡ ይሕጽጽ ። ዕብ ፡ ሐጻጽ፤ ከፈለ)፤** መጕደል ፡ ማነስ፤ መከፈል ፡ መቀነስ፤ እኩሌታ ፡ እስከ ፡ መኾን ፡ ድረስ ። ንጠጠን ፡ እይ፤ የዚህ ፡ ጎር ፡ ነው ። ሐጸ ፡ ማይ ። የሐጽጽ ፡ ልቡ ፡ ከመ ፡ ወርኅ ። እለ ፡ የሐጽፆሙ ፡ አእምሮ ። ኢየሐጽጽ ፡ መዐተ ፡ ንጉሥ ፡ እመዐተ ፡ አንበሳ ። ኢይሕጽጽ ፡ እክልከ ። (ዘፍ፰ ፡ ፫ ፡ ሚራ፳፯ ፡ ፲፩ ፡ ምሳ፱ ፡ ፬ ፡ ፳ ፡ ፪ ፡ ኩፋ ፡ ፴፩) ።

**ሕጹጽ፤ (ጻን ፡ ጻት ፡ ጽጽት ። ዕብ ፡ ሐጺ፤ እኩሌታ)፤** ያነሰ ፡ የጐደለ፤ ታናሽ ፡ ጐደሎ፤ ደካማ ፡ ምኑን ። ሕጹጽ ፡ አነ ፡ እምነ ፡ ዐደው ፡ ጻድቃን ። ኩኑ ፡ ፍጹማነ ፡ ወአኮ ፡ ሕጹጻነ ። ብእሲት ፡ ሕጽጽት ፡ እምፍጥረተ ፡ አንስት ። አርባዕቱ ፡ ሕጹጻን ፡ ውስተ ፡ ምድር ፡ (ማር ፡ ይሥ፴፩ ፡ ግንዘ ፡ ፍ ፡ ነ ፡ ፳፱ ፡ ፯ ፡ ምሳ፳፱ ፡ ፶፱) ።

**ሕጹጻን፤** የመጽሐፍ ፡ ስም፤ ዜና ፡ መዋዕል ። ትራፋት ፡ ነገሥት ፡ ማለት ፡ ነው፤ በነገሥት ፡ የሌሉ ፡ ከነገሥት ፡ የቀሩ ፡ ጥቃቅን ፡ ቃሎች ፡ ታናናሽ ፡ ታሪኮች ፡ በላሉበት፤ ስሙ ፡ ሕጹጻን ፡ ተብሏል፤ ይኸውም ፡ ፪ ፡ ክፍል ፡ ነው ። ወክልኤቱ ፡ ሕጹጻን ። ሕጹጻን ፡ ቀዳማዊ ። ካልእ ፡ (ፍ ፡ ነ ፡ ፪ ፡ ዜና ፡ ፩ ፡ ፪) ።

**ሕጸት፤** ማነስ ፡ መጕደል፤ አጕዳደል ፡ ጐደሎነት፤ ጕድለት ። ዘእንበለ ፡ ተውሳክ ፡ ወኢሕጸት ። አልቦ ፡ ባዕለ ፡ እግዚ ፡ ተወስኮ ፡ ወኢሕጸት ። ሕጸተ ፡ አእምሮ ፡ እግዚ ። ሕጸተ ፡ ሃይማኖት ። በእንተ ፡ ሕጸተ ፡ ምክሮን ፡ ለአንስት ፡ (ዮሴፍ ። ቀሌ ። ጥበ፲፫ ፡ ፩ ። ኪዳ ። ዮሴፍ) ።

**ሑጻጼ፤** ዝኒ ፡ ከማሁ፤ መጕደል ፡ ማነስ፤ ጕድለት፤ ነውር ። ዘአልቦ ፡ ሑጻጼ ። ፍድፋዴ ፡ ወሑ

ጻጼ ። እምኢከነክሙ ፡ ሐኳጼ ፡ ወዘለፋ ፡ (አዋል ። ፍ ፡ ነ ፡ ፴፩ ። ዮሴፍ) ።

**ሕጻጽ** ፤ በቁሙ ፤ ጕዳይ ፡ ጕድለት ፤ ቅሬታ ፡ ቀሪት ፤ እንከን ፤ ስሕ ፤ ጸያፍ ። በሕጻጸ ፡ ወርኅ ። እፎ ጽም ፡ ሕጸጸ ፡ ሕማሙ ። ሕጻጸ ፡ ነፍስ ፡ ይትወለድ ፡ እምሕጻጸ ፡ አሚን ። እንከሰ ፡ ሕጻጽ ፡ ውስተ ፡ ማዐ ርገ ፡ ክህነት ፡ (ሔኖ፻፰ ፡ ፰ ። ቆላ፩ ፡ ፳፬ ። አፈ ፡ ድ ፲፱ ። ፲፫) ።

**አሕጸጸ** ፤ አጕደለ ፤ አስጕደለ ፤ አሳነሰ ፤ ከፈለ ፤ ቀነሰ ፤ ናቀ ፡ አቃለለ ። ወይቤ ፡ አሐዱ ፡ እምጸሐፍት ፡ ሐሳብ ፡ ዘሀሎ ፡ እምኍልቆሙ ፡ ለአይሁድ ፡ እለ ፡ አ ምኑ ፡ ወተጠምቁ ፡ ብእሲ ፡ ማእምረ ፡ ኦሪት ፡ ወ መጻሕፍተ ፡ ነቢያት ። ወውእቱ ፡ ቦአ ፡ ኀበ ፡ ቈስጠ ንጢኖስ ፡ ንጉሥ ፡ ወአይድዖ ፡ ከመ ፡ ካህናት ፡ አይ ሁድ ፡ አሕጸጹ ፡ እምዓመታተ ፡ ልደቶሙ ፡ ለአበው ፡ ቀደምት ፡ ዘይትዌሰክ ፡ ዐሠርተ ፡ ወኀምስተ ፡ ም እተ ፡ (ሺሕ ፡ ከ፭፻) ፡ ዓመተ ፡ ወፈቀዱ ፡ በዝንቱ ፡ ያ ብጥሉ ፡ ምጽአቶ ፡ ለክርስቶስ ። ሰብዓ ፡ ዓመተ ፡ አሕ ጸጸ ፡ እምዐሠርቱ ፡ ምእት ፡ ዓመት ። ሕቀ ፡ አሕጸጽከ ፡ እመላእክቲከ ። ግፍዐ ፡ ያሐጽጽ ፡ መዋዕለ ። ተቀጸለ ፡ ጌራ ፡ ዐቢየ ፡ አሕጺጾ ፡ ጌራ ፡ ክህነት ፡ ቅዱስ ፡ (ጊ ፡ ወ ፡ ሐ ፡ ገ፻፰፭ ። ኩፋ ፡ ፱ ። መዝ ፡ ፰ ። ፈላስ ፡ ገ፴፱ ። ዮሴፍ) ።

**ተሐጸ** ፤ **ተሓጸጸ** ፤ ተካፈለ ፡ ተከፋፈለ ፤ ተና ነሰ ፡ ተቀናነሰ ።

**ታሕጻጽ** ፤ **ታሕጻጺት** ፤ ጕዳይ ፡ ሕጸጽ ፤ ማ ነስ ፡ ታናሽነት ። በአይኒ ፡ ታሕጻጽ ፡ ወእቢድ ፡ ዘኮነ ። እለ ፡ ይኄልዩ ፡ ድካመ ፡ ወታሕጻጸ ፡ ለወልደ ፡ እ ግዚ ። አርጌንስ ፡ ይሜህር ፡ ታሕጻጸ ፡ ወልድ ፡ እም አብ ። ታሕጻጺተ ፡ ደቂቃት ፡ ኀጣውእ ፡ (ፊልክ ፡ ፶ ፫፩ ። ሃይ ፡ አበ ። መጽ ፡ ምስ ። ቀሌ) ።

**ትሕጻጼ** ፤ (**ጽያት**) ፤ መጕደል ፤ መጓደል ፤ ጕ ድለት ፡ ጕደሎነት ። በእንተ ፡ ትሕጻጼ ፡ ራእዩ ። ኮነ ፡ ሎቱ ፡ ትሕጻጼ ፡ ኅዳጥ ፡ (ፊልክ ፡ ፺ ። ፶፺፫) ።

**ትሕጽጽት** ፤ ዝኒ ፡ ከማሁ ። መፀት ፡ ምስለ ፡ ትሕጽጽተ ፡ ልቡና ፡ ይወልድ ፡ ጽዕለተ ፡ ወጽልአ ፡ ወቀቲለ ፡ (ፊልክ ፡ ፻፱) ።

**ሐጽ** ፤ (**ብ ፡ አሕጻጽ** ፤ **አሕጻ ፡ ጻት ። ዕብ ፡ ሔጽ**) ፤ ፍላጻ ፤ ስለቱ ፡ የሚፈልጥ ፡ የሚቈርጥ ፤ የሚከፍል ፤ የሚሠጥቅ ፤ በቀስት ፡ የሚነደፍ ፤ የሚወረ ወር ። ፪ኛም ፤ ፀጫር ፡ ቀጭን ፡ ታናሽ ፡ ቀላል ፤ ከዘገር ፡ ካበታ ፡ ጦር ፡ የሚያንስ ፡ ሕጹጽ ፡ ማለት ፡ ነው ። ይበ



ሐጽ ፡

ውእዋ ፡ በሐጽ ፡ ወበቀስት ። ፈነወ ፡ አሕጻሁ ፡ ወዘረ ዎሙ ። አስተዳለዉ ፡ አሕጻቲሆሙ ። ይደራበዩ ፡ በ አሕጻት ፡ (ኢሳ፯ ፡ ፳፬ ። መዝ ፡ ፲፯ ። ፲ ፡ ፪ ። ፊልክ ፡ ፶) ።

**ሐጻ** ፤—**አሸዋ ፡ ድቡሽት** ፤—**ኀዊጽ ፡ ኖጸ** ።

**ሐጺር** ፤ **ሮት** ፤ (**ሐጸረ ፡ የሐጽር ፡ ይሕ ጽር ። ዕብ ፡ ሐጻር ። ዐረ ፡ ሐጸረ**) ፤ ማጠር ፡ መ ቅጠር ፤ መከበብ ፡ ዙሪያውን ፡ መዝጋት ፡ መወሰን ፤ መ ጠበቅ ፡ መሰወር ። ሐጸሩ ፡ አርእስተ ፡ አድባር ። ሐጸ ሩኒ ፡ በሐሰት ። አሐጽር ፡ ፍኖታ ፡ በሦክ ። ሐጸሮ ፡ ለ ማይ ፡ በትእዛዙ ። ሐጸርከዋ ፡ ለባሕር ፡ በአናቅጽ ። ይሕጽርከሙ ፡ በሐጺረ ፡ መስቀሉ ፡ (ዮዲ፭ ፡ ፩ ። ሆሴ ፲፩ ፡ ፲፪ ። ፪ ፡ ፰ ። ኢዮ፳፯ ፡ ፲ ። ፴፰ ፡ ፰ ። ግንዘ) ።

**ሐጻሪ** ፤ (**ሪት ፡ ርያን ፡ ያት** ፤ **ጸርት**) ፤ የሚ ያጥር ፡ የሚከብ ፤ ዐጣሪ ፡ ከባቢ ።

**አሕጸረ** ፤ አሳጠረ ፡ አስቀጠረ ፤ ዐጥር ፡ ቅጥር ፡ አሠራ ፤ አስከበበ ።

**ተሐጽረ** ፤ ታጠረ ፡ ተከበበ ፤ ተዘጋ ፡ ተጠበቀ ። በወላትወ ፡ ነኪር ፡ ተሐጺረከ ። ፍኖትየ ፡ ተሐጽረ ፡ በ ሦክ ። ከመ ፡ ትትሐጸር ፡ በመስቀልከ ፡ (ተረ ፡ ቄር፰ ። ስንክ ፡ ኅዳ፲፯ ። ቅዳ) ።

**ሕጹር** ፤ (**ራን ፡ ራት ፡ ጽርት**) ፤ የታጠረ ፡ የተቀጠረ ፤ የተከበበ ። ሕጹር ፡ በጽጌ ። ሀገር ፡ ሕጽርት ፡ (ማሕ፯ ፡ ፫ ። ኢሳ፩ ፡ ፰) ።

**ሐጹር** ፤ (**ራት ። ዕብ ፡ ሐጼር**) ፤ ዐጥር ፡ ቅ ጥር ፡ ከለላ ፤ ወልወል ፡ ከቤት ፡ ውጭ ፡ ከቅጥር ፡ ግቢ ፡ በቤት ፡ ግራና ፡ ቀኝ ፡ ፊት ፡ ለፊት ፡ ያለ ፡ ደጅ ፡ ዐጥረ ፡ ገጥ ። ሐጹር ፡ የዐውደ ። ማይ ፡ ሐጹራ ። ደስያተ ፡ ሙሴ ፡ ወአሮን ፡ ሕዝበ ፡ እስራኤል ፤ ዘሐጹረ ፡ ገጸሙ ፡ ኮነ ፡ ፍቅረ ፡ አምልኮ ፡ ዕፀ ፡ አስራብ ፡ (ድጓ ። ናሖ፫ ፡ ፰ ። ቅኔ) ።

—፤ የሾኽ ፡ ዘለሳ ፤ በረት ፡ ዳስ ። ወገብረ ፡ ሀየ ፡ ሐጹረ ፡ ሎቱሂ ፡ ወለእንስሳሁ ፡ (ዘፍ፴፫ ፡ ፲፯) ።

— ፤ ዕርድ ፡ ምሽግ ፤ መታኰሻ ፡ ግንብ ። ትነድቅ ፡ ሐ ጹረ ፡ ላዕለ ፡ ይእቲ ፡ ሀገር ፡ እንተ ፡ ትገብር ፡ ጸብአ ፡ ምስሌከ ። ሕጽሩ ፡ ሐጹረ ፡ ውስተ ፡ ሀገር ፡ (ዘዳ፳ ፡ ፳ ። ፫ነገ ፡ ፳ ፡ ፲፪) ።

**ተሓጸረ** ፤ ተጣጠረ ፡ ተካበበ ፤ ርስ ፡ በርሱ ። እ ስመ ፡ ተሓጸራ ፡ ምስለ ፡ ቢጾን ፡ (ሄርማ ፡ ገ፱) ።

**ሐጻረ ፡ ዔናን** ፤ ስመ ፡ ሀገር ፤ የደማስቆ ፡ ክ ፍል ፤ የምድረ ፡ እስራኤል ፡ ዳርቻ ፡ (ሕዝ፵፰ ፡ ፩) ።

**ሐጽረ** ፤—**ዐጭር ፡ ሽነ** ፤—**ኀጺር ፡ ኀ ጽረ** ።

**ሕጸት** ፤—**መጕደል** ፤—**ሐጺጽ ፡ ሐጸ** ።

**ሐፅይ** ፤ **ዮት** ፤ (**ሐፀየ ፡ የሐፂ ፡ ይሕፂ ። ፈኀረ**) ፤ ማጨት ፤ ማጫ ፡ ማሥመሪያ ፡ ዐረቦን ፡ መስ ጠት ፤ የልጃገረድ ። ለአከ ፡ ንጉሥ ፡ ይሕፀያ ፡ ሎቱ ። የ ሐፂ ፡ ሕፄሃ ፡ ለአቡሃ ። ብእሲትየ ፡ እንተ ፡ ሐፀይክዋ ፡ በምእት ፡ ቍልፈት ፡ (ዮሴፍ ። ዘፀ፳፪ ፡ ፲፮ ። ፪ነገ ፡ ፫ ፡ ፲፬) ።

**ሐፃዪ፤ (ዪት፡ ይያን፡ ያት፤ ፀይት)።** የሚያጭ፤ ማጫ፡ የሚሰጥ፤ ዐጭታ።

**አሐፀየ፤** አሳጨ፤ ማጫ፡ አሰጠ።

**ተሐፀየ፤** ታጨ፤ ማጫ፡ ወሰደ፡ ተቀበለ። ድንግል፡ እንተ፡ ተሐፀየት፡ (ፍ፡ ነ፡ ፵፭። ፵፰)።

**ተሓፀየ፤** ተማጨ፤ የጋብቻ፡ ውል፡ ተዋዋለ።

**ሕፁይ፤ (ያን፡ ያት፡ ዪት)፤** የታጨ፤ የተማጨ፤ ባለጮኛ። ድንግል፡ እንተ፡ ይእቲ፡ ሕፂት፤ አው፡ ተፍኅረት፡ ለብእሲ፡ (ፈ፡ መ፡ ፯፡ ፰)።

**ሕፀየት፤** ማጨት፤ መታጨት፤ መተማጨት፤ አስተማጨት። እለ፡ ይመሥጡ፡ ወለተ፡ ሕፀየት፡ (ሕፀይተ)፡ አው፡ ዘኢተሐፀየት፡ (ፍ፡ ነ፡ ፵፰)።

**ሕፄ፤** ዝኒ፡ ከማሁ፤ ማጨት፡ መታጨት፤ ማጫ፡ መስጠት፡ መቀበል። ዕድሜ፡ ሐዘን፡ ይከልእ፡ እምአውስቦ፤ ወኢይከልእ፡ እምሕፄ፡ ወእምፍኅረት፡ (ፍ፡ ነ፡ ፳፬፡ ፱)።

—፤ ማጫ፡ መታጫ፡ የጋብቻ፡ ዐረቦን፤ ወንድ፡ ለሴት፡ አባት፡ የሚሰጠው፡ ገንዘብ። ሕፄሃ፡ ለመርዓት። እመ፡ ፈቀደ፡ ፈኃሪ፡ አው፡ ዘተፍኅረት፡ ምንዝስና፡ እምድኅረ፡ ወሀበ፡ ሕፄ፡ ይደልዎ፡ ለፈኃሪ፡ ዘወሀባ፡ ቅድመ፡ ከመ፡ ይንሣእ፤ ወለፍኅርቱኒ፡ ከመ፡ ታግብእ፡ ዘነሥአተ፡ ዘእንበለ፡ ካዕበት። ይደሉ፡ አውስቦ፡ ዘእንበለ፡ ትልወት፡ ወኢሕፄ፡ (ፍ፡ ነ፡ ፳፬፡ ፫)። ሴትም፡ ወደ፡ ባሏ፡ የምትወስደው፡ ገንዘብ፡ ሕፄ፡ ይባላል፤ መዳፊያ፡ ማለት፡ ነው። ዘጸሐፈ፡ ትእዛዘ፡ የሀብ፡ ለአዋልዲሁ፡ ለለ፡ አሐቲ፡ መክፈልተ፡ ሕፄ፡ ሆነ፡ (ፍ፡ ነ፡ ፵፭፡ ፬)።

**ሐፄ፤ (ሐፃዪ)፤** ዐጤ፤ የመንግሥት፡ ዕጮኛ፤ በዓለ፡ መንግሥት፡ ሕዝብና፡ ካህናት፡ ዘውዱን፡ ዙፋኑን፡ እንደ፡ ሙሽራ፡ ባርከው፡ መርቀው፡ የሚሰጡት፤ ተቀጽላ፡ ጽጌ፡ የሚሉት። እከ፡ በቃለ፡ ሐፄ፡ ወእከ፡ በመኳንንት፡ (ታሪ፡ አዞ)። የንግሥና፡ የተክሊል፡ ሥርዐት፡ አንድ፡ ስለ፡ ኾነ፡ ሙሽሮችም፡ በማኅላቸው፡ ወራት፡ ሐፄና፡ እቴጌ፡ ወይም፡ ንጉሥና፡ ንግሥት፡ ይባላሉ። ወይወስዱ፡ ለንጉሥ፡ ደናግለ፡ ድኅሬሃ፡ ወያበውእዎን፡ ውስተ፡ ጽርሐ፡ ንጉሥ፤ ማኅሌ፡ (መዝ፡ ፵፬)። ሐፄና፡ ዐጤ፡ ስለ፡ ማለት፡ በዐረብና፡ ባማርኛ፡ ብዙ፡ ተረትና፡ አፈ፡ ታሪክ፡ አለ።

**ሐፄጌ፤** ሐፃዪ፡ ምድር፤ ፈኃሪሃ፡ ለምድር፤ ንጉሥ፡ ምድር፡ እግዚአ፡ ምድር። ባለርስትን፡ ባለጌ፡ እንዲሉት፤ የጌን፡ አፈታት፡ እይ። ተቀጸል፡ ጽጌ፡ ሐፄጌ፡ (የድጓ፡ ግስ)።

**ሐፄጌ፤ (ማእከላይ፡ ስም)፤** ዘይቤው፡ ዕጨ፡ ዕጨጌ፤ ሹታፌ፡ ንጉሥ፤ ባለሚስ፡ መንግሥት። ምስጢሩ፡ ሊቀ፡ ሀገር፡ ሊቀ፡ ካህናት፤ ርእሰ፡ አድባራት፡ ወገዳማት። ኢትዮጵያ፡ እንደ፡ ኒቅያ፡ ሕግ፡ ትምርቱንና፡ ንጽሕናውን፡ ጠባዩንና፡ አናዎሩን፡ አስተዳደሩን፡ አይታ፡ መርምራ፤ ይደልዎ፡ ብላ፡ መርጣ፡ መስክራ፡ ባልኾመችው፡ ሌሎች፡ ከወገናቸው፡ መርጠው፡ በሚኾሙት፤ ቋንቋውን፡ በማታውቀውና፡ ቋንቋዋን፡ በማያውቅላት፡ በባዕድ፡ በንግዳ፡ በውጭ፡ አገር፡ ጳጳስ፡ ታዝ፡ ተናዝ፡ መኖርን፡ ስለ፡ ወደደች፤ ፪ኛም፡ ክብሯንና፡ መንበረ፡ ክብሯን፡ አካታ፡ ፈጽማ፡ ይቅርብኝ፡ ብላ፡ ለባዕድ፡ መስጠትን፡ ስለ፡ ጠላች፤ አፍኣዊ፡ ስሙን፡ መለካዊ፡ ወይም፡ ባስልዮስ፡ እንደ፡ ማለት፡ ሐፄጌ፡ ብላዋለች፡ እንጂ፡ ውሳጣዊ፡ ስሙ፡ ጳጳስ፡ ሊቀ፡ ጳጳስ፡ ነው። ጳጳስ፡ ሲታጣም፡ በግልጥ፡ የጳጳስ፡ ሥራ፡ እየሠራ፡ አቡንና፡ ዕጨጌ፡ ይባላል፤ ጳጳስም፡ ቢኖር፡ ላገሩ፡ እንግዳ፡ ለሕዝቡ፡ ባዳ፡ ስለ፡ ኾነ፤ አፈ፡ ድዳ፡ ቀንደ፡ ጉዳ፡ መስሎ፡ ያቀረቡለትን፡ ቅስና፡ ዲቁና፡ ከመሾም፡ በቀር፡ ሊፈርድና፡ ሊተች፡ ሊሰብክ፡ ሊያስተምር፡ አይችልምና፤ በሕዝብና፡ በካህናት፡ ላይ፡ ሥልጣኑ፡ መብቱ፡ ፍትሑ፡ ነገሥቱ፡ ወትሮ፡ የጨጌ፡ ነው። ወፈታሒሰ፡ ውእቱ፡ ሊቀ፡ ካህናት፤ ወውእቱ፡ ሊቀ፡ ጳጳሳት፤ አው፡ ኤጲስቆጶስ፤ አው፡ ዘአትለውዎ፡ እሙንቱ፡ ወረሰይዎ፡ ህየንቴሆሙ፡ በእንተ፡ ፍትሕ። ይኩን፡ ድኍነ፡ ልሳን፡ ወዘየአምር፡ ነገረ፡ ልሳን፡ እንተ፡ ኢትትከሀል፤ ልሳነ፡ ሰብእ፡ ሚመቱ፡ በዘይትናገሩ፡ በበይናቲሆሙ፡ (ፍ፡ ነ፡ ፵፫)። በዕግዕና፡ በዕጋዕ፡ ዘይቤም፡ ሲፈቱት፤ ወምስማካስ፡ ለመንግሥትክሙ፡ ውእቱ፡ ክርስቶስ፡ እንዳለው፡ ኹሉ፡ (ቈር)፡ መጨጊያ፡ መከዳ፡ ያስኛልና፤ ይህ፡ ስም፡ ዕጨግናን፡ ከጵጵስና፡ አዛምዶ፡ አዋሕዶ፡ አጣምሮ፡ አስተባብሮ፡ ያሳያል። ይኸውም፡ እንደ፡ ግራና፡ ቀኝ፡ መከዳ፡ ንጉሡን፡ አማኽለው፡ አቡኑ፡ በቀኝ፡ ዕጨጌው፡ በግራ፡ በመቀመጣቸው፡ ይታወቃል፤ አቡን፡ ሲታጣ፡ ግን፡ ቀኙ፡ የጨጌ፡ ነው። ዕጨግንትም፡ የተጀመረ፡ ባ፲፪፻፸፫(፸፫)፡ ዓመት፡ ይኩኖ፡ አምላክን፡ ቀብተው፡ ባነገሡ፡ በዳግማይ፡ ተክለ፡ ሃይማኖት፡ ነው፤ ርሳቸውም፡ በናታቸው፡ የነገሥታት፡ ወገን፡ የይኩኖ፡ አምላክ፡ ያክሥት፡ ልጅ፡ ወይም፡ የናት፡ ወንድም፡ አጎት፤ ወዲህም፡ የደብረ፡ ሊባኖስ፡ አበ፡ ምኔት፡ ነበሩ፡ ይባላል። ፊት፡ በሕግ፡ ቀብተው፡ በኋላ፡ መንኰሰው፡ አቡን፡ ስለ፡ ኾኑ፡ ያልተማሩ፡ ሰዎች፡ የማይገባ፡ መስሏቸው፤ አበ፡ ብልንት፡ ዕጨግንት፡ ከሚሰት፡ ብለዋቸዋል። ዳግማይ፡ ማለትም፡ በ፪ኛው፡ (ሴክል)፡ መቶ፡ ይሆን፡ ሐዲስ፡ ስም፡ ተክለ፡ ሃይማኖት፡ መባልን፡ እንደ፡ ያዕቆብ፡ በጌታ፡ ቃል፡ ለተሰየሙት፤ ለጻድቁና፡ ለቅዱሱ፡ ለታላቁ፡ ሐዋርያ፡ እንጂ፤ ባ፲፫ኛው፡ (ሴክል)፡ መቶ፡ መንግሥትን፡ ከድልነዓድ፡ ወስዶ፡ መዠመሪያ፡ ከዛጔ፡ ወገን፡ ለነገሠው፡ መሬ፡ ተክለ፡ ሃይማኖት፡ ለተባለው፡ ለላስታው፡ ንጉሥ፡ አይደለም። በጻድቁና፡ በጨጌው፡ መካከል፡ ያለው፡ ዘመን፡ ከ፳፻፶፱፡ ቢበልጥ፡ እንጂ፡ አያንስም፡ (ታሪክና፡ ገድል)። ጳጳስን፡ እይ።

**ሐፂን፤ ኖት፤ (ሐፀነ፡ የሐፅን፡ ይሕፅን)፤** ማቀፍ፤ ማጥባት፤ ማሳደግ፤ የልጅ። እንተ፡ ተሐፅኖ፡ ወታጠብዎ። ተሐፅነ፡ ሳራ፡ ሕፃነ። እለ፡ የሐፅና።

ወለት፡ አንተ፡ ሐፀና ። መፍትው፡ ሕዝበ፡ ክርስቲያን፡ እለ፡ አልቦሙ፡ ውሉድ፡ ይሕፀንዎሙ፡ ለዕጓለ፡ ማውታ፡ (ኵፉ፡ ፵፯ ። ዘፍ፴፩፡ ፯ ። ማቴ፴፱፡ ፲፱ ። አስቴ፪፡ ፯ ። ዲድ፡ ፲፰) ። ለንጨትና፡ ለሣር፡ ለጠጕርም፡ ይነገራል ። ማይ፡ ሐፀኖ ። ሐፂኖቱ፡ ወፀፊሮቱ፡ (ሕዝ፴፩፡ ፬ ። ፍ፡ ን፡ ፶፩) ። በሴስየ፡ ፈንታ፡ ሐፀነ፡ ይላል፤ ምስጢሩ፡ ከማጥባት፡ ይገባል ። የሐፀኖ፡ ለሚበትኪ፤ ያረጀ፡ ሰውነትሽን፡ (ሩት፬፡ ፲፭) ።

**ሐፃኒ፤ (ኒት፡ ንያን፡ ያት፤ ፀንት)፤** የሚያቅፍ፡ የሚያጠባ፤ አሳዳጊ፡ ሞግዚት ። ሐፃንያትኪ ። ወልደ፡ ሐፃኒቱ ። መምህር፡ ወሐፃኒ ። ሐፀንተ፡ ደቂቁ፡ (ኢሳ፵፱፡ ፳፫ ። ግብ፲፫፡ ፩ ። አፈ፡ ድ፴፬ ። ፬ ነገ፡ ፲፡ ፩) ።

**ተሐፅነ፤** ጠባ፡ ጠጣ፤ አደገ፤ ታቀፈ፡ ዕቅፍ፡ ኾነ ። ተሐፀንኩ፡ በጥብ ። ትትሐፀኒ፡ ሐሊበ፡ አሕዛብ ። ደቂቅ፡ እለ፡ ተሐፀኑ፡ ምስሌሁ ። ተሐፀነ፡ በሖሉ፡ ምግባረ፡ ሠናይ ። ዘከመ፡ ተሐፀንኪ፡ ውስተ፡ እዴየ፡ (ኢዮ፫፡ ፲፪ ። ኢሳ፷፡ ፲፮ ። ፪ዜና፡ ፲፡ ፰ ። ስንክ፡ ጥቅ፲፫ ። አስቴ፬፡ ፰) ።

**ሕፁን፤ (ናን፡ ናት፡ ፅንት)፤** ያደገ፡ የጠባ፤ የታቀፈ፡ በክንድ፡ የተያዘ ።

**ሕፅነት፤** ማደግ፤ ማሳደግ፤ እድገት፡ አስተዳደግ ። ለዝንቱ፡ ቅዱስ፡ ሐፀኖ፡ ሠናየ፡ ሕፅነተ፡ ቴዎፍሎስ፡ እኁወ፡ እሙ ። ዘያሤኒ፡ ሕፅነተ፡ ደቂቁ፡ (ቄር፡ ገ፪ ። ፍ፡ ነ፡ ፭) ።

**ሕፃን፤ (ናት)፤** በቁሙ፤ ዐራስ፡ ጨቅላ፤ ጡት፡ ያልተወ፡ ራሱን፡ ያልቻለ፡ ታናሽ፡ ለጋ፡ ርጥብ፡ ልጅ፡ ወንድ፤ ሴት ። ያደገውም፡ ቢኾን፡ እስኪባልቅ፡ ድረስ፡ ሕፃን፡ ይባላል፤ ደቦል፡ ጕብል፡ አሽከር፡ ብላቴና፡ ማለት፡ ነው ። ሕፃን፡ ጥብሉል ። እለ፡ ይእዜ፡ ተወልዱ፡ ሕፃናት ። ሕፃን፡ ንስቲት ። ሕፃን፡ ንኡስ ። ሕፃን፡ ውእቱ፡ ወልደ፡ ዐሠርቱ፡ ወአርባዕቱ፡ ዓመት ። ወሬዛ፡ ወሕፃን፡ (ሉቃ፪፡ ፲፪ ። ፩ጴጥ፡ ፪፡ ፪ ። ኢሳ፲፩፡ ፯፡ ፰ ። ኵፉ፡ ፲፩ ። ፩ዜና፡ ፳፱፡ ፩) ። ሕፃንና፡ ዕጣን፡ ባማርኛ፡ ይተባበራሉ፤ (ሙሾ፤ በክፉ፡ ቀን፡ ልጇን፡ እንደ፡ ድመት፡ ዐንቃ፡ የበላች፡ ሆዳም፤ ቀን፡ በወጣ፡ ጊዜ፡ ስትቄዝም)፤ አላስገባም፡ ብሎ፡ ቢያባረኝ፡ ወዳጄ፤ ክፉ፡ ቀን፡ አወጣኝ፡ የወልድኩት፡ ልጄ ። ዝባድ፡ ለመነገድ፡ ከመውረድ፡ መተማ፤ ዕጣኑ፡ ይሻላል፡ ለለት፡ እራትማ ። ዳግመኛ፡ ለመውጣት፡ በሌላ፡ መንገድ፤ ተመልሶ፡ ገባ፡ ልጅ፡ ከናቱ፡ ሆድ ። ልጅ፡ የሚችለውን፡ ዐዋቂ፡ እንዳይችል፤ በኒቆዲሞስ፡ ፊት፡ ይመስከር፡ ወንጌል ። የልጆች፡ ተረት፤ ምን፡ እናት፡ ታስጠላ፡ ድመት ።

**ሕፃንና፤** ሕፃንነት፤ ዐፍላ፡ ጕብዝና፡ ልጅነት ።

**ሕፅን፤ (ፅብ፡ ሐጼን ። ዐረ፡ ሒፅን)፤** በቁሙ፤ ማቀፊያ፡ መታቀፊያ፤ ጭን፡ ደረት፤ የደረትና፡ የእጅ፡ መካከል፤ ብብት፡ ጐን፡ ግብጣ፡ እንብርቢጣ ። የቀሚስ፡ ሠላጤ፡ በሠላጤው፡ ላይ፡ የሚሰፋ፡ ኪስ፡ ጀብ፤ ጥግ፡ ቅርብ፡ አጠገብ፤ የቦታ ። ውስተ፡ ሕፀነ፡ እሞሙ ። አንበሮሙ፡ ውስተ፡ ሕፀኑ ። ደይ፡ እዴከ፡ ውስተ፡ ሕፀንከ ። ሕፀነ፡ ልሳነ፡ ባሕር፡ (ሰቈ፪፡ ፲፪ ። ማር፲፡ ፲፯ ። ዘፀ፬፡ ፯፡ ፯ ። ኵፉ፡ ፰) ።

**ማሕፀን፤ (ናት፤ መሓፅን)፤** በቁሙ፤ የሴት፡ ሆድ፡ ከዚያውም፡ ለብቻው፡ የተለየ፡ የፅንስ፡ የሽል፡ ቦታ፤ ልጅ፡ ተፀንሶ፡ እስኪወለድ፡ የሚኖርበት ። ዕትብት፡ እየጠባ፡ የሚያድግበት ። ተዐቍረ፡ ውስተ፡ ማሕፀን ። ዘእንበለ፡ ትፃእ፡ እማሕፀን ። እንዘ፡ ባ፡ ውስተ፡ ማሕፀና ። ተሀውከ፡ ማሕፀና፡ በእንተ፡ ወልዳ፡ (ቅዳ ። ኤር፩፡ ፭ ። ማቴ፩፡ ፲፰ ። ፪ነገ፡ ፫፡ ፳፯) ።

**አማሕፀነ፤ (ዲ፡ ቃ፡ ግ)፤** አማጠነ፡ አረዳ፤ ከለከለ ። ዐደራ፡ አለ፤ ዐደራ፡ ሰጠ፡ አስጠበቀ ። ብፁር፡ ዘአማሕፀነ፡ ኀበ፡ ራጉኤል ። አማሕፀንኩክሙ፡ ፊቤንሃ፡ እኅተነ ። አባ፡ ውስተ፡ እዴከ፡ አማሕፀን፡ ነፍስየ፡ (ጦቢ፬፡ ፩ ። ሮሜ፲፮፡ ፩ ። ሉቃ፳፫፡ ፵፮) ።

**ማሕፀንት፤ (ታት)፤** ዐደራ፤ ያደራ፡ ገንዘብ፤ እንደ፡ ፅንስ፡ እንደ፡ ሽል፡ በፍጹም፡ ጥንቃቄ፡ የሚጠበቅ ። (ተረት)፤ ዐደራ፡ ጥብቅ፤ ሰማይ፡ ሩቅ ። ታገብእ፡ ምድር፡ ማሕፀንታ ። ዕቀብ፡ ማሕፀንተከ ። ኅፍረት፡ ሰሪቅ፡ እምንዋየ፡ ማሕፀንት፡ (ሔኖ፶፩፡ ፩ ። ፩ጢሞ፡ ፮፡ ፳ ። ሢራ፵፩፡ ፲፱) ።

**ተማሕፀነ፤** ተማጠነ፤ ይግባኝ፡ አለ ። ተማሕፀንኩ፡ ሎሙ፡ በቄሳር፡ (ግብ፳፭፡ ፲፩) ።

—፤ ዐደራ፡ አኖረ፤ ዐደራ፡ ተባለ፤ ጠበቀ፡ ተከናከነ፤ ዐደራውን ። ኢይፈዲ፡ ዘተማሕፀነ ። ተሰቃሒ፡ ወተማሕፃኒ ። ዘየዐቅብ፡ አፉሁ፡ ይትማሐፀን፡ ነፍሶ ። ይትማሕፀንከ፡ እምሖሉ፡ እኩይ፡ (ዘፀ፳፪፡ ፲ ። ፍ፡ ነ፡ ፴፪ ። ምሳ፲፫፡ ፫ ። ኵፉ፡ ፲፪) ።

—፤ ሸሸ፡ ተጠጋ፡ የሙጥኝ፡ አለ፤ ራሱን፡ ለሌላ፡ ዐደራ፡ ሰጠ ። ፍና፡ ኀበ፡ ይትማሐፀን፡ ቀታሊ ። ኀበ፡ መኑ፡ ትትማሐፀኑ ። ተማሕፀነ፡ ኀበ፡ ቤተ፡ ክርስቲያን፡ (ዘፀ፳፩፡ ፲፫ ። ኢሳ፲፡ ፫ ። ቀሌ) ። ይትጋባእ፡ ይረውጽ፡ በማለት፡ ፈንታ፡ ይትማሐፀን፡ ይላል፡ (ኢሳ፶፬፡ ፲፭ ። ፶፭፡ ፭) ።

**ምሕፁን፤ (ናን፡ ናት፡ ፅንት)፤** የተማጠነ፤ ሙጥኝ፡ የሙጥኝ፡ ያለ፤ የደወለ ።

**ምሕፅና፤** ምጥንታ፤ ዐደራ ። ቀሲሳን፡ እለ፡ ዐቀቡ፡ ምሕፀናሆሙ፡ በጽድቅ፡ (ቅዳ፡ ዮሐ) ።

**መምሕፅን፤ (ናን)፤** ጠባቂ፡ ባልደረባ፤ መልአክ፡ ዑቃቤ፡ (አርጋ) ።

**መምሕፃን፤** መማጠኛ፤ መሸሻ፡ መጠጊያ፡ የሙጥኝ፡ መስያ፤ ገዳም ። ድንቅ፡ ታምራት፡ የረዴት፡ ምልክት ። ነደቀ፡ ምሥዋዐ፡ ወሰመየ፡ ስሞ፡ መምሕፃን፡ (ዘፀ፲፯፡ ፲፭) ። ሽቦሌት፡ በማለት፡ ፈንታ፡ መምሕፃን፡ ይላል፤ የተሳሳተ፡ ነው፤ ሰብለን፡ እይ፡ (መሳ፲፪፡ ፯) ።

**ጠባሒ** ፤ (ሒት ፡ ሕያን ፡ ያት) ፤ የሚ ያርድ ፡ የሚበልት ፤ ዐራጅ ፡ ገፋፊ ፤ በጋማች ፡ ሥጋ ፡ ቤት ። ጠባሕያነ ፡ አልሕምት ፡ (ማር ፡ ይሥ) ።

**አጥብሐ** ፤ አሳረደ ፡ አስጠባ ፤ አስበጣ ፡ አስገፈፈ ።

**ተጠብሐ** ፤ ታረደ ፤ ተጠባ ፡ ተበለተ ፡ ተገፈፈ ። መጽአ ፡ ይጠባሕ ፡ ከመ ፡ በግዕ ። ከመ ፡ ላሕም ፡ ዘየሐውር ፡ ለተጠብሖ ፡ (ኢሳ፶፫ ፡ ፯ ። ምሳ፯ ፡ ፳፪ ። ዘኍ ፲፩ ፡ ፳፪) ።

—፤ ተበጣ ፤ ተተፈተፈ ፤ ተፈቃ ። ይጠባሕ ፡ ገጸሙ ፡ (ሕዝ፮ ፡ ፱) ።

**ጥቡሕ** ፤ (ሓን ፡ ሓት ፡ ብሕት) ፤ የታረደ ፡ የተበለተ ፤ የተበጣ ፡ ብጥ ።

**ጥብሐት** ፤ (ታት) ፤ ማረድ ፤ መታረድ ፤ አስተራረድ ፤ ዐረዳ ፡ ዕርደት ፤ ዕርድነት ። ዘያሥብሕ ፡ ላሕመ ፡ ለዕለተ ፡ ጥብሐት ፡ (ያዕ፭ ፡ ፭) ።

**ጥብሕ** ፤ (ሓት) ፤ ዕርድ ፡ ፍሪዳ ፤ መሚዕት ። ዐቢይ ፡ ጥብሕ ። ዘብሕት ፡ ዘዚኣሃ ፡ ጥብሐ ። ለእከ ፡ ያምጽኡ ፡ ለከ ፡ ሥጋ ፡ እምጥብሕከ ፡ ዘጠባሕከ ፡ በውስተ ፡ ቤትከ ። ተአዘዘ ፡ በበዓል ፡ አዕርጎ ፡ መባእ ፡ ወጥብሕ ፡ (ኢሳ፴፱ ፡ ፮ ። ምሳ፱ ፡ ፪ ። ዮሴፍ ። አርጋ ። ዘዳ፲፰ ፡ ፫) ።

**ምጥባሕ** ፤ ማረጃ ፡ ቦታ ፤ ምሚዕ ፡ መንበረ ፡ ታቦት ። ምጥባሐ ፡ ሥጋሁ ፡ ወምቅዳሐ ፡ ደሙ ፡ ለክርስቶስ ፡ (አርጋ ፡ ፯) ።

**መጥባሕት** ፤ (ብ ፡ መጣብሕ ፡ ት) ፤ ማረጃ ፡ መቍረጫ ፤ ካራ ፡ ቢላዎ ፡ ስንጢ ፤ ስለታም ፡ ብረት ፤ ጕራዴ ፡ ስለቱ ፡ ባንድ ፡ ወገን ፡ ብቻ ፡ የኾነ ፤ ወይም ፡ ፪ ፡ አፍ ፡ ያለው ፤ ሰይፍ ፡ ሾተል ፤ አፉ ፡ ጩቤ ፤ ጕዶ ፡ ዱቢት ፤ ቀሜኔ ፡ ዋልሴ ፤ ዐጥንት ፡ አይመልሴ ። መጥባሕት ፡ ዘእብን ፤ (ሱፋጭ ፡ ቡልጭት) ። መጥባሕት ፡ ዘጠባሕያነ ፡ አልሕምት ። መጥባሕት ፡ ጸሓፊ ። አነዳ ፡ ድማሁ ፡ በመጥባሕት ፡ ጠብሖ ። መጥባሕት ፡ ዘክልኤ ፡ አፉሁ ። ይጸውሩ ፡ መጥባሕት ፡ ንኡሳነ ፡ ወበሊኃነ ፡ ወየኀብእዎሙ ፡ ውስተ ፡ ልብሶሙ ። ነሥኡ ፡ መጣብሒሆሙ ፡ (ኢያ፭ ፡ ፪ ። አዋል ። ኤር፴፫ ፡ ፳፫ ። ስንክ ፡ ሐም፲፫ ። ምሳ፳ ፡ ፬ ። ዮሴፍ ። ዘፍ፴፱ ፡ ፳፭) ።



መጥባሕት ፡

**መጥባሕታዊ** ፤ የካራ ፡ ወገን ፤ የካራ ፡ ዐይነት ፡ ስለታም ። ባለካራ ፤ ባለሾተል ፤ ወይም ፡ ሃይማኖቱ ፡ ካራ ፡ የሚባል ። እሉሰ ፡ መጥባሕታውያን ፡ ይትናገሩ ፡ ፈጠራ ፡ (ምእላድ) ። የካራ ፡ ባህል ፡ ስልቱ ፡ ፩ ፡ ነው ። ፩ኛው ፤ መንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ቃል ፡ የነሣውን ፡ ሥጋ ፡ አለዘር ፡ ቢከፍልና ፡ ቢፈጥር ፡ ቅብዕ ፡ ተባለ ፡ ይላል ። ፪ኛው ፤ ከአዳም ፡ ፍዳ ፡ ስላነጻው ፡ ቅብዕ ፡ ተባለ ፡ ብሎ ፡ መጣፍ ፡ ይጠቅሳል ፡ (ሮሜ፩ ፡ ፲፱ ፡ ፲፩) ። ፫ኛው ፤ የብሉዩ ፡ ሊቀ ፡ ካህናት ፡ ፱ቱን ፡ ሽቱ ፡ ባ፩ኛ ፡ ዘይት ፡ ያዋሕዳቸው ፡ ነበረና ፤ መንፈስ ፡ ቅዱስም ፡ አዋሐጅ ፡ ስለ ፡ ኾነ ፡ ቅብዕ ፡ ተባለ ፡ ይላል ። ፬ኛው ፤ በሰውነቱ ፡ ለኛ ፡ አብነት ፡ ሊኾን ፡ ተቀባ ፡ እንጂ ፤ መቀባቱ ፡ ለርሱ ፡ አልጠቀመውም ፡ ይላል ። እነዚህ ፡ አራቱ ፡ ኹሉ ፡ መንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ቅብዕ ፡ የሚሉ ፡ ናቸው ፤ ባህላቸው ፡ ግን ፡ ገባሬ ፤ መንጽሒ ፤ ደማሪ ፤ ዘኢይረብሕ ፡ ቢያሰኝ ፡ እንጂ ፤ ቅብዕ ፡ አያሰኘውም ። ፭ኛው ፤ ወልድ ፡ ቅብዕ ፤ በሰውነቱ ፡ አምላክ ፤ ሥጋውን ፡ በተዋሕዶ ፡ ስላከበረ ፡ ቅብዕ ፡ ተባለ ፤ ተቀብዐ ፡ ማለትም ፡ ተዋሐደ ፡ ማለት ፡ ነው ፡ እንጂ ፤ እንደኛ ፡ በመንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ከበረ ፡ ተሾመ ፡ ማለት ፡ አይደለም ፡ ይላል ። ከኹሉ ፡ አስቀድሞ ፡ በሱስንዮስ ፡ ዘመን ፡ የበቀለው ፤ ኋላም ፡ በቴዎድሮስ ፡ የተሳለው ፡ ይህ ፡ ፭ኛው ፡ ነው ፤ ያንቁትም ፡ ሰዎች ፡ አዛዥ ፡ ዘድንግል ፡ አባ ፡ ክርስቶስ ፡ ይባላሉ ፤ የተሳለበትም ፡ ምክንያት ፡ ይህ ፡ ነው ። (ታሪክ) ፤ የጐንደሮች ፡ መንግሥት ፡ ዘውዱ ፡ ብቻ ፡ ሲቀር ፡ ግዛቱ ፡ ኹሉ ፡ ባ፲፯፻፷፯ ፡ ዓመት ፡ ወደ ፡ መሳፍንት ፡ ከኼደ ፡ በኋላ ፡ ራስ ፡ ወልደ ፡ ሥላሴ ፡ ትግሬን ፡ ለብቻቸው ፡ ሲገዙ ፡ በርሳቸው ፡ ዘመን ፤ ከትንቤን ፡ ከደብረ ፡ ዳሞ ፡ ከባ ፡ ገሪማ ፡ ከነዚህ ፡ ከሦስቱ ፡ አህጉር ፡ አባ ፡ ኪኑ ፡ ደብተራ ፡ በትሩ ፡ አለቃ ፡ ዐምደ ፡ መንሱት ፡ የሚባሉ ፡ ሦስት ፡ ሐሳውያን ፡ ተንሥተው ፡ ፲፪ ፡ ክሕደት ፡ ፈጥረው ፡ ጥፈው ፡ በኢትዮጵያ ፡ እንደዚህ ፡ የሚሉ ፡ ብዙ ፡ መናፍቃን ፡ ተንሥተው ፡ አስቸግረውናል ፤ የሊህም ፡ መረቻ ፡ አፋቸው ፡ የሚዘጋበት ፡ ወልድ ፡ ቅብዕ ፡ ማለት ፡ ነው ፤ ያለዚህ ፡ አይረቱምና ፡ ይህን ፡ ሃይማኖት ፡ አጽኑልን ፤ የተላከ ፡ ካ፴፱ቱ ፡ አድባራት ፡ ከጐንደር ፡ ብለው ፡ ወደ ፡ ግብጽ ፡ ላኩ ። (ተረት) ፤ የገባያ ፡ ግርግርታ ፡ ለቀጣፊ ፡ ትመቸው ። ግብጦችም ፡ ያባቶቻቸው ፡ ትምርትና ፡ ቋንቋ ፡ በተንባላት ፡ ዘመን ፡ ዕልም ፡ ድርግም ፡ ብሎ ፡ ስለ ፡ ጠፋ ፡ እውነት ፡ መስሏቸው ፡ ተቀበሉት ። «በእንተ ፡ ብዝኀ ፡ ተደምሮቶሙ ፡ ምስለ ፡ ተንባላት ፡ እስመ ፡ ጠፍአ ፡ ልሳኖሙ ፡ ቅብጥ ፡ ዘእምኔሁ ፡ የአምሩ ፡ ጽድቀ ፡ ሃይማኖቶሙ ፤ ወኮኑ ፡ ዘኢይሰምዑ ፡ ዝክረ ፡ ሥሉስ ፡ ቅዱስ ፡ ማእከሌሆሙ ፡ ዘእንበለ ፡ ኅዳጣን ፤ ወኢለወልደ ፡ እግዚ ፡ ተዘከርዎ» ፡ (ሳዊ ፡ ዘእስ ፡ ድ፲) ። ከለማበት ፡ የተጋባበት ፡ እንደሚሉት ፡ ኹሉ ፤ ከዚያ ፡ ወዲህ ፡ የመጡት ፡ ጳጳሳት ፡ እናባ ፡ ኢዮሳብ ፤ ይልቁንም ፡ ጥንተ ፡ ስማቸው ፡ ሚናስ ፡ እንድራዎስ ፡ የነበረ ፡ ቄርሎስ ፡ ሰላማ ፡ ወልድ ፡ ቅብ ፡ በማለት ፡ ጸንተው ፡ ሲሰደዱና ፡ ሲያሰድዱ ፡ ሲያሳስሩና ፡ ሲያስገርፉ ፡ ሲያስይፉ ፡ ኖሩ ፤ ከዚህ ፡ የተነሣ ፡ የግብጦች ፡ ሃይማኖት ፡ ተብሎ ፡ ባዋጅ ፡ በግዝት ፡ የማርቆስን ፡ ስም ፡ ተቀብቶ ፡ እስከ ፡ ዛሬ ፡ ነግሧል ፤ የትርጓሜውን ፡ መጥፎነት ፡ ወልድ ፡ ዋሕድ ፡ ማለትን ፡ እንዲያፈርስ ፡ በክርስቶስ ፡ ፍች ፡ ተመ

ልከት ። ምድራዊ፡እንጥረኛ፡የሠራውን፡መስቀል፡ ግብዞችና ፡ አታላዮች ፡ ከሰማይ ፡ ወርዷል ፡ እንደሚ ሉት ፡ ይህም ፡ እንደዚያ ፡ ነው ። (ተረት ፤ ስለ ፡ ቅርናታም ፡ ሴት) ፤ ወይዘሮ ፡ ስሙኝ ፡ ለማያውቁሽ ፡ ታጠኝ ። ቀድሞም ፡ በ፲፱፻ ፡ ዓመት ፥ የሽፍቶች ፡ እናት ፡ የፈላሾች ፡ እኅት ፡ ከምትኾን ፡ ከዚያች ፡ ከመንግሥ ፡ ከጕዲት ፡ በፊት ፡ እንደነዚሁ ፡ ሚናስ ፡ እንድራዎስ ፡ የሚባሉ ፡ ፪ ፡ ሐሳውያን ፡ ያውጣኪ ፡ ወገኖች ፡ መጥተው ፡ ጳጳሳት ፡ ሳይኾኑ ፡ ጳጳሳት ፡ ነን ፡ ብለው ፡ ኢትዮጵያን ፡ በሐሰት ፡ በስሕተት ፡ በክለዋታል ፤ በሰውነቱ ፡ አምላክ ፥ ፩ ፡ ባሕርይ ፥ ፩ ፡ ግብር ፡ ማለትና ፡ ልደትን ፡ በ፫፫ ፡ ማክበር ፡ በነሱ ፡ ጊዜ ፡ ተዠምሯል ። በመጨረሻውም ፡ ሐሰታቸው ፡ ታውቆ ፡ በሰይፍ ፡ ስለ ፡ ተቀጡና ፡ ወዲያው ፡ ያ ፡ ጕደኛ ፡ የጕዲት ፡ መንግሥት ፡ ስለ ፡ ተዠመረ ፡ በዚህ ፡ ምክንያት ፥ ከልጆቿ ፡ ይልቅ ፡ ባዕድ ፡ የንጀራ ፡ ልጅ ፡ የምቶደው ፡ እናታችን ፡ ኢትዮጵያ ፡ ፫ ፡ ዘመን ፡ ያኽል ፡ ያለጳጳስ ፡ ያለኤጲስቆጶስ ፡ ኑራለች ፡ (ስንክ ፡ መጋ፳) ። ፊተኞቹንና ፡ ኋለኞቹን ፡ የሚያስተባብር ፡ ምሳሌ ፤ ዘሺዬ ፡ ወልደ ፡ ምሳሌ ፤ የደብረ ፡ ሊባኖስ ፡ መነኰሴ ፤ ዘዖደ ፡ ኵሎ ፡ አድያማተ ፡ ግብጽ ፡ ወጽርአ ፡ ወሶርያ ። ሄሮድስ ፡ ወጲላጦስ ፡ ተንሥኡ ፡ ቅድመ ፡ እንበለ ፡ ፍትሕ ፡ ላዕለ ፡ አቡሁ ፡ ቀባዒ ፡ ወላዕለ ፡ ወልዱ ፡ ቅቡዕ ። ከማሆሙ ፡ ዓዲ ፡ ተንሥኡ ፡ በግፍዕ ፤ ዘእምግብጽ ፡ ሚናስ ፡ ሐሳዊ ፡ ወእንድራዎስ ፡ ጽሉእ ። ወበከመ ፡ ተሡላት ፡ እምአባግዕ ፤ ይትኀጥኡ ፡ እሉ ፡ እምይትኀጣእ ፡ ሰብእ ፤ እስመ ፡ ከኑ ፡ አርኣያ ፡ ለጸብእ ።

**ጠብጠበ**፤—ፈጠነ፤ገረፈ፤—ጠቢብ፡ ጠበ ።

**ጦብያ**፤ጦቢት፤—የሰው፡ስም፤—ጠወበ ።

**ጠባይዕ** ፤—ባሕርይ ፤—ጠቢዕ ፡ ጠብዐ ።

**ጠቢል** ፤ ሎት ፡ (ጠበለ ፡ ይጠብል ፡ ይጥብል ። ዕብ ፡ ጣበል) ፤ መነከር ፡ መዝፈቅ ፤ ገላን ፡ በውሃ ፡ ማጠብ ፡ መታጠብ ፤ ማጥመቅ ፡ መጠመቅ ። ጠመቀን ፡ እይ ፤ የዚህ ፡ ጎር ፡ ነው ።

**ጠበል** ፤ (ላት) ፤ በቁሙ ፤ የጥምቀት ፡ ውሃ ፡ የተባረከ ፡ የተጸለየበት ፤ ወይም ፡ በታምራት ፡ የፈለቀ ፡ ከደዌ ፡ የሚያድን ፡ የሚፈውስ ፤ እንደ ፡ ሚጣቅና ፡ እንዳንበ ፡ እንዳትጋፈኝ ፡ ውሃ ፡ ያለ ። ጠበለተኛ ፤ ጠበል ፡ ረጪ ፡ እንዲሉ ።

**ጠብለለ** ፤ (ተቀ ፡ ግ) ፤ ጠቀለለ ፤ ሸበለለ ፤ አሰረ ፡ ጠመጠመ ። ጠብለሉ ፡ ልብሰ ፡ ሐመር ። ወጠብለላ ፡ ለክርታስ ፡ ወንተማ ። ጠብልሎ ፡ ውስተ ፡ ክሣድከ ፡ (አፈ ፡ ተ፵፬ ። ስንክ ፡ ሚያ፳ ። ምሳ፯ ፡ ፳፩) ።

—፤ ሸፈነ ፡ አለበሰ ፤ አጐናጠፈ ፤ በልብስ ፡ ለፈፈ ። በጊሜ ፡ ጠብለልክዋ ። ወጠብለለቶ ፡ በአጽርቅት ። ጠብልሎቶሙ ፡ ለሙታን ፡ በአልባስ ፡ ሐዲሳት ፡ (ኢዮ ፴፰ ፡ ፱ ። ሉቃ፪ ፡ ፯ ። ግንዘ) ። በወግአና ፡ በቦአ ፡ ፈንታ ፡ ጠብለለ ፡ ይላል ፤ ስሕተት ፡ ነው ። ይጠበልሎን ፡ ሦክ ፡ ወአሜከላ ፡ (ሄርማ ፡ ገ፶፯) ።

**ተጠብለለ** ፤ ተጠቀለለ ፡ ተሸፈነ ፤ ተጠመጠመ ። ሰማያት ፡ ይጠበለሉ ። በአጽርቅት ፡ ተጠብለለ ። ከይሲ ፡ ተጠብለለ ፡ ውስተ ፡ ክሣዱ ፡ (ኪዳ ። ድጓ ። ስንክ ፡ ሐም፳፬) ።

**ጥብሉል** ፤ (ላን ፡ ላት ፡ ልልት) ፤ የተጠቀለለ ፤ ጥቅልል ፡ ሽፍን ። ሰበን ፡ ዘዲበ ፡ ርእሱ ፡ እንተ ፡ ባሕቲቱ ፡ ጥብሉል ። ወገጹኒ ፡ ጥብሉል ፡ በሰበን ። ጥብሉል ፡ በአጽርቅት ። የማነ ፡ እዴሁ ፡ ጥብልልት ፡ ይእቲ ፡ በኩናት ፡ (ዮሐ፳ ፡ ፯ ። ፲፩ ፡ ፵፬ ። አፈ ፡ ድ፳፯ ። ገድ ፡ ተክ) ።

**ጥብላሌ** ፤ (ላ ፡ ጥ) መጠቅለል ፡ መሸብለል ፤ መሸፈን ፤ መጠምጠም ። ጥብላሌክ ፡ በአጽርቅት ፡ (ኢርጋ ፡ ፪) ። አጠቀላለል ፤ ጥቅለላ ፡ ሽፈና ። ፅንብልን ፡ እይ ፤ የጠብለለ ፡ ዘር ፡ ነው ፤ ጠና ፡ ፀ ፡ ተወራራሾች ፡ ስለ ፡ ኾኑ ፡ ወደዚያ ፡ ኺዷል ፤ ጠንበለልም ፡ ማለት ፡ እንደ ፡ ፅንብል ፡ ከዚህ ፡ የወጣ ፡ ነው ።

**ጠቢዕ** ፤ ዖት ፤ (ጠብዐ ፡ ይጠብዕ ፡ ይጥባዕ ፤ ተብዐ ። ዕብ ፡ ጣባዕ ፤ ሰጠመ ፡ አሰጠመ) ፤ በጠባይ ፡ መውደድ ፡ መፍቀድ ፤ ቈራጥ ፡ መኾን ፡ መጨከን ፡ መድፈር ፤ መቸኰል ። ተብዐን ፡ ተመልከት ፤ የዚህ ፡ መንቲያ ፡ ነው ። ጠብዑ ፡ መላእክት ። በየዋህ ፡ ልብ ፡ ጠባዕኩ ፡ ዘንተ ፡ ኵሎ ። ተቃተሉ ፡ ጠቢያሙ ። ንጥባዕ ፡ ለመዊት ። ጥባዕኬ ፡ እኁየ ፡ ጳውሎስ ፡ (፩ዜና ፡ ፳፱ ፡ ፮ ፡ ፲፯ ። ዮሴፍ ። ድጓ) ።

—፤ ባሕርይን ፡ መመሥረት ፡ ማቆም ፤ የባሕርይን ፡ ሕግ ፡ መፈጸም ፤ ባለባሕርይ ፡ መኾን ፤ የፈጣሪና ፡ የፍጡር ። አነሰን ፡ እይ ፡ (ገድ ፡ አዳ) ። አንዳንድ ፡ መጽሐፍ ፡ ግን ፡ በጠብዐ ፡ ፈንታ ፡ አጥብዐ ፡ ይላል ፤ ስሕተት ፡ ነው ። ወአጥብዐ ፡ ዳንኤል ፡ በልቡ ፡ ከመ ፡ ኢይብላዕ ፡ እማእደ ፡ ንጉሥ ። መኑ ፡ እንከ ፡ ዘያጠብዕ ፡ ይፈጽም ፡ እደዊሁ ። ለእመ ፡ አጥባዕከ ፡ እምነፍስከ ። አጥብዕት ፡ ለተኰንኖ ። ወአጥብዑ ፡ ሕዝብ ፡ በቃለ ፡ ሕዝቅያስ ፡ (ዳን፩ ፡ ፰ ። ፩ዜና ፡ ፳፱ ፡ ፭ ። ሚራ፯ ፡ ፴፪ ። ስንክ ፡ ጥቅ፲፩ ። ፪ዜና ፡ ፴፪ ፡ ፰) ።

**ጠባዒ** ፤ ጥቡዕ ፤ (ዓን ፡ ዓት ፡ ብዕት) ፤ የወደደ ፤ የጨከነ ፡ ጨካኝ ፡ ደፋር ፤ ቈራጥ ፤ ጥኑ ፡ ጠንካራ ፤ ጠባየ ፡ ብርቱ ። ጥቡዕ ፡ ልቡ ፡ ለተወክሎ ። ብእሲ ፡ ጥቡዕ ፡ ጥቀ ። እመ ፡ ጥቡዓን ፡ አንትሙ ። ንሕነሰ ፡ ጥቡዓን ፡ ወኢንብል ፡ አሆ ። ለእመ ፡ ኮነት ፡ ጥብዕተ ፡ ለንስሓ ፡ (መዝ ፡ ፻፲፩ ። ፩ዜና ፡ ፳ ፡ ፯ ። ዳን፫ ፡ ፲፮ ። መቃ ፡ ገ፪ ። ቀሌ) ።

**ጥብዐት** ፤ (ታት) ፤ መውደድ ፤ መጨከን ፤ አጨካከን ። ጭከና ፡ ጭካኔ ፡ ድፍረት ፤ ቍርጥ ፡ ሐሳብ ። ተመይጠ ፡ ፍርሀቱ ፡ መንገለ ፡ ጥብዐት ። ጥብዐተ ፡ ኀሊናሁ ። ኣጸንዐ ፡ ጥብዐቶሙ ፡ ለዐቂበ ፡ ሃይማኖት ።

ለይቴኑ ፡ ጽንዐከ ፡ ወኀይልከ ፡ ወጥብዐታቲከ ፡ ለሞት ፡ (ስንክ ፡ ሠኔ፳ ። ኅዳ፳፰ ። ዮሴፍ) ።

**ጥብዕና** ፤ ጭከና ፤ ድፍረት ። ጨካኝነት ፡ ቈራጥነት ፡ ደፋርነት ፡ (ቈር) ።

**አጥብዐ** ፤ አሶደደ ፤ አስጨከነ ፡ አስደፈረ ፤ አጸና ፡ አበረታ ። አጥብዐ ፡ አልባቢሆሙ ። መንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ አጥብዓ ፡ ከመ ፡ ትኩን ፡ ስምዐ ። ቀድሳ ፡ ወአጥብዓ ። አጥብዖሙ ፡ ለመዋእያን ፡ ሰማዕት ። አጥብዑ ፡ ልቦሙ ፡ (፪ዜና ፡ ፴፪ ፡ ፮ ። ስንክ ፡ መስ፮ ። ኪዳ ። አርጋ ፡ ፩ ። ቀሌ) ።

**ጠባይዕ ፤ (ዓት ። ዐረ ፡ ጠቢዕ ፤ ጠቢዐት ። ዕብ ፡ ጤባዕ) ፤** በቁሙ ፤ ጠባይ ፤ ባሕርይ ፤ የፍጥረት ፡ ኹሉ ፡ ጥንት ፡ ሥር ፡ መሠረት ፤ አኳኋን ፡ ኹነታ ። ጠባይዕ ፡ ውስጠ ፡ ብዙ ፡ ነው ፤ ላንድም ፡ ለብዙም ፡ ይኾናል ። ተሐደሰ ፡ ጠባይዐ ፡ ዕጓለ ፡ መሕያው ፡ በትንግሌሁ ፡ ለመድኀኒነ ። ፍትወት ፡ እንስሳዊት ፡ እምከመ ፡ ተሠልጠት ፡ ትሬሲ ፡ ጠባይዒሁ ፡ ለብእሲ ፡ ከመ ፡ ጠባይዐ ፡ እንስሳ ። አርባዕቱ ፡ ጠባይዐ ፡ ፍጥረቱ ፡ ለአዳም ፡ ዘመሬት ፡ ወማይ ፡ ዘነፋስ ፡ ወእሳት ። እሉ ፡ እሙንቱ ፡ ጠባይዓቲሁ ፡ ለአዳም ፡ (አቡሻ ፡ ፬ ። ፈላስ ፡ ገ፲፭ ። ሳታት ። አዋል) ።

**ጠባይዕ** ፤ አካል ፤ መልክ ፡ ቁመት ፤ የባሕርይና ፡ የሥራ ፡ ባለቤት ፤ ገኸ ፡ አዛኸ ። እመ ፡ ቦ ፡ ዘይብል ፡ ክልኤቱ ፡ ጠባይዕ ፡ እምድኅረ ፡ ተዋሕዶ ። ዘረሰዮ ፡ ለክርስቶስ ፡ ክልኤተ ፡ ጠባይዓተ ። የአምኑ ፡ በአሐቲ ፡ ጠባይዕ ፡ ዘእግዚአብሔር ፡ ቃል ፡ ዘተሰብአ ። ይሬእዩ ፡ ጠባይዖ ፡ ዘስዉር ፡ እምነ ፡ ዅሉ ፤ አካሉን ፡ መልኩን ፡ (ያዕ ፡ ዘእል ። ስንክ ፡ መስ፯ ። ነሐ፳፫ ። አረጋ ፡ ድ፲፬) ። የጠባይዕ ፡ ፍች ፡ በዐረብም ፡ እንደ ፡ ህላዌ ፡ ነው ፤ ለባሕርይ ፡ በሚመችበት ፡ ባሕርይ ፤ ለአካል ፡ በሚመችበት ፡ አካል ፡ ይባላል ፡ እንጂ ፤ ፍችው ፡ ባሕርይ ፡ ብቻ ፡ አይደለም ። ይኸውም ፡ ሊታወቅ ፤ ግእዙ ፡ ህላዌ ፡ ህላውያት ፡ የሚለውን ፡ ኹሉ ፡ የዐረቡ ፡ ሃይማኖት ፡ አበው ፡ ጠቢዓ ፤ ጠቢዕቴን ፡ ይለዋል ። በአንቀጸ ፡ ተዋሕዶ ፡ ፍችው ፡ አካል ፡ ስለ ፡ ኾነ ፡ አሐዱ ፡ ህላዌ ፡ እንደ ፡ ማለት ፡ ዋሕድ ፡ ጠቢዓ ፡ ይላል ። በአንቀጸ ፡ ተፀቅቦም ፡ ፍችው ፡ ባሕርይ ፡ ስለ ፡ ኾነ ፡ ክልኤቱ ፡ እንደ ፡ ማለት ፡ ጠቢዕቴን ፡ ይለዋል ፤ ፪ ፡ ባሕርያት ፡ ማለት ፡ ነው ፤ ህላዌን ፡ ተመልከት ። ይችን ፡ የሊቃውንት ፡ ዐዋጅ ፡ ያላዩ ፡ ያልሰሙ ፡ መምራን ፡ ግን ፡ ያፌታውያንም ፡ እንዲልማን ፡ እንኳ ፡ ሳይቀሩ ፡ ያውጣኪን ፡ አሠር ፡ ተከትለው ፡ ጠባይዕን ፡ ሲተረጕሙ ፡ በቦታው ፡ ኹሉ ፡ ባሕርይ ፡ ብቻ ፡ እንጂ ፡ አካል ፡ አይሉትም ። ስለዚህ ፡ ነገር ፡ ባህላቸውና ፡ ትርጓሜያቸው ፡ ታሪካቸውና ፡ ፍቻቸው ፡ ከቋንቋ ፡ ከመጽሐፍ ፡ አይገጥምም ። ከለመግጠሙም ፡ የተነሣ ፡ ተለያይታለች ፡ ከኒሳ ፤ ይኸውም ፡ እስመ ፡ አበዊነ ፡ ሰመይዎን ፡ በዝንቱ ፡ ገጸ ፡ መካን ፡ (ሲጠባይዓት) ፡ ለህላውያት ፡ አካላተ ፡ ባለው ፡ ይታወቃል ። ጠባይዕን ፡ በአካል ፡ ቦታና ፡ በአካል ፡ ፈንታ ፡ ባሕርይ ፡ ብሎ ፡ መፍታት ፤ በመንፈስ ፡ ቦታ ፡ እንደ ፡ ገባው ፡ እንደ ፡ ወልድ ፡ ቅብዕ ፡ ምስጢራትን ፡ ኹሉ ፡ ያፈርሳል ። መዠመሪያ ፡ እንደ ፡ ሰባልዮስ ፡ ቅድስት ፡ ሥላሴን ፡ አንድ ፡ አካል ፡ ብቻ ፡ ነች ፤ ያችውም ፡ ሰው ፡ ኾነች ፡ ያሰኛል ፤ የሦስቱ ፡ አካል ፡ ባሕርይ ፤ ምንታዌ ፡ ተከፍሎ ፡ የሌለው ፡ አንድ ፡ ሥር ፤ አንድ ፡ ነቅ ፤ አንድ ፡ መለኮት ፡ ነውና ። ኹለተኛም ፡ በተለየ ፡ አካሉ ፤ በተለየ ፡ ስሙ ፡ የኛን ፡ ባሕርይ ፡ ነሥቶ ፡ ከኀጢአት ፡ በቀር ፡ እንደኛ ፡ ፍጹም ፡ ሰው ፡ ለኾነው ፡ ለዚህ ፡ ላንዱ ፡ አካል ፡ ላንዱ ፡ ልጅ ፡ በተፀቅቦ ፡ ፪ ፡ ባሕርያት ፡ ከሌሉት ፡ ባንዲት ፡ ባሕርይ ፡ ብቻ ፡ ፪ ፡ ሥራ ፡ መሥራት ፤ ኢመዋቲና ፡ መዋቲ ፡ ግዙፍና ፡ ረቂቅ ፡ መኾኑ ፤ ወልደ ፡ አብ ፡ ወልደ ፡ ማርያም ፤ ፍጹም ፡ አምላክና ፡ ፍጹም ፡ ሰው ፡ መባል ፡ አይቻልምና ፤ በግድ ፡ እንዳውጣኪ ፤ ሥጋ ፡ ወደ ፡ ቃል ፡ ባሕርይ ፡ ተለወጠ ፡ ተቀላቀለ ፡ ያሰኛል ። ተዋሕዶ ፤ ቃልና ፡ ሥጋን ፡ አንድ ፡ አካል ፡ አንድ ፡ ልጅ ፡ ቢያሰኝ ፡ እንጂ ፤ ባሕርያትንና ፡ ግብራትን ፡ ቀላቅሎ ፡ ደባልቆ ፡ አንድ ፡ ባሕርይ ፡ አንድ ፡ ግብር ፡ አያሰኝም ፤ ተፀቅቦ ፡ ይከለክለዋል ። የአካልንና ፡ የባሕርይን ፡ የተዋሕዶን ፡ ፍች ፡ ተመልከት ። (ግጥም) ፤ ዐዋቆች ፡ ካልሰጡት ፡ ማረሚያና ፡ ዐራሚ ፤ ንፍጥ ፡ ይለቀልቃል ፡ አላዋቂ ፡ ሳሚ ። ምስጢሩን ፡ ሳያውቁ ፡ መተርጐም ፡ መፍታት ፤ ደፍሮ ፡ ሳይበጡ ፡ ዐግሞ ፡ ደም ፡ እንደ ፡ ማውጣት ።

**ጠባይዓዊ** ፤ ባሕርያዊ ፤ የባሕርይ ። ንፍረቱ ፡ ጠባይዓዊ ። ሕግ ፡ ጠባይዓዊ ። እሙንቱ ፡ ኢገብሩ ፡ አውስቦ ፡ ጠባይዓዌ ፡ (ፈ ፡ መ ፡ ፲፪ ፡ ፳ ። አፈ ፡ ተ፱ ። አቡሻ ፡ ፶) ።

**ጥብዕ ፤ (ዓት) ። አው ፡ ጥብዖት ፡ (ታት) ፤** የሥራ ፡ ትእዛዝ ፤ ቍርጥ ፡ ቃል ፡ ጌታ ፡ ለሎሌው ፡ የሚሰጠው ። ኢትትማከር ፡ ምስለ ፡ ዐሱብ ፡ እንበይነ ፡ ጥብዓት ፡ (ሢራ፴፯ ፡ ፲፩) ።

— ፤ ጡብ ፤ የጡብ ፡ ሥራ ፤ ወይም ፡ ቍጥሩና ፡ ልኩ ። አምጣነ ፡ ጥብዖቶሙ ፡ ዘይገብሩ ። አልቦ ፡ ዘያሐጸክሙ ፡ እምጥብዖትክሙ ። ለምንት ፡ ኢትፌጽሙ ፡ ጥብዖትክሙ ፡ ግንፋለ ፡ (ዘፀ፭ ፡ ፰ ፡ ፲፩ ፡ ፲፬ ፡ ፲፰ ፡ ፲፱) ።

**ጠቢቅ ፤ ቆት ፤ (ጠበቀ ፡ ይጠብቅ ፡ ይጥብቅ) ፤** ዐጕልና ፡ ገቢር ። መጥበቅ ፤ መታሰር ። መጠበቅ ፤ ጠባቂ ፡ መኾን ፤ ጥብቅና ፡ መሾም ፡ (ዐማርኛ) ። መጣበቅ ፤ ጥብቅ ፡ ልጥፍ ፡ ማለት ፤ አንዱ ፡ ካንዱ ፡ ጋራ ፡ መያያዝ ፤ በችንካር ፡ በመጣብቅ ፡ በማሰሪያ ። ማጥበቅ ፤ ማጣበቅ ፡ ማስጨነቅ ፤ አጥብቆ ፡ አጣብቆ ፡ መያዝ ። ወይጡብቆ ፡ ውስተ ፡ ሐቌሁ ። ይጡብቆ ፡ ሕማም ፡ ከመ ፡ ማይ ። እመ ፡ ጠበቆ ፡ ዡያንው ። ጠበቆ ፡ ሦክ ፡ ወኀነቆ ፡ (ኢዮ፲፭ ፡ ፳፯ ። ፳፯ ፡ ፳ ። ማ፩ ፡ ፲፯ ። ማቴ፲፫ ፡ ፯) ።

— ፤ መከበብ ፤ ማጠር ፤ ምስጢሩ ፡ ከጠባቂነት ፡ ይገባል ። ወአሜሃ ፡ ተላጸቀት ፡ በበይናቲሃ ፡ ወጠበቀቶ ፡ ለሥጋ ፡ አዳም ፡ እምድኅረ ፡ ወረደ ፡ (አቡሻ ፡ ፵፯) ። በጠበቀ ፡ ፈንታ ፡ ጠፀቀ ፡ ይላል ፤ የጣፊ ፡ ስሕተት ፡ ነው ።

**አጥበቀ**፤ አጠበቀ፤ አስጠበቀ። አጣበቀ፡ ጣፈ፡ ለጠፈ፤ ቸንከረ፡ አጣመረ። አጥበቃ፡ ለምትርት፡ የማኑ። አጥበቃ፡ በምድር። ውስተ፡ አረፍት፡ አጥበቀ፡ ወጸንዖ፡ በንጺን፡ (ስንክ፡ ጥቅ፳፪። ሰቈ፪፡ ፪። ጥበ፲፫፡ ፲፭)።

**አጥበቂ**፤ **መጥብቅ**፤ በቁሙ፤ የሚያጠብቅ፤ የሚያጣብቅ፡ አጣባቂ።

**መጥበቅ፡ ት**፤ (ብ፡ **መጣብቅ፡ ት**)፤ ማጥበቂያ፤ ማጣበቂያ፡ መጣብቅ፤ ሙጫ፡ ችንካር። መጥበቅተ፡ አዕማዲሆን፡ (ዘፀ፴፯፡ ፲፭። ኢሳ፵፩፡ ፯)።

**ተጣበቀ**፤ በቁሙ፤ ተጠባበቀ፤ ተያያዘ፡ ተጣመረ። አሐዱ፡ ምስለ፡ ካልኡ፡ ተጣበቁ፤ ይጣበቁ፡ ወኢይትፋትሑ። ኩናት፡ ተጣበቀት፡ ምስለ፡ እራኁ፡ (ኢዮ፵፩፡ ፯፡ ፰። ገድ፡ ተክ)።

**ጥቡቅ**፤ (**ቃን፡ ቃት፡ ብቅት**)፤ የጠበቀ፤ የተጣበቀ፤ የገጠመ፡ የተያያዘ፤ ልክክ፡ ያለ። ሥጋ፡ ነፍስቱ፡ ጥቡቅ። እንዘ፡ ጥቡቃን፡ በክሣዶሙ። ጊዜ፡ ልደቱ፡ ለሰብእ፡ እደዊሁ፡ ጥቡቃት፡ ወዕራቁ፡ ይትወለድ። ከናፍሪሁ፡ ለዘይትሜጦ፡ ቍርባነ፡ ይኩና፡ ጥቡቃተ፡ በፍርሀት፡ ከመ፡ ኢይደቅ፡ እምኔሁ፡ ምንትኒ፡ (ኢዮ፵፩፡ ፲፬። ራእ፡ ማር። ግንዘ። ፈ፡ መ፡ ፳፯፡ ፯)።

**አስተጣበቀ**፤ አጣበቀ፡ አያያዘ፡ አጋጠመ፤ አገጣጠመ። ከመ፡ ዘያስተጣብቅ፡ አግልዕተ። አስተጣበቅዋ፡ ከመ፡ እብነ፡ ኵኵሕ። ግብር፡ ዘያስተጣብቅዎ፡ (ሚራ፳፪፡ ፯። ኢዮ፴፰፡ ፴፰። ኤር፲፡ ፲፭)።

**ጠቢስ**፤ **ሶት**፤ (**ጠበሰ**፤ **አው፡ ጠብሰ፡ ይጠብስ፡ ይጥብስ**)፤ መጥበስ፤ በእሳት፡ ማብሰል፤ ከእሳት፡ ላይ፡ መጣል፤ የሥጋ፡ የሸት። ይጠብሱ፡ ሥጋ፡ ወይበልዑ፡ ጠቢሶሙ፡ ጥብሶ። ዓሣሁኒ፡ ጠበሱ፡ ወበልዑ። ጠበሰቶ፡ በእሳት። ይጠብሱ፡ ፍሥሐ፡ በእሳት። ይጥብስዎ፡ በእሳት፤ ወአልቦ፡ ሰቢረ፡ ዐፅም፡ እምውስቴቱ፡ ምንትኒ፡ (ኢሳ፵፬፡ ፲፮፡ ፲፱። ጦቢ፮፡ ፮። ዮሴፍ። ፪ዜና፡ ፴፭፡ ፲፫። ኵፋ፡ ፵፱)።

**ተጠብሰ**፤ ተጠበሰ፤ ለእሳት፡ ተሰጠ፡ ተረመጠ፡ እስኪበስል።

**ጥቡስ**፤ (**ሳን፡ ሳት፡ ብስት**)፤ የተጠበሰ፡ ጥብስ፤ አለውሃ፡ በእሳት፡ ብቻ፡ የበሰለ። መክፈልተ፡ ዓሣ፡ ጥቡስ። ይብልዑ፡ ጥቡሰ፡ ወብሱለ፡ በእሳት፡ (ሉቃ፳፬፡ ፵፪። ኵፋ፡ ፵፱)። ጠባሳ፤ ጥብሳት፡ ዕትራት፤ ተተኵሶና፡ እሳት፡ በልቶት፡ የሻረ፡ ገላ።

**ጥብሰት**፤ መጥበስ፤ መጠበስ፤ ጥብስነት፤ አጠባበስ፡ ጠበሳ።

**ጥብሶ**፤ ጥብስ፤ ጥብሱን። ይብልዑ፡ ሥጋሁ፡ ጥብሶ፡ በእሳት፡ (ዘፀ፲፪፡ ፰፡ ፱)።

**መጥበስ፡ ት**፤ መጥበሻ፤ መጠበሻ፡ የብረት፡ ሠቅሠቅ፤ ምሢዐ፡ ብርት። መጥበስ፡ ለአፍሓም፡ ወዕፀው፡ ለእሳት። ወትገብር፡ መጥበስቶ፡ ሠቅ ሠቀ፡ ዘብርት፡ ከመ፡ መሥገርት፡ ዓሣ። ወአግብር፡ ላቲ፡ ለመጥበስት፡ አርባዕተ፡ ሕልቀታተ፡ (ምሳ፳፯፡ ፳፩። ዘፀ፳፯፡ ፬፡ ፭)።


መጥበስ፡

**ጣቢታ**፤—**ጠለየ**፤—**ጣሊታ**።

**ጣቢታ**፤—**ጠወበ**፤—**ጦቢት**።

**ጤገን**፤—**ምጣድ**፤—**ጠየገን**።

**ጠጊዕ**፤ **ዖት**፤ (**ጠግዐ፡ ይጠግዕ፡ ይጥጋዕ። ፀግዐ**፤ **ጠቅዐ**)፤ መጠጋት፡ መደገፍ፤ ጥግ፡ ደገፋ፡ መያዝ፤ ልጥቅ፡ ልጥፍ፡ ማለት፤ መጣበቅ፡ አንድ፡ መኾን። ወጠግዐት፡ በምድር፡ ከርሥነ። ይጥጋዕ፡ ልሳንየ፡ በጕርዔየ። በከመ፡ ይጠግዕ፡ ዝ፡ ሞራእ፡ ውስተ፡ ሐቌ፡ ብእሲ። እስከ፡ ይጠግዕ፡ ማእሰ፡ ሥጋሁ፡ ዲበ፡ ዐፅሙ፡ (መዝ፵፫። ፻፴፯። ኤር፲፫፡ ፲፩። ገድ፡ ተክ)።

—፤ መቆም፡ መገታት፤ መጽናት፡ መርጋት፡ ርጉዕ፡ መኾን፤ መጥበቅ፡ መድረቅ፤ የፈሳሽ። ወጠግዐ፡ ከመ፡ አረፍት፡ ማይ። በረድ፡ ወአስሐትያ፡ ዘጠግዐ። ከመ፡ አስሐትያኑ፡ ጠጋዕከ። ወትጠግዕ፡ እዴሁ፡ በእደ፡ ካልኡ፡ (ዘፀ፲፭፡ ፰። ኢዮ፮፡ ፲፮። ፲፭፡ ፯። ዘካ፲፬፡ ፲፫)።

**ጠጋዒ**፤ (**ዒት፡ ዕያን፡ ያት**)፤ የተጠጋ፤ የሚጠጋ፤ ተጠጊ፡ ጥግ፡ ፈላጊ፤ ጥገኛ።

**ጥጉዕ**፤ (**ዓን፡ ዓት፡ ግዕት**)፤ የተጠጋ፡ ጥግ፡ የያዘ፤ የተለበጠ፡ ልብጥ። ዕፀወ፡ ሰውሕ፡ ጥጉዓን፡ በአረፍት፡ (ክብ፡ ነገ፶፯)።

**አጥግዐ**፤ አስጠጋ፡ አስደገፈ፤ አጣበቀ፡ አጸና። ያጥግዕ፡ ላዕሌከ፡ ወላዕለ፡ ዘርዕከ፤ በከመ፡ መዋዕለ፡ ሰማይ፡ ዲበ፡ ምድር፡ (ኵፋ፡ ፲፱)።

**ተጣግዐ**፤ ተጣጋ፡ ተጠጋጋ፤ ተነባበረ።

**ተጣጋዒ**፤ **ጥጉዕ**፤ የተጣጋ፡ የተጠጋጋ፤ ስግስግ፡ ንብብር።

**አስተጣግዐ**፤ አጣጋ፡ አጠጋጋ፤ ሰገሰገ፡ ጽፍቅ፡ አደረገ፤ አያያዘ፡ አጣበቀ። አስተጣግዖሙ፡ ለዓሣተ፡ ፈለግከ፡ በቅሣርከ። ማህው፡ ለእመ፡ ተሰብረ፡ አልቦ፡ ዘያስተጣግዖ፡ ዘእንበለ፡ ገባሪሁ። ከመ፡ እብነ፡ ጳዝዮን፡ ዘአስተጣግዕዎ፡ በወርቅ፡ ጽሩይ። አስተጣግዑ፡ አባላቲሆሙ፡ ምስለ፡ ሥጋ፡ በግዕ። ያስተጣግዕ፡ በሾላ፡ (ሕዝ፳፱፡ ፬። ያዕ፡ ዘእል። መጽ፡ ምስ። አቡሻ፡ ፶። ኢሳ፵፩፡ ፲፫)።

**ምጥጋዕ**፤ (**ዓት**)፤ መጠጊያ፡ ማስጠጊያ፡ ቦታ። መጨጊያ፡ መከዳ፤ ድጋፍ። ዕጋዕንና፡ ምዕጋዕን፡ እይ፤ ከዚህ፡ ጋራ፡ አንድ፡ ነው።

**ጠገራ ፤ (ዐማርኛ) ፤** በቁሙ ፤ ብረት ።

**ጥድ ፤ (ዐማርኛ) ፤** በቁሙ ፤ ጽሕድ ። ጽሕ ደን ፡ እይ ።

**ጥሂር ፤ ሮት ፤ (ጠሀረ ፡ ይጥሀር ፡ ይጥ ሀር ። ዐረ ፡ ጠሁረ ። ዕብ ፡ ጣሄር) ፤** መንጻት ፤ መጥራት ፤ ከርስሐትና ፡ ከንጢአት ፡ ንጹሕ ፡ ጥሩ ፡ መ ኾን ፡ በውሃ፡ በንስሓ ፡ (ሕዝ፴፮ ፡ ፳፭) ።

**ጥሀረት ፤** ዝኒ ፡ ከማሁ ፡ (ዮሐ፫ ፡ ፳፭) ።

**ጣሀር ፤ ጥሀር ፤** ንጽሕ ፡ ጽሬት ፤ ቅድስና ፡ (ገድ ፡ አዳ) ።

**አጥሀረ ፤** አነጻ ፡ አጠራ ፤ ዐጠበ ፡ አጠመቀ ። በዘ ያጥህሩ ፡ አይሁድ ። በእንተ ፡ አጥህሮ ፡ (ዮሐ፪ ፡ ፮ ። ፫ ፡ ፳፭ ። መጽ ፡ ምስ) ።

**አጥሃሪ ፤ መጥሀር ፤** የሚያነጻ ፡ የሚያጠራ ፤ ዐጣቢ ፡ አጥማቂ ፤ ወይም ፡ ውሃ ።

**ተጣሀረ ፤** ተናጻ ፡ ተጣራ ፤ ተጣጠበ ፡ ተጠማ መቀ ። ኢትትነፀቡ ፡ ዡሎ ፡ ጊዜ ፡ ወኢትግበሩ ፡ ዘከመ ፡ ያሰምዱ ፡ ተጣህሮ ፡ (ዲድ ፡ ፴፫) ።

**ጥሁር ፤ (ራን ፡ ራት ፡ ሀርት) ፤** የነጻ ፡ የተ ናጻ ፤ የጠራ ፡ የተጣራ ፤ ንጹሕ ፡ ጥሩ ። እነዝህከሙ ፡ በማይ ፡ ጥሁር ፡ ወትጥህሩ ፡ (ሕዝ፴፮ ፡ ፳፭) ።

**ጥሀረ ፤—ጮኸ ፤—ጥሒር ፡ ጥሕረ ።**

**ጦበ ፤ ጠወበ ፤ (ጠዊብ ። ዕብ ፡ ጦብ ፤ ሡነየ) ፤** ጡብ ፡ ሠራ ፤ መሠረተ ፡ አስጌጠ ፡ አሳመረ ፤ ሥራውን ። ጡብ ፡ ጤት ፡ ጠይት ፡ ማለት ፡ ከዚህ ፡ የ ወጣ ፡ ነው ።

**ጦብያ ፤ ጦቢት ፤ (ዕብራ) ፤** የሰው ፡ ስም ፤ ሠናይ ፡ ልሑይ ፤ ጻድቅ ፡ ኄር ። መጽሐፈ ፡ ጦብያ ፡ ወልደ ፡ ጦቢት ፡ (ጦቢ፩ ፡ ፩ ። ፍ ፡ ን ፡ ፪) ።

**ጣቢታ ፤ (ሱር ፡ ጣብያእ ። ጽር ፡ ታ ቢታ ፤ ዶርከስ) ፤** ፌቆ ፤ ወይጠል ፡ እግረ ፡ ቀላል ፡ ቀ ንዳም ፡ ዘላይ ፡ ፈዊ ፤ ውብ ፡ መልክ ፡ መልካም ። ሲ በዝ ፡ ጣብያት ፡ ያሰኛል ፤ ድርቃስና ፡ ወይጠል ፡ ጣቢታ ፡ እነዚህ ፡ ሦስቱ ፡ ፩ ፡ ስም ፡ ናቸው ፡ (ግብ፱ ፡ ፴፮ ፡ ፵) ። እንጀራንም ፡ ስላይናማነቱ ፡ ጣቢታ ፡ ማለት ፡ ከዚህ ፡ ወ ጥቷል ፤ ምስጢሩ ፡ ከጡብ ፡ ይስማማል ።

**ጡበ ፤ ጦቢ ፤ (ቅብጥ ፡ ቶበ ፡ ቶቢ ። ዕብ ፡ ጤቤት) ፤** ወር ፤ የወር ፡ ስም ፤ ጥር ፡ (አቡሻ ፡ ፰) ።

**ጡጥ ፤ (ዐረ) ፤** ጥጥ ፤ የጥጥ ፡ ፈትል ። ጡጥ ፡ ርስሕት ፡ እው ፡ ሠናይት ፡ (ፊልክ ፡ ፻፶፮) ። ጠጣ ፡ ማለት ፡ ከዚህ ፡ ወጥቷል ፤ ጥጥማ ፡ ጠጉረ ፡ ጥጥ ፡ ማ ለት ፡ ነው ፤ ጠጉሯ ፡ ከርዝመቱና ፡ ከጥቍረቱ ፡ በቀር ፡ እንደ ፡ ጥጥ ፡ መኾኑን ፡ ያሳያል ፤ ጥጥንና ፡ ሐለስትዮን ፡ እይ ።

**ጠውይ ፤ ዮት ፤ (ጠወየ ፡ ይጠዊ ፡ ይ ጥወይ ። ዐረ ፡ ጠወይ ። ዕብ ፡ ጣዋሀ) ፤** ገቢርና ፡ ዐጕል ። ማከረር ፡ መፍተል ፤ ማጥመም ፡ መቈልመም ፤ ማጠፍ ፡ ማጕበጥ ፤ መጠቅለል ፡ መጠምጠም ። ይጠ ውይዋ ፡ ለጽድቅ ፡ በዐመፃሆሙ ። እጠዊ ፡ ኀሊና ሆሙ ፡ (ኢሳ፳፱ ፡ ፳፮ ። መቃ ፡ ገ፳፪) ።

—፤ መጥመም ፤ መጣመም ፤ መክፋት ፡ ጠማማ ፡ መ ኾን ። ትጠዊ ፡ እምአቅርንቲሁ ፡ ለሀየል ። ወምስለ ፡ ጠዋይ ፡ ትጠዊ ። እፌኑ ፡ ሎቱ ፡ ጠዋያነ ፡ ወይጠው ይዎ ፡ (መጽ ፡ ምስ ። መዝ ፡ ፲፯ ። ኤር፴፩ ፡ ፲፪) ። አንዳ ንድ ፡ መጽሐፍ ፡ ግን ፡ በጠወየ ፡ ፈንታ ፡ አጥወየ ፡ ተጠ ውየ ፡ ይላል ፤ ስሕተት ፡ ነው ። ዘእግዚአብሔር ፡ አጥ ወየ ። ዘያጠዊ ፡ ፍኖት ። ዐውሎሁ ፡ ለነፋስ ፡ ዐረባዊ ፡ ያጠውያ ፡ ለመንፈስ ። እስከ ፡ ይጠወይ ፡ ሥጋሁ ፡ (መክ፯ ፡ ፲፬ ። ምሳ፲፬ ፡ ፪ ። ሚራ፵፫ ፡ ፲፯ ። ስንክ ፡ መ ጋ፲፯) ።

**ጠዋይ ፤ (ያን ፡ ያት) ፤** ጠማማ ፡ ወልጋዳ ፤ ክፉ ፡ መጥፎ ። ቀስት ፡ ጠዋይ ። ዕፀ ፡ ጽኑዕ ፡ ወጠ ዋይ ። ጠዋያነ ፡ ሃይማኖት ። ፍናው ፡ ጠዋያት ። አ እባን ፡ ጠዋያት ፡ (ሆሴ፯ ፡ ፲፮ ። ጥበ፲፫ ፡ ፲፫ ። ሲኖዶ ። ምሳ፰ ፡ ፲፫ ። ሔኖ፶፱ ፡ ፩) ።

**ጥውየት ፤** መጥመም ፡ መጣመም ፤ ጥመት ፡ ክፋት ፤ ጠማምነት ። የውጣ(፲) ፡ ዘእንበለ ፡ ጥውየት ። በከመ ፡ ጥውየተ ፡ ልበሙ ፡ ይሜህሩ ፡ ቢጾሙ ። ም ንተ ፡ ርኢከ ፡ በላዕሌየ ፡ ጥውየተ ። ራትዕ ፡ ዘእንበለ ፡ ጥውየት ። ኢክህለ ፡ ጥውየቱ ፡ ከመ ፡ ይማእ ፡ ርት ዐተ ፡ ልቡ ። ስምዐ ፡ ኮነ ፡ ሎቱ ፤ አኮ ፡ በጥውየት ፡ (መጽ ፡ ምስ ። መቃ ፡ ገ፳ ። ኩፋ ፡ ፴፩ ። ቅዳ ፡ ኤጲ ። ፍ ፡ ነ ፡ ፲ ፡ ፯ ። ፈ ፡ መ ፡ ፳፭ ፡ ፫) ።

**ጥዋይ ፤** ብስና ፤ ክፉ ፡ ግማት ፡ እንደ ፡ ፈስ ፡ የሚሸት ፡ (ሚራ፴፱ ፡ ፰) ።

**ጥውዮ ፤** ጥምዝ ፡ ሥራ ፤ ጥልፍ ፡ ቍልፍ ፤ ቀለበት ። ክልኤቱ ፡ ጥበበ ፡ ጥውዮ ፡ (ዘፀ፴፮ ፡ ፳፫) ። በዕብራይስጥ ፡ ግን ፡ (ዘፀ፳፰ ፡ ፳፭) ፡ ነው ።

**አጥወየ ፤ (አስደራጊ) ፤** አስከረረ ፡ አስጠመ ዘዙ ፤ አስጠመመ ፤ አስቀለሰ ፡ አስጐነበሰ ። ልማዱ ፡ ግን ፡ አድራጊነት ፡ ነው ።

**አጥዋዪ ፤ መጥወዪ ፤** የሚያስጠምም ፡ የ ሚያስቈለምም ፤ ጠምዛዥ ፡ ቈልማሚ ። መጥወዪ ፡ ከጠ ወየና ፡ ከአጥወየ ፡ ከኹለቱ ፡ ዐምዶች ፡ ስለ ፡ ወጣ ፡ በ፪ ፡ ስልት ፡ ይፈታል ። መጥወዩ ፡ ክሣድ ፡ (ስንክ ፡ ጥር፲፭) ።

**መጥወይ ፤ (ያት ፤ መጣውይ) ፤** ማጥመ ሚያ ፡ መቈልመሚያ ፤ መጠምዘዣ ፡ ማስጠምዘዣ ። ኵነንዎ ፡ በመጥወይ ፡ ወበመጥባሕት ። እንዘ ፡ ው እቱ ፡ ሀሎ ፡ በመጥወይ ፡ ቍቡለ ፡ (ስንክ ፡ ግን፫ ። ሐም ፳፭) ። በመጥወይ ፡ ፈንታ ፡ መጥመይ ፡ ይላል ፤ የጣፊ ፡ ስሕተት ፡ ነው ። ግበር ፡ መጥመየ ፡ ወመዋሥርተ ፡ (ስንክ ፡ ጥር፲፭) ።

**ጦልሎ ፤ ሎት ፤ (ጦለለ ፡ ይጦልል ፡ ይጦልል ። ዕብ ፡ ጣሌል) ፤** መከደን ፡ ማልበስ ፡ መሸፈን ፤ የባጥ ፡ የጣራ ። ዳስ ፡ መጣል ፡ በስተላይ ፡ መጋ

ረድ፤ ጥላ፡ አጐበር፡ ማድረግ። ጸለለን፡ እይ፤ የዚህ፡ ጎር፡ ነው።

**አንጦለለ**፤ ነጠለ፤ ተረተረ። ተነጠለ፤ ተተረ ተረ። ለታጠፈ፡ ለተጠቀለለ፡ ይነገራል፤ ቤትን፡ ገራህ ትን፡ ሰፊ፡ በታን፡ ኹሉ፡ ጠላላ፡ ማለት፡ ከዚህ፡ የወጣ፡ ነው። ከመ፡ ኢያንጦልል፡ ልብሰ፡ ሎግዮን፡(ዘፀ፴፮፡ ፳፮)።

**ጦልዐ**፤ (ተቀ፡ ግ፤ ጦለለ። ዕብ፡ ጣላእ)፤ ዐ፡ የ፪ኛው፡ ለ፡ ተውላጥ፡ ነው። ጣፈ፡ ለገበ፤ ሰፋ፡ ጠቀመ፤ ቀዳዳን፡ ነገር፡ በሚመስለው፡ ቊራጭ። ለልብስና፡ ለማእስ፡ ለሚቀደድ፡ ኹሉ፡ ይነገራል፤ ፪ኛ ም፡ ለጌጥ፡ ለሽልማት፡ ለስደቃ፡ ልብስ፡ ዝንጕርጕር፡ ኹኖ፡ የሚሠራ፡ ጥልፍን፡ መረሻትን፡ ግብረ፡ መርፌን፡ ኹሉ፡ ያሳያል።

**አንጦልዐ**፤ ዘረጋ፡ ጋረደ፤ ሸፈነ። ተዘረጋ፡ ተጋረደ፤ ተሸፈነ። አርሕቢ፡ መታክለኪ፡ ወአንጦልዒ፡ ደባትረኪ። አንጦልዐ፡ ውስተ፡ ገጽየ፡ ጽልመተ። አንጦልዐ፡ ደመና፡ ወሰወሮሙ። ሶበ፡ ርእዮ፡ አ ቡሁ፡ አንጦልዐ፡ ገጸ፡ እምኔሁ፤ ወይቤሎ፡ ረሐቅ፡ እምኔየ፡(ስንክ፡ መጋ፳፪። ኢዮ፲፱፡ ፰። መዝ፻፬። ዮሴፍ)። አንጐድጐደ፥ አንበልበለ፥ አንቦሰወ፡ ብሎ፡ በአን፡ ልማድነት፡ የሚገሰስ፡ ኹሉ፡ በማድረግና፡ በመ ደረግ፡ በ፪፡ ጾታ፡ ቢፈታ፡ እንጂ፤ ተንጐድጐደ፡ ተን በልበለ፡ ተንቦሰወ፡ እንዳይል፥ ተንጦልዐ፡ አይልም። አንዳንድ፡ መጽሐፍ፡ ግን፡ በደራሲና፡ በጸሓፊ፡ ስሕተት፡ ተንጦልዐ፡ ይላል፤ አያስኼም። ሶበ፡ ተንጦልዐ፡ ሥጋሁ፡ ለኢየሱስ። በመብረቀ፡ ስብሐት፡ ተገልበበ፡ ወበ ደመና፡ እሳት፡ ተንጦልዐ። በከመ፡ ተንጦልዐ፡ ሥ ጋከ፡ ዲበ፡ ዕፀ፡ መስቀል። ተንጦልዐ፡ ኀጢአትየ፡ ማእከሌየ፡ ወማእከለ፡ እግዚ፡(መጽ፡ ምስ። ቅዳ፡ ያዕ። አርጋ፡ ፩)።

**እንጡሉዕ**፤ የተሸፈነ፡ የተጋረደ፤ ሽፍን። እንጡሉዓን፡ በመብረቀ፡ ስብሐት፡ ወግልቡባን፡ በነደ፡ እሳት። እንጡሉዕ፡ በደመና፡ እሳት፡(መጽ፡ ምስ)።

**እንጡላዔ**፤ (ላ፡ ጥ) መዘርጋት፡ መጋረድ፤ አዘረጋግ፡ አገራረድ፤ ግርደሽ። ክዱናን፡ በስዋሬ፡ ወኅ ቡኣን፡ በእንጡላዔ፡(መጽ፡ ምስ)።

**መንጦላዕት**፤ (ብ፡ መንጠዋልዕ፡ ት፡ ዓት)፤ መጋረጃ፤ ግርደሽ፡ ጥላ፡ ከለላ፤ ልብስ፡ ክዳን፤ ልባጥ፡ ሽፋን፡(ዘፀ፳፮፡ ፴፩—፴፮)። ውሳጤ፡ መንጦላ ዕት። ትከድኖሙ፡ በመንጦላዕትከ። መንጠዋልዕ፡ ዘወርቅ፡(ዕብ፮፡ ፲፱። መዝ፡ ፴። ፫ነገ፡ ፮፡ ፴፪)።

—፤ ጕርጆ፤ መከዘን፡ የዕቃና፡ የልብስ፡ የገንዘብ፡ ቤት፤ ጐተራ። ዲበ፡ መንጠዋልዕ፡ ወዲበ፡ ንጽሐ፡ ቅድ ሳት። ቤተ፡ መንጠዋልዕ፡(፩ዜና፡ ፳፫፡ ፳፰። ፪ዜና፡ ፴፩፡ ፲፩)።

**ጦሊት**፤ (ዕብ፡ ጣሊት)፤ በቁሙ፤ መጠ ብር፤ ነጠላ፡ ያንገት፡ ልብስ። ገበርባሬ፡ ባለጥቍር፡ ጥለት፤ አይሁድ፡ በጸሎት፡ ጊዜ፡ የሚለብሱት።

**ጠዊም**፤ ሞት፤ (ጦመ፡ ይጠውም፡ ይጡም)፤ ማጠፍ፤ መጠቅለል፡ መሸብለል፤ ማዞር፡ መጠምጠም፤ የመጣፍ፡ የምንጣፍ፡ የልብስ፡ የገመድ፤ ጠብለለን፡ እይ፥ የዚህ፡ ጎር፡ ነው። ነሥአ፡ ሐሜለቶ፡ ወጦማ። ወከመ፡ ሞጣሕት፡ ትጠውሞሙ፡(፬ነገ፡ ፪፡ ፰። ዕብ፡ ፩፡ ፲፪)። ወጦማ፡ ባለው፡ ወጠመ፡ ይ ላል፤ ስሕተት፡ ነው።

**ጠዋሚ**፤ መጥውም፤ የሚያጥፍ፤ ጠቅ ላይ፤ ጠምጣሚ።

**ተጠውመ**፤ ታጠፈ፡ ተጣጠፈ፤ ዕጥፍጥፍ፡ አለ፡ ተጠቀለለ። ትጠወም፡ ሰማይ፡ ከመ፡ መጽ ሐፍ። ወሰማይኒ፡ ተጠውመት፡ ከመ፡ ክርታስ፡(ኢሳ፴፬፡ ፬። ራእ፮፡ ፲፬። ሔኖ፲፡ ፳፰)።

**ጥዉም**፤ (ማን፡ ማት፡ ውምት)፤ የታጠፈ፤ የተጠቀለለ፡ ጥቅልል።

**ጥዋሜ**፤ ጡመት፤ ማጠፍ፤ መታጠፍ፤ አ ስተጣጠፍ፤ ዐጠፌታ፡ ዕጥፍነት።

**ጦማር**፤ (ራት። ጽር፡ ቶማሪዎን። ዐረ፡ ጡማር)፤ መጽሐፍ፤ ደብዳቤ፡ ከታብ፤ የመል እክትና፡ የትእዛዝ፡ የሰላምታ፡ ቃል፡ ያለበት፤ ክገር፡ ወዳገር፡ በፖስታ፡ የሚላክ፤ ወይም፡ በሰው፡ እጅ፡ የሚ ሰደድ። ንሣእ፡ ለከ፡ ጦማረ፡ ክርታስ። ወኢበጽሐ፡ እምኀቤሁ፡ ጦማረ፡ መልእክት። ተነበት፡ ጦማረ፡ ሚመቱ። ጦማረ፡ ልዮን። መጻሕፍት፡ ወጦማ ራት፡ እለ፡ ነበሩ፡ ምስሌሁ፡(ኢሳ፰፡ ፩። ፈ፡ መ፡ ፲፪፡ ፮። ስንክ፡ መስ፬ና፡ ፮። ጥቅ፳፪)። ባለቅኔዎች፡ ግን፡ ጦመረ፡ ጣፈ፡ ብለው፡ ይገሱና፤ ጦማርን፡ ከዚህ፡ ያወጣሉ።

**ጠዊዕ**፤ ዖት፤ (ጦዐ፡ ይጠውዕ፡ ይ ጡዕ። ጠወየ)፤ መሠሠት፡ መሣሣት፤ መንፈግ፡ መቈጠብ፤ መቤስ፡ መቀቀት፤ ይኸን፡ ብሰጥ፡ ምን፡ እውጥ፡ ማለት። ሀሰወ፡ ዘይብዕል፡ በብዝን፡ ጠዊዐ። ዘለነፍሱ፡ ይጠውዕ፡ ለመኑ፡ ሀለዎ፡ ይጸጉ። አልቦ፡ ዘየአክዮ፡ ለዘይጠውዕ፡ እምነፍሱ። ዐይኑ፡ ለሐ ማሚ፡ ይጠውዕ፡ እክለ፡(ሢራ፲፩፡ ፲፰። ፲፬፡ ፭፡ ፮፡ ፲። ፪ቆሮ፡ ፱፡ ፯)። ደንጸወን፡ እይ።

**ጠዋዒ**፤ (ዒት፡ ዕያን፡ ያት)፤ የሚሣሣ፤ ሥሡ፡ ሥሥታም፤ ቂቂይ፡ ንፉግ፡ ቢስ፤ ጨባጭ፡ ቈ ጣቢ። ለብእሲ፡ ጠዋዒ፡ ኢይደልዎ፡ ንዋይ። እኩይ፡ ዐይኑ፡ ጠዋዒ፡(ሢራ፲፬፡ ፫፡ ፰)።

**ጠዊቅ**፤ ቆት፤ (ጦቀ፤ ጠወቀ፡ ይጠ ውቅ፤ ይጡቅ)፤ ማስጨነቅ፡ ማስጠበብ፤ አጥብቆ፡ ማሳዘን፡ መሣቀይ፤ መቅጣት፡ መከራ፡ ማምጣት። መ ጽሐፍ፡ ግን፡ በጦቀና፡ በጠወቀ፡ ፈንታ፡ አጦቀ፡ አጠ ወቀ፡ ጠውቀየ፡ ይላል፤ ስሕተት፡ ነው። ኣጠውቃ፡ ለነፍስየ፡ ወኣገርሮ፡ ለሥጋየ። ወርእዮ፡ ንጉሥ፡ ከመ፡ ጥቀ፡ ያጠውቅዎ። ግርማከ፡ ኢያጡቅኒ። ዘአ

ጦቆ ፡ ጋኔን ። አመቅሠፍት ፡ እንተ ፡ ታጠውቅ ። ለነ ፡ ያጠውቀነ ፡ (፩ቆሮ ፡ ፱ ፡ ፳፯ ። ዳንጀ ፡ ፴ ። ኢዮ፲፫ ፡ ፳፩ ። ኪዳ ። አርጋ ፡ ፩ ። ቀሌ) ። የጦቀ ፡ ፍች ፡ ዐማርኛው ፡ እስ ፡ ስላለበት ፤ ምስጢሩ ፡ ማድረግ ፡ ማስደረግ ፡ ነውና ፤ ፪ኛ ፡ አጥወቀ ፡ አያሰኝም ።

**ተጠው(ወ)ቀ** ፤ ተጨነቀ ፤ ተጠበበ ፡ በቦታ ፤ በሐሳብ ፡ በመከራ ። ተጠውቀት ፡ በጻቄን ። ትጠወቅ ፡ ነፍስየ ። ኢይጠወቅ ፡ አሐዱ ፡ ምስለ ፡ ካልኡ ። ወተጠወቀ ፡ በሕቁ ፡ እስከ ፡ ይደዊ ። ተጠውቀ ፡ ወተዐጽበ ፡ (ዘኍ፳፪ ፡ ፳፮ ። ኢዮ፲ ፡ ፩ ። ሚራ፲፯ ፡ ፳፰ ። ፪ነገ ፡ ፲፫ ፡ ፪ ። ፊልክ ፡ ፳፫) ።

**ጥዉቅ** ፤ (ቃን ፡ ቃት ፡ ውቅት) ፤ የተጨነቀ ፤ የጨነቀው ፤ ጭንቅ ፡ የያዘው ። ኮነ ፡ ጥዉቀ ፡ እምሕዋሳቲሁ ። ተዘከር ፡ እግዚኦ ፡ ጥዉቃነ ፡ ወጽቡቃነ ። ዕደው ፡ ጥዉቃን ። ሆላ ፡ ነፍስ ፡ ምንድብት ፡ ወጥው ት ፡ (ፊልክ ፡ ፵፯ ። ግንዘ ። ኢሳ፳፰ ፡ ፲፬ ። መስተ) ።

**ጡቀት** ፤ **ጥውቀት** ፤ (ቃት) ፤ መጨነቅ ፤ ማስጨነቅ ፤ ጭንቀት ፡ ጥበት ፤ ጭንቅንት ፤ መከራ ፡ የጭንቅ ፡ ሥራ ። በእንተ ፡ ጥውቀት ፡ ዘይመጽእ ፡ ላዕሌሁ ፡ በውስተ ፡ ዓለም ። ከሠተ ፡ ሎቱ ፡ ግብረ ፡ ጥውቀቱ ፡ (ፊልክ ፡ ፭ ። ፺፬) ።

**ጥዋቄ** ፤ (ቅያት) ፤ ዝኒ ፡ ከማሁ ። ውስተ ፡ ተቃትሎ ፡ ምስለ ፡ ጥዋቄሁ ፡ (ፊልክ ፡ ፸፪) ።

**ተጣወቀ** ፤ ተጫነቀ ፡ ተጨናነቀ ፤ ተጣበበ ። ይጣወቅኑ ፡ ዓለም ፡ (ሱቱ ፡ ዕዝ፫) ። በጦቀ ፡ ፈንታ ፡ ጠውቀየ ፡ ካለ ፡ ዘንድ ፤ ይጣወቅኑ ፡ ባለው ፡ ይጠዋቀይኑ ፡ ይላል ።

**አስተጣወቀ** ፤ አጫነቀ ፤ አጨናነቀ ፤ አጋፋ ፡ አጣበበ ። (ተረት) ፤ ይጸድቅ ፡ አይጸድቅ ፡ አይታወቅ ፤ ቤተ ፡ ክሲያን ፡ ያጫንቅ ። አስተጣወቀ ፡ ባለውም ፡ አስተጠዋቀየ ፡ ይላል ፤ ፍችው ፡ አንድ ፡ ነው ።

**ጣውር** ፤ (ዕብ ፡ ጡር) ፤ ክብ ፤ ናስ ፡ ግንብ ፤ ደንጊያው ፡ የተሰደረ ፤ ስድር ፡ ድርድር ። ወጣውር ፡ ቅድሜሆሙ ፡ ለአርባዕቲሆሙ ፡ (ሕዝ፵፮ ፡ ፳፫) ።

**ጣዎስ** ፤ (ጽር ፡ ታዎስ ። ሱር ፡ ጣውሳ ። ዕብ ፡ ጣዋስ ። ዐረ ፡ ጣዉስ) ፤ ቍንጪም ፡ ወፍ ፤ ላባው ፡ ዝንጕርጕር ፡ ዐይናማ ፡ ነብርማ ፡ የኾነ ፤ ጥሩ ፡ ውብ ፡ መልክ ፡ መልካም ፤ ከመልኩ ፡ ውበት ፡ የተነሣ ፡ ግምጃ ፡ ሠሮች ፡ ኹሉ ፡ በየሶራው ፡ በየሱቲው ፡ ላይ ፡ የሚሥሉት ፡ (ስንክ ፡ ሐም፲) ። ያፌ ፡ ጣዎስ ፡ ሠናይ ፡ ውእቱ ። ጸጕረ ፡ ጣዎስ ፡ (አፈ ፡ ተ፴፪ ። ቄስጠ ፡ ፶፪) ።



ጣዎስ ፡

ልጃገረዶችም ፡ የጥምቀት ፡ ለት ፤ የሶራ ፡ ላይ ፡ ወፌ ፡ የሶራ ፡ ላይ ፤ ላይ ፡ ላዩን ፡ ነይ ፤ እያሉ ፡ ይዘፍኑበታል ።

**ጣዝማ** ፤ (ዐማርኛ) ፤ በቁሙ ፤ የጸደና ፡ ማር ፡ መድኀኒት ፡ የሚኾን ። (ተረት) ፤ ጣዝማ ፡ ይሰረስራል ፤ ዳኛ ፡ ይመረምራል ። ጸደናን ፡ እይ ።

**ጥሒል** ፤ **ሎት** ፤ (**ጠሐለ** ፤ **አው** ፤ **ጥሕለ ፡ ይጥሕል ፡ ይጥሐል**) ፤ መጣል ፤ ከውሃ ፡ ማግባት ፡ መበጥበጥ ፡ መዘለል ፤ መጥመቅ ፡ መጠጀት ፤ የማር ፡ የድፍድፍ ፡ የወይን ።

**ጠሓሊ** ፤ (**ሊት ፡ ልያን ፡ ያት** ፤ **ሐልት**) ፤ የሚጥል ፡ የሚጠምቅ ፤ ጠማቂ ።

**አጥሐለ** ፤ አስጣለ ፤ አስጠመቀ ፡ አስበጠበጠ ።

**ተጥሕለ** ፤ ተጣለ ፤ ወደቀ ፤ ተጠጀ ፡ ተጠመቀ ። ዘቀጠ ፡ አተላ ፡ ኾነ ፤ ተሰበሰበ ፡ ተከማቸ ። ውስተ ፡ መንጠፍት ፡ ይጠሐል ፡ ሐሠር ፡ (ሚራ፳፯ ፡ ፱) ።

**ጥሑል** ፤ (**ላን ፡ ላት ፡ ሕልት**) ፤ የተጣለ ፡ የወደቀ ፤ ውድቃን ፡ ውዳቂ ፡ (ገድ ፡ አዳ ፡ ገ፭ ፡ ፱ ፡ ፲፰ ፡ ፰ ፡ ፺፯) ።

**ጣሕል** ፤ (**ዐረ ፡ ጠሒል** ፤ **ጕሽ ፡ ድፍርስ**) ፤ አተላ ፡ አንብላ ፤ ዝቃጭ ፡ ትራዋጭ ፤ ገፈት ፡ ፍላቂ ፤ ሐሠር ፡ ጥማቂ ፤ የጠላ ፡ የጠጅ ፡ የወይን ፡ ያረቂ ። ምጻሕተ ፡ ወይን ፡ ዘእንበለ ፡ ጣሕል ። ወጣሕሉኒ ፡ ኢይትከዐው ፡ (መጽ ፡ ምስ ። መዝ ፡ ፸፬) ።

**ጥሕሎ** ፤ (**ትግሬኛ**) ፤ የበሶ ፡ ሊጥ ፤ እንደ ፡ ፍትፍት ፡ በገር ፡ የሚዋጥ ፡ የሚሰለቀጥ ፤ እንዳማሩ ፡ በሶ ፡ አላምጡኝ ፡ ለንቅጡኝ ፡ የማይል ። (ግጥም) ፤ ጥሕሎ ፡ ለልብ ፡ ያጠልሎ ፤ ለረኀብ ፡ ይቀትሎ ።

**ጥሒን** ፤ **ኖት** ፤ (**ጥሕነ** ፤ **ጠሐነ ፡ ይጥሕን ፡ ይጥሐን ። ዕብ ፡ ጣሐን ። ሱር ፡ ጥሓን ። ዐረ ፡ ጠሐነ**) ፤ መፍጨት ፤ ማድቀቅ ፡ መሰለቅ ። ማሸት ፤ ማፍተልተል ፡ መሰበቅ ፤ ፪ ፡ እጅን ፡ እንደ ፡ ወፍጮ ፡ ገጥሞ ። የሸት ፡ የቁሎ ፡ የንኵቶ ፤ ደሐየንና ፡ ሐረጻን ፡ እይ ።

**ጠሓኒ** ፤ (**ኒት ፡ ንያን ፡ ያት** ፤ **ሐንት**) ፤ የሚፈጭ ፤ ፈጫይ ፡ ፈጭታ ፤ ባለወፍጮ ።

**ጣሕን** ፤ (**ናት**) ፤ መፍጫ ፤ ወፍጮ ፤ መንጋጋ ።

**ጥሕን** ፤ (**ዐረ ፡ ጢሕን**) ፤ ጥሩ ፡ ደቄት ፤ ስልቅ ፡ በሶ ። ወመልእት ፡ ጽፍነታ ፡ ጥሕነ ፡ ወበለሰ ፡ (ዮዲ፲ ፡ ፭) ።

— ፤ የታሸ ፡ ቈሎ ፤ ጥብስ ፡ እሸት ። ንማእ ፡ ለእንዊክ ፡ ዘንተ ፡ መስፈርተ ፡ ጥሕን ፤ ቈሎ ። ኀምስተ ፡ መስፈርተ ፡ ጥሕን ። ወፀበጠ ፡ ላቲ ፡ ጥሕነ ፤ እሸት ፡ (፩ነገ ፡ ፲፯ ፡ ፲፯ ። ፳፭ ፡ ፲፰ ። ሩት፪ ፡ ፲፬) ።

**ጥሒር** ፤ **ሮት** ፤ (**ጥሕረ ፡ ይጥሕር ፡ ይጥሐር ። ሱር ፡ ጥሓር**) ፤ መጮኽ ፡ ማግሣት ፤ ከረኀብ ፡ ከቍጣ ፡ የተነሣ ፤ የንስሳ ፡ ያንበሳ ፡ ያራዊት ፡ ኹሉ ። ጥሕኑ ፡ ላዕሌሁ ፡ አናብስት ። በከመ ፡ ይጥሕር ፡ አንበሳ ፡ ወዕጓለ ፡ አንበሳ ። አራዊት ፡ እለ ፡ ይጥሕሩ ፡ በጥ

ራእ ፡ ቃል ፡ መፍርህ ፡ (ኤር፪ ፡ ፲፩ ። ኢሳ፴፩ ፡ ፬ ። ጥበ ፲፯ ፡ ፲፰) ።

**ጥሕረት** ፤ ዝኒ ፡ ከማሁ ፤ መጮኽ ፡ ማግሣት ፤ አጪጪኽ ፡ አገሣሥ ። ግርማ ፡ ያለው ፡ ጩኸት ፡ ግሣት ። መዐተ ፡ ንጉሥ ፡ ከመ ፡ ጥሕረተ ፡ አንበሳ ፡ (ምሳ፲፱ ፡ ፲፪) ።

**ጣሕር** ፤ ድምፀ ፡ አራዊት ፤ ጩኸት ፡ ግሣት ። ድምፀ ፡ ጣሕሩ ፡ ከመ ፡ ጣሕረ ፡ አንበሳ ፡ (ሕዝ፲፱ ፡ ፯) ።

**አጥሐረ ፤ አስተጥሐረ** ፤ አስጮኸ ፤ አስገሣ ።

**አስተጣሐረ** ፤ አጪጪኸ ፤ አጋሣ ፡ አገሣሣ ። ያስተጣሕር ፡ ነገሥተ ፡ ከመ ፡ አንበሳ ፡ (መጽ ፡ ምስ) ።

**ጥጥ** ፤ በቁሙ ፤ ያታክልት ፡ ወገን ፡ ፍሬው ፡ ቅባታም ፤ ጠጕሩ ፡ ፈትልና ፡ ልብስ ፡ የሚኾን ፤ መጠኑ ፡ ከፀምር ፡ መጠን ፡ የሚያንስ ፡ የሚቀጥን ፤ ጡጥን ፡ እይ ። ዘይትዐሰብ ፡ እንስሳ ፡ ከመ ፡ ያጼራ ፡ መክሊተ ፡ ጥጥ ፡ ኢይደልዎ ፡ ከመ ፡ ያጼራ ፡ መክሊተ ፡ ኀጺን ። ፈትለ ፡ ጥጥ ፡ (ፍ ፡ ነ ፡ ፴፯ ። ስንክ ፡ መጋ፴) ።

**ጢጢ** ፤ ዐለንጋ ፡ ጅራፍ ። ቀሠፍዎ ፡ በጢጢ ፡ (ገድ ፡ ተክ) ።

**ጢጤን** ፤ (ጽር ፡ ቲቴን) ፤ ደቅማ ፤ የደቅማ ፡ ዐይነት ፡ ዛፍ ፤ መልካም ፡ ሽታ ፡ ያለው ፡ (ኩፋ ፡ ፳፩) ።

**ጢጣኖስ ፡ ን** ፤ (ጽር ፡ ቲታኔስ) ፤ ኀያላን ፡ ነዊኃን ፤ የዔናቅ ፡ ልጆች ፤ መጠናቸው ፡ ከሰው ፡ የሚበልጥ ፤ እንደ ፡ ዖግ ፡ ንጉሠ ፡ ባሳን ፡ ያሉ ፤ ዛፍ ፡ የሚያክሉ ። ወረዱ ፡ ውስተ ፡ ቈላተ ፡ ጢጣኖስ ። አኮ ፡ ደቂቀ ፡ ጢጣኖን ፡ ዘቀተልዎሙ ፡ (፪ነገ ፡ ፳ ፡ ፲፰ ። ዮዲ ፲፯ ፡ ፳) ።

**ጤገን** ፤ (ናት ። ሱር ፡ ጢጋና ። ዐረ ፡ ጣጂን) ፤ የብረት ፡ ሉሕ ፡ ሰሌዳ ፤ ምንን ፡ ምጣድ ። ንሣእ ፡ ለከ ፡ ጤገነ ፡ ኀጺን ። ወአብአቶ ፡ በጤገኑ ። ዲበ ፡ ጤገናት ፡ ወዲበ ፡ ብሑእ ፡ (ሕዝ፬ ፡ ፫ ። ፪ነገ ፡ ፲፫ ፡ ፱ ። ፩ዜና ፡ ፳፫ ፡ ፳፱) ።

**ጤገነ** ፤ (ዐረ ፡ ጠጀነ ። ሱር ፡ ወዕብ ፡ ጣጌን) ፤ አበሰለ ፤ ቈላ ፡ ጋገረ ፤ ዐመሰ ፡ ጠበሰ ። እለ ፡ ጤገኖሙ ፡ ንጉሠ ፡ ባቢሎን ፡ በእሳት ፡ (ኤር፴፯ ፡ ፳፪) ።

—፤ ተገነ ፤ ጋረደ ። ጠገነ ፤ ዐደሰ ፡ አጸና ፤ የሰባራና ፡ ያሮጌ ፡ የድኻ ፡ የደካማ ፡ (ዐማርኛ) ።

**ጤጋኒ** ፤ አብሳይ ፤ ጋጋሪ ። የሚያድስ ፤ የሚጠግን ፡ ጠጋኝ ።

**ተጤገነ** ፤ በሰለ ፤ ተቈላ ፡ ተጋገረ ። ታደሰ ፡ ተጠገነ ።

**ጢጉን ፤ ጤጉን** ፤ የበሰለ ፡ የተጋገረ ፤ አንባሻ ፡ ዳቦ ፡ ቈሎ ፡ ዕንጕቻ ። ኅብዝተ ፡ ጤጉን ፡ (፪ነገ ፡ ፮ ፡ ፲፱) ። የታደሰ ፤ የተጠገነ ፡ ጥግን ።

**ጤግሮስ** ፤ (ጽር ፡ ቲግሩስ ። ዕብ ፡ ሔዴቄል) ፤ ስመ ፡ ፈለግ ፤ ከ፬ቱ ፡ ዐበይት ፡ አፍላጋት ፡ አንዱ ፡ ሦስተኛው ፡ ወንዝ ፤ በአሶር ፡ አገር ፡ በነነዌ ፡ ወደ ፡ ባቢሎን ፡ የሚፈስ ፤ ከኤፍራጥስ ፡ ገጥሞ ፡ ወደ ፡ ባሕረ ፡ ፋርስ ፡ ወደ ፡ ህንድ ፡ ውቅያኖስ ፡ የሚገባ ። ሔዴቄል ፤ በሊኅ ፡ ማይ ፡ ጽሩየ ፡ ማይ ፡ ቀሊለ ፡ ማይ ፡ ማለት ፡ ነው ፤ በሊኅ ፡ ፍጥነትን ፡ ያሳያል ፡ (ዘፍ፪ ፡ ፲፬) ።

**ጢግሩስ ፤ ጢግሪስ** ፤ (ዕብራ) ፤ ታላቅ ፡ ነብር ፤ በወንዝ ፡ ዳር ፡ በባሕር ፡ ጠረፍ ፡ የሚኖር ፤ ቍጡ ፡ ብስጩ ፡ ክፉ ፡ ጨካኝ ። እንደ ፡ ፏፏቴ ፡ የሚዘል ፡ የሚወረወር ፤ ቀላልና ፡ ፈጣን ፡ ስለ ፡ ኾነ ፡ ስሙን ፡ ከውሃ ፡ ወሰዲል ። ቲግርን ፡ እይ ፤ ከዚህ ፡ ጋራ ፡ ፩ ፡ ነው ።

**ጠዩዕ ፤ ዖት** ፤ (ጤዐ ፡ ይጠይዕ ፡ ይጢዕ ። ዕብ ፡ ጡዋሕ ። ዐረ ፡ ጣኅ) ፤ መምረግ ፡ መለሰን ፤ በጭቃ ፡ መዝጋት ፡ መድፈን ፤ የዠሮ ። ጤዑ ፡ እዘኒሆሙ ፡ ከመ ፡ ኢይስምዑ ፡ (ኢሳ ፡ ፯ ፡ ፲ ። ሚክ፯ ፡ ፲፯) ።

—፤ መቅባት ፡ መለቅለቅ ፤ ማስር ፡ ማጣበቅ ፤ የኖራ ፡ የሙዳኒት ። ንሣእ ፡ ዐጽቀ ፡ በለስ ፡ ወጢዕ ፡ ቦቱ ፡ ኀበ ፡ ተኀምም ። ዘይጠይዕዎ ፡ ሥራዩ ፡ (፬ነገ ፡ ፳ ፡ ፯ ። ኢሳ፩ ፡ ፯) ።

**ተጤዐ** ፤ (ይጠያዕ) ፤ ተመረገ ፡ ተለሰነ ፤ ተደፈነ ፡ ተቀባ ።

**ጥዩዕ** ፤ (ዓን ፡ ዓት ፡ ይዕት) ፤ የተመረገ ፡ ምርግ ፤ ድፍን ፡ ዝግ ፤ ደንቈሮ ። ለሕሙማን ፡ ለቈረ ፡ እዘኒሆሙ ፡ ጥዩዓተ ፡ ከመ ፡ ይስምዑ ፡ ቃለ ፡ ሃይማኖት ። ይሰቍር ፡ እዝነ ፡ ጥይዕተ ፡ (ቀሌ ። ቅዳ ፡ ዮሐ) ።

**ጤፍ ፤—በቁሙ ፤—ጣፍ ።**

**ጠያፌሳ** ፤ ፀሓየ ፡ ፊሳ ፤ ዕንቈ ፡ ባሕርይ ፤ ሰደፍ ፡ ከፀሓይ ፡ የምቶልደው ። እብን ፡ ባሕርይ ፡ ዘስሙ ፡ ጠያፌሳ ፡ (አረጋ) ።

**ጠይቆ ፤ ቆት** ፤ (ጠየቀ ፡ ይጤይቅ ፡ ይጠይቅ ። ሰአለ ፤ ሐተተ) ፤ መጠየቅ ፤ መመርመር ፤ ለማግኘት ፡ ለማወቅ ። ጠይቆ ፡ መርምሮ ፡ ማወቅ ፡ መረዳት ፤ ልኩን ፡ ድርሱን ፡ ርግጡን ፡ ማግኘት ። ጠየቅዎ ፡ ለአሐዱ ፡ እምእለ ፡ ይቀውሙ ። ቅድመ ፡ ጠይቅ ፡ ወድኅረ ፡ ትጌሥጽ ። ጠይቅ ፡ ነገራ ፡ ለትምህርትከ ። ወነፍስየ ፡ ትጤይቆ ፡ ጥቀ ። ከመ ፡ ያእምሩ ፡ ወይለብዉ ፡ ወይጠይቁ ፡ ወይእመኑ ፡ (ዳን፯ ፡ ፲፮ ። ሢራ፲፩ ፡ ፯ ። ፲፯ ፡ ፳፩ ። መዝ ፡ ፻፴፰ ። ኢሳ፵፩ ፡ ፳) ። አንዳንድ ፡ መጣፍ ፡ በጠየቀ ፡ ፈንታ ፡ ተጠየቀ ፡ ይላል ፤ ስሕተት ፡ ነው ። ወተጠየቀ ፡ እምኔቤሆሙ ፡ መዋዕሊሁ ። ይፈርሁ ፡ ተጠይቆቱ ፡ በእንተ ፡ ዝ ፡ ነገር ። ወተጠየቆ ። እመ ፡ ተጠየቀ ፡ ብእሲ ፡ ደዌሁ ። በኀበ ፡ ጠቢባን ፡ ተጠየቅ ፡ በኵሉ ፡ ጊዜ ፡ (ማቴ፪ ፡ ፯ ። ሉቃ፱ ፡ ፵፭ ። ፳፪ ፡ ፶፯ ። ፪ዜና ፡ ፯ ፡ ፳፪ ። ሢራ፳፯ ፡ ፲፪) ።

**ጠያቂ** ፤ (ቂት ፡ ቅያን ፡ ያት) ፤ በቁሙ ፤ የሚጠይቅ ፡ የሚመረምር ፤ መርማሪ ። (ተረት) ፤ አጥብቆ ፡ ጠያቂ ፡ እናቱን ፡ ይረዳል ።

**አጠየቀ** ፤ አስጠየቀ ፤ አስመረመረ ። አስረዳ ፤ አሳወቀ ፡ አስታወቀ ፤ ነገረ ፡ አሰማ ፡ አስተማረ ። አጠይቀኒ ፡ ኵልቆሙ ። ወአጠይቅዎ ፡ ለንጉሥ ፡ ቃላተ ።

ተጋብኡ ፡ ኀበ ፡ ዕዝራ ፡ ከመ ፡ ያጠይቅሙ ፡ ዙሎ ፡ ቃለ ፡ ኦሪት ፡ (፩ዜና ፡ ፳፰ ፡ ፪ ። ፪ዜና ፡ ፴፱ ፡ ፳፰ ። ዕዝ፰ ፡ ፲፫) ።

**አጠያቂ ፤ መጠይቅ ፤ (ቅት ፡ ቃን ፡ ቃት) ፤** የሚያስጠይቅ ፤ አስጠያቂ ፡ አስመርማሪ ። የሚያስረዳ ፡ አስረጅ ፤ መምር ፡ አስተማሪ ። ወሌዋውያን ፡ መጠይቃን ፡ ለሕዝብ ፡ መጽሐፈ ፡ (ነሐ፰ ፡ ፯) ።

**ተጠየቀ ፤** በቁሙ ፤ ተመረመረ ፤ ታወቀ ፡ ተረዳ ፡ ተረገጠ ፤ ታየ ፡ ተገለጠ ። በዝ ፡ ተዐውቀ ፡ ወተጠየቀ ፡ ከመ ፡ (አቡሻ ፡ ፲፪) ። ወበዝ ፡ ተዐውቀ ፡ ሕልመ ፡ አቡሆሙ ። ለእመ ፡ ተጠየቀ ፡ ሞተ ፡ ንጉሥ ። ወተጠየቀ ፡ ሰቤሃ ፡ ነገረ ፡ አረጋዊ ፡ (ዮሴፍ) ።

**ጥዩቅ ፤** የተጠየቀ ፤ የተመረመረ ። የታወቀ ፡ የተረዳ ፡ የተረገጠ ። ዕለት ፡ ጥይቅት ። አይድዐኒ ፡ ፍካሬሁ ፡ ጥዩቀ ። ለአከቶ ፡ ይስማዕ ፡ ጥዩቀ ፡ ነገረ ፡ (ቅዳ ፡ ግሩ ። ዳን፯ ፡ ፲፮ ። አስቴ፱ ፡ ፳) ።

**ጥዩቀ ፤** ርግጥ ፡ በርግጥ ፤ እውነት ፡ በውነት ፡ በግልጥ ፤ ፈጽሞ ። ጥዩቀ ፡ እንከ ፡ ያእምሩ ። ጥዩቀኬ ፡ ወገሃደ ። ለሊክሙ ፡ ተአምሩ ፡ ጥዩቀ ፡ ከመ ፡ ዕለተ ፡ እግዚእነ ፡ ትመጽእ ፡ (ግብ፪ ፡ ፴፮ ። ቴር ፡ ጳላ ። ፩ተሰ ፡ ፭ ፡ ፪) ።

**ጥያቄ ፤ (ቅያት) ፤** በቁሙ ፡ መጠየቅ ፤ (ጥ ፡ ጠ) መጠየቅ ፤ አጠያየቅ ፡ ጥየቃ ፤ ምርመራ ። መረዳት ፤ ማስረዳት ፤ መግለጥ ፡ ማስረገጥ ። በብዙኅ ፡ ጥያቄ ፡ ፈለጠ ። ናመጽእ ፡ ካልአ ፡ አምሳለ ፡ ለጥያቄ ፡ ዝንቱ ፡ (አፈ ፡ ድር ። ተ፲፫) ። ርግጥ ፤ ርግጥነት ። ኅሥሥ ፡ በእንተ ፡ ዝንቱ ፡ ነገር ፡ እስከ ፡ ትረክብ ፡ ጥያቄሁ ። ኢያእመረ ፡ ጥያቄሁ ፡ ለዝንቱ ። የሀብዎ ፡ መዋዕለ ፡ ዕድሜ ፡ ለአብጽሖተ ፡ ጥያቄሁ ፡ (ዮሴፍ ። ፍ ፡ ነ ፡ ፳፱ ። ማ፫ ፡ ፯) ።

**ጥይቅና ፤** ዝኒ ፡ ከማሁ ፤ መረዳት ፡ ማስረገጥ ፤ ርግጥነት ። አእምሩ ፡ ዘንተ ፡ በጥይቅና ። ነባብያን ፡ በጥይቅና ፡ (ሃይ ፡ አበ ። መቅ ፡ ወን) ።

**ጠይሮ ፤ ሮት ፤ (ጠየረ ፡ ይጤይር ፡ ይጠይር ። ዐረ ፡ ጣረ) ፤** መብረር ፡ መክንፍ ፤ ያሞራ ፡ የወፍ ።

**ተጠየረ ፤ (ዐረብ ። ዕብ ፡ ጣዬር) ፤** ተነባ ፤ ጠነቈለ ፤ አሟረተ ፤ በወፍ ፡ ጮኸት ፡ በድምፀ ፡ አራዊት ፡ በሌላውም ፡ ፍጥረት ። ዘሟርቱና ፡ ከጥንቈላው ፡ ጋራ ፡ አምልኮትንም ፡ ያሳያል ። ኢትጠየሩ ፡ በዖፍ ። ዘይጤየሩ ፡ በሐሳበ ፡ ፀሓይ ፡ ወወርኅ ፡ (ዘሌ፲፱ ፡ ፳፮ ። አርጋ ፡ ፪) ። ዘይጤየር ፡ በዖፍ ፡ ወበማይ ፡ ወበእሳት ። እመ ፡ ቦ ፡ ዘተጠየረ ፡ በአዕዋፍ ፤ አው ፡ በአራዊት ፡ አው ፡ በካልእ ፤ አው ፡ በዘኮነ ፡ ከዊኖ ፡ (ቀሌ) ።

**ተጠያሪ ፤ (ሪት ፡ ርያን ፡ ያት) ፤** የሚያሟርት ፡ ሟርተኛ ፤ ጠንቋይ ፤ ወፍ ፡ ጠያቂ ፤ እንዳገውና ፡ እንዳርማጭሖ ፡ ሰው ፡ የወፍ ፡ ቋንቋ ፡ የሚያውቅ ። ኢትኩን ፡ ተጠያሬ ፡ በዖፍ ። ተጠያሪ ፡ በመሬት ፡ ወበሐመድ ፡ ወበፍሬ ፡ ዕፀው ። ተጠያርያን ፡ (መጽ ፡ ምስ ። ሲኖ ። ቄድር) ።

**አጠየረ ፤ አስተጠየረ ፤** አበረረ ፤ አስበረረ ፤ አክነፈ ፡ አክነፈነፈ ። አስጠነቈለ ፤ ወፍ ፡ አስጠየቀ ፤ አስመለከ ። አድራጊና ፡ አስደራጊ ፡ ነው ።

**አጠያሪ ፤ መጠይር ፤ መስተጠይር ፤** አስጠንቋይ ፤ ወፍ ፡ አስጠያቂ ፡ (ሲኖ) ።

**ጠያር ፤ ጥያራ ፤ (ራት) ፤** ሰው ፡ ሠራሽ ፡ አሞራ ፤ ዘመን ፡ አመጣሽ ፡ ወፍ ፡ በአየር ፡ የሚበር ፡ የሚክንፍ ፡ አይሮፕላን ፡ የውቀት ፡ ብዛትና ፡ የፍጻሜ ፡ ዘመን ፡ ምልክት ፡ (ዮኤ፫ ፡ ፫—፭ ። ፩ተሰ ፡ ፬ ፡ ፲፯) ።



ጠያር ፡

**ጢር ፤** ጥንቈላ ፡ ሟርት ፤ አምልኮ ፡ ባዕድ ። ዑጥር ፡ ቅጥርንም ፡ ያሳያል ። ጣውርን ፡ እይ ።

**ጢሮት ፤** ጣራ ፡ ባጥ ፤ ጠፈር ፡ መዋቅር ፤ ድንኳን ፡ (ሕዝ፳፭ ፡ ፬) ።

**ጥር ፤** በቁሙ ፤ ስመ ፡ ወርኅ ፡ ኃምስ ፡ እመስከረም ፤ ጠር ። ምስጢሩ ፡ ምጥቀት ፡ ርዝመት ፡ ነው ፤ ቢ፲፭ ፡ ምዕራፍ ፡ ኑኀና ፡ ርሕብ ፡ ዓ ፡ ዘመን ፡ ምሉ ፡ ተሠርቶ ፡ ቁመቱ ፡ ፭ ፡ ሺሕ ፡ ካ፱፻፹፫ ፡ ክንድ ፡ ከ፪ ፡ ስንዝር ፡ ሲኾን ፡ በጥር ፡ በ፯ ፡ ከፈረሰው ፡ ከጥቅመ ፡ ሰናዖር ፡ ይስማማል ። ድርሳነ ፡ ሥላሴ ፡ ተመልከት ፡ (ኩፋ ፡ ፲ ። ዘፍ፲፩ ፡ ፩—፯) ።

**ጠዩስ ፤ ሶት ፤ (ጤሰ ፡ ይጠይስ ፡ ይጢስ ። ተነ) ፤** መጤስ ፤ መትነን ፡ መብነን ፡ መትጉልጐል ፤ ከሚነድና ፡ ከሚቃጠል ፡ ነገር ፡ ጭጋግና ፡ ጉም ፡ ጥቍር ፡ ደመና ፡ መስሎ ፡ መውጣት ። ትንታጋት ፡ እለ ፡ ይጠይሱ ። ሡዕ ፡ ዘይጠይስ ። ዘእንበለ ፡ ይጢስ ፡ ሥብሕ ። እቶን ፡ ዘይጠይስ ፡ (ኢሳ፯ ፡ ፬ ። ዓ፪ ፡ ፫ ። ፩ነገ ፡ ፪ ፡ ፲፭ ። ዘፍ፲፭ ፡ ፲፯) ። ከሰው ፡ ልቡና ፡ ለሚነቁና ፡ ለሚፈልቁ ፡ ለኀሊናትም ፡ ይነገራል ።

**ጢስ ፤** በቁሙ ፤ ጪስ ፡ ጭጋግ ፡ የሚመስል ። ላበት ፡ እንፋለት ፡ ስልባቦት ፤ ከሙቅ ፡ ከትኵስ ፡ ነገር ፡ የሚወጣ ። ለእሳት ፡ ይቀድሞ ፡ ተነ ፡ ጢስ ። ጢስ ፡ ምንሃብ ። ወዐርገ ፡ ጢስ ፡ እምቀላይ ፡ ከመ ፡ ጢስ ፡ እቶን ፡ ዐቢይ ። ወወፅአኒ ፡ ጢስ ፡ ውስተ ፡ አዕይንትየ ፡ ወተሥዕዐ ፡ እምብንተ ፡ አዕይንቲሁ ፡ ዝኩ ፡ ጢስ ፡ (ሢራ፳፪ ፡ ፳፬ ። ፴፰ ፡ ፳፰ ። ራእ፱ ፡ ፪ ። ጦቢ፪ ፡ ፲ ። ፲፩ ፡ ፲፪) ።

**አጤሰ ፤** በቁሙ ፤ አጬሰ ፡ አበነነ ፤ ዐጠነ ። አጤሰ ፡ ልቦ ፡ ወሐሞቶ ፡ ለዓሣ ። በቀላ ፡ ቍልቍሊተ ፡ ወአጤሰ ፡ መትሕቴሃ ፡ እሳተ ። ለተነ ፡ ፂሜ ፡ ዘያጤ

ይሶ ። አጤስ ፡ ቦቱ ፡ (ስንክ ፡ መስ፲፮ ። ጥቅ፲ ። መጽ ፡ ምስ ። ጦቢ፯ ፡ ፲፯) ።

**ጤት ፤ (ዕብራ)** ፤ ስመ ፡ ፊደል ፡ ታስዕ ። ሠ ናይት ፡ ላሕዩት ፡ ጠባብ ፡ ኄርት ፡ ማለት ፡ ነው ፡ (መዝ ፡ ፻፲፰ ፡ ፷፭—፸፪ ። ሰቈ፩ ፡ ፱ ። ፪ ፡ ፱ ። ፫ ፡ ፷፭ ። ፬ ፡ ፱) ።

**ጠይት ፤ (ግእዝ)** ፤ ዝኒ ፡ ከማሁ ፤ ዘጠንኛ ፡ ፊደል ፡ ጠ ። ጤትና ፡ ጠይት ፡ ጦብያና ፡ ጦቢት ፡ በዕብ ራይስጥ ፡ አንድ ፡ ዘር ፡ ናቸው ፤ ጠወቦን ፡ እይ ።

(ጥ) **ጠየተ ፤ (ይጤይት ፡ ይጠይት)** ፤ በቁሙ ፤ ጥይት ፡ ሠራ ። መረጠ ፡ መራረጠ ፤ አበጀ ፡ አዘጋጀ ፤ የሽ ትን ፡ ዛላ ፡ ለመጥበስ ፡ ለማሸት ፡ (ዐማርኛ) ። እንደዚህ ፡ ያለው ፡ ግስ ፡ ቅጥይ ፡ ተቀጥላ ፤ ወይም ፡ ክልስ ፡ ዲቃላ ፡ ይባላል ፤ ይህን ፡ የመሰለ ፡ ብዙ ፡ አለ ።

**ጠያቲ ፤ (ቲት ፡ ትያን ፡ ያት)** ፤ የሚጠይት ፡ ጠያች ፤ ጥይት ፡ ሠሪ ።

**አጠየተ** ፤ አስጠየተ ፤ ጥይት ፡ አሠራ ።

**መጠይት ፤ (ታን)** ፤ የሚያስጠይት ፡ አስጠ ያች ፤ ወይም ፡ ጠያች ።

**ተጠየተ** ፤ በቁሙ ፤ ተመረጠ ፡ ተዘጋጀ ።

**ጥዩት ፤ (ታን ፡ ታት ፡ ይት)** ፤ የተጠየተ ፤ የታሰረ ፡ የተዘጋጀ ።

**ጥይት ፤ (ታት)** ፤ በቁሙ ፤ ጥሩ ፡ እሸት ፤ ተመ ርጦ ፡ የታሰረ ፤ ለመጠበስ ፡ የተደከረ ። ዐረር ፡ ርሳስ ፡ የሚ ፈነዳ ፡ የሚተኰስ ፡ እንደ ፡ ዛላ ፡ ኹኖ ፡ የተሠራ ፤ ዝግጁ ፡ ማለት ፡ ነው ። ወለሲና ድር ፡ ንይልክ ፡ አመ ፡ በጥይት ፡ ብጐምካ ፤ ትግራይ ፡ አሽከር ፡ ቦሬሳ ፡ በይእቲ ፡ አቅ መሰከ ፡ (ትግሪኛ ፡ ቅኔ) ።



ጥይት ፡

**ጠል ፤—በቁሙ ፤—ጠሊል ፡ ጠለ ።**

**ጠልጠለ ፤—ጣለ ፤—ጠሊል ፡ ጠለ ።**

**ጠልይ ፤ ዮት ፤ (ጠለየ ፡ ይጠሊ ፡ ይ ጥሊ ። ጠለ)** ፤ መርጠብ ፡ መታደስ ፤ ልምላሜ ፡ ማ ግኘት ፤ ርጥብ ፡ ለጋ ፡ መኾን ፤ የዐጽቅ ፡ የልጅ ። መው ጣት ፡ መብቀል ፡ ማጨልጨል ፤ የቡቃያ ፡ የሣር ። ፋኑ ሔል ፡ ዝክርከ ፡ እምቀናንም ፡ ዘይጠሊ ፡ (ደራሲ) ።

**ጠሊ ፤ (ዕብ ፡ ጣሌ ። ዐረ ፡ ጠሊይ ፤ ጠ ለን ። ሱር ፡ ጥላያ)** ፤ ግልገል ፤ እንቦሳ ፤ ውርንጭላ ፤ ለጋ ፡ ቀንበጥ ፤ ርጥብ ፡ ጨሌ ፤ ዐራስ ፡ ጨቅላ ። ልጅነት ፡ ላለው ፡ ለታናናሽ ፡ ኹሉ ፡ ይነገራል ፤ በዕብራይስጥ ፡ ግን ፡ ለበግ ፡ ብቻ ፡ ነው ።

**ጠሊ ፤ (ሊት ፤ ብ ፡ አጣሊ ፤ ልያት)** ፤ ተባት ፡ ፍየል ። ጸጕረ ፡ ጠሊ ። ማእሰ ፡ ጠሊ ። ያም ጽእ ፡ በግዐተ ፤ አው ፡ ጠሊተ ። ይፈልጥ ፡ አባግዐ ፡ እምአጣሊ ፡ (ዘፀ፳፭ ፡ ፬ ። ዘኍ፴፩ ፡ ፳ ። ዘሌ፭ ፡ ፯ ። ማቴ፳፭ ፡ ፴፪) ። እንስቶቹን ፡ አጣልያት ፡ በማለት ፤ ፈንታ ፡ አጣሊ ፡ አንስት ፡ ይላል ፤ አያስኼም ፡ (መቃ ፡ ገ፩) ፡ አን ፡ ትቶ ፡ በንና ፡ በየ ፡ ሲበዛ ፡ ግን ፤ ጠሊ ፡ ጣል ያን ፤ ጣሊት ፡ ጣልያት ፡ ያሰኛል ።



ጠሊ ፡

**ጣሊታ ፤ (ሱር ፡ ጣልያታ ። ጽር ፡ ታ ሊታ)** ፤ ታናሽ ፡ ሴት ፡ ልጅ ፤ ለጋ ፡ ቈንጆ ፡ ድንግል ፤ ከዘጠኝና ፡ ካሥር ፡ ዓመት ፡ በላይ ፡ ያለች ፤ ገና ፡ አካለ ፡ መጠን ፡ ያልሞላች ። ወይቤላ ፤ ጣሊታ ፡ ተንሥኢ ፤ ዘ በትርጓሜሁ ፡ ወለት ፡ (ማር፭ ፡ ፵፩) ። አንዳንድ ፡ መ ጣፍ ፡ ግን ፡ በጣሊታ ፡ ፈንታ ፡ ጣቢታ ፡ ይላል ፤ የጣፊ ፡ ስሕተት ፡ ነው ።

**ጠሊል ፤ ሎት ፤ (ጠለ ፤ ጠለለ ፡ ይጠ ልል ፡ ይጥልል ። ዐረ ፡ ጠለ)** ፤ መጥለል ፡ መጥ ራት ፤ የጠላ ፡ የጠጅ ። መውረድ ፡ መረጨት ፤ የጠል ፡ የ ክረምት ። መራስ ፡ መረስረስ ፤ መርጠብ ፡ መለምለም ፤ መ ርካት ፡ ጠል ፡ መንሣት ፤ ከውሃ ፡ ከቅባት ። ትጠልል ፡ ምድር ፡ እምሥብሖሙ ። ወይጠልል ፡ በቅብዕ ፡ ሚበትየ ። ሖላ ፡ ነፍስ ፡ እንተ ፡ ትባርክ ፡ ትጠልል ፡ (ኢሳ፴፬ ፡ ፯ ። መዝ ፡ ፺፩ ። ምሳ፲፩ ፡ ፳፭) ።

**ጥሉል ፤ (ላን ፡ ላት ፡ ልልት)** ፤ የጠለለ ፡ ጥሩ ። የለመለመ ፡ የረጠበ ፤ ለምለም ፡ ርጥብ ። ብሔር ፡ ጥሉል ። ዒያት ፡ ጥሉል ። ደብር ፡ ጥሉል ። ርሥኣን ፡ ጥሉል ፡ (ኢሳ፭ ፡ ፩ ። ሕዝ፴ ፡ ፲፪ ። መዝ ፡ ፷፯ ። ፺) ።

—፤ ሥጋ ፡ ቅቤ ፤ ዕንቍላል ፡ ወተት ፤ የብሉት ፡ ምግብ ። ትወርድ ፡ ማእድከ ፡ እንዘ ፡ ምሉእ ፡ ወጥሉል ። መባልዕት ፡ ጥሉላት ። ኢይብልዑ ፡ ጥሉላተ ፡ (ኢዮ ፴፯ ፡ ፲፯ ። ፈ ፡ መ ፡ ፲፬ ፡ ፭ ። ስንክ ፡ ጥር፲) ።

**ጠል ፤ (ላት)** ፤ በቁሙ ፤ የሰማይ ፡ ወዝ ፤ የአ የር ፡ ላበት ፡ ሌሊት ፡ አለደመና ፡ የሚወርድ ፤ ምድርን ፡ የሚያርስ ፡ የሚያረሰርስ ፤ እንደ ፡ ጤዛ ፡ በሣር ፡ በቅጠል ፡ ላይ ፡ የሚታቈር ፡ የሚንቈረዘዝ ። እስመ ፡ ርእስየኒ ፡ ምሉእ ፡ ጠለ ። ወይረይ ፡ ከመ ፡ ጠል ፡ ነቢብየ ። ወ ወረደ ፡ ጠል ፡ ዲበ ፡ ፀምር ፡ ባሕቲቱ ፡ (ማሕ፭ ፡ ፪ ። ዘዳ፴፪ ፡ ፪ ። መሳ፮ ፡ ፴፯) ።

—፤ ካፊያ ፤ የጉም ፡ ሽንት ፤ ልዝብ ፡ ዝናም ። ይመ

ናት ፡ ያውሕዙ ፡ ጠላተ ፡ (ምሳ፫ ፡ ፳) ። ቅባት ፤ ዘይት ። እሉኬ ፡ ይቂቀ ፡ ጠላት ፡ እሙንቱ ፡ (ዘካ፬ ፡ ፲፬) ።

**ጥላል** ፤ ርጥበት ፡ ልምላሜ ፤ ጣዕም ፡ ሥን ። ጥላሊሁ ፡ ለማእድ ፡ (ገድ ፡ ላሊ) ።

**አጥለለ** ፤ አጠለለ ፡ አወረደ ፤ የጠላ ፡ የጠል ። አራስ ፡ አረጠበ ፡ አለመለመ ፤ አረካ ። ያጠልል ፡ አዕፅምተ ፡ እምብዝኀ ፡ ጣዕሙ ። መሥዋዕቱ ፡ ለጻድቅ ፡ ያጠልሎ ፡ ለምሥዋዕ ። ያጥልል ፡ ለከ ፡ ቍርባነከ ። በማየ ፡ ጸሎቱ ፡ ጽምአ ፡ ነጋድያን ፡ አጥለለ ። በጠለ ፡ ምሕረቱ ፡ እግዚ ፡ ያጥልል ፡ ነፍሳቲክሙ ፡ (ቅዳ ፡ ሕር ። ሚራ፴፪ ፡ ፳ ። መዝ ፡ ፲፱ ። ስንክ ፡ ኅዳ፲፱ ። ግንዘ) ። በስትየ ፡ ፈንታ ፡ አጥለለ ፡ ይላል ፤ ስሕተት ፡ ነው ። እንበለ ፡ ይብልዑ ፡ እክለ ፡ ወማየ ፡ ያጥልሉ ፡ (ስንክ ፡ ሠኔ፲፱) ።

**መጥለሊ** ፤ **መጥልል** ፤ የሚያጠል ፡ የሚያለመልም ፤ የሚያረካ ። አስተየኒ ፡ ዘንተ ፡ ወይነ ፡ ኀይል ፡ መጥለሌ ፡ (ጥበ ፡ ጠቢ) ።

**መጥለል** ፤ ማጥለያ ፡ ማጥሪያ ፤ ወንጠፍት ። ከመ ፡ ዘመጥለል ፡ ሙሓዝ ፡ (ስንክ ፡ ግንጃ) ።

**ጠልጠለ** ፤ (ተቀ ፡ ግ ። ዕብ ፡ ጣልጤል) ፤ ጣለ ፡ ወረወረ ፤ ረጨ ፡ በተን ፡ በየጥቂቱ ፤ እንደ ፡ ጠልና ፡ እንደ ፡ ጠበል ። ንቀለ ፡ አኃዘ ፡ ወሰደ ።

**አንጠልጠለ** ፤ በቁሙ ፤ አንጠለጠለ ፡ አንግ ፡ ያዘ ፤ ለመውሰድ ፡ ለመጣል ፤ ወይም ፡ ለማኖር ። ተያዘ ፡ ተንጠለጠለ ፤ ተወዘወዘ ፤ ለመውደቅ ። ተቀሥፈ ፡ አባለ ፤ እስከ ፡ ሥጋሁ ፡ አንጠልጠለ ፡ (ስንክ ፡ መጋ፲፯) ።

**ጠለመ** ፤ (**ጸልመ** ፤ **ጸለመ** ። **ሱር ፡ ጥላም** ። **ዐረ ፡ ዘለመ**) ፤ ካደ ፡ ከዳ ፤ ሸፈጠ ፡ ተ ፤ ውል ፡ አፈረሰ ፤ ሰደበ ፡ ነቀፈ ። ጠለሙ ፡ በበይናቲሆሙ ፡ ... ወበእንተ ፡ ዝ ፡ ይከውን ፡ ቀትል ፡ ማእከሌሆሙ ፡ (አዋል) ። ፪ኛም ፡ መስጠምንና ፡ መዝቀጥን ፡ ያሳያል ። ጠ ፡ የጸ ፡ ለወጥ ፡ ነው ፤ ጸልመን ፡ ተመልከት ።

**ጥልማ** ፤ **ጥልም** ፤ (**ዕብ ፡ ያህሎም**) ፤ ከቡር ፡ ደንጊያ ፤ ዕንቍ ፤ ልዩ ፡ ሕብር ፡ የሌለው ፡ የውሃ ፡ ዐይነት ። ኢያስጲስን ፡ እይ ፤ ከዚህ ፡ ጋራ ፡ አንድ ፡ ነው ፡ (መቃ ፡ ገ፫ ። ክብ ፡ ነገ፲፯ ። ዘፀ፴፯ ፡ ፲፰) ። ኢያስጲስ ፡ ወጥልም ፡ አሐዱ ፡ (ጥሬ ፡ ስዋ) ።

**ጥልማክስ** ፤ **ጥልምያክስ** ፤ ስመ ፡ ሰይጣን ፤ የሲኦል ፡ በረኛ ፡ አጋፋሪ ፤ ከሓዲ ፡ ግፈኛ ፡ ማለት ፡ ነው ፡ (ራእ ፡ ማር) ።

**ጠልዐ** ፤ (**ዐረ ፡ ጠለዐ**) ፤ ወጣ ፡ በቀለ ፤ አደገ ፡ ረዘመ ። ናሁ ፡ ትጠልዕ ፡ (ሕዝ፲፯ ፡ ፲) ። ዕብራይስጡ ፡ ግን ፡ ሸቱላ ፡ ይላል ፤ ትክልት ፡ ማለት ፡ ነው ።

**ጠሊቅ** ፤ **ቆት** ፤ (**ጠለቀ ፡ ይጠልቅ ፡ ይጥልቅ** ። **ዐረ ፡ ጠለኀ** ፤ **አሳደፈ**) ፤ መጥለቅ ፤ ጥልቅ ፡ ዕሙቅ ፡ መኾን ፤ ወይም ፡ ጥልቅ ፡ ብሎ ፡ መግባት ፤ መንከር ፡ መዘፈቅ ፤ ማደፍ ፡ መኰለፍለፍ ፤ መርከስ ፡ መጨማለቅ ። ኢጠለቀ ፡ ኀዲሮ ፡ ውስተ ፡ ማሕፀና ። ልቡና ፡ ሰብእ ፡ ዘኢጠለቀ ፡ በኀጢአት ፡ (ተረ ፡ ቄር) ።

—፤ መጥገብ ፡ መርካት ፤ መጥላት ፡ መሰልቸት ። ትሰክር ፡ ምድር ፡ እምደሞሙ ፡ ወትጠልቅ ፡ እምሥብሖሙ ። ሰቄራረ ፡ ኮንክሙኒ ፡ ወጠለቁክሙ ፡ (ኢሳ፴፬ ፡ ፯ ። ፩ ፡ ፯) ።

—፤ መጥለቅለቅ ፡ መቅለሽለሽ ፤ ልውጣ ፡ ልውጣ ፤ አውጡኝ ፡ አውጡኝ ፡ ማለት ፤ የምግብ ፤ አብዝቶ ፡ ከመብላት ፡ ከመጋፈፍ ፡ ወይም ፡ ከሆድ ፡ ማደፍ ፡ የተነሣ ። እለ ፡ ጠለቀት ፡ ነፍስኪ ፡ እምኔሆሙ ፡ (ሕዝ፳፫ ፡ ፳፪ ፡ ፳፰) ። በጠለቀ ፡ ፈንታ ፡ አጥለቀ ፡ ይላል ፤ ስሕተት ፡ ነው ። ብልዑ ፡ ሥብሐ ፡ እስከ ፡ ያጠልቀክሙ ፡ (ሕዝ፴፱ ፡ ፲፱ ። ሆሴ፲፫ ፡ ፯) ። ፪ኛም ፡ በጠቀለ ፡ ፈንታ ፡ ጠለቀ ፡ ይላል ፤ የጣፊ ፡ ስሕተት ፡ ነው ፡ (ኩፋ ፡ ፴፱) ።

(ጥለ) **ጠለቀ** ፤ (**ዐረብ**) ፤ ፈታ ፤ ለቀቀ ፡ ሰደደ ፤ ኢወጣ ፡ አሶጣ ፤ አሰናበተ ፤ የሚስት ፡ የገረድ ። በቁሙ ፡ ነከረ ፡ ጠቀሰ ፡ እጁን ፡ አገባ ፤ የወጥ ። ቀዳ ፡ ጨለፈ ፡ ደነበቀ ፤ የውሃ ፡ የመጠጥ ፡ (ዐማርኛ) ።

**ጥሉቅ** ፤ (**ቃን ፡ ቃት ፡ ልቅት**) ፤ የጠለቀ ፤ ጥልቅ ፡ ጠሊቅ ፤ ዕሙቅ ። ያደፈ ፡ የረከሰ ፤ እድፋም ፡ ጨምላቃ ፤ የሚያስጠይፍ ። አውገዝነ ፡ ፀዊጋተ ፡ ውጥሉቃተ ፡ ትምህርታቶ ፡ (ተረ ፡ ቄር፲፬ ። ገድ ፡ አዳ) ።

**ጥልቀት** ፤ (**ቃት**) ፤ መጥለቅ ፡ ጥልቅነት ፤ ማደፍ ፡ አስተዳደፍ ። አደፍ ፡ እድፍ ፡ ጭቅቅት ፤ ርኵስ ፡ ኀጢአት ፤ ውሃና ፡ ንስሓ ፡ የሚያስፈልግ ። ንጹሕ ፡ እምጥልቀት ። እምዘሱ ፡ ጥልቀተ ፡ ኀጢአት ። ጥልቀተ ፡ ዝሙት ። እንዘ ፡ አልቦ ፡ ጥልቀት ፡ (ቄድር ፡ ገ፰ና ፡ ፲፪ ። አርጋ ፡ ፯ ። ቅዳ) ።

**ጥላቄ** ፤ ዝኒ ፡ ከማሁ ፤ መጥለቅ ፡ አጠላለቅ ፤ ጥልቂያ ፡ ጥልቆሽ ። እድፍ ፡ ጥላቂ ፡ ጭላፊ ። ጥላቄ ፡ ኀጢአት ። ወመልአ ፡ ጥላቄ ፡ ዘሎቱ ፤ ቀለም ፡ (ቄድር ፡ ገ፴፬ ። ጥበ፲፫ ፡ ፲፬) ።

**አጥለቀ** ፤ አጠለቀ ፤ አስጠለቀ ፤ የቀሚስ ፡ የሱሪ ። አጥለቀለቀ ፡ አሳደፈ ፤ አረከሰ ። ርሡሱ ፡ ሊብእሲ ፡ ቀታሊ ፡ ያጠልቆ ፡ (ምሳ፳፬ ፡ ፲) ።

**ጠሊስ** ፤ **ሶት** ፤ (**ጠልሰ** ፤ **ጠለሰ ፡ ይጠልስ ፡ ይጥልስ**) ፤ መጥለስ ፤ መጥፋት ፡ መጥቈር ፤ የእሳት ፡ የከሰል ። ከንጨት ፡ ይልቅ ፡ ለሣር ፡ ለገለባ ፡ ይስማማል ።

**ጠለስ** ፤ በቁሙ ፤ ጥቍር ፡ ዐመድ ፤ ጥላት ፤ የሣር ፡ የገለባ ፡ የቅጠል ፡ ሕመት ፤ ቀለም ፡ የሚኾን ። ጠለሸት ፤ የደን ፡ ውስጥ ፡ ጥላ ፤ ጨለማ ፡ (ዐማርኛ) ።

**አጥለሰ** ፤ አጠለሰ ፤ አጠቈረ ፡ አከሰለ ፤ አጠላ ፡ አጨለመ ።

**አጥላስ** ፤ (**ሳት**) ፤ በቁሙ ፤ ጥቍር ፡ የሐዘን ፡ ልብስ ፤ ከል ፡ እማሎሚ ፤ የጠለስና ፡ የጥላ ፡ የጨለማ ፡ ዐይነት ።

**ጠልሰም ፤ (ማት ። ዐረ ፡ ጢልሰም ። ጽር ፡ ቴሌስማ)** ፤ በቁሙ ፤ ክታብ ፤ ጠንቋዮች ፡ በጥቍር ፡ ቀለም ፡ ጥፈው ፡ ጠልስመው ፡ የሚያሲዙት ። ክታብ ፡ አስማቱ ፤ ጠልሰም ፡ በያስማቱ ፡ ውስጥ ፡ የሚጣል ፡ ሥዕልና ፡ ሐረግ ፡ ስንጠረዥ ፡ ሙጭርጭር ፡ ጥፈት ፡ ነው ። ጠልሰማት ፡ (አቡሻ ፡ ፶፩) ። አቀሙ ፡ ጠልሰማተ ፡ ዘውእቱ ፡ ግልፎ ፡ ጣዖት ፡ (ጊ ፡ ወ ፡ ሐ ፡ ገ፩) ።

**ጠሊሳን ፤ (ዐረ ፡ ጠይለሳን)** ፤ ክቡር ፡ ልብስ ፤ ልብሰ ፡ ተክህኖ ፡ ታላቅ ፡ መንዲል ፤ ወይም ፡ ሞጣሕት ፡ ካህን ፡ ባንገቱ ፡ በራሱ ፡ የሚያደርገው ። ወጠሊሳኑኒ ፡ ይኩን ፡ ጽዕድወ ። እትሜነይ ፡ ለስዒም ፡ ጠሊሳኒ ፡ ጳውሎስ ፡ (ፈ ፡ መ ፡ ፴፩ ፡ ፳ ። ድጓ) ።

—፤ የላይ ፡ ልብስ ፤ መጐናጠፊያ ። ጠሊሳኒ ፡ ንጉሥ ፡ ሶቤሃ ፡ ከደና ፡ (ድጓ) ።

**ጠመ ፤ ጦመ ፤—ዐጠፈ ፤—ጠዊም ፡ ጦመ ።**

**ጤሜዎስ ፤ (ጽር ፡ ቲሜዎስ ። ዕብ ፡ ጢማይ)** ፤ የሰው ፡ ስም ፤ ጠንባሳ ፡ ዕዉር ፤ ዐይን ፡ ስዉር ፡ (ማር፲ ፡ ፵፮) ።

**ጤሜን ፤ (ጽር ፡ ቴሜኒ)** ፤ መስጊድ ፤ ቤተ ፡ ጣዖት ፤ ምኵራብ ፡ ጣዖት ፡ (ሆሴ፫ ፡ ፲፬) ።

**ጠመነ ፤ (ዕብ ፡ ጣማን)** ፤ ደፈነ ፡ ቀበረ ፤ ሸፈነ ፡ ሰወረ ። ቀባ ፤ ለቀለቀ ። ጣመን ፤ ተጠማኝ ፡ ማለት ፡ ከዚህ ፡ ወጥቷል ፤ ኹሉም ፡ ዐማርኛ ፡ ነው ።

**ጠመኔ ፤ (ዐማርኛ)** ፤ በቁሙ ፤ በረቅ ፡ ነጭ ፡ ደንጊያ ፤ ዐፈር ፡ የኖራ ፡ ዐይነት ፤ ለቤት ፡ የሚቀባ ፡ የሚለቀለቅ ።

**ጠሚዕ ፤ ዖት ፤ (ጠምዐ ፡ ይጠምዕ ፡ ይጥማዕ ። ዕብ ፡ ጥማዕ ፤ ሰጠመ ። ጣማአ ፤ ረከሰ)** ፤ መጥማት ፤ መንከር ፡ መዝፈቅ ፤ ማግባት ፡ ማጥለቅ ፤ ማሳደፍ ፡ ማርከስ ። ኢትጥምዖ ፡ ውስተ ፡ ማይ ። ውስተ ፡ ሠሉ ፡ ዘርኢከ ፡ ኢትጥማዕ ፡ እዴከ ። ትጠምዐኒ ፡ ውስተ ፡ ርስሐት ። ይጥማዕ ፡ ካህን ፡ አጽባዕቶ ፡ ውስተ ፡ ደም ። ጠምዖ ፡ ለቤት ፡ (ኤር፲፫ ፡ ፩ ። ሚራ ፴፬ ፡ ፲፬ ። ኢዮ፱ ፡ ፴፩ ። ዘሌ፬ ፡ ፮ ። ሔኖ፹ ፡ ፹፪) ።

**ተጠምዐ** ፤ ተነከረ ፡ ተዘፈቀ ፤ ገባ ፡ ጠለቀ ። በከመ ፡ ይዴመር ፡ ሠርዌ ፡ ምስለ ፡ ፀምር ፡ ተጠሚዖ ። አጽፋረ ፡ እግርከ ፡ በደመ ፡ ቅንዋት ፡ እለ ፡ ተጠምዓ ። ለእመ ፡ ተጠምዐት ፡ ነፍስከ ፡ ውስተ ፡ ኀሊናት ፡ እኩት ፡ ትከውን ፡ ጸሎትከ ፡ ዘኢንጽሕት ፡ (ቄር ፡ እስት ። ፊልክ ፡ ፻፰፩) ።

**ጥሙዕ ፤ (ዓን ፡ ዓት ፡ ምዕት)** ፤ የተነከረ ፡ የተዘፈቀ ፤ ቀለም ፡ የገባ ። ጥሙዓኒ ፡ ደም ፡ (ስንክ ፡ ጥቅ፰፱) ።

**ጥምዐት ፤ (ታት)** ፤ መንከር ፡ መንከር ፡ መዝፈቅ ፤ ቀለም ፡ መግባት ፤ እንከከር ፡ ቀለም ፡ አገባብ ። ጥምዐተ ፡ ሕበሪሁ ። ጥምዐታተ ፡ ሕብር ፡ (መሳ፭ ፡ ፴ ። ሔኖ፰ ፡ ፩) ።

—፤ ቀለም ፤ የቀለም ፡ ዐይነት ፡ ሴቶች ፡ የሚቀቡት ፡ የሚለቀለቁት ። አንስት ፡ ኢይግበራ ፡ ላዕለ ፡ መላትሒሆን ፡ ጥምዐታተ ፡ ቀይሓተ ። ርቱዕ ፡ ለአንስት ፡ ይትገልበባ ፡ ርእሶን ፡ በንጽሕ ፤ ወአኮ ፡ በአሥንዮ ፡ ላሕየ ፡ ገጾን ፡ ወጥምዐታት ፡ ወተሠሕሎ ፡ ወተሰርግዎ ፡ (ፈ ፡ መ ፡ ፴፬ ፡ ፰ ። ዲድ ፡ ፫) ።

**መጠማ** ፤ ምጥማዕ ፤ መንከሪያ ፤ ጢቆሽ ፡ የውሃ ፡ መርጫ ፡ መፈንጠቂያ ። ንሣእ ፡ መጠማ ፡ ዘማይ ፡ ወንፋኅ ፡ ውስተ ፡ ሰማይ ፡ (ሄርማ ፡ ገ፵፬) ።

**ጠሚቅ ፤ ቆት ፤ (ጠመቀ ፡ ይጠምቅ ፡ ይጥምቅ ። ዕብ ፡ ጣባል)** ፤ መጥመቅ ፡ ማጥመቅ ፤ መንከር ፡ መዝፈቅ ፤ ከውሃ ፡ ማግባት ፤ በውሃ ፡ ማጠብ ፤ ወይም ፡ ውሃውን ፡ በራስ ፡ በገላ ፡ ላይ ፡ ማፍሰስ ፡ መቸለስ ፤ መርጨት ፡ ማረብረብ ። ጠሚቀ ፡ ትጠምቆ ፡ (ቀሌ) ። ብዙው ፡ መጽሐፍ ፡ ግን ፡ በጠመቀ ፡ ፈንታ ፡ አጥመቀ ፡ ይላል ፤ ስሕተት ፡ ነው ። አንሰ ፡ አጠምቀክሙ ፡ በማይ ፤ ውእቱሰ ፡ ያጠምቀክሙ ፡ በመንፈስ ። አጥመቁ ፡ አጽርቅተ ፡ ዘሠቀ ፡ ጸጕር ፡ ውስተ ፡ ብሒእ ። አጥመቃ ፡ ሲምድር ፡ በማየ ፡ አይኅ ፡ (ማቴ፫ ፡ ፲፩ ። ስንክ ፡ ነሐ፮ ። መቃ ፡ ገ፯) ።

—፤ መዘለል ፡ መበጥበጥ ፤ ከውሃ ፡ ማዋሐድ ፡ ማስማማት ፤ የድፍድፍ ፡ የማር ፡ የጠላ ፡ የጠጅ ። ጠላ ፡ ጠማቂ ፡ እንዲሉ ። ጸመቀን ፡ እይ ፤ የዚህ ፡ መንቲያ ፡ ነው ።

**ጠማቂ ፤ መጥምቅ** ፤ በቁሙ ፤ የሚጠምቅ ፡ የሚያጠምቅ ፤ አጥማቂ ። ዮሐንስ ፡ መጥምቅ ። ሐናንያ ፡ ለጳውሎስ ፡ መጥምቁ ፡ (ማቴ፫ ፡ ፩ ። ስንክ ፡ ጥቅ፱) ።

**መጥምቃዊ** ፤ ዝኒ ፡ ከማሁ ፤ ያጥማቂ ፡ የጠማቂ ፡ ወገን ፤ አጥማቂነት ፡ ያለው ። ዮሐንስ ፡ መጥምቃዊ ፡ (ፊልክ ፡ ፻፲፪) ።

**አጥመቀ** ፤ አስጠመቀ ፤ አስነከረ ። ሶበ ፡ ተወልደ ፡ ሕፃን ፡ ጥዑየ ፡ ይትዐገሡ ፡ አጥምቆቶ ። እናት ፡ አባቱ ፡ ርሱን ፡ ከማስጠመቅ ፡ (ፈ ፡ መ ፡ ፳፯ ፡ ፯) ። ለካህናት ፡ ግን ፤ ጠሚቅሁ ፡ ጠሚቆቶ ፡ እንጂ ፤ አጥምቆቶ ፡ አያሰኝም ።

**አጥማቂ ፤ መጥምቅ** ፤ የሚያስጠምቅ ፤ አስጠማቂ ። መጥምቅ ፡ ከጠመቀና ፡ ከአጥመቀ ፡ ከኹለቱ ፡ አዕማድ ፡ እንደ ፡ ወጣ ፤ ሌላውም ፡ መስም ፡ እንዲሁ ፡ እንዲወጣ ፡ አስተውል ።

**ምጥማቅ ፤ (ቃት)** ፤ መጥመቂያ ፡ ማጥመቂያ ፤ መጠመቂያ ፡ መታጠቢያ ፤ ቦታ ። ቤተ ፡ ምጥማቅ ። ዋዜማ ፡ ዘደብረ ፡ ምጥማቅ ። ወረደ ፡ ወልድ ፡ እምሰማያት ፡ ውስተ ፡ ምጥማቃት ። በኀበ ፡ ምጥማቃት ፡ እንተ ፡ ላዕላይ ፡ ፍኖት ። ምጥማቃተ ፡ ሰሊሆም ፡ (ኪዳ ። ድጓ ። ኢሳ፯ ፡ ፫ ። ዮሐ፱ ፡ ፯) ።

**ተጠምቀ** ፤ ተጠመቀ ፤ ተነከረ ፤ ታጠበ ፡ ተጣጠበ ፡ በገዛ ፡ እጁ ፤ ወይም ፡ በሰው ፡ እጅ ፤ ስርየት ፡ ልጅነት ፡ ለማግኘት ። ሖር ፡ ተጠመቅ ፡ ውስተ ፡ ተከዜ ፡

ዮርዳኖስ ። ትወፅእ ፡ በሌሊት ፡ ወትጠመቅ ፡ ውስተ ፡ ንቅዐ ፡ ማይ ። ወተጠምቀ ፡ ውስተ ፡ ይእቲ ፡ ዐዘቅት ፡ ዘናጥራን ። ተጠምቀ ፡ ህየ ፡ በማይ ፡ (፬ነገ ፡ ፭ ፡ ፲ ፡ ፲፬ ። ዮዲ ፲፪ ፡ ፯ ። ስንክ ፡ ጥቅ፲፫ ። ኅዳ፲፭) ። ወእም ድኅረ ፡ ተጠምቀ ፡ ሕዝብ ፡ ተጠምቀ ፡ ኢየሱስኒ ። ሖኪ ፡ ፈቂዶ ፡ ለተጠምቀ ፤ አላ ፡ ጽሕቀ ፡ ያብርህ ፡ ማያተ ፡ ወያኀይል ፡ መካናተ ፡ ለእለ ፡ ሀለዎሙ ፡ ይጠመቁ ፡ ውስቴቱ ። ወተጠሚቀ ፡ ወፅአ ፡ እማይ ። እለ ፡ ተጠመቅነ ፡ በእግዚእነ ፡ ውስተ ፡ ሞቱ ። ተጠመቅነ ፡ በአሚነ ፡ አብ ፡ ወወልድ ፡ ወመንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ (ሉቃ፫ ፡ ፳፩ ። ሃይ ፡ አበ ፡ ባዊ ። ተረ ፡ ቄር፲፯ ። ማቴ፫ ፡ ፲፯ ። ሮሜ፯ ፡ ፫ ። ቀሌ) ።

**ጥሙቅ** ፤ (ቃን ፡ ቃት ፡ ምቅት) ፤ የተጠመቀ ፤ እምነትና ፡ ጥምቀት ፡ ያለው ፡ ፍጹም ፡ ክርስቲያን ። እንዘ ፡ ሀሎ ፡ በዝየ ፡ እመሂ ፡ ጥሙቅ ፤ አው ፡ ንኡስ ፡ ክርስቲያን ። እለ ፡ ጥሙቃን ፡ በመንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ (አፈ ፡ ተ፲፫ ። ቀሌ) ።

**ጥምቀት** ፤ (ታት) ፤ በቁሙ ፤ ማጥመቅ ፡ መጠመቅ ፤ አጠማመቅ ፡ ጠመቃ ፤ የማጥመቅና ፡ የመጠመቅ ፡ ሥራ ፡ ኅፅበት ፤ በጥሩ ፡ ውሃ ፡ የሚፈጸም ። የበዓል ፡ ስም ፤ ጌታችን ፡ የተጠመቀበት ፡ ቀን ። (ተረት) ፤ ለጥምቀት ፡ ያልኾነ ፡ ቀሚስ ፡ ይበጣጠስ ። ጥምቀታት ፡ ዘዘ ፡ ዚኣሁ ። በእንተ ፡ ሥርዐተ ፡ ጥምቀት ፤ ውሉድ ፡ እለ ፡ ሞቱ ፡ ዘእንበለ ፡ ጥምቀት ። ጥምቀት ፡ ዘዳግም ፡ ልደት ። ቅዱስ ፡ ጥምቀት ። እምድኅረ ፡ ነሥኡ ፡ ጥምቀተ ። ስመ ፡ ጥምቀትየ ። ኀፀበ ፡ በማየ ፡ ጥምቀት ፡ (ዕብ፱ ፡ ፲ ። ፈ ፡ መ ፡ ፳፯ ፡ ፭ ። ዲድ ፡ ፵ ። ኪዳ ። ቀሌ ። ስንክ ፡ ጥር፲፭ ። ነሐ፱) ።

ጥምቀት ፡

ጠማር ፤—ክታብ ፤—ጠወማር ።

**ጠኒን** ፤ ኖት ፤ (ጠነ ፡ ይጠንን ፡ ይጥንን ። ዕብ ፡ ጣናን) ፤ መርጠብ ፡ መራስ ፤ ርጥብ ፡ መኾን ፡ መታደስ ። መጥናት ፡ መጠንከር ፤ ማየል ፡ መበርታት ፤ እያደጉና ፡ ኀይል ፡ እየጨመሩ ፡ መኼድ ፤ የሕዋሳትና ፡ የዕፀዋት ። ጠለየን ፡ እይ ፤ የዚህ ፡ ጎር ፡ ነው ።

**ጥን** ፤ (ብ ፡ ኣጥናን) ፤ ርጥብ ፡ ለጋ ፡ ወጣት ። ጥኑ ፡ ጠንካራ ፤ ኀይለኛ ፡ ጕበዝ ። ወገብረ ፡ ኀይለ ፡ ዘአጥናን ፡ (፩ነገ ፡ ፲፱ ፡ ፵፰) ። ዘአጥናን ፡ ትርፍ ፡ ንባብ ፡ ነው ፤ ከግእዝ ፡ በቀር ፡ በጽርኡም ፡ በዕብራይስጡም ፡ አይገኝ ።

**አጥናን** ፤ ቅድስት ፡ ሥላሴ ፤ ወይም ፡ ስባቱ ፡ ሀብታት ፡ (ኢሳ፲፩ ፡ ፪) ። በኀይለ ፡ አጥናን ፡ ዘሞአ ፡ ለሰይጣን ። ኀይልከ ፡ ኀይለ ፡ አጥናን ። ኀይል ፡ ዘአጥናን ፡ (ድጓ ። ስንክ ፡ ኅዳ፲፫ ። አርጋ ፡ ፮) ። አንዳንድ ፡ ሰዎች ፤ ትጋት ፡ ትጉህነት ፡ ሙቀት ፤ መንፈሳዊ ፡ ቅንአት ፡ ይሉታል ፤ ምስጢሩ ፡ ከሀብታት ፡ ይገባል ።

**ጠነይ** ፤ ዋሻ ፡ ጕሬ ፤ ባሕር ፡ ኵሬ ፤ ወይም ፡ ደሴት ፡ የባሕር ፡ ተሬ ። ጣና ፡ ማለት ፡ ከዚህ ፡ ወጥቷል ፤ ምስጢሩ ፡ ባሕርነትና ፡ ርጥበት ፡ ነው ፤ ስፋትም ፡ ያሳያል ። ቦአ ፡ ጠነየ ፡ ወኢረከበ ፡ (አዋል) ። ዲልማን ፡ ግን ፡ ኀሠሠ ፡ ብሎታል ።

**ጥንፍ** ፤ (ብ ፡ ጥነፍ ። ጽንፍ ፡ ጽነፍ ፤ ጸነፈ ። ዐረ ፡ ጠንፍ ፤ ጡንፍ ፤ የቤት ፡ አፍ አዊ ፡ ክፍል) ፤ የዐምድ ፡ ክባስ ፤ የባላና ፡ የወጋግራ ፡ ራስ ፤ ዘንድ ፡ ጋድም ፤ የድንኳን ፡ ዘንግ ፡ መሎጊያ ፡ ተራዶችን ፡ እንደ ፡ ዋልታና ፡ እንደ ፡ ጋድም ፡ ኹኖ ፡ የሚያያይዝና ፡ የሚያጠና ። በስተላይ ፡ ለሚኾን ፡ ለሥራ ፡ ጌጥ ፡ ኹሉ ፡ ይነገራል ። ጠንፋ ፡ የሚሉት ፡ ስም ፡ ከዚህ ፡ ወጥቷል ፤ ዘሩ ፡ ጸነፍ ፡ ነው ። ጥነፊሁ ፡ ዘብሩር ፤ ጥነፊሁ ፡ ለዐምድ ፡ (ዘፀ፳፯ ፡ ፲ ፡ ፲፩) ።

**አጥነፈ** ፤ አያያዘ ፤ አዋደደ ። ወታጠንፎ ፡ በጥንፍ ፡ (ዘፀ፴ ፡ ፱) ።

**ጥንፍሕ** ፤ አው ፡ ጥፍንሕ ፤ (ጸነፈ ፡ ጸፈነ) ፤ ሸውራራ ፤ ጨፋና ፤ ጨንቋራ ፡ ሎልጨላ ፤ ዐይኑና ፡ አስተያየቱ ፡ የማያምር ። አዕይንቲሁ ፡ በአምሳለ ፡ ጥንፍሕ ፡ (ቄስጠ ፡ ፯) ። ባ፲ኛው ፡ ደግሞ ፡ ጥፍንሕ ፡ ይላል ።

**ጠንቄለ** ፤ (ጠቀለ) ፤ ጠነቈለ ፤ ጠነቀለ ፤ በማር ፡ በሥንጥር ፡ በጣት ፡ ነካ ፡ ጠቈመ ። መጠንቈል ፡ መጣፍን ፡ ገልጦ ፡ ስንጠረዥን ፡ በማር ፡ እየወጉ ፡ ቍጥሩን ፡ ከስጠንቋዩ ፡ ስም ፡ አስማምቶ ፡ የንባቡን ፡ ነገር ፡ መፈለግ ፡ ነው ። ሥራይ ፡ ወጠንቍሎ ፡ (ፍ ፡ ነ ፡ ፳፫) ። መጠንቀል ፡ ግን ፡ በጥቂቱ ፡ ለሚላስና ፡ ለሚቀመስ ፡ ለሚሸተት ፡ ነው ። (ተረት) ፤ አላርፍ ፡ ያለች ፡ ጣት ፡ ዐር ፡ ጠንቅላ ፡ መጣች ። ተንኰለ ፤ ተንኰል ፡ ሠራ ፡ ተንኰለኛ ፡ ኾነ ። ጠና ፡ ተ ፡ ይዋረሳሉ ፤ ውስጠ ፡ ውስተ ።

**ጠንቋሊ** ፤ (ሊት ፡ ልያን ፡ ያት ፤ ቄልት) ፤ የሚጠነቍል ፡ ጠንቋይ ፡ ሟርተኛ ፤ መጻእያትን ፡ የሚናገር ፡ ሥጋዊና ፡ ሰይጣናዊ ፡ ነቢይ ፤ ተንኰለኛ ። ሡሉ ፡ ዘተሰወ ፡ ማሪተ ፡ ወጠንቋሌ ። ዘየአምን ፡ ነገረ ፡ ጠንቋልያን ፡ ወመሠርያን ። አይቴ ፡ ሀለዉ ፡ ርኩሳን ፤ ዘማውያን ፡ ወጠንቋልያን ። ጠንቋልት ፡ (ቄድር ፡ ገ፳፭ ። ፍ ፡ ነ ፡ ፭ ፡ ፳፫ ። ግንዘ ። ገድ ፡ አዳ ፡ ገ፺፬) ።

**መጠንቍል** ፤ (ልት ፡ ላን ፡ ላት) ፤ ዝኒ ፡ ከማሁ ። እመሂ ፡ ዘያጣዑ ፤ እመሂ ፡ መጠንቍል ፤ እመሂ ፡ ዘማዊ ፡ ወሐሳዊ ፡ (ቄድር ፡ ገ፳፯) ።

**ጥንቋሌ** ፤ መጠንቈል ፤ አጠንቋቈል ፤ ሟርት ፡ ጥንቈላ ፤ የተንኰል ፡ ሥራ ፡ (ገድ ፡ አዳ) ።

**ጠንቀቀ** ፤ (ጠቀቀ) ፤ ጠነቀቀ ፤ አስተዋለ ፤ አስተካከለ ፤ ልክ ፡ አደረገ ፤ መላ ፡ ፈጸመ ፡ ጨረሰ ፤ ያግብር ፡ የነገር ፡ የስፍር ፡ የቍጥር ። ኢጠንቀቀ ፡ ዐቂቦቶ ። ዘተወክፈ ፡ ዛተ ፡ መጽሐፈ ፡ ወጠንቀቃ ። ወመጠነ ፡ ርሕበ ፡ ሕንጻ ፡ ወጠንቀቀ ፡ በኀለት ። ዘጠንቀቀ ፡ ኆምሳ ፡ ዓመተ ። ኢይደሉ ፡ አውስቦ ፡ ብእሲት ፡ ዘኢጠንቀቀት ፡ ዐሠርተ ፡ አውራኀ ፡ እምድኅረ ፡ ሞተ ፡ ምታ ፡ (ፍ ፡ ነ ፡ ፴፫ ፡ ፫ ። መጽ ፡ ጠማ ። ሕዝ፵ ፡ ፭ ፡ ፯ ። ዲድ ፡ ፱ ። ፈ ፡ መ ፡ ፭ ፡ ፲፯) ። በጠንቀቀ ፡ ፈንታ ፡ አጠንቀቀ ፡ ይላል ፤ ስሕተት ፡ ነው ። ሸሉ ፡ ምክሩ ፡ ዘከመ ፡ ያጠንቅቅ ፡ ኆሪወ ፡ ማኅተም ። አጠንቀቀ ፡ ነገረ ፡ (ሚራ፴፰ ፡ ፳፯ ። መጽ ፡ ምስ) ።

**ጠንቃቂ** ፤ (ቂት ፡ ቅያን ፡ ያት) ፤ በቁሙ ፤ የሚጠነቅቅ ፡ የሚያሳምር ፤ አስተዋይ ፡ ተመልካች ። ማእምር ፡ ወጠቢብ ፡ ወልብው ፡ ወጠንቃቄ ፡ መጻሕፍት ፡ (ዮሴፍ) ።

**አጠንቀቀ** ፤ አስጠነቀቀ ፤ አስለበመ ፤ ሠሪን ፡ በሥራ ፡ ላይ ።

**አስተጠንቀቀ** ፤ ዝኒ ፡ ከማሁ ። አስተጠንቀቀ ፡ ሎቱ ፡ ወነገሮ ፡ ዘከመ ፡ ይገብራ ፡ (ቀሌ) ።

**ተጠንቀቀ** ፤ ተጠነቀቀ ፤ ሥራው ፡ ወይም ፡ ሠሪው ። ሶበሰ ፡ ኢተዐውቀት ፡ ወኢተጠንቀቀት ፡ ዛቲ ። ዝንቱ ፡ ተጠንቀቀ ፡ በብዙኅ ፡ ቀኖናት ፡ (ፈ ፡ መ ፡ ፱ ፡ ፲ ። ፵፩ ፡ ፱) ።

**ተጠናቀቀ** ፤ ተራቀቀ ፤ መራቀቅ ፡ አበዛ ። ሀለወ ፡ ዘይጠበብ ፡ ወይጠናቀቅ ፡ እንዘ ፡ ይዔምፅ ። ተጠናቀቀ ፡ ለገቢረ ፡ አምሳሉ ፡ በዘይሜኒ ፡ ወይኄይስ ። በተጠናቅቆ ፡ (ሚራ፲፱ ፡ ፳፭ ። ጥበ፲፬ ፡ ፲፱ ። ቀሌ) ።

**ጥንቁቅ** ፤ (ቃን ፡ ቃት ፡ ቅቅት) ፤ በቁሙ ፤ የተጠነቀቀ ፡ ጠንቃቃ ፤ ፍጹም ። ጥንቁቅ ፡ ውስቴታ ። ጥንቁቅ ፡ በርእሱ ። ጼናከሙ ፡ ጥንቁቅ ፡ (ዮሴፍ ። ቄር ፡ ጸላ ። ስንክ ፡ ጥቅ፯) ።

**ጥንቁቀ** ፤ ፈጽሞ ፤ ጠንቅቆ ፡ ጠንቃቃ ፡ ኹኖ ፤ በጥንቃቄ ፡ በጭራሽ ። መኑ ፡ ይክል ፡ ነጊረ ፡ ምሕረቱ ፡ ጥንቁቀ ፡ (ሚራ፲፰ ፡ ፭) ።

**ጥንቃቄ** ፤ በቁሙ ፤ (ላጥጠ) መጠንቀቅ ፤ አጠነቃቀቅ ፡ ጥንቀቃ ፤ ጠንቃቅነት ። በጥንቃቄ ፡ ንኅሥሥ ። ይንግር ፡ ድጢይ ፡ ኀጣውኢሁ ፡ ለካህን ፡ በጥንቃቄ ። ፈጠረ ፡ ሰማየ ፡ በጥንቃቄ ፡ (ቄር ፡ ጸላ ። ቄድር ፡ ገ፴፱ ። ደራሲ) ።

**ጥንቅቅና** ፤ ጥንቁቅነት ፤ ጠንቃቅነት ፤ ጥንቁቅ ፡ ጠንቃቃ ፡ መኾን ፤ መተካከል ። እስመ ፡ ሸሉ ፡ ምሳሌ ፡ ዘበዝንቱ ፡ ይደክም ፡ እምጥንቅቅና ፤ ወይውኅድ ፡ እምአማን ፡ (ቄር ፡ ጸላ) ።

**አስተጠናቀቀ** ፤ አጠናቀቀ ፤ አራቀቀ ፤ አታጋ ። ጠባዩ ፡ ማደራረግና ፡ ማስደረግ ፡ ነው ፤ ባስደራጊነቱ ፡ ከአጠንቀቀና ፡ ከአስተጠንቀቀ ፡ ይስማማል ፤ ተደራራጎቹ ፡ ግብራት ፡ ሕዋሳት ፡ ሲኾኑ ፡ ምስጢሩ ፡ ከማድረግና ፡ ከማስደረግ ፡ ከኹለቱ ፡ ኹሉ ፡ ይገባል ። ፈድፋደ ፡ ናስተጠናቅቅ ፡ ኅሊናነ ፤ አልቦ ፡ ዘይክል ፡ አስተጠናቅቆ ። ያስተጠናቅቁነ ፡ ለገቢረ ፡ ሠናይ ፡ (ቄር ፡ ጸላ ። ቀሌ) ።

**ጥንቃቅ** ፤ (ቃት) ፤ የተራራ ፡ ሥር ፡ መሠረት ፤ በባሕር ፡ ውስጥ ፡ ያለ ፡ ቈላ ፡ ማዕምቅት ፡ ዕርድ ፡ ምሽግ ፡ መቀራቅርት ። ናሁ ፡ ርእስየ ፡ ውስተ ፡ ጥንቃቃተ ፡ ደብር ። ፈቀደ ፡ ከመ ፡ ይቤዙ ፡ ሸሎ ፡ ነፍሳተ ፡ እለ ፡ ሙቁሓን ፡ ኀበ ፡ ጽልመተ ፡ ሞት ፡ ወጥንቃቃተ ፡ ሲኦል ፡ (ዮና፪ ፡ ፯ ። መቅ ፡ ወን) ።

**ጥንቁር** ፤ (ራት ። ነቍር ፡ ነቈረ) ፤ ጭንቁር ፤ የቍስል ፡ ስም ፡ ፩ ፡ ዐይነት ፡ ቍስል ፤ በሺዋ ፡ ሻሕኝ ፤ በዕብራይስጥ ፡ ሽሒን ፡ ይባላል ፤ (ዘፀ፱ ፡ ፱ ፡ ፲) ።

—፤ ያይጥ ፡ ወገን ፡ ጕርጥ ፤ ዐይጠ ፡ መጐጥ ፡ አፈ ፡ ሹል ፡ ጥርስ ፡ ስል ፤ ባፉ ፡ የሚያንቍር ፡ የሚሸንቍር ። ከመ ፡ ኢይርከቦሙ ፡ አንጼዋ ፡ አው ፡ ጥንቁር ፡ (ቄድር) ።

**ጥንት** ፤—በቁሙ ፤—ወጠነ ፡ ወጠነ ።

**ጥንትዮን** ፤—አበቅቴ ፡ ፀሓይ ፤—ፕንትዮን ፡ ፐ ።

**ጥዒው** ፤ ዎት ፤ (ጠዐወ ፡ ይጥዑ ፡ ይጥዐው ። ዕብ ፡ ጣዓህ ። ሱር ፡ ጥዓእ ። ዐረ ፡ ጠዓ) ፤ መሳት ፡ መሳሳት ፤ ከመንገድ ፡ መውጣት ፤ ጣዖት ፡ ማምለክ ፡ መቅረጽ ፡ መሥራት ። ከልክ ፡ ያለፈ ፡ ዝሙትና ፡ ፍቅረ ፡ ንዋይም ፡ አምልኮ ፡ ጣዖት ፡ ይባላል ። መጽሐፍ ፡ ግን ፡ በጠዐወ ፡ ፈንታ ፡ አጥዐወ ፡ ይላል ። ዘያስግል ፡ ወያጥዑ ፡ አጥዕዎ ፡ (ሲኖድ) ። ፪ኛም ፡ በባረከ ፡ ቤት ፡ ጣዕዎ ፡ ጣዐወ ፡ ይጣዑ ፡ ይላልና ፤ ይህነን ፡ ደግሞ ፡ አጣዐወ ፡ ያጣዑ ፡ እያለ ፡ ባስደራጊ ፡ አንቀጽ ፡ ይጥፋል ። እለ ፡ ያጣዕዉ ፡ በከርሥ ። አጣዕዎ ፡ ወሥራይ ። ይመርሕ ፡ ውስተ ፡ አጣዕዎ ፤ ኢታስግሉ ፡ ወኢታጣዕዉ ፡ (፪ዜና ፡ ፴፫ ፡ ፮ ። ገላ፭ ፡ ፳ ። ዲድ ፡ ፴፭) ።

**ጠዓዊ** ፤ (ዊት ፡ ውያን ፡ ያት) ፤ የሳተ ፡ የሚስት ፤ መምለኬ ፡ ጣዖት ። ጠዓውያን ፡ (ቀሌ) ።

**መጥዕው** ፤ መጣዕው ፤ (ዋን ፡ ዋት ፡ ዑት) ፤ ዝኒ ፡ ከማሁ ። መጣዕዋን ፡ (ዲድ) ።

**መጥዐዊ** ፤ ዝኒ ፡ ዓዲ ፡ ከማሁ ። መጥዐዊ ፡ ወመጸብሓዊ ። አረሚ ፡ መጥዐውያን ፡ (ፍ ፡ ነ ፡ ፭ ። ቅዳ ፡ ሕር) ። በመጣዕውና ፡ በመጥዐዊ ፡ ፈንታ ፡ መጣዓዊ ፡ ይላል ፡ አያስኝም ። (ቀሌ) ።

**ጣዕዋ** ፤ (ዋት) ፤ ጥጃ ፡ እንቦሳ ፡ ውርንጫ ፡ ግልገል ። ከመ ፡ ጣዕዋ ፡ ዘተፈትሐ ፡ እማእሰሩ ። ጣዕዋ ፡ ላሕም ፡ ወፈረስ ፡ ወአድግ ፡ ወገመል ። ኢታብስል ፡ ጣዕዋ ፡ በሐሊበ ፡ እሙ ፡ (ሚል፬ ፡ ፪ ። ፍ ፡ ነ ፡ ፵ ። ዘፀ፳፫ ፡ ፲፱) ።

—፤ ወይፈን ፤ ጊደር ። ጣዕዋ ፡ እምአልሕምት ። ጣዕዋ ፡ ዘሠለስቱ ፡ ዓመት ። ጣዕዋ ፡ አንስቲያዊት ። እልኩ ፡ ጣዕዋት ፡ ወአልሕምት ። በግዕ ፡ ንጹሕ ፡ ወልደ ፡ ቅድስት ፡ ጣዕዋ ፡ (ኩፋ፯ ፡ ፲፬ ። ሔኖ፹፭ ፡ ፫ ። ፹፮ ፡ ፫ ። አርጋ) ።

**ጣዖት ፤ (ታት ። ዕብ ፡ ጣዑት) ፤** ስሕተት ፡ የስሕተት ፡ ሥራ ። በቁሙ ፤ ግልፎ ፡ ስብኮ ፤ የጥጃ ፡ የንብሳ ፡ የሰው ፡ የንስሳ ፡ ምስል ፤ ስሑታን ፡ ሰዎች ፡ የሚያመልኩት ። ገብረ ፡ ጣዖተ ። ቤተ ፡ ጣዖት ። ድኩም ፡ ወጽኑስ ፡ ጣዖተ ፡ ዝ ፡ ዓለም ። ከመ ፡ ይሕንጽ ፡ ምሥዋዕ ፡ ወይሥርዓሙ ፡ ለጣዖታት ፡ (ኩፋ ፡ ፲፩ ። ፲፪ ። ገላ፭ ፡ ፱ ። ቅዳ ፡ ዮሐ) ።



ጣዖት ፡

**አጥዐወ ፤ አጣዐወ ፤** አሳተ ፡ አሳሳተ ፤ ጣዖት ፡ አስመለከ ። ልማዱ ፡ ግን ፡ አድራጊነት ፡ ነው ። እመ ፡ ቦ ፡ እምአኀው ፡ ዘያጥዑ ። እለ ፡ ያሰግሉ ፡ ወእለ ፡ ያጣዕዉ ። ተምዐ ፡ መንፈሱ ፡ ሶበ ፡ ርእየ ፡ ያጣዕዉ ፡ ኵሉ ፡ ሀገር ፡ (፩ቆሮ ፡ ፩ ፡ ፲፩ ። ቀሌ ። ግብ፲፯ ፡ ፲፮) ።

**አጥዓዊ ፤ መጥዐዊ ፤ መጥዕው ፤ መጣዕው) ፤** የሚያስት ፡ አሳች ፤ ጣዖት ፡ አስመላኪ ። ከአጥዓዊ ፡ በቀር ፡ ሣስቱ ፡ እንደ ፡ ፊተኛው ፡ ባድራጊነትም ፡ ይፈታል ።

**ጣዕጥዐ ፤—ጠረገ ፤—ጣእጥአ ፡ ጣእጥአ ።**

**ጥዕየ ፤ ዮት ፤ (ጥዕየ ፡ ይጥዒ ፡ ይጥዐይ) ፤** መጤን ፤ ጤና ፡ ማግኘት ፡ መሻር ፤ መፈወስ ፡ መዳን ፤ ጤናማ ፡ ባለጤና ፡ መኾን ። ለጥዕይ ፡ ከመ ፡ ይጥዐይ ፡ ኵሉ ፡ ዘይሠርጽ ፡ ወይልህቅ ፡ ዲበ ፡ ምድር ። ኢይጥዒ ፡ ቍስልየ ። ሶበ ፡ ትጥዒ ፡ እምሕማምከ ። እስከ ፡ ይጥዒ ፡ ወይትፌወስ ፡ (ኩፋ ፡ ፱ ። ኢዮ ፲፭ ፡ ፯ ። አፈ ፡ ተ፲፯ ። ዮሴፍ) ።

**ጥዑይ ፤ (ያን ፡ ያት ፡ ዒት) ፤** የጤነ ፤ ጤና ፡ ያገኘ ፡ ጤነኛ ፤ ጤናማ ፡ ባለጤና ፤ ታሞ ፡ የዳነ ፡ ወይም ፡ ያልታመመ ፡ ደኅና ። ነዳይ ፡ ጥዑይ ። ወአኮ ፡ ጥዑያን ። ሕዐይንት ፡ ጥዑያት ፡ (ሚራ፵ ፡ ፲፱ ። ማቴ፱ ፡ ፲፪ ። አፈ ፡ ተ፲፮) ።

**ጥዑየ ፤** ድኖ ፡ ጤና ፡ አግኝቶ ፤ ባለጤና ፡ ኹኖ ፤ በጤና ፡ በሰላም ። ትሰፍሕ ፡ ጥዒታ ። ውሉድ ፡ እለ ፡ ተወልዱ ፡ ጥዑያኒሆሙ ። ኖመ ፡ ጥዑየ ፡ ወሰከበ ፡ ሐዋዘ ፡ (ጥበ፳ ፡ ፩ ። ፈ ፡ መ ፡ ፳፮ ፡ ፱ ። ስንክ ፡ ኀዳ፯) ።

**ጥዕየት ፤** መዳን ፡ ጤና ፡ ማግኘት ፤ ባለጤናነት ።

**ጥዒና ፤ (ናት) ፤** በቁሙ ፤ ጤና ፡ ደኅንነት ፤ የሕዋሳት ፡ ሰላም ፤ የምግብና ፡ የሆድ ፡ መስማማት ፤ ከርን ፡ ብስና ፡ የጕመን ፡ ጤና ፡ እንዲሉ ። ሠረቀ ፡ ፀሓይ ፡ ላዕሌሆሙ ፡ ለጥዒና ። ለጥዒና ፡ አዘማድየ ። እምቅድመ ፡ ይርከብ ፡ ፍጻሜ ፡ ጥዒና ። ዕቀቦ ፡ በሰላም ፡ ወበጥዒና ፡ (ኩፋ ፡ ፱ ። ዮሴፍ ። አፈ ፡ ተ፳፱ ። ቅዳ) ።

**አጥዐየ ፤** አጤነ ፤ ልብ ፡ አደረገ ፡ ዐሰበ ፡ አስተዋለ ፡ (ዐማርኛ) ። አዳነ ፤ አሻረ ፡ ፈወሰ ፤ ጤነኛ ፡ አደረገ ። አጥዐየ ፡ መፃጕዐ ። ፈውሳት ፡ እለ ፡ ያጥዕያ ፡ ቍስላተ ። ዝንቱ ፡ ደዌ ፡ ይከውን ፡ ዕጹበ ፡ ፈውሶቱ ፡ ወአጥዕዮቱ ። ሕጸጸ ፡ ቅንአት ፡ ያጥዒ ፡ ሥጋ ፡ (ግንዘ ። ፈ ፡ መ ፡ ፫ ፡ ፫ ፡ ፯ ። ፈላስ) ።

**አጥዓዪ ፤ መጥዐዪ ፤ (ዪት ፡ ይያን ፡ ያት) ፤** የሚያሽር ፡ አዳኝ ፤ ፈዋሽ ።

**መጥዕይ ፤ (ያን ፡ ያት ፡ ዒት) ፤** ዝኒ ፡ ከማሁ ።

**ምጥዓይ ፤ (ያት) ፤** መዳኛ ፤ ጤና ፡ ማግኛ ፡ መፈወሻ ፤ በታ ፡ መድኀኒት ፡ ምክንያት ።

**ጥዒም ፤ ሞት ፤ (ጥዕመ ፤ ጠዐመ ፡ ይጥዕም ፡ ይጥዐም ። ዕብ ፡ ጣዐም ። ሱር ፡ ጥዔም ። ዐረ ፡ ጠዒመ) ፤** መቅመስ ፡ መሞከር ፤ ማጣጣም ፡ ከጣዕም ፡ መድረስ ፤ ጣዕም ፡ ማወቅ ። ኢይክል ፡ ጥዒመ ፡ መብልዐ ። ዘእንበለ ፡ እጥዐም ፡ እክለ ። እመ ፡ ቦ ፡ ዘጥዕመ ፡ ወኢውኅጠ ። ጥዕም ፡ ለሞት ። ወጥዒሞ ፡ አበየ ፡ ሰትየ ። ጥዕመት ፡ ከመ ፡ ሠናይ ፡ ተቀንዮ ፡ (ኢዮ፴፫ ፡ ፳ ። ጦቢ፪ ፡ ፱ ። ቀሌ ። ዕብ፪ ፡ ፱ ። ማቴ፳፯ ፡ ፴፬ ። ምሳ፴፩ ፡ ፴፩) ።

—፤ መጣም ፡ መጣፈጥ ፤ ጥፍጥ ፡ መኾን ፤ ደስ ፡ ማሰኘት ። ምንት ፡ ይጥዕም ፡ እመዓር ። ሐልቦ ፡ ዘይጥዕም ፡ እምነ ፡ ዐቂበ ፡ ትእዛዙ ፡ ለእግዚ ። ቦ ፡ እክል ፡ ዘይጥዕም ፡ እምእክል ። ለዘማዊ ፡ ኵሉ ፡ እክል ፡ ይጥዕሞ ። ጥዕመ ፡ መዐዛየ ። ይጥዕም ፡ እመዓር ፡ ዝክርየ ። ይጥዕሞሙ ፡ ንዋም ። ጥዕመቶ ፡ እኪት ፡ ውስተ ፡ አፉሁ ፡ (መሳ፲፬ ፡ ፲፰ ። ሢራ ፡ ፳፫ ፡ ፳፯ ። ፴፮ ፡ ፳፫ ። ፳፫ ፡ ፲፯ ። ፳፱ ፡ ፲፰ ፡ ፳ ። አፈ ፡ ድ፳፱ ። ኢዮ፳ ፡ ፲፪) ።

**አጥዐመ ፤** አበላ ፡ አቀመሰ ፤ አስበላ ፡ አስቀመሰ ። አጥዐመ ፡ ሥጋ ፡ ለአኀው ። ወአጥዐሞ ፡ ሞተ ። እግዚ ፡ አጥዐሞሙ ፡ በከመ ፡ አጥዐሙ ፡ ለሰብእ ፡ ረኃበ ፡ (ፊልክ ፡ ፻፱፫ ። ቄር ፡ ድ፷፱ ። ዮሴፍ) ።

—፤ አጣመ ፡ አጣፈጠ ፤ ጣፋጭ ፡ አደረገ ። ጼው ፡ ዘአጥዐሞ ፡ ለልቡሕ ። አጥዕሙ ፡ መዐዛክሙ ። አጥዕማ ፡ ለማሕሌትየ ፡ ውስተ ፡ አፈ ፡ ኵሉ ፡ (ቅዳ ፡ ዮሐ ። ሢራ ፡ ፵፱ ፡ ፲፬ ። ስንክ ፡ ታኅ፭) ።

**አስተጥዐመ ፤ አስተጠዐመ ፤ (ያስተጥዕም) ፤** ዝኒ ፡ ከማሁ ፤ አጣፈጠ ፡ አሰናዳ ፤ አደነቀ ። ዘኅቡረ ፡ አስተጠዐምከ ፡ ሲተ ፡ መባልዕተ ። በከናፍሪሁ ፡ ያስተጥዕም ፡ ለከ ፡ ቃሉ ። እመ ፡ አስተጠዐምከ ፡ ሎቱ ፡ ምግባሮ ፡ ቀተልኮ ፡ ለእኁከ ። ሥጋ ፡ ያስተጥዕም ፡ ለነፍስ ፡ ምግባረ ፡ ሕሡመ ፡ (መዝ ፡ ፶፱ ። ሢራ፲፪ ፡ ፲፯ ። ዲድ ፡ ፯ ። ዮሴፍ) ።

—፤ ደስ ፡ ፈቅ ፡ አሰኘ ፤ አስጐመዠ ። ሰይጣን ፡ ያስተጥዕም ፡ ሎሙ ፡ በኀዲጥ ፡ ወይኬንን ፡ ሎሙ ፡ በብዙኅ ፡ (ቀሌ) ።

**ተጥዕመ** ፤ ተቀመሰ ፤ ተጣፈጠ ።

**ጥዑም** ፤ (ማን ፡ ማት ፡ ዕምት) ፤ የተቀመሰ ፤ የተጣፈጠ ። በቁሙ ፤ የጣመ ፡ የጣፈጠ ፡ ጥፍጥ ፤ ውብ ፡ መልካም ፡ ደስ ፡ የሚያሰኝ ። መዓር ፡ ጥዑም ። ልሳን ፡ ጥዑም ። ጥዑማነ ፡ ዜና ፡ ወዝክር ። ብልዑ ፡ ወስተዩ ፡ ጥዑማተ ። ጥዕምት ፡ በቃላ ፡ (ሕዝ፫ ፡ ፫ ። ሚራ፯ ፡ ፳ ። ስንክ ፡ መስ፲፱ ። ነሐ፳ ፡ ፲ ። ድጓ) ።

**ጥዕመት** ፤ መቅመስ ፡ መቀመስ ፤ አቀማመስ ፡ ቀመሳ ፡ ቅምሻ ። መጣም ፡ መጣፈጥ ፡ አጠፋፈጥ ፤ ጣዕም ፡ ጥፍጥንት ። ወሀበት ፡ ፍተታተ ፡ በረከት ፡ እምነ ፡ አውሎግያ ፤ ወሰበ ፡ በልዓ ፡ ኮነ ፡ ጥዕመታ ፡ ውስተ ፡ አፉሁ ፡ ከመ ፡ መዓር ፡ (ስንክ ፡ ሠኔ፲፱) ።

**ጣዕም** ፤ (ማት) ፤ በቁሙ ፤ ጣም ፡ ጥፍጥንት ፤ ወይም ፡ መራርነትና ፡ ጥፍጥንት ፤ የመብል ፡ የመጠጥ ፡ የነገር ፡ የምስጢር ፡ ጠባዩና ፡ ቃናው ፡ ሐሳቡና ፡ ስልቱ ፤ ጉረሮና ፡ ገሮ ፡ ለይቶ ፡ የሚያውቀው ። ጉርዔ ፡ ይፈልጦ ፡ ለሖሉ ፡ ጣዕመ ፡ እክል ። ፍሬያት ፡ ዘበበ ፡ ጣዕሙ ። ሞገሰ ፡ ቃሉ ፡ ወጣዕመ ፡ ነገሩ ። አንክረ ፡ ንጉሥ ፡ እምጣዕመ ፡ ቃሉ ፡ (ሚራ፴፮ ፡ ፳፱ ። ቀሌ ። ድጓ ። ስንክ ፡ ነሐ፳) ።

—፤ ጥሩ ፡ ምግብ ፤ የላመ ፡ የጣመ ፡ የሚያስጐመኝ ። ከመ ፡ ይጹም ፡ እምእሉን ፡ ጣዕማት ። ናሁ ፡ በላዕኩ ፡ ሖሎ ፡ ጣዕማተ ፡ ወኢረከብኩ ፡ ዘይጥዕም ፡ እምነ ፡ ጥዒና ፡ (ፊ ፡ መ ፡ ፲፬ ፡ ፱ ። ፊላስ ፡ ገ፳፭) ።

—፤ ተድላ ፡ ደስታ ፡ ምቾት ፤ ብዕል ፡ ሹመት ። ኢይብልዑ ፡ ለጣዕም ። ይደሉ ፡ ለሰ ፡ አሐዱ ፡ ከመ ፡ ይልበስ ፡ በጣዕመ ፡ ዘመን ። እንዘ ፡ ያአምሩ ፡ ጣዕሞ ፡ ለዓለም ፡ ወምረራ ፡ ለሞት ። መነኑ ፡ ፍትወታተ ፡ ወጣዕመ ፡ ዝ ፡ ዓለም ፡ (ፍ ፡ ነ ፡ ፲ ። ፳፫ ። መቃ ፡ ገ፲፱ ። ቀሌ) ።

—፤ ፍትወት ፡ እንስሳዊት ፤ የፍትወት ፡ ሥራ ፤ ፈቃደ ፡ ሥጋ ። ተሰጥሞ ፡ ውስተ ፡ ጣዕማት ፡ እንስሳውያት ፡ (ፊ ፡ መ ፡ ፲፯ ፡ ፬) ።

**ተጣዐመ** ፤ ተጣጣመ ፤ ተቃመሰ ።

**አስተጣዐመ** ፤ (ያስተጣዕም) ፤ አቃመሰ ፡ አቀማመሰ ፤ አጠፋፈጠ ፤ አስነዳዳ ። ኢናስተጣዕም ፡ ለክርሥነ ፤ አላ ፡ ናስተጣዕም ፡ ትምህርተ ፡ መንፈሳዌ ፡ (አዋል) ።

**ጣፍ** ፤ (ዕብ) ፤ ስመ ፡ ሕፃናት ፡ ንኡሳን ፤ ጉባኤ ፡ ሕፃናት ፤ ከቤት ፡ የሚውሉ ፤ ራሳቸውን ፡ ያልቻሉ ፡ ታናናሽና ፡ ጥቃቅን ፡ ልጅ ፡ ኹሉ ። በትግሬና ፡ በትግሪኛ ፡ ግን ፡ ጤፍ ፡ ማለት ፡ ነው ፤ የባሕር ፡ ጤፉንም ፡ ጤፋዊ ፡ እንደ ፡ ማለት ፡ ጣፍጣፎ ፡ ይሉታል ፡ (ሐባበኙ) ።

**ጠፍአ** ፤ **አት** ፤ (**ጠፍአ ፡ ይጠፍእ ፡ ይጥፋእ ። ዐረ ፡ ጠፍአ**) ፤ መጥፋት ፡ መድለም ፤ ዕልም ፡ ድርግም ፡ ማለት ፤ መበላሸት ፡ ከንቱ ፡ መኾን ፤ የእሳት ፡ የመብራት ፡ የዐይን ፡ የብርሃን ፡ የልብ ፡ የገንዘብ ፡ የሥራ ፡ የመንገድ ። መሸሽ ፡ መኰብለል ፤ መሰወር ፡ መደበቅ ፤ ካይን ፡ መራቅ ፡ መርቀቅ ፤ መሞት ፡ መታጣት ፤ መውደም ፡ መፈታት ፤ የሰው ፡ የንስሳ ፡ ያገር ። ጠፍአ ፡ ይጠፍኡ ፡ (ዮዲ፯ ፡ ፬) ።

**ጠፋኢ** ፤ (ኢት ፡ እያን ፡ ያት) ፤ የሚጠፋ ፡ ጠፊ ፤ ኰብላይ ።

**ጥፉእ** ፤ (**ኣን ፡ ኣት ፡ ፍእት**) ፤ የጠፋ ፡ ጥፉ ፤ ብልሹ ፡ መጥፎ ፤ ደካማ ። ኢያሌዕል ፡ ገጾ ፡ ጥፉእ ፡ ኀበ ፡ እግዚእ ፡ (ተረ ፡ ቁር፩ ። ፍ ፡ ነ ፡ ፴፯ ። ዘዳ ፳፰ ፡ ፷፭) ።

**ጥፍአት** ፤ መጥፋት ፡ መታጣት ፤ ጥፋት ፡ አጠፋፍ ፤ አደጋ ፡ ሞት ፤ ምርኮ ፡ ስደት ፤ ኰብለላ ፡ ሽሽት ። እሳት ፡ ዘአልቦ ፡ ጥፍአት ። ጥፍአተ ፡ መሀይምናን ። ከመ ፡ ዝኬ ፡ ጥፍአቶሙ ፡ ለኃጥኣን ፡ በምዕር ። ጥፍአተ ፡ ልብ ። በጽሐቶሙ ፡ ጥፍአት ፡ ለኃጥኣን ፡ (ቀሌ ። መቃ ፡ ገ፳፩ ። ፍ ፡ ነ ፡ ፶ ። ዕን፩ ፡ ፱) ። ጢስ ፡ ነበልባል ፡ በማለት ፡ ፈንታ ፡ ጥፍአት ፡ ይላል ፤ የመላሽ ፡ ስሕተት ፡ ነው ፡ (መሳ፳ ፡ ፵) ።

**ጠፍእ** ፤ (**ኣት**) ፤ በቁሙ ፤ ጠፍ ፡ ባድ ፡ ባድማ ፤ ብርሃኑ ፡ ሕዝቡ ፡ የጠፋበትና ፡ ያለቀበት ፡ ጨረቃ ፡ ሀገር ። ከጌታው ፡ የጠፋ ፡ ባሪያ ፡ ከብት ። ወራሽ ፡ የሌለው ፡ ገንዘብ ፡ ርስት ፤ የመሰለው ፡ ኹሉ ።

**አጥፍአ** ፤ አጠፋ ፡ አስጠፋ ፤ አወደመ ፡ ጠፍ ፡ አደረገ ። ለእሳት ፡ እንተ ፡ ትነድድ ፡ ያጠፍኣ ፡ ማይ ። ከመ ፡ ኣጥፍእ ፡ እምኔሃ ፡ ሰብአ ፡ ወእንስሳ ። እብነ ፡ በረድ ፡ አጥፍአ ፡ ሖሎ ፡ ዘይሠርጽ ፡ (ሚራ፫ ፡ ፴ ። ሕዝ፲፬ ፡ ፲፱ ። ኩፋ ፡ ፵፰) ።

**መጥፍኢ** ፤ **እ** ፤ የሚያጠፋ ፡ አጥፊ ፤ አስጠፊ ፡ (አቡሻ ፡ ፲፫) ። መጥፊያ ፡ ማጥፊያ ፤ ማስጠፊያ ፤ መሠሪያ ፡ ምክንያት ።

**ምጥፋእ** ፤ መጥፊያ ፡ ማጥፊያ ፡ ስፍራ ፤ የጥፋት ፡ ቦታ ።

**ተጣፍአ** ፤ ተጣፋ ፤ ተጠፋፋ ፤ ተጋደለ ።

**ጠፈሐ** ፤ **ሐት** ፤ (**ጠፍሐ ፡ ይጠፍሕ ፡ ይጥፋሕ ። ዕብ ፡ ጣፋሕ ፤ ሳፋቅ ። ዐረ ፡ ጸፈሐ ፤ ጸፈቀ**) ፤ ማጨብጨብ ፡ ኹለት ፡ እጅን ፡ መጥፋት ፤ ማማታት ፡ ማጋጨት ፡ መስበቅ ፡ ማፋጨት ፤ የደስታና ፡ የዘፈን ፡ የቍጭት ፡ የሐዘን ፤ ያገና ፡ የገባያ ፤ ለክንፍም ፡ ይኾናል ። ጠፍሑ ፡ እደዊሆሙ ፡ ላዕሌኪ ። አሉ ፡ ይጠፍሑ ፡ ወየኀብሩ ፡ ምስለ ፡ ቃለ ፡ አንዚራ ። ጥፍሑ ፡ እደዊክሙ ፡ ወየብቡ ። ጥፋሕ ፡ እዴከ ፡ በዲበ ፡ እዴከ ። ወጠፍሐ ፡ እደዊሁ ፡ ላሜኽ ፡ በእንተ ፡ ሐዘኑ ፡ ላዕለ ፡ ቃየል ። ብእሲ ፡ አብድ ፡ ይጠፍሕ ፡ እዴሁ ። መላእክት ፡ ይጠፍሑ ፡ ክነፊሆሙ ፡ (ሰቈ፪ ፡ ፲፭ ። ዓሞ፯ ፡ ፭ ። መዝ ፡ ፵፯ ። ሕዝ፳፩ ፡ ፲፬ ። ቀሌ ። ምሳ፲፯ ፡ ፲፰ ። ስንክ ፡ ግን፳፩) ።

—፤ ማጠፍጠፍ ፤ መጠፍጠፍ ፡ ጠፍጣፋ ፡ ማድረግ ፡ ወይም ፡ መኾን ፤ የጡብ ፡ የኰበት ። ንዑ ፡ ንጥፋሕ ፡ ግንፋለ ፡ ወናብስሎ ፡ በእሳት ፡ (ዘፍ፲፩ ፡ ፫) ። መጋት ፤ ቤ

ጋት ፡ መስፈር ፤ በጥፊ ፡ መምታት ፡ ማጮል ። ወግዐንና ፡ ጸፍዐን ፡ ገዐተን ፡ እይ ።

**ጠፋሒ** ፤(ሒት ፡ ሕያን ፡ ያት)፤ የሚያጨበጭብ ፡ አጨብጫቢ ፤ ጠፍጣፊ ።

**ጥፍሐት** ፤ ማጨብጨብ ፡ አጨባጨብ ፤ ጭብጨባ ፡ ግጭት ፤ የእጅና ፡ የክንፍ ፡ መማታት ። ወበጥፍሐተ ፡ እደዊሁ ፡ ሰከዩ ፡ ለወልዱ ፡ ወቀተሎ ። ኢመጠነ ፡ ጥፍሐተ ፡ አክናፊ ፡ አንስርት ፡ (ቀሌ ። መጽ ፡ ምስ) ።

**ጥፍሕ** ፤ (ዕብ ፡ ጦፋሕ) ፤ ጥፊ ፡ ጋት ፤ ያራት ፡ ጣት ፡ መጠን ፤ ገዐተን ፡ እይ ። እመት ፡ ወጥፍሕ ፡ (ሕዝ፵ ፡ ፭ ። ፵፫ ፡ ፲፫) ። በጥፍሕ ፡ ፈንታ ፡ ስዝር ፡ ይላል ፤ ስሕተት ፡ ነው ።

**ጣፍያ** ፤ ጣፊያ ፤ የሆድ ፡ ዕቃ ፡ መሣሪያ ፡ እንደ ፡ ጕበት ፡ ያለ ፤ ሞላላ ፡ ጠፍጣፋ ፤ ምስጢሩ ፡ ጠፍጣፍነት ፡ ነው ። የብሰ ፡ ሥጋሁ ፡ እምብዝኀ ፡ ትሕርምት ፡ እስከነ ፡ ይትሔዘብዎ ፡ ከመ ፡ ዘአልቦ ፡ ውስተ ፡ ከርሡ ፡ ልብ ፡ ወኢጣፍያ ፡ (ፊልክ ፡ ፲፯) ።

**ተጣፍሐ** ፤ ተጣፋ ፤ እጅ ፡ ለእጅ ፡ ተማታ ፤ ያገና ፡ የገባያ ። ሸያጭና ፡ ገዥ ፡ በዋጋ ፡ ተስማምተው ፡ ነገር ፡ ሲጨርሱ ፡ እንደ ፡ መማል ፡ እንደ ፡ መፈጣጠም ፡ ይጣፋሉ ።

**አስተጣፍሐ** ፤ አጣፋ ፤ አማታ ፡ አጋጨ ። ይስፍሑ ፡ ወያስተጣፍሑ ፡ እደዊሆሙ ። እንዘ ፡ ያስተጣፍሕ ፡ ክነፊሁ ፡ (ፍ ፡ ነ ፡ ፩ ። ገድ ፡ ተክ) ።

(ጥ) **ጥፉሕ** ፤—የተክል ፡ ስም ፤—ትፉሕ ።

**ጣፌጥ** ፤ (ጽር ፡ ታፌት ። ዕብ ፡ ቶፌት) ፤ የቦታ ፡ ስም ፤ ምድኛ ፡ የልጆች ፡ ማንደጃ ፤ የኢየሩሳሌም ፡ ቅርብና ፡ አጠገብ ፡ የገሃነም ፡ ክፍል ፤ እስራኤል ፡ ልጆቻቸውን ፡ ሞሎክ ፡ ለሚባለው ፡ ለዓሞናውያን ፡ ጣዖት ፡ ያቃጥሉበት ፡ የነበረ ። አፈየን ፡ እይ ፤ ቶፌት ፡ ማለት ፡ ከዚያ ፡ የወጣ ፡ ነው ። ፪ኛ ፡ አፈታት ፡ ቶፍ ፡ ከበሮ ፡ ነውና ፤ ሕፃናቱን ፡ ካህናተ ፡ ጣዖት ፡ ሲሠዉ ፡ እናት ፡ አባት ፡ የልጆችን ፡ ጩኸት ፡ እንዳይሰሙና ፡ እንዳይራሩ ፡ እንዳይጠጠቱ ፡ ከበሮ ፡ እየመቱ ፡ የሚያረግዱበት ፡ ስለ ፡ ኾነ ፡ ስሙ ፡ በቤት ፡ አንቀጽ ፡ ቶፌት ፡ ተብሏል ፤ ከበሮም ፡ ባለከበሮ ፡ ማርገጃ ፡ ከበሮ ፡ ማንጕጃ ፡ ማለት ፡ ነው ፤ ሞሎክንና ፡ ገሃነምን ፡ እይ ፡ (፬ነገ ፡ ፳፫ ፡ ፲ ። ኤር፲፱ ፡ ፲፩—፲፬) ።

**ጠፌል** ፤ ሎት ፤ (ጠፈለ ፡ ይጠፍል ፡ ይጥፍል ። ዕብ ፡ ጣፋል) ፤ መጨመር ፤ ዕጥፍ ፡ ድርብ ፡ ጥንድ ፡ ከዕብ ፡ ማድረግ ፤ ሥንጥቅ ፡ ወይም ፡ ኹለት ፡ እጅ ፡ ማትረፍ ፤ ያበዳሪና ፡ የነጋዴ ።

**ጠፍልሕ** ፤ (ብ ፡ ጠፋልሕ ፤ ሓት) ፤ የገንዘብ ፡ ስም ፤ ጥሩ ፡ ብር ፤ የብር ፡ ገንዘብ ፡ ምዝምዙ ፡ ጠገራው ፤ ወይም ፡ በንጉሥ ፡ መልክ ፡ የተሠራው ፡ ታላቁም ፡ ታናሹም ። ጠፍ ፡ ያለ ፤ ጠፍተኛ ፡ ማለት ፡ ከዚህ ፡ ወጥቷል ። ምንት ፡ ውእቱ ፡ አርባዕቱ ፡ ምእት ፡ ጠፋልሕ ። ጠፋልሐ ፡ ብሩር ። ዲናራት ፡ ወጠፋልሓት ፡ (ዘፍ፳፫ ፡ ፲፭ ፡ ፲፮ ። ፍ ፡ ነ ፡ ፳፮) ።

**ጥፍንሕ** ፤—ጨፋና ፡ ሸውራራ ፤—ጥንፍሕ ፡ ጥንፍ ።

**ጥፉንቂስ** ፤ (ጽር ፡ ቲፎኒኮስ) ፤ የባሕር ፡ ዐውሎ ፡ ብርቱ ፡ ነፋስ ፤ ማዕበል ፡ ሞገድ ፡ የሚያስነሣ ፤ ባሕር ፡ የሚደርጥ ፡ መርከብ ፡ የሚያናውጥ ፡ (ግብ፳፯ ፡ ፲፬) ። አውራቂስን ፡ እይ ፤ ከዚህ ፡ ጋራ ፡ አንድ ፡ ነው ።

(ጥ) **ጠፊር** ፤ ሮት ፤ (ጠፈረ ፡ ይጠፍር ፡ ይጠፍር) ፤ መጠፈር ፡ መማገር ፤ አጥብቆ ፡ ማሰር ፤ ጣራን ፡ ባጥን ፡ በግድግዳ ፡ ላይ ፡ መሥራት ፡ ማዋቀር ። አኮ ፡ በዕፀ ፡ ዘትሰውቆን ፡ ወትቄምሮን ፤ ወአኮ ፡ በአሕባል ፡ ዘትጠፍሮን ። ዘይጠፍር ፡ በማይ ፡ ጽርሖ ፡ (ገድ ፡ ላሊ ። መዝ ፡ ፻፫) ። መማገር ፡ ለኹሉ ፡ ይኾናል ፤ ማዋቀር ፡ ግን ፡ ለጣራ ፡ ብቻ ፡ ነው ። ጠብቆ ፡ እንደ ፡ ቀተለ ፡ የሚኼድ ፡ ይህን ፡ የመሰለ ፤ ላልቶም ፡ እንደ ፡ ቀደሰ ፡ የሚኼድ ፡ ገረመን ፡ ጸዐለን ፡ የመሰለ ፡ ብዙ ፡ ግስ ፡ አለና ፤ መንገዱንና ፡ አካኼዱን ፡ ለይተኽ ፡ ጠንቅቀኽ ፡ አስተውል ።

**ጠፋሪ** ፤ (ሪት ፡ ርያን ፡ ያት) ፤ በቁሙ ፤ የሚማግር ፡ የሚያዋቅር ፡ አጥብቆ ፡ የሚያስር ፡ የሚጠፍር ። ከበሮ ፡ ጠፋሪ ፡ እንዲሉ ።

**አጠፈረ** ፤ **አስተጠፈረ** ፤ አስጠፈረ ፡ አስማገረ ፤ ጠፈር ፡ መዋቅር ፡ አሠራ ።

**ተጠፈረ** ፤ በቁሙ ። አጥፈረ ፡ ተጠፍረ ፡ ቢል ፡ ግን ፡ የቀተለ ፡ ቤት ፡ ነው ።

**ጥፉር** ፤ (ራን ፡ ራት ፡ ፍርት) ፤ የተጠፈረ ፤ የተሠራ ፤ ጥፍር ። ይኄይስ ፡ ነቢር ፡ ውስተ ፡ ማእዘንት ፡ ዘኢኮነ ፡ ጥፉረ ። ወማኅደሩ ፡ በማይ ፡ ጥፉር ፡ (ምሳ፳፩ ፡ ፱ ። ቅዳ) ።

**ጠፈር** ፤ (ራት) ፤ በቁሙ ፤ ሰማይ ፡ የምድር ፡ ባጥ ። ለይኩን ፡ ጠፈር ፤ ወገብረ ፡ ጠፈረ ፡ ወሰመዮ ፡ ለውእቱ ፡ ጠፈር ፡ ሰማየ ፡ (ዘፍ፩ ፡ ፮ ፡ ፯ ፡ ፰) ።

—፤ የባጥ ፡ ማገር ፤ ጣራ ፡ መዋቅር ። ዕፀው ፡ ለጠፈረ ፡ ቤት ፡ ወለሠራዊት ። ዐርጉ ፡ ናሕስ ፡ ወነሡቱ ፡ ጠፈረ ። ቦኡ ፡ አራዊት ፡ ታሕተ ፡ ጠፈር ። ንበ ፡ አልቦ ፡ ጠፈር ። ውስተ ፡ ጠፈረ ፡ ጽርሕ ፡ አርያም ፡ (፪ዜና ፡ ፴፬ ፡ ፲፩ ። ሉቃ፭ ፡ ፲፱ ። ኢዮ፴፯ ፡ ፰ ። ኢሳ፳፫ ፡ ፪ ። አርጋ ፡ ፫) ።

**ጠፍር** ፤ በቁሙ ፤ ማሰሪያ ፡ መጠፈሪያ ፡ መማገሪያ ፤ የተተለተለ ፡ ቁርበት ፡ ርጥቡ ፡ ወይም ፡ የለፋው ፤ ቅሪላ ፡ ቅራና ፡ መጫኛ ፡ ምራን ፡ መርገጥ ፡ ማነቆ ።

**ጣቃ** ፤ **ጣቅ** ፤ (ብ ፡ ጣቃት ። ዐረብ) ፤ በቁሙ ፤ ልብስ ፡ የልብስ ፡ መዳ ፡ ነደ ፤ የታጠፈ ፡ የተጠቀለለ ፡ (አቡሻ ፡ ፶) ። ጭጋግ ፡ ጉም ፡ ጢስ ፤ ጥቍር ፡ ደመና ፡ ጠቀርማ ፡ የቀን ፡ ጨለማ ፡ ጥቅጥቅ ፡ ያለ ፤ እንደ ፡ ልብስ ፡ ጣቃ ፡ የሚጋርድና ፡ የሚሸፍን ። ቆባርን ፡ እይ ፤ የዚህ ፡ መንቲያ ፡ ነው ፡ (ዘፀ፳ ፡ ፳፩ ። ዘዳ፬ ፡ ፲፩ ። ፭ ፡ ፲፱ ። ዕብ፲፪ ፡ ፲፰) ።

**ጥቀ፤—እጅግ፡ ብዙ፤—ጠቂቅ፡ ጠቀ።**

**ጥቃ፤—ቅርብ፡ አጠገብ፤—ጠቂዕ፡ ጠቅዐ።**

**ጠቂብ፤ ቦት፤ (ጠቀበ፡ ይጠቅብ፡ ይጥቅብ፤ ጠቀመ። ዐረ፡ ሰቀበ፤ በሳ፡ ነደለ)፤** መጥቀም፡ መጠቃቀም፤ መስፋት፡ መደረት፤ መጣፍ፡ መለገብ፤ ያሮጌ፡ ልብስ፡ ያሮጌ፡ ጫማ። ጠቀመን፡ እይ። ነሥአ፡ ቈጽለ፡ በለስ፡ ወጠቀበ፡ ወገብረ፡ ሎቱ፡ ምራአ፡ ወከደነ፡ ኀፍረቶ። አልቦ፡ ዘይጠቅብ፡ (ኵፉ፡ ፫። ማቴ፱፡ ፲፮)።

**ጠቃቢ፤ (ቢት፡ ብያን፡ ያት፤ ቀብት)፤** የሚጠቅም፡ የሚለግብ፤ ጣፊ፡ ለጣፊ፡ ድሪቶ፡ ሰፊ፤ አሮጌ፡ ጠጋኝ፤ የጨርቅ፡ ወጌሻ።

**አጥቀበ፤** አስጠቀመ፡ አስለገበ፤ አስደረተ፤ ልብሱን፡ ጫማውን፡ አስጠገነ።

**ተጠቅበ፤** ተሰፋ፡ ተጠቀመ፤ ተጣፈ፡ ተለገበ፤ ታደሰ፡ ተጠገነ። ከመ፡ ትትሐጸር፡ በመስቀልከ፡ ወትጠቀብ፡ በመጽለብትከ፡ እማእከለ፡ መንሱት፡ (ቅዳ፡ ዮሐ)። ምስጢሩ፡ መራቅ፡ መጠበቅ፡ ነው፤ አንዳንድ፡ መጣፍ፡ ትጠበቅ፡ ትጠቀም፡ ይላል።

**ጥቁብ፤ (ባን፡ ባት፡ ቅብት)፤** የተጠቀመ፤ የተጠቃቀመ፤ ድሪቶ፡ ጥቅምቅም። ዝቅ፡ ብሉይ፡ ወሥጡጥ፡ ወጥቁብ። ሀሎ፡ ዲቤሁ፡ ልብስ፡ ጥቁብ፡ (ኢዮ፱፡ ፬። ፊልክ፡ ፻፲፯)።

**ጥቅበት፤ (ታት)፤** መጥቀም፡ መስፋት፤ መሰፋት፡ አሰፋፍ፤ ስፌት፡ ጥቅማት። በህየ፡ ተምህረ፡ ግብረ፡ እድ፡ ጽሕፈተ፡ ወጥቅበተ። ያነቅዎ፡ ጥቅበቱ፡ (ስንክ፡ ግን፲፱። ማር፪፡ ፳፩)።

**ተጣቀበ፤** ተጣቀመ፡ ተጠቃቀመ፤ ተሰፋፋ።

**አስተጣቀበ፤** አጣቀመ፤ አጠቃቀመ፤ የጨርቅና፡ የጨርቅ፤ ለነገርና፡ ለሰውም፡ ይኾናል።

**መጥቀብት፤ (ብ፡ መጣቅብት)፤** መጥቀሚያ፡ መጠቃቀሚያ፤ የስፌት፡ መሣሪያ።

**ጠቂል፤ሎት፤(ጠቀለ፡ ይጠቅል፡ ይጥቅል)፤** መጥቀል፤ በነገር፡ መንካት፡ መጕንጥ፤ ጠቅ፡ ማድረግ፡ ማሽሟጠጥ፡ ፊት፡ ለፊት፤ ወይም፡ በስተኋላ፡ ማማት፡ መንቀፍ፤ መዋሸት፡ መቅጠፍ፤ መክሰስ፡ ማሳጣት። አፍ፡ ዘይጠቅል፡ ወይሔሱ። ወጠቀለቶ፡ ቅድመ፡ እግዚእ። ሶበ፡ ጠቀለቶ፡ (ጥበ፭፡ ፲፭። ኵፉ፡ ፴፱። መጽ፡ ምስ)። ጠንቈለን፡ እይ፤ የዚህ፡ ስሯጽ፡ ነው።

**ጠቃሊ፤ (ሊት፡ ልያን፡ ያት፤ ቀልት)፤** የሚነካ፡ ጕናጭ፡ አሽሟጣጭ፤ ሰብቀኛ፡ ከሳሽ፡ አሳጭ፤ ቀጣፊ፡ የሰው፡ ስም፡ አጥፊ፤ ሹላፍ፡ እሾኻፍ።

**መጥቍል፤ (ልት፡ ላን፡ ላት)፤** ዝኒ፡ ከማሁ። የሰው፡ ስም፤ ምትሀታም፡ አስማታም፤ ጠንቋይ፡ መሠሪ፤ ጋኔን፡ ጠሪ፡ ሙት፡ አናጋሪ፡ ማለት፡ ነው፡ (ነገ፡ ማር)።

**ጠቅለለ፤ (ተቀ፡ ግ። ጠቀለ)፤** በቁሙ፤ ጠቀለለ፤ ጠቀላለለ፡ ጠመጠመ፤ የልብስ፡ የገመድ። ጠብለለን፡ እይ፤ ተቀጥላነቱ፡ እንደዚያ፡ ነው።

**አጠቅለለ፤ አስተጠቅለለ፤** አስጠቀለለ፤ አስጠመጠመ።

**ተጠቅለለ፤** ተጠቀለለ፤ ተሸበለለ።

**ጥቅሉል፤ (ላን፡ ላት፡ ልልት)፤** የተጠቀለለ፤ ጥቅልል፤ መዳ፡ ጣቃ። አልባስ፡ ጥቅሉላት፡ (ፍ፡ ነ፡ ፴፫)።

**ጠቂም፤ ሞት፤ (ጠቀመ፡ ይጠቅም፡ ይጥቅም። ጠቀበ)፤** መጥቀም፤ መጠገን፡ ማደስ፤ ያሮጌ። ሐነጸ፡ አብያተ፡ ክርስቲያናት፡ ብዙኃተ፡ ወጠቀመ፡ ወሐደሰ፡ እምኔሆሙ፡ (ስንክ፡ ሐም፳፯)።

—፤ መንደቅ፡ መገንባት፤ ማጠር፡ መቅጠር፤ ቅጥር፡ መሥራት፡ በቅጥር፡ መክበብ፤ ዙሪያውን፡ በግንብ፡ መወሰን፡ መከለል፤ የከተማ፡ የቤት፡ የቦታ፡ የመሬት። ከመ፡ ይሕንጽ፡ ውእተ፡ መካነ፡ ወይጥቅም፡ ዐጸደ። እለ፡ ያፈቅሩ፡ ሕገ፡ ይጠቅሙ፡ ሰርአሶሙ፡ ቅጽረ፡ (ኵፉ፡ ፴፪። ምሳ፳፰፡ ፬)።

—፤ በቁሙ፤ መርባት፡ መጥቀም፤ ሥራ፡ መያዝ፡ ማገልገል፤ በቍዐንና፡ ረብሐን፡ እይ።

**ጠቃሚ፤(ሚት፡ ምያን፡ ያት)፤** በቁሙ፤ (ተረት)፤ ጠቋሚ፡ ጠቃሚ።

**ተጠቅመ፤** ተጠቀመ፡ ተሠራ፤ ታጠረ፡ ተከበበ፤ ጥቅም፡ አገኘ። ከመ፡ ትጠቀብ፡ ባለው፡ ትጠቀም፡ እንዲል፡ (ቅዳ፡ ዮሐ)።

**ጥቁም፤ (ማን፡ ማት፡ ቅምት)፤** የተገነባ፡ የተናሰ፤ የተቀጠረ።

**ጥቅም፤ (ማት)፤** ግንብ፡ ናስ፤ የግንብ፡ ቅጥር፡ መከበቢያ፤ የደንጊያ፡ ድሪቶ፡ ጥቅምቅም፡ በኖራ፡ ፈትልነት፡ የተሰፋ፡ የተጠቀመ፤ የተሳከ፡ የተጋጠመ፤ ብርቱ፡ ሥራ። ንቃወ፡ ምዝባሬ፡ ዘጥቅመ፡ ሰናዖር፡ ያፍ። ሀገር፡ ዘንኅሰ፡ ጥቅማ። አህጕር፡ እለ፡ ቦን፡ ጥቅም። መኑ፡ ይወስደኒ፡ ሀገረ፡ ጥቅም። በከመ፡ አንኅልከ፡ ጥቅማ፡ ለኢያሪኮ፤ ከማሁ፡ አንኅል፡ ጥቅመ፡ ኀጢአትየ፡ (ቅኔ። ምሳ፳፭፡ ፳፰። ኢሳ፴፯፡ ፳። መዝ፡ ፶፱። ቅዳ)።



ጥቅም፡

**ጥቅምት፤** በቁሙ፡ ስመ፡ ወርኅ፡ ካልእ፡ እመስከረም። ዘይቤው፡ የተሠራች፡ ሥር፤ ሥስጢሩ፡ ወርኅ፡ ግብር፡ ጥንተ፡ ግብር፡ ማለት፡ ነው፤ ሥነ፡ ፍጥረትን፡ ያሳያል፤ አታሚንን፡ ተመልከት። እንደ፡ ወራቱ፡ ግን፡ ሲፈቱት፤ ጽጌውን፡ መደብ፡ አድርገ፡ ፍሬ፡ ወርኅ፡ ፍሬ፡ መዋዕለ፡ ሠዊት፡ ያሰኛል። (ተረት)፤ ል

ጅን ፡ በጡት ፤ እኽልን ፡ በጥቅምት ፡ (ክልጠበቁትና ፡ ክልቈጠቡት) ።

**ጠቂዕ፤ ዖት፤(ጠቅዐ ፡ ይጠቅዕ ፡ ይጥ ቃዕ ። ዕብ ፡ ታ ቃዕ)፤** መደወል ፡ ማቃጨል ፤ መም ታት ፡ ማንኳኳት ፤ የንጨት ፡ የብረት ። ማጨብጨብ ፤ እጅ ፡ መጽፋት ። መንፋት ፡ ማጋፈት ፡ እፍ ፡ እፍ ፡ ማ ለት ፤ እየነፉ ፡ ድምጥ ፡ ማሰማት ፤ የንቢልታ ፡ የዋሽንት ፡ የቱልቱላ ፡ የቀንዳ ፡ መለከት ። ትጠቅዐ ፡ መጥቅዐ ፡ ወ ይትጋብኡ ፡ ሕዝብ ። ካህናት ፡ እሙንቱ ፡ እለ ፡ ይጠ ቅዕዎ ፡ ለመጥቅዕ ፡ (ግንዘ ። ዘኍ፲ ፡ ፫ ፡ ፰ ፡ ፲ ። ኢያ፯ ፡ ፰—፲፯) ።

—፤ በቁሙ ፤ መጥቃት ፡ ጠቅ ፡ ማድረግ ፤ ማጥቃት ፤ ማስጮኽ ፡ ማስለቀስ ፤ ማሸነፍ ፡ በላይ ፡ መኾን ። ለወይ ፈንና ፡ ላለሌም ፡ ይኾናል ፤ አጠቃ ፡ መታ ፡ እንዲሉ ። መጠጋት ፡ መቅረብ ፤ ቅርብ ፡ አጠገብ ፡ መኾን ፤ ለመም ታት ፡ ለመጥቃት ።

**ጠቃዒ፤ መጥቅዕ፤(ዕት ፡ ዓን ፡ ዓት)፤** የሚደውል ፡ የሚነፋ ፡ ጠቂ ፡ አጥቂ ።

**መጥቅዕ ፤ (ብ ፡ መጣቅዕት) ፤** በቁሙ ፤ መጥቅ ፡ ድወል ፡ ቃጭል ፤ መረዋ ፡ ነጋሪት ፤ ቱልቱላ ፡ ዋሽንት ፤ እንቢልታ ፡ መለከት ። መጥቅዐሰ ፡ ተወጥነ ፡ በኖኅ ፤ ወገብረ ፡ መጥቅዐ ፡ እምዕፀወ ፡ አብኖስ ፡ ዘ ኑኁ ፡ ሠለስቱ ፡ በእመት ፡ ወግድሙ ፡ አሐዱ ፡ በእ መት ፤ ወሶበ ፡ አኀዘ ፡ ይግበር ፡ ታቦተ ፡ ይጠቅዕ ፡ ሎሙ ፡ ዙሉ ፡ ዕለተ ፡ ሠለስተ ፡ ጊዜ ። ድምፀ ፡ መጥ ቅዕ ። ቃለ ፡ መጥቅዕ ። ሰብዐቱ ፡ መላእክት ፡ እለ ፡ ያጸንዑ ፡ ሰብዐተ ፡ መጣቅዕተ ። ግበር ፡ ለከ ፡ ክል ኤተ ፡ መጣቅዕተ ፡ ዘብሩር ፡ (ቀሌ ። ዕብ፲፪ ፡ ፲፱ ። ራእ፱ ፡ ፩ ። ፰ ፡ ፯ ። ዘኍ፲ ፡ ፪) ።



መጥቅዕ ፡

—፤ በዓል ፡ የበዓል ፡ ስም ፤ የዕብራውያን ፡ ዐውዳመት ፡ ቱልቱላ ፡ መለከት ፡ የሚነፋበት ፤ በ፯ኛው ፡ ወር ፡ የጥቅ ምት ፡ ጨረቃ ፡ በምትበቅልበት ፡ ቀን ፡ የሚውል ። አታሚ ንን ፡ እይ ፤ ከዚህ ፡ ጋራ ፡ አንድ ፡ ነው ፡ (ዘሌ፳፫ ፡ ፳፬) ።

**አጥቅዐ ፤** አስመታ ፡ አስነፋ ፤ አስጠቃ ፡ ጋ ።

**ተጠቅዐ ፤** ተመታ ፡ ተነፋ ፤ ተጠቃ ፤ ተጠጋ ።

**ጥቁዕ ፤ (ዓን ፡ ዓት ፡ ቅዕት) ፤** የተጠቃ ፡ ጥቁ ፤ ወራዳ ።

**ጥቅዐት ፤** መጠቃት ፡ መሸነፍ ፤ በታች ፡ መ ኾን ። በቁሙ ፡ ጥቃት ፤ ውርደት ።

**ጥቅዕ ፤ ጥቃዕ ፤ ጥቃ ፤** አጠገብ ፤ ጕን ፡ ላይ ፤ ቅርብ ፤ የቅርብ ፡ ቅርብ ፡ ሊይዙት ፡ ሊነኩት ፡ ወ ይም ፡ በጨበጣ ፡ ሊመቱት ፡ ሊወጉት ፡ የሚቻል ። ዳርቻ ። ጠረፍ ፤ ወሰን ፡ ደንበር ፤ ጎር ፡ ጎረቤት ፤ የቦታ ። አብ ፡ ጥቅዖም ፡ (ትግሪኛ) ። ጥቃሆሙ ። ጥቃ ፡ ማያት ። ጥቃ ፡ ጽህርት ፡ ዘሥጋ ። ማይ ፡ ዘጥቃ ፡ ባሕር ። በ ጥቃ ፡ ኵሎሙ ። በጥቃ ፡ ፍኖት ፤ ላይ ፡ (ኢዮ፩ ፡ ፲፬ ። ዘፀ፲፩ ፡ ፳፯ ። ፲፯ ፡ ፫ ። ኢሳ፲፱ ፡ ፭ ። መዝ ፡ ፻፵ ። አፈ ፡ ድ፬) ።

**ጠቂቅ ፤ ቆት ፤ (ጠቀ ፤ ጠቀቀ ፡ ይጡ ቅቅ ፡ ይጥቅቅ ። ደቀ ፤ ደግደገ) ፤** መጠቀን ፡ ማነስ ፤ ጥቃቅን ፡ ታናናሽ ፡ መኾን ፤ ተፈጭቶ ፡ ደቆ ፡ ተሰ ባብሮ ፡ ወይም ፡ ተቈርሶ ፡ ተፈርፍሮ ። መቈጠብ ፡ መን ፈግ ፡ ጩቅ ፡ መኾን ፤ ቈርጠ ፡ በጥሶ ፡ ቈንጥሮ ፡ አሳንሶ ፡ መስጠት ። ጢቆ ፡ ጥቂት ፡ ማለት ፡ ከዚህ ፡ ወጥቷል ፤ ጢቆ ፡ ጋልኛ ፡ ነው ። አደሬ ፡ ጢቆ ፡ እንዲሉ ። መብ ዛት ፡ መፈድፈድ ፤ እጅግ ፡ መኾን ፤ በመሰበርና ፡ በመድ ቀቅ ፡ በመፈለጥና ፡ በመቈረጥ ፤ እንደ ፡ ሸክላ ፡ እንደ ፡ ግንድ ። ተባረከ ፡ ዳግን ፡ ወኮነ ፡ ምእተ ፤ እስመ ፡ ቢ ዝኀ ፡ ወመልአ ፡ መሬተ ፡ (ቅኔ) ። የምስጢር ፡ ጥቅስ ፡ ነው ።

**ጥቀት ፤** መብዛት ፤ ብዙነት ። ማነስ ፤ ጥቂት ነት ፤ የቍጥር ፡ የመጠን ። መንፈግ ፡ መቤስ ፤ ንፍገት ፡ ጩ ቅነት ። በጥቀት ፡ መብልዐ ፡ ወሀብኩ ፡ (መጽ ፡ ኑዛ) ።

**ጥቅ ፤** እጅግ ፤ ብዙ ፡ ዐያሌ ፤ ጥቃቅንነቱ ፡ እን ዳሸዋ ፡ እንደ ፡ ጤፍ ፡ ቅንጣት ፡ እንዳፈርና ፡ እንደ ፡ ዱ ቄት ፡ ያለ ፤ የብዛቱ ፡ መጠን ፡ በስፍር ፡ በሚዛን ፡ ክል ኾነ ፡ በቍጥር ፡ ሊታወቅ ፡ የማይቻል ፡ የማይቈጠር ።

**ጥቀ ፤ (ንኡስ ፡ አገባብ) ፤** እጅግ ፤ ብዙ ፡ እምብዛ ፤ ለካ ፡ ፈጽሞ ፤ ይልቅ ፡ በጣም ፤ እንኳን ። ተ ምዐ ፡ ጥቀ ። ጥቀ ፡ ተሰብሐ ፡ ስምከ ። ጥቀ ፡ ሠኒ ይኪ ፡ ወጥቀ ፡ አደምኪ ። ገቢረ ፡ ጽድቅ ፡ ሥሙር ፡ በኀበ ፡ እግዚ ፡ ጥቀ ፡ እምዘቢሐ ፡ መሥዋዕት ። ማየ ፡ ጥቀ ፡ ኢያስተይከ ፡ ለጽሙእ ። መላእክት ፡ ጥቀ ፡ ስሕቱ ፡ በሰማይ ፡ (ማቴ፪ ፡ ፲፯ ። መዝ ፡ ፰ ። ማሕ፯ ፡ ፯ ። ምሳ፲፮ ፡ ፭ ። ኢዮ፳፪ ፡ ፯ ። ደራሲ) ። (ዕር፳ ፡ ቍ፺፯) ።

**ጠቂር ፤ ሮት ፤ (ጠቀረ ፡ ይጠቅር ፡ ይ ጥቅር ። ደመነ ፤ ጸልመ) ፤** መጥቀር ፡ መጥቈር ፤ ጠቀራ ፡ መኾን ፤ ጥቀርሻ ፡ መምሰል ፤ የጣራ ፡ የፊት ፡ የደ መናት ።

**ጠቀር ፤** በቁሙ ፤ ጠቀራ ። ጥቀርሻ ፤ ጥቍር ፡ ጠቋራ ፡ ጥላት ፤ የጢስ ፡ ስልባቦት ፡ በማድ ፡ ቤት ፡ ጣራ ፡ በማሩም ፡ በንጨቱም ፡ የሚገኝ ። ማሩም ፡ ጠቀራ ፡ ጠ ገብ ፡ ስለ ፡ ኾነ ፡ ጠቀራ ፡ ይባላል ። (ተረት) ፤ ያፈና ፡ በሬ ፡ ጠቀራ ፡ ይመዛል ። ረገዝዎ ፡ በኲናት ፡ ጸሊም ፤ ጠቀራ ፡ ጠገብ ፡ (ቅዳ ፡ ግሩ) ።

**ጠቂስ ፤ ሶት ፤ (ጠቀሰ ፡ ይጠቅስ ፡ ይ ጥቅስ ። ሱር ፡ ትክስ ። ዕብ ፡ ጣቈስ ፤ ሰደረ) ፤** መጥቀስ ፤ ማመልከት ፤ ባይን ፡ በጅ ፡ በቃል ፤ የሰው ፡ የወጥ ፡ የነገር ፡ (ምሳ፮ ፡ ፲፪) ። መኰስተር ፡ መተርከስ ፤ የመብራት ፡ የቀንዲል ። መብራቱን ፡ ጥቅሰው ፡ እንዲሉ ።

**ጥቅስ፤ (ሳት)፤** ጥቅሻ፤ ምልክት ። ባይን ፡ ጥቅሻ፤ በክንፈር ፡ ንክሻ ፡ እንዲሉ ። በቁሙ ፡ የመጽሐፍ ፡ ቃል፤ ዐጭር ፡ ቍርጭኝ ፡ ንባብ፤ ምሳሌ ፡ መስል ፡ ማስረጃ ፡ ምስክር ፡ የሚኾን ። ጕመን ፡ ጥቅስ፤ ዐልጫ ፡ ጥቅስ ፡ እንዲሉ ። ዘመረንና ፡ ቀጸበን ፡ እይ፤ የዚህ ፡ ጎር ፡ ነው ።

**ጥር፤—በቁሙ ፡ ጠር፤—ጠይሮ ፡ ጠየረ ።**

**ጠሪአ፤ አት፤ (ጠርአ ፡ ይጠርእ ፡ ይጥራእ ። ጸርሐ)፤** መጥራት ፡ መጮኽ፤ አቤት ፡ አቤት ፡ ማለት፤ ቡታ ፡ መስደድ ። ኢይኬልሕ ፡ ወኢይጠርእ ። እንዘ ፡ ይጠርኡ ፡ (ኢሳ፵፪ ፡ ፪ ። ግብ፳፭ ፡ ፲፩) ።

**ጠራኢ፤** ጠሪ ፡ ጪኺ፤ ቡታ ፡ ሰዳጅ ።

**ጥራእ፤ ጥርእ፤** ጥሪ ፡ ጩኸት፤ ቡታ ፡ እሪታ ። ጥራአ ፡ ቃል ፡ መፍርህ ፡ (ጥበ፲፯ ፡ ፲፰) ።

**ጥሬቡኖስ፤ (ብ ፡ ጠርባናት ። ሮማይ ፡ ትሪቡኑስ)፤** የሹመት ፡ የማዕርግ ፡ ስም፤ ደጅ ፡ አዝማች ፡ ራስ ፡ ቢቶደድ ፡ እንደ ፡ ማለት ፡ ያለ ። ፈነውዎ ፡ ለክቡር ፡ ጥሬቡኖስ ። ተፈነዉ ፡ ጠርባናት ፡ (ተረ ፡ ቄር፲፬ ። መጽ ፡ ምስ) ።

**ጠርቤንቶስ፤ (ጽር ፡ ቴሬቢንቶስ)፤** የንጨት ፡ ስም ፡ ቡጥም፤ መልካም ፡ ሽታና ፡ ብዙ ፡ ቅጠል ፡ ደም ፡ ወተት ፡ ያለው፤ ቅጠሉና ፡ ፍሬው ፡ ታናናሽ፤ ቍንድ ፡ በርበሬ ፡ የሚመስል ፡ (ኢሳ፮ ፡ ፴ ። ፮ ፡ ፲፪ ። ኩፋ ፡ ፲፫ ። ኢያ፳፬ ፡ ፳፮) ።

**ጠራው፤** ትርያ፤ ጉቡኣን ፡ ከዋክብት ፡ እንደን ስድስቶ ፡ ያሉ፤ ባንድነት ፡ ተጻፍቀው ፡ ተሰናስለው ፡ አበባ ፡ መስለው ፡ የሚታዩ ። ኮከብ ፡ ጠራው ፡ (ሰንክ ፡ መስ፲፩) ። ስመ ፡ ሀገር፤ ከዋክብት ፡ የሚመለኩበት ፡ ሥዕላቸው ፡ ምስላቸው ፡ ያለበት፤ የኮከብ ፡ ቈጣሮች ፡ አገር ። ሀገረ ፡ ጠራው ፡ (ስንክ) ። ትርያን ፡ እይ፤ ከዚህ ፡ ጋራ ፡ ፩ ፡ ነው ።

**ጠሪዝ፤ ዘት፤ (ጠረዘ ፡ ይጠርዝ ፡ ይጥርዝ ። ዐረ ፡ ጠሪዘ ። ዕብ ፡ ጣራዝ፤ ጣራስ)፤** መጠረዝ ፡ መጥለፍ፤ መዘምዘም፤ ፈትልን ፡ በመርፌ ፡ ማቈላለፍ፤ በልብስ ፡ ላይ ፡ ዛፍና ፡ ሐረግ ፡ መሣል፤ ልብስን ፡ በስፌት ፡ በሐር ፡ ማስጌጥ ፡ ማንቈጥቈጥ ፡ ስራ ፡ ማስመሰል፤ ረቀመን ፡ እይ ።

**ጠራዚ፤ (ዚት ፡ ዝያን ፡ ያት)፤** የሚጠርዝ ፡ ጠራዥ፤ ጠላፊ ፡ ጥልፍ ፡ ሰፊ ።

**ጥራዝ፤ (ዛት)፤** ግብረ ፡ መርፌ፤ ጥልፍ ፡ ዝምዝማት ፡ ቍልፍልፍ ፡ ስፌት፤ በልብስ ፡ ላይ ፡ ወይም ፡ ርሱን ፡ ራሱን ፡ ፈትሉን ፡ ብቻ ፡ እንደ ፡ ወንፊት ፡ ሐረግ ፡ አበባ ፡ ዛላ ፡ ዘለላ ፡ እያስመሰሉ ፡ የሚጠልፉትና ፡ የሚታቱት ። የመጽሐፍ ፡ ስፌት ፡ ቶታን፤ ሥራው ፡ የጥልፍ ፡ ሐረግ ፡ የሚመስል፤ ዥማቱና ፡ ሚሩ ፡ ርስ ፡ በርሱ ፡ የተጣለፈ ፡ የተቈላለፈ ። በቁሙ፤ የመጽሐፍ ፡ ነደ፤ ብራናው ፡ ወይም ፡ ወረቀቱ ፡ ካራትና ፡ ካምስት ፡ በመታጠፍ ፡ ሉሑ ፡ ቅጠሉ ፡ ፰ ፡ ፲፤ ገጹ ፡ ፲፮ ፡ ወይም ፡ ፳ ፡ ኹኖ ፡ ባንድነት ፡ የሚያዝ ፡ የሚሰፋና ፡ የሚጠረዝ ። ስሙን ፡ ከስፌቱ ፡ ከቶታኑና ፡ ከዥማቱ ፡ ወሰዲል ። ወምስሌሃ ፡ አሐዱ ፡ ጥራዝ ፡ እመጽሐፈ ፡ መልእክቱ ፡ ለጳውሎስ፤ ወተቤሎ ፡ ተማየጥ ፡ እምኔየ፤ ወነሥኣ ፡ ለይእቲ ፡ ጥራዝ ። ሠለስቱ ፡ ጥራዛት ፡ ካልኣን ፡ (ስንክ ፡ መጋ፲፫) ።

**ጠርዝ፤** በቁሙ፤ የልብስ ፡ ዳርቻ ፡ ዝሓው ፡ ዕጥፍ ፡ ድርብ ፡ ኹኖ ፡ ጥራዝና ፡ ጥልፍ ፡ የሚመስል ፡ (ዐማርኛ) ።

**ጠርዘዘ፤ (ተቀ ፡ ግ)፤** አንጠረዘዘ፤ የፊት ፡ የሆድ ።

**ተጠርዘዘ፤** ተንጠረዘዘ፤ ጠርዛዛ ፡ ኾነ ።

**ጥርዙዝ፤** የተንጠረዘዘ፤ እንጥርዝ፤ ፊተ ፡ ክባድ፤ ርጉዝ፤ ጋን ፡ ሆድ ፡ (ዐማርኛ) ።

**ጥሬዝቢጤር፤—ከህን ፡ ቄስ፤—ጥሬዝ ፡ ጥ ።**

**ጠርይ፤ (ዮት፤ ጠርየ፤ ጠረየ ፡ ይጠሪ ፡ ይጥሪ ። ጸርየ)፤** መጠረት፤ ጥሪት ፡ ማጥራት፤ ገንዘብ ፡ ማግኘት ፡ መሰብሰብ፤ የሌላውን ፡ ጥሪት ፡ መዋጀት ፡ መግዛት ፡ መውረስ፤ ጥሩ ፡ ገንዘብ ፡ ማድረግ ። መጽሐፍ ፡ ግን ፡ በአመረ ፡ ፈንታ ፡ አእመረ ፡ እንዲል፤ በጠረየም ፡ ፈንታ ፡ አጥረየ ፡ ይላል፤ ስሕተት ፡ ነው ። ንዋይ ፡ ዘአጥረየ ። አጥረይኩ ፡ ሠናየ ፡ ጥሪተ ። ኅሩያንየ ፡ እለ ፡ አጥረይኩ ። እንተ ፡ አጥረያ ፡ በደሙ ። ልብነ ፡ እምከመ ፡ አጥረየ ፡ ክንፈ ፡ ወርሐቀ ፡ እምግብራተ ፡ ለም ። ንጽሐቅ ፡ ለአጥርዮተ ፡ ዝንቱ ፡ (ኢዮ፳ ፡ ፳፱ ። ሚራ፵፩ ፡ ፳፩ ። ኢሳ፵፫ ፡ ፳፩ ። ግብ፳ ፡ ፳፩ ። አፈ ፡ ተ፳፪ ። ፴፬) ። ጥሬ ፡ መኾን፤ አለመብሰል፤ የምግብ ።

**ጠራዪ፤ መጥረዪ፤ መጥሪ፤ (ሪት ፡ ርያን ፡ ያት)፤** ገዥ ፡ ወራሽ፤ ጥሪታም ፡ ባለጥሪት ።

**አጥረየ፤** ጥሪት ፡ አስገዛ፤ አሷጀ ፡ ገንዘብ ፡ አስደረገ ።

**ተጠርየ፤** ተገዛ ፡ ተዋጀ፤ ተገኘ ፡ ተሰጠ፤ ጥሩ ፡ ገንዘብ ፡ ኾነ ። አንተ ፡ ኀለይከ ፡ ከመ ፡ ጸጋ ፡ እግዚ ፡ ትጠረይ ፡ በብሩር ። ንዋይ ፡ ዘይጠረይ ፡ እምግብር ። ሃይማኖት ፡ እንተ ፡ ትጠረይ ፡ እምተምህሮ ። ትሩፋት ፡ እንተ ፡ እምኔሃ ፡ ትጠረይ ፡ ንጽሐ ፡ ልብ ። ጸጋ ፡ መንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ እንተ ፡ ትጠረይ ፡ በጥምቀት ፡ (ፈ ፡ መ ፡ ፳፭ ፡ ፩ ። ፍ ፡ ነ ፡ ፴፬ ። ማር ፡ ይሥ ። ፊልክ ፡ ፬ ፡ ፳) ።

**ጥሩይ፤ (ያን ፡ ያት ፡ ሪት)፤** የተገዛ ፡ ግዝ፤ ውጁ ፡ ውርስ ።

**ጥሪት፤ (ታት)፤** በቁሙ፤ ጥሩ ፡ ገንዘብ፤ ብዕል ፡ ሀብት፤ ብዙ ፡ ክብት፤ ቋም ፡ መንጋ ፡ የሚንጋጋ ። ሑር ፡ ወሢጥ ፡ ጥሪተከ ፡ ወሀብ ፡ ለምስኪናን፤ ወሖረ ፡ ትኩዘ፤ እስመ ፡ ብዙኅ ፡ ጥሪቱ ። አጥርዮ ፡ ጥሪታት ፡ (ማቴ፲፱ ፡ ፳፩ ፡ ፳፪ ። ፍ ፡ ነ ፡ ፳፱ ፡ ፬) ።

**መጥሪት ፤ (ብ ፡ መጥርያት ፡ ታት) ፤** ጥሪት ፡ ማጥሪያ ፤ ዕቃ ፡ መሣሪያ ፤ ወፍጮ ፡ መኪና ፤ ወይም ፡ የሚከራይ ፡ ገመል ፡ አህያ ፡ ፈረስ ፡ በቅሎ ፡ ባሪያ ፡ የመሰለው ፡ ኹሉ ። በእንተ ፡ አንስቲያሆሙ ፡ ወውሉዶሙ ፡ ወመጥርያታቲሆሙ ፡ ወኪነታቲሆሙ ፡ (ፊልክ ፡ ፫) ።

**ጥራይ ፤ (ያን) ፤** ጥሬ ፡ ገንዘብ ፡ ፍራጣ ፤ ሩብ ፡ አላድ ፡ ቤሳ ፡ መሐልቅ ፤ ጥሬ ፡ ብር ፡ ጥሬ ፡ ወርቅ ። ወአልብክሙ ፡ ጥራያኒሆሙ ፡ (ሔኖ፲፱ ፡ ፯) ።

**ጥራይ ፤ (ዕብ ፡ ጣሪይ ። ዐረ ፡ ጠሪይ) ፤** ጥሬ ፤ ያልበሰለ ፡ እሳት ፡ ያልነካው ።

**ጥራዩ ፤** ጥሬውን ፡ በጥሬው ፡ ሳይበስል ፤ ወይም ፡ ብቻውን ፡ (ዘፀ፲፪ ፡ ፱ ። ኩፋ ፡ ፵፱) ። ኮኑ ፡ ይበልዑ ፡ ኅጠተ ፡ ሥርናይ ፡ ጥራዮ ። የሐምል ፡ ሐምለ ፡ ገዳም ፡ ወይበልዕ ፡ ጥራዮ ፡ እምኔሁ ፡ (ዮሴፍ ። ገድ ፡ ተክ) ።

**ጥሬ ፤** በቁሙ ፤ ያልበሰለ ፡ ቅንጣት ፡ ፍሬ ፤ ያልተፈታ ፡ ቋንቋ ፡ በዚያው ፡ በበቀለበት ፡ የሚነገር ። ሃሌ ፡ ሉያ ፡ ኦደናይ ፡ ኤሎሄ ፤ ይህን ፡ የመሰለ ። ከዘር ፡ ከአንቀጽ ፡ የሚወጣ ፡ ፍሬ ፡ ቃል ፡ ስምና ፡ ቅጽል ፤ ያውም ፡ ዘመድና ፡ ባዕድ ፡ የሚባል ። ዘመደንና ፡ በዐደን ፡ ተመልከት ።

**ጠሪቅ ፤ ቆት ፤ (ጠረቀ ፡ ይጠርቅ ፡ ይጥርቅ ። ዕብ ፡ ጣራቅ ፤ መታ) ፤** መጠረቅ ፡ መጠርነቅ ፤ መጠርቄሽ ፡ መብሳት ፡ መንደል ፤ አጣብቆ ፡ መውጋት ፡ መቸንከር ፤ መለበጥ ፡ ማስጌጥ ። መጠርቀቅ ፡ ማስጨነቅ ፤ ማነቅ ፡ መፈጥረቅ ፤ አጥብቆ ፡ አጣብቆ ፡ መያዝ ፤ የሰው ፡ የንስሳ ፤ እስኪቱን ፡ ሲያሹት ፡ ሲያኰላሹት ፤ ሌባም ፡ ቢኾን ፡ እውነት ፡ እስኪያወጣ ። ባለብሉዮች ፡ ግን ፡ መቅዘን ፡ ይሉታል ፤ ይኸውም ፡ ወይፈን ፡ ሲቀጠቀጥ ፡ በግድ ፡ የሚቀዝን ፡ ስለ ፡ ኾነ ፡ ነው ። መጠርቃት ፡ ማገገም ፤ በመብል ፡ መታደስ ፡ ማፈርጠም ፤ ከተኰላሹና ፡ ከተቀጠቀጡ ፡ በኋላ ። በዐረብ ፡ ቋንቋ ፡ ግን ፡ ጠሪቅ ፡ ጥሬ ፡ ዘር ፡ ነው ፤ መንገድ ፡ ጐዳና ፡ ጥርጊያ ፡ ይኾናል ።

**ጠራቂ ፤** በቁሙ ፤ የሚጠርቅ ፡ የሚጠረንቅ ። (ተረት) ፤ ነገር ፡ ባዋቂ ፤ ብረት ፡ በጠራቂ ።

**አጥረቀ ፤** አስጠረቀ ፤ አስመታ ፡ አስቀጠቀጠ ፤ እስኪቀዝን ፡ ድረስ ።

**አጥራቂ ፤** የሚያስሞክት ፤ የሚያስነጋ ። ባለብሉዮች ፡ ግን ፡ ጡርቂያም ፡ እንደ ፡ ማለት ፡ ቅዘናም ፡ ይሉታል ፤ ፍችው ፡ አይደለም ።

**ተጠርቀ ፤** ተጠረቀ ፤ ተቀጠቀጠ ፡ ተኰላሸ ።

**ጥሩቅ ፤ (ቃን ፡ ቃት ፡ ርቅት) ፤** የተጠረቀ ፡ ጥርቅ ፤ የተስነጋ ፡ ፍሬው ፡ የወጣ ፤ ኰልሹ ፡ ስንጋ ፡ ቅጥቅጥ ። ዘምቱር ፡ ወዘጥሩቅ ፡ ኢታቅርቡ ፡ ለእግዚ ፡ (ዘሌ፳፪ ፡ ፳፬) ። ወዘጥሩቅ ፡ ባለው ፡ ወዘአጥራቂ ፡ ይላል ፤ የመላሽና ፡ የጣፊ ፡ ስሕተት ፡ ነው ።

**ጠሪስ ፤ ሶት ፤ (ጠርሰ ፤ ጠረሰ ፡ ይጠርስ ፡ ይጥርስ ። ዕብ ፡ ጣሬሽ) ፤** መጠርሰም ፤ መስበር ፤ መሠንጠቅ ፡ መፍለጥ ፤ መምታት ፡ መቀጥቀጥ ፡ ለማድቀቅ ፤ የደንጊያ ፡ የገል ፤ ወይም ፡ የመብል ፤ መጨረስ ፤ መጨራረስ ፡ መፈጸም ፤ የሥራ ። ጥርስ ፡ ማውጣት ፡ ማብቀል ፤ የሕፃን ። (ተረት) ፤ እኔ ፡ እበላው ፡ ሳጣ ፡ ልጄ ፡ ጥርስ ፡ አወጣ ። መጥረስ ፡ መደንዝ ፤ ወይም ፡ ጥርሳም ፡ ገጣጣ ፡ መኾን ። ፀርስን ፡ እይ ።

**ጥርስ ፤ (ብ ፡ ጥረስ ፤ አጥራስ) ፤** በቁሙ ፤ መንጋጋ ፡ ክራንቻ ። ወሰእመ ፡ ሰበረ ፡ ጥርሰ ፡ ወስነ ። አንገፍክዎሙ ፡ እማእከለ ፡ ጥረሲሆሙ ፡ ዘመሠጡ ። ጥረሲሆሙ ፡ ለአናብስት ። ስነነ ፡ መጥባሕት ፡ ቦቱ ፡ ወጥረሲሁ ፡ መከርከር ። መሊኅ ፡ አጥራስ ፡ (ዘፀ፳፩ ፡ ፳፯ ። ኢዮ፳፱ ፡ ፲፯ ። መዝ ፡ ፶፯ ። ምሳ፳፬ ፡ ፴፯ ። ስንክ ፡ መስ፲፰) ።



ጥረስ ፡

**ጠረጴዛ ፤ (ዛት ። ጽር ፡ ትራፔዛ) ፤** ስደቃ ፡ ገበታ ፤ አራት ፡ እግር ፡ ያለው ፡ ማናቸውም ። ምሧዕ ፡ መንበረ ፡ ታቦት ፡ ከንርከኑ ፡ ከናጐበሩ ፤ መቅደስ ፡ ቅድስተ ፡ ቅዱሳን ። ኢይትወከፍዎሙ ፡ ውስተ ፡ ቅድስት ፡ ጠረጴዛ ። ኢይደልዎሙ ፡ ይባኡ ፡ ውስተ ፡ ቅድስት ፡ ጠረጴዛ ፡ ወምሥዋዒሁ ፡ ለእግዚ ። ጠረጴዛት ፡ ዘምስጢር ። ሰላም ፡ ለታእድራ ፡ ዘሐነጸት ፡ ጠረጴዛ ። አሪታዊት ፡ ጠረጴዛ ፡ (ቀሌ ። አርጋ ፡ ፮ ። ስንክ ፡ መጋ፲፩ ። ታኅ፫) ።

**ጠስ ፤** የመጽሐፍ ፡ ስም ፤ የፍትሐ ፡ ነገሥት ፡ መዠመሪያ ፡ ክፍል ፤ ካራት ፡ አንዱ ። ጠስ ፡ መክ ፡ መግ ፡ መጅ ፡ (ፍ ፡ ነ ፡ መቅ) ።

**ጠስይ ፤ ዮት ፤ (ጠሰየ ፡ ይጠሲ ፡ ይጠሲ ። ዕብ ፡ ጣሽጤሽ) ፤** ማጥፋት ፡ መደምሰስ ፤ መፋቅ ፡ መሠረዝ ፤ የጥፈት ። መጣስ ፡ መጠምሰስ ፤ ማስተኛት ፡ መለጠስ ፤ ምስጢሩ ፡ ያው ፡ ማጥፋት ፡ ነው ። ቤቱ ፡ የጠፈረ ፡ ነው ፤ እንደ ፡ ቀተለም ፡ ይኼዳል ። ኅድገኒ ፡ እጥስዮሙ ። እኪይዖሙ ፡ ወእጠስዮሙ ። ጠስየኒ ፡ ምስሌሆሙ ። አነ ፡ ጠሰይክዎሙ ፡ በመፀትየ ። ተሀበኒ ፡ መድኀኒተ ፤ ደዌ ፡ ኀጢአት ፡ ዘይጠሲ ፡ (ዘፀ፴፪ ፡ ፲ ። ፪ነገ ፡ ፳፪ ፡ ፵፫ ። ክብ ፡ ነገ፱ ። መቃ ፡ ገ፯ ። ስንክ ፡ መስ፳፪) ። መስፈር ፡ መለካት ፡ ልክ ፡ ማድረግ ፡ ሳይተርፍም ፡ ሳይጐድልም ፡ የርጥብ ፡ የደረቅ ። ጣሳ ፡ ማለት ፡ ከዚህ ፡ ወጥቷል ። ማርጀት ፡ ማፍጀት ፤ መጠስጠስ ፡ የድሜን ፡ ልክ ፡ ማድረስ ።

**ጠሳዪ ፤ (ዪት ፡ ይያን ፡ ያት) ፤** የሚያጠፋ ፡ አጥፊ ፤ ጣሽ ፡ ጠምሳሽ ።

**ተጠስየ ፤** ጠፋ ፡ ተደመሰሰ ፤ ተፋቀ ፡ ተጣሰ ። ተመስወ ፡ ልቦሙ ፡ ወተጠስየ ፤ ወኀጥኡ ፡ ዘይኄልዩ ፤ ጠፋ ፡ (ኢያ፭ ፡ ፩) ።

**ጥሱይ፤(ያን፡ያት፡ሲ.ት)**፤የጠፋ፡የተጣሰ።

**ጥስየት**፤መጥፋት፤ጥፋት፡አጠፋፍ፤ጥሶሽ፡አጣጣስ።

**ጥስን**፤ጠስኝ፤የደጋ፡ቅጠል፤ከድልኽ፡ቅመም፡የሚገባ።

**ጤት፤—ስመ፡ፊደል፤—ጠይት።**

# የ

**የ**፤፲ኛ፡ፊደል፡በግእዝ፡አልፍ፡ቤት፡በአበገደ፤ስሙ፡የማን፤ቍጥሩ፡ዐሥር፤አኃዝ፡ሲኾን፡የ፡ዐሠርት፡ቱ፡ይባላል።

**የ**፤የአካል፡ዝርዝር፤አን፡ለሚል፡ብቻ። **ለልየ፤ኪ.ያየ፤ ዚ.ኣየ፤ ነፍስየ።**

**የ**፤ሥርወ፡ትንቢት፤የካልኣይ፡አንቀጽ፡መነሻ፡ለሦስት፡ስራዊት፤ለሩቅ፡ለሩቆች፡ወንዶችና፡ሴቶች። ግእዙ፡ብቻ፡ስለ፡ተነገረ፡ራብዑና፡ሳድሱ፡አይቀሩም። ይህም፡ **ፆቀ፡(ፆቁ፡ፆቃ)፡የዐውቅ፡(ቁ፡ቃ)፡ይዑቅ።አፆቀ፡(ቁ፡ቃ)፡ያዐውቅ፡ያዑቅ፡** እያለ፡ሌላውን፡ኹሉ፡ያሳያል። የትንቢት፡አሥራው፡፬፡ብቻ፡ናቸው፤የ፡ተ፡አ፡ነ።

**ዩ**፤የቅጽል፡ምእላድ፤ወይም፡የስም፡አርቲክል፤በሴት፡አንቀጽ፡ለሚነገር፡ቃል። ሐዳስዩ፡ድንግልዩ፡ብሊትዩ፡ዕቤርዩ፡እያለ፡ይህን፡በመሰለ፡ይገባል። ሲፈታም፡ዐዲሷ፡ዐዲሲቱ፤ባልቴቷ፡ባልቴቲቱ፡ያሰኛል። **ይዌድስዋ፡መላእክት፡ለማርያም፡በውስተ፡ውሳጤ፡መንጦላዕት፡ወይብልዋ፡በሓኪ፡ማርያም፡ሐዳስዩ፡ጣዕዋ፡(ሳታት)።**

**ዪ—ዬ**፤የማልስና፡የኃምስ፡ሥረዮች፤ዪ፡የማልስ፡ዬ፡የኃምስ። የማልስ፡የኃምስ፡ድምፅ፡ኹሉ፡ከዪና፡ከዬ፡ወጥቷል፤ቅጥላቸውም፡ኢ፡ኤ፡የዪና፡የዬ፡ምልክት፡ነው። ፊደል፡ኹሉ፡አለየ፡መሪነት፡ማልስና፡ኃምስ፡አይኾንም።

**ዪ—ይ**፤የጥሬና፡የስም፡ምእላድ፤ወገናዊ፡ቅጽል፡የ፡ኛ። ዊና፡ይን፡ተመልከት።

**ያ**፤የጥሬና፡የስም፡ምእላድ፤ፍችው፡ኛ፡የ። **ኬንያ፡ሐዋርያ**፤ብልኀተኛ፡መንገደኛ። **ኢትዮጵያ፡እስክንድርያ**፤የኢትዮጲስ፡የእስክንድር፡አገር፤ወይም፡ኢትዮጳዪት፡እስክንድራዪት፡ያሰኛል፤ይኸውም፡በተጸውዖ፡ስም፡ሲገባ፡ነው።

**ያ**፤አብገር፡ምእላድ፤ክንና፡ክት፡እየተደረበ፡በማልስ፡ቅጽል፡በማልስ፡መስም፡ይገባል። **ቀታሊ.ልያን፡ያት፤መምለኪ.፡ክያን፡ያት።** ብዙዎቹን፡ወንዶችና፡ሴቶች፡በሚያስተባብር፡በመድበል፡ቅጽል፡ግን፡ተውጠ፡ተጕርዶ፡ይቀራል። **ቀተልት**፤መምለክት።

**ዮ**፤ቃለ፡ብካይ፡ወሰቈቃው፤በቁሙ፤ዮ፡ወዮ፡ወየው፤ይብላኝ። **ብክይዎ፡ወላሕውዎ፡እለ፡ታፈቅርዎ፤ዮ፡ዮ፡ዮ፡ዐማኑኤል፡አምላክነ፡(ቅዳ፡አፈ)።**

**ዮ**፤ቃለ፡ትፍሥሕት፡ወአንክሮ፤ዕሦ፡ዕሠይ፡ኢዮሃ፤እንሆ። **ዮ፡መስቀል፡ጸገየ።ዮ፡ዮ፡ዮ፡መንክር፤** እንሆ፡ድንቅ፡(ድጓ)።(ዕርኟ፡ቍ፺፬)።

**ይ—ዩ**፤የቅጽል፡ምእላድ፤እንደ፡ዊ፡በጥሬና፡በስም፡እየገባ፡ወገን፡የሚያሳይ። **ቅድም፡ቀዳማይ—ዩ፤(ዩት፡ይያን፡ያት)**፤ፊተኛ፤የፊት። **ፊደታይ**፤የወንበደች፡ወገን፤ቀማኛ። **ላዕላይ፡ታሕታይ**፤ላይኛ፡ታችኛ፤የላይ፡የታች፤በላይ፡በታች፡ያለ። **ግብጻይ፡ግብጻዩ**፤የግብጽ፡ሰው። **ቀርናይ—ዩ**፤ቀንደኛ፡ቀንዳም፡ባለቀንድ፤የቀንድ፡ከብት፡ተዋጊ፡እያሰኘ፡እንደ፡ሙሻዘር፡እንደ፡ማልስ፡ቅጽል፡በሚያምርለት፡ስልት፡ይፈታል። ምክንያቱም፡ዊና፡ዩ፡ማልሶች፡ስለ፡ኾኑ፡ነው፤በዪ፡ፈንታ፡ግን፡ይ፡መጣፉ፡ስለ፡ተለመደ፡ነው፡እንጂ፡የሚገባው፡ኹኖ፡አይደለም፤ማልስና፡ሳድስ፡ምን፡ገጥሞት። ባማርኛ፡ግን፡ሳድሱን፡ሲጣኑት፡ድምጡ፡እንደ፡ማልስ፡ስለ፡ኾነ፡ማልስና፡ሳድስ፡ይዋረሳሉ፤ስጪ፡ገዢ፤ስጭ፡ገዥ፤የመሰለው፡ኹሉ፤የዊን፡ፍች፡እይ።

**ዮ፤(ያ፡ዮሙ፡ዮን)**፤ድርብ፡ዝርዝር፤የገቢር፡ዐጸፋ፡ባራት፡ስራዊት፡በሩቅ፡በሩቆች፡የሚነገር። ኪያሁ፡(ሃ፡ሆሙ፡ሆን)፡በማለት፡ፈንታ፤እየገባ፤ያን፡ያንን፡ርሱን፡ያሰኛል። **ሀበኒዮ፡እምውእቱ፡ማይ። ከመ፡የሀበኒያ፡ለይእቲ፡መጽሐፍ። ወሊተ፡ወሀብከኒዮሙ። አልቦ፡ዘየሀይደኒዮን፤እስመ፡አቡየ፡ዘወሀበኒዮን፡ውእቱ፡የዐቢ፡እምኵሉ፡** (ዮሐ፬፡፲፭። ራእ፲፡፱። ዮሐ፲፯፡፮። ፲፡፳፰፡፳፱)።

**ይእዜ፤(ይእቲ፡ጊዜ)**፤አኹን፡በዚች፡ሰዓት፤ዛሬ፡ዘንድሮ። አኹን፡ማለት፡ቅጽበት፡ደቂቃ፡ሳይቀር፡የጊዜን፡መቅረብና፡ማጠር፤ያሉበትን፡ክፍል፡ያሳያል። **ይእዜ፡ትስዕሮ፡ለገብርከ። ይእዜኒ፡ወዘልፈኒ። እምእስየ፡እስከ፡ይእዜ። እምይእዜ፡ወእስከ፡ለዓለም፡**(ሉቃ፪፡፳፱። ይሁ፡፳፭። መዝ፡፩። ኤፍ፡፭)። አንዳንድ፡ጊዜም፡በእንክ፡ዘይቤ፡ይፈታል፤ዮምን፡ተመልከት፤የዚህ፡መንቲያ፡ነው።

**ይእቲ፤—ያት፡ርሷ፤ነች፡ናት፤—ውእቱ ።**

**ይቤ፤(በዪል፤ሎት፤ቤለ፡ይበይል፡ይቢል።አው፡ቤለ፡ይቤ፡ይበል)፤** የቤለ፡ ክልኣይ፤ትንቢት፡አንቀጽ ። ፍችው፤ ይል፤ ይላል፤ ይል፡ ነበር ። የቤለ፡ ትንቢቶች፡ ክልኣዮቹ፡ ይቤና፡ ይበይል፡ ኹለት፡ እንደ፡ ኾኑ፡ አስተውል ። መምህራን፡ ግን፡ በቤለ፡ ፈንታ፡ ይቤን፡ ከብህለ፡ ደርበው፡ ቀዳማይ፡ አንቀጽ፡ ያደርጉታል፤ ፪ኛም፡ ዘሩና፡ አርእስቱ፡ በዪል፡ ሲኾን፡ አርእስት፡ የለውም፤ ነባር፡ አንቀጽ፡ ነው፡ ይሉታል፤ ብሂልን፡ እይ ።

**የብበ፤ ቦት፤(የበበ፡ ይዬብብ፡ ይየብብ።ዕብ፡ወሱር፡ያቤብ፤ጮኸ፡አለቀሰ)፤** እልል፡ ማለት፤ በደስታ፡ ቃል፡ መጮኽ፡ ማመስገን፤ የዘፈን፡ የማሕሌት ። ባበየን፡ እይ፤ የዚህ፡ ግልባጭ፡ ነው ። የበበት፡እሌኒ።ቦ፡እመላእክት፡ዘይዜምር፡ወቦ፡ዘይዬብብ፡(ድጓ ። ቀሌ ። መዝ፡ ፵፯ ። ፹፰) ።

**ይባቤ፤(ብያት)፤** በቁሙ፤ እልልታ፡ ጩኸት፤ ምስጋና፡ መዝሙር፡ በደስታ፡ ቃል፡ የሚነገር ። ወአልቦ፡ብዝኀ፡ለይባቤነ።ዐርገ፡እግዚ፡በይባቤ።ማርያም፡በይባቤ፡ትዘብጥ፡ከበሮ፡(መዝ፡ ፵፮ ። ፮ ። መዋሥ) ።

**የቢስ፤ ሶት፤(የብሰ፡ ይየብስ፡ ይይበስ። ዕብ፡ ያቤሽ። ሱር፡ ዩቢሽ። ዐረ፡ የቢሰ)፤** መድረቅ፡ መክረር፤ ርጥበት፡ ልምላሜ፡ ማጣት።ፈለግ፡ይነፅፍ፡ወይየብስ። ወውእቱ፡የብሰ፡ከመ፡እብን።ይየብስ፡ተክሎሙ።የብሰ፡ማእረረ፡ምድር፡(ኢዮ፲፬፡ ፲፩ ። ፩ነገ፡ ፳፭፡ ፴፯ ። ኢዮ፳፬፡ ፲፱ ። ራእ፲፬፡ ፲፭) ።

**ይቡስ፤(ሳን፡ ሳት፡ ብስት)፤** የደረቀ፡ የከረረ፤ ደረቅ፡ ክሩሩ ። ይብስት፡ባሕር።አዕፅምት፡ይቡሳት። ይቡሳነ፡ልብ።ዕፀ፡ይቡስ።ኀብስት፡ይቡስ።ክሣድ፡ይቡስ፡(ዘፀ፲፬፡ ፳፱ ። ሕዝ፴፯፡ ፬ ። ሔኖ፭፡ ፬ ። ሚራ፯፡ ፫ ። ቄድር ። ኩፉ፡ ፩) ።

**ይብሰት፤** መድረቅ፡ አደራረቅ፤ ድርቀት፡ ድርቅና፡ ደረቅነት ። ሐዘንከኑ፡ በእንተ፡ ይብሰተ፡ ሐምሐም። ይብሰተ፡ ኀብስት፡(ስንክ፡ መስ፳፭ ። ፈልክ፡ ፸፱) ።

**ይበስ፤** ድርቅ፤ ድርቀት ። ይበሰ፡ ኀብስት፡(ስንክ፡ ነሐ፲፱) ።

**የብስ፤** በቁሙ፤ ደረቅ፡ ምድር፡ ባሕር፡ የሌለው፤ ውሃ፡ ያልሸፈነው ። ይቤ፤ ያስተርኢ፡ የብስ፤ ወአስተርአየ፡የብስ፤ ወሰመዮ፡ እግዚ፡ለየብስ፡ምድረ። እለ፡ የኀድሩ፡ የብሰ። በየብስ፡ ወበባሕር፡(ዘፍ፩፡ ፱ ። ሔኖ፴፯፡ ፭ ። ዮሴፍ) ።

**አይበሰ፤** አደረቀ፤ አስደረቀ ። አየብሶሙ፡ ለአፍላግ።ለሥርዉኢ፡ ያየብሶ፡ ነፋስ ። አየብስ፡ ዕፀ፡ርጡበ። ያረጥባ፡ ለምድር፡ ወያየብሳ፡ ለባሕር። ያየብስዎ፡በፀሓይ፡(ኢሳ፶፡ ፪ ። ኢዮ፲፭፡ ፴ ። ሕዝ፲፯፡ ፳፬ ። ሳታት ። መ፡ ፈ) ።

**ዮጊ፤—እንሆ፡ ወይ፤—የወጊ ።**

**ዮድ፤—ስመ፡ ፊደል፤—የወድ ።**

**ይዶን፤(ሮማይ፡ ይዱስ)፤** ክፍለ፡ወርኀ፤ የወር፡ እኩሌታ፤ በዱሮ፡ አከፋፈል፡ የየካቲት፡ ፲፫ኛ፡ ወይም፡ በሠግር፡ ጊዜ፡ ፲፭ኛው፡ ቀን ። ወበወርኀ፡ሮሜ፡ቅድመ፡ሰማኒቱ፡ይዶን፡ፍርፍርዮን፡(ተረ፡ ቄርሏ፭) ።

**የዲዕ፤ ዖት፤(የድዐ፡ ይየድዕ፡ ይይዳዕ። ዕብ፡ ያዳዕ። ሱር፡ ዪዳዕ)፤** ማወቅ፡ መረዳት፤ ልኩን፡ ርግጡን፡ ማግኘት፤ በጠባያዊ፡ ዕውቀት፡ ፈልጎ፡ መርምሮ፡ ተመራምሮ፤ እንደ፡ አብርሃም፡ እንደ፡ ሙሴ፡ ጸሊም ።

**አይድዐ፤(ብህለ፤ ነበበ)፤** አለ፡ ነገረ፡ አስተማረ፤ አመለከተ፤ አሳወቀ፡ አስታወቀ፤ አስረዳ ። ወአነ፡ ኣየድዕ፡ግብርየ፡ለንጉሥ። መፍትወ፡ ኣየድዕ።አይድዕ፡ከመ፡ ኣሐይዋ፡ ለምድር። ኢያይድዐት፡ ብሔራ። ይእቲ፡አይድዐቶ፡ለንጉሥ፡ምክሮሙ፡(መዝ፡ ፵፬ ። ምሳ፳፡ ፯ ። ሔኖ፲፡ ፲፭ ። አስቴ፪፡ ፳፡ ፳፪) ።

**ተየድዐ፤** ታወቀ፡ ተረዳ፤ ተሰማ፡ ተባለ፡ ተነገረ ። ከመ፡ይትየዳዕ፡ ስምየ፡ ውስተ፡ ኵሉ፡ ምድር። ተየድዐ፡ነገሩ፡ ውስተ፡ ሀገር። በከመ፡ ተየድዐ፡ወተነግረ፡ በዐሠርቱ፡ ወክልኤቱ፡ አንቀጽ፡(ዘፀ፱፡ ፲፮ ። ዮሴፍ ። አቡሻ፡ ፴፱) ።

**ይዱዕ፤(ዓን፡ ዓት፡ ድዕት)፤** የታወቀ፡ የተረዳ፤ የተነገረ ።

**ደዐት፤** ማወቅ፡ መታወቅ፤ ዕውቀት፡ አነጋገር፤ ንግግር ።

**ዳዒ፤(ዕብ፡ ዴዒ፤ ዴዓ፤ ዳዐት)፤** ዕውቀት፡ ዕውቂያ፤ ማስተዋል ።

**እንዳዒ፤(ዕብ፡ ኤን፡ ዴዒ፤ አልቦ፡ ዑቀት)፤** አሉታ፤ አላውቅም፡ አላወቅኹም፤ አላስተዋልኹም ። ወይም፡ ጥርጥር፤ እንጃ፤ ምናልባት ። እንጋን፡ እይ፤ የዚህ፡ መንቲያ፡ ነው ። እንዳዒ፤ እግዚ፡ የአምር። እንዳዒ፤ ኢያእመርኑ፡ ከመ፡ ይመልእ፡ ኵሉ፡ ዝቅ፡ ወይነ። እንዳዒ፤ እመ፡ቦ፡ ዘንለይክ፡(፪ቆሮ፡ ፲፪፡ ፪፡ ፫ ። ኤር፡ ፲፫፡ ፲፪ ። ሄርማ፡ ገ፫) ። ከማሁ፡ በማለት፡ ፈንታ፡ እንዲሁ፡ እንደ፡ ማለት፡ እንዳዒ፡ ይላልኹ በሌላም፡ በብዙ፡ ቦታ፤ እንዳዒ፡እንጋ። እፈርህክሙ፡እንዳዒ፡ እያለ፡ አለ፡ ስልቱ፡ ገብቶ፡ ይገኛል፤ የመላሽ፡ ስሕተት፡ ነው፡ (፪ቆሮ፡ ፲፭፡ ፫ ። ሮሜ፭፡ ፯ ። ገላ፬፡ ፲፩) ።

**ያህ፤(ዕብ። ሱር፡ ይያ)፤** ዐጭር፡ ስመ፡ አምላክ፤ የይሆዋ፡ ክፋይ ። ዘይቤው፡ እግዚእ፤ ምስጢሩ፡ ምላትና፡ ስፋት፡ ልዕልናና፡ ርቀት፡ ያሳያል ። ዕብራውያንም፡ ሲፈቱ፤ ዐቢይ፡ ወጽኑዕ፡ ስፉሕ፡ ወም

ሉእ፤ እግዚእ፥ ዘበአማን፥ ዘያገምር፥ ኵሎ፥ ወኢያገምሮ፥ መካን፤ ይሉታል። ሃሌ፡ ሉያ፡(ዕብ፡ ሀልሉ፡ ያህ)፤ የሃሌ፥ ሉያን፥ ፍች፥ እይ።

**የሂድ፤ ዶት፤** (የሀደ፥ ይየሀድ፥ ይይሀድ። ዕብ፥ ያሄድ)፤ ይሁዲ፥ ማድረግ፤ አሕዛብን፥ ወደ፥ ሕዝብ፥ መሳብ፤ ማስጠጋት፥ ማቅረብ፤ መግዘር፥ በኦሪት፥ ማሳመን፤ ከዚህ፥ የተነሣ፥ እግዜርን፥ ማመስገን፥ ማስመስገን። ገየረንና፥ አፍለስን፥ እይ፤ የዚህ፥ ጎሮች፥ ናቸው፥ (ማቴ፳፫፥ ፲፭)።

**ይሁዳ፤ (ዕብራ)፤** የሰው፥ ስም፤ ምስጋና፥ እምነት፤ ወይም፥ እማኒ፥ ምእመን፥ ማለት፥ ነው፥ (ዘፍ፳፱፥ ፴፭)። ስመ፥ ነገድ፤ ስመ፥ ሀገር፤ ይሁዳ፥ የወለደውና፥ የወረሰው፥ የይሁዳ፥ ዘር፥ የይሁዳ፥ ምድር። ወኮነ፡ ይሁዳ፡ መቅደሶ፡ ወእስራኤልኒ፡ ምዙናኖ። በእንተ፡ ይሁዳ፡ ወኢየሩሳሌም፡ (መዝ፥ ፻፲፫። ኢሳ፩፥ ፩። ማቴ፪፥ ፳፪። ፫፥ ፭። ፱፥ ፳፭)።

**አይሁድ፤** በቁሙ፤ ይሁዶች፥ የይሁዳ፥ ዘሮች። ይህ፥ ስም፥ እስከ፥ ባቢሎን፥ ምርኮ፥ ድረስ፥ የይሁዳ፥ ብቻ፥ ነበረ፤ ከምርኮ፥ በኋላ፥ እስከ፥ ክርስቶስ፥ ድረስ፥ ለእስራኤል፥ ኹሉ፥ ተሰጥቷል። ፈላሻና፥ እስራኤል፥ ሕዝብና፥ አሕዛብ፥ ሲኾኑ፥ በይሁዳ፥ ስም፥ አይሁድ፥ መባላቸው፤ ኋላ፥ ከይሁዳ፥ ወገን፥ በሚመጣው፥ በክርስቶስ፥ ክርስቲያን፥ ለመባል፥ ምሳሌ፥ ነው፥ (ግብ፲፩፥ ፳፮)። ወፈቀደ፡ ያጥፍአሙ፡ ለኵሎሙ፡ አይሁድ፡ ዘውስተ፡ ደወለ፡ መንግሥቱ፡ ለአርጤክስስ። ቦኑ፡ ለባሕቲቶሙ፡ ለአይሁድ፡ እግዚ፡ አኮኑ፡ ለአሕዛብኒ። እስመ፡ መድኀኒት፡ እምነ፡ አይሁድ፡ (አስቴ፫፥ ፯። ሮሜ፫፥ ፱። ዮሐ፬፥ ፳፪)። ከክርስቶስ፥ ወዲህ፥ ግን፥ በክሕደታቸው፥ ስለ፥ ተነቀፉ፥ አይሁድነታቸው፥ ወዳረመኔነት፥ ተለውጧል። ጉባኤ፡ አይሁድ፡ እለ፡ ይሰመዩ፡ በከንቱ፡ አይሁደ። ፀርፈተሙ፡ ለእለ፡ ይብሉ፡ አይሁድ፡ ንሕነ፡ ወኢኮኑ፤ አላ፥ ማኅበሩ፡ ለሰይጣን፡ (ዲድ፥ ፲፱። ራእ፪፥ ፱)።

**አይሁዳዊ፤ (ዊ—ይ)፤** በቁሙ፤ የአይሁድ፥ ወገን፥ ይሁዲ፥ እስራኤላዊ፤ ወይም፥ ፈላሻ፥ ግዙር። ወነገርዎ፡ ከመ፡ መርዶኪዎስ፡ አይሁዳዊ፡ ውእቱ። ቦኑ፡ አነ፡ አይሁዳዊ። አይሁዳይ። አይሁዳውያን። ወእሙስ፡ አይሁዳዊት፡ (አስቴ፫፥ ፬። ዮሐ፲፰፥ ፴፭። ሲኖ ደ። ስንክ፥ ኅዳ፳፭። ግብ፲፮፥ ፩)።

**ይሁድና፤** ይሁዲነት፤ ይሁዲ፥ መኾን፥ መባል፤ እምነት። ይሁድና፡ ዘአይሁድ። ጾረ፡ ንጢአት፡ ዘአመ፡ ይሁድና፡ (ቄር፥ አላ። ተረኅ ፲፱)።

**ተይሀደ፤** ይሁዲ፥ ኾነ፤ በኦሪት፥ በግዝረት፥ አመነ። ቦኑ፡ ለዐይነ፡ ሰብእ፡ ይትየሀዱ። አኮኑ፡ በክዱን፡ ይትየሀዱ። ምንት፡ ረባሁ፡ ለተይሀዶ። እለ፡ ይትየሀዱ፡ ምጽአተ፡ ዚኣሁ፡ (ሮሜ፱፡ ፳፰፡ ፳፱። ፪፥ ፩። ገላ፪፥ ፲፱)።

**ትይህድና፤** ይሁዲነት፤ የአይሁድ፥ እምነትና፥ ሥርዐት፤ ለሐዲስ፥ ኪዳን፥ አምሳል፥ መርገፍ፥ ኹኖ፥ የተሰጠ፥ (መጽ፥ ምስ። ስንክ፥ ግንቦ፳፫)።

**ይሆዋ፤ (ዕብ፥ ይሆዋህ)፤** ስመ፥ አምላክ፤ ከፍጡራን፥ ስም፥ የተለየ፤ ከፈጣሪ፥ በቀር፥ ለማንም፥ ፍጡር፥ የማይሰጥ፤ ፍጡራን፥ የማይጠሩበት። መጽሐፍ፥ ግን፥ በይሆዋ፥ ፈንታ፥ ይሆባ፥ ይላል። ይሆባ፡ ጸባኦት፡ አዶናይ፡ (ድር፥ ሚክ)። ፍችውም፥ እግዚአ፥ ኵሉ፤ አምላክ፥ ኵሉ፤ ፈጣሬ፥ ኵሉ፥ ዓለም፤ ንጉሠ፥ ኵሉ፥ ዓለም፥ ያሰኛል። እግዚአብሔርን፥ ተመልከት፤ ከዚህ፥ ጋራ፥ አንድ፥ ነው።

**ዮጊ፤ (ንኡስ፥ አግ)፤** እንሆ፤ አኹን፥ ዛሬ፥ (ይህ፥ ጊዜ)፤ ወይ፤ ምናልባት። ዮጊ፡ በጽሒት፡፡ እምትሡዒ፡ ለአማልክት፡ ወእምዕጣነ፡ ታዐርጊ፤ ተመትሮተ፡ ክሣድ፡ አብደርኪ፡ ወኀረይኪ፡ ዮጊ፡፡ መኑ፡ የአምር፡ ዮጊ፡ በዝንቱ፡ መዋዕል፡ ንግሥኪ፡፡ ገሥጾ፡ ለዐርክከ፤ ዮጊ፡ ኢገብረ፡፡ ኢትፍቅድ፡ ከዊነ፡ መኰንነ፤ ዮጊ፡ ኢትክል፡ ተበቅሎቶ፡ ለዘአበሰ፤ ወዮጊ፡ ታደሉ፡ ለገጸ፡ ዐቢይ፡ (ሉቃ፲፩፥ ፰። ስንክ፥ ግንቧ። አስቴ፬፥ ፲፬። ሢራ፯፥ ፮። ፲፱፥ ፲፫፥ ፲፱)። (ዕርሺ፥ ቍ፲፯)።

**ዮድ፤ (ዕብ፥ ዩድ)፤** ስመ፥ ፊደል፤ ፲ኛ። ፍችው፥ እጅ፥ (መዝ፻፲፰፥ ፸፫—፹። ሰቈ፩፥ ፲። ፪፥ ፲። ፫፥ ፳፱። ፬፥ ፲)። በመዝሙር፡ ዮድ፡ (መጽ፥ ምስ)።

**ዮዳሄ፤ (ጽር። ዕብ፥ ይሆያዳዕ)፤** የሰው፥ ስም፤ እግዜር፥ ያውቃል፥ (፬ነገ፥ ፲፩፥ ፬)። ዳግመኛም፥ በዮዳሄ፥ ፈንታ፥ ኢዮአዳ፥ ይላል፤ ስሕተት፥ ነው፥ (፬ዜና፥ ፳፬፥ ፬)።

**የውሀ፤ ሆት፤ (የውሀ፤ ይዩውህ፥ ይየውህ)፤ (ገቢር)፤** ማለዘብ፥ ማለዛዘብ፤ ማግራራት፥ ማቈላመጥ፤ ቅንነት፥ ማስተማር፤ ገር፥ የዋህ፥ ቅን፥ ማድረግ። ሀሎ፡ ዘይጠብብ፡ ለነፍሱ፡ ወይዩውህ፡ በቃሉ፡፡ አንዘ፡ ይየውሃ፡ በቃል፡ ሠናይ፡፡ እትጋነይ፡ ላቲ፡ ወእዩውሃ፡፡ ትዩውሆሙ፡ ለኃጥአን፡ ወትመይጦሙ፡ በብዝኃ፡ ምሕረትከ፡፡ መዐተ፡ ንጉሥ፡ ከመ፡ መልአከ፡ ሞት፤ ወብእሲ፡ ጠቢብ፡ ይዩውሆ፡ (ሢራ፴፯፥ ፳፱። አስቴ፥ ፩። ኢዮ፲፮። ፲፮። ዲድ፥ ፴፯። ምሳ፲፮፥ ፲፬)። ማሞኘት፥ ማታለል፤ መደለል፥ መሸንገል፤ የከፋ። ዘይዩውሁ፡ ለከንቱ፡፡ ኢየዋህናከሙ፡ በቃል፡ (ቆላ፪፥ ፳። ፩ተሰ፥ ፪፥ ፭)። በየውሀ፥ ፈንታ፥ አየውሀ፥ ይላል፤ ስሕተት፥ ነው። አየውህዎ፡ (ስንክ፥ ሚያ፳፭)።

**የዋሂ፤ (ሂት፥ ህያን፥ ያት)፤** የሚያለዝብ፥ የሚያግራራ፤ የሚያሞኝ፥ ሸንጋይ፥ አታላይ።

**ተየውሀ፤ (ተገብሮ)፤** የዋህ፥ ኾነ፤ ቀና፥ ለዘበ፤ ተገራ፥ ለመደ፤ የወይፈን፥ የበቅሎ፥ ላውሬም፥ ይኾናል። ተሞኘ፥ ተታለለ፥ ተሸነገለ። አኮ፡ ከመ፡ ሰብእ፡ ዘይትዩዋህ፡ እግዚአብሔር፡፡ በተየውሆ፡ (ዘኍ፳፫፥ ፲፱። ሮሜ፲፮፥ ፲፰)።

**የውሀ፤ (ዐጕል። ዕብ፥ ያአህ፤ አማረ፥ ተዋበ)፤** ገኘ፥ ከማሁ፤ የዋህ፥ ኾነ፥ ለዘበ፥ ቀና፤ በገዛ፥ እጁ።

**የዋህ ፤ (ሃን ፡ ሃት)** ፤ በቁሙ ፤ የቀና ፡ ቅን ፡ ልዝብ ፤ ገር ፡ ገራም ፡ ጭምት ፤ ደግ ፡ ጥሩ ፤ እውነተኛ ። ቅጽልነቱ ፡ ዐጕል ፡ ሕገ ፡ ወጥ ፡ ስለ ፡ ኾነ ፡ ወንድና ፡ ሴት ፡ ያስተባብራል ፤ አዳምን ፡ እይ ። ተመሀሩ ፡ እምኔየ ፤ እስመ ፡ የዋህ ፡ አነ ። ብእሲ ፡ የዋህ ። በየዋህ ፡ ኵነኔ ፡ ይኴንን ። ቅሩብ ፡ እግዚ ፡ ለየዋሃነ ፡ ልብ ፡ (ማቴ፲፩ ፡ ፳፱ ። ሚራ፳፩ ፡ ፳ ። ኢሳ፲፩ ፡ ፬ ። መዝ ፡ ፴) ። ብእሲት ፡ የዋህ ። እመሰ ፡ የዋህ ፡ ይእቲ ፡ ወሠናይ ፡ ቃላ ፡ (ሚራ፳፮ ፡ ፲፱ ። ፴፯ ፡ ፳፰) ። ብዙ ፡ መጻሕፍት ፡ ይህም ፡ የጠቀስነው ፡ ሚራክ ፡ ሳይቀር ፡ በየዋህ ፡ ፈንታ ፡ የዋሂት ፡ ይላሉ ፤ አያሰኝም ። ብእሲት ፡ የዋሂት ፡ እም እከይ ። ርግብ ፡ የዋሂት ። በግዕት ፡ የዋሂት ፡ (ፍ ፡ ነ ፡ ፲ ፡ ፰ ። አፈ ፡ ተ፵፪ ። ስንክ ፡ ግንቦ) ። ለክፉ ፡ ሲኾን ፡ ሞኝ ፡ አላዋቂ ፤ ያልተማረ ፡ ያሰኛል ። የዋህ ፡ የአምን ፡ ኵሎ ፡ ነገረ ፡ (ምሳ፲፬ ፡ ፲፭) ።

**የውሀት ፤ የውሀና** ፤ በቁሙ ፤ የዋህ ፡ መኾን ፡ የዋህነት ፤ ገርነት ፡ ቅንነት ። በየውሀት ፡ ተናገረኒ ። ዘየሐውር ፡ በየውሀት ። ይኩነኒ ፡ በከመ ፡ የውሀትየ ። ርግብየ ፡ ይቤላ ፡ በእንተ ፡ የውሀታ ። ከመ ፡ በየውሀና ፡ ንሕዮ ፡ (ዕር ፡ ኢሳ፯ ፡ ፯ ። ምሳ፲ ፡ ፱ ። መዝ ፡ ፯ ። ድጓ ። ቄር ፡ ጸላ) ።

**ይዋሄ** ፤ ዝኒ ፡ ከማሁ ። በፍርሀት ፡ ወበይዋሄ ። ይዋሄ ፡ ወህድአት ፡ ወአርምሞ ፡ (አፈ ፡ ድ፪ ። ዮሴፍ ። አርጋ ፡ ፩) ።

**የውጣ ፤ (ጽር ፡ ዮታ)** ፤ ስመ ፡ ፊደል ፡ የ፤ ፲ኛ ፤ ዐሥር ፡ (ማቴ፭ ፡ ፲፰) ። ቀዳሚ ፡ ስሙ ፡ ለኢየሱስ ፡ የውጣ ፡ በኈልቈ ፡ (፲) ዐሠርቱ ። ፈጻሚት ፡ ቃላት ፡ የውጣ ፡ (ዲድ ፡ ፳ ። ውዳ ፡ ማርያ ። ስንክ ፡ ነሐ፲፰) ። የሱስ ፡ በማለት ፡ ፈንታ ፡ የውጣ ፡ ይላል ፤ ስሕተት ፡ ነው ። መርቆሬዎስ ፡ ስማዕተ ፡ የውጣ ፡ (ስንክ ፡ መስ፲፰) ።

**የዊም ፤ ሞት ፤ (ዮመ ፡ ይየውም ፡ ይዩም)** ፤ ጊዜን ፡ መስፈር ፡ መቍጠር ፤ መክፈል ፡ መተንተን ፤ ቅጽበትን ፡ በከልኢት ፡ ከልኢትን ፡ በደቂቅ ፡ ደቂቅን ፡ በሰዓት ፡ ሰዓትን ፡ በዕለት ፡ ዕለትን ፡ በ፳፬ ፡ ሰዓት ፡ መወሰን ፡ መቀመር ፤ የፈጣሪ ፡ የሰዓት ፡ ሠሪ ።

**ዮም ፤ (ዕብ ፡ ዮም ። ሱር ፡ ያውማ ። ዐረ ፡ የውም ፤ ዕለት ፤ መዓልት)** ፤ ዛሬ ፡ አኹን ፤ ዘንድሮ ፤ የተወሰነ ፡ ክፍል ፡ መዓልትና ፡ ሌሊት ፤ ዕለት ፡ ወርኅ ፡ ዓመት ፤ ቀመር ። ያሉበትን ፡ ቀን ፡ ወራትና ፡ ዘመን ፡ ከመባቻው ፡ እስከ ፡ መከተቻው ፡ ያሳያል ። የሰውም ፡ ዕድሜ ፡ ተወልደ ፡ እስኪሞት ፡ ተኹሞ ፡ እስኪሻር ፡ የሚኖረው ፡ ዮም ፡ ይባላል ፤ ይእዜንና ፡ ዕለትን ፡ ተመልከት ። ዘትማልም ፡ ወዮም ። ዮም ፡ ወለድኩከ ፤ ወዮም ፡ ብሂል ፡ እኮ ፡ ዘንሰፈ ፡ መዋዕል ፡ ዘይነግር ፡ አላ ፡ ዘሀሎ ። ዮምኬ ፡ ሰብእ ፡ ወጌሠመ ፡ መሬት ። ንጉሥ ፡ ለዮም ፡ ወጌሠመ ፡ ይመውት ፡ (ዕብ፲፫ ፡ ፰ ። ቄር ። ድጓ ። ሚራ፲ ፡ ፲) ።

**ዮማዊ** ፤ ሙያተኛ ፤ የዕለት ፡ ምንደኛ ፡ ከጧት ፡ እስከ ፡ ማታ ፡ የሚሠራ ። የዕለት ፡ መፍቅድ ፡ በየቀኑ ፡ የሚወጣ ፡ ወጪ ፤ ወይም ፡ ገቢ ፡ ገንዘብ ። ዮምዬ ፡ እንዲል ፡ (ዐረብ) ። ዘመናይ ፤ ሹም ፡ ባለጊዜ ፤ ዐፍለኛ ፡ ጐበዝ ፤ ወጣት ፡ ልጅ ፡ እግር ።

**ዮን ፤ ዮና ፤ (ዕብራ)** ፤ ርግብ ፤ ዮን ፡ ተባቱ ፤ ዮና ፡ እንስቲቱ ፤ ሲያባዛ ፡ ዮኒም ፡ ይላል ። ፪ኛም ፡ ዮና ፡ ዮናስ ፡ የሰው ፡ ስም ፡ ይኾናል ፤ ስምነቱም ፡ እንደ ፡ ደስታ ፡ ወንድና ፡ ሴት ፡ ያስተባብራል ፡ (ስንክ ፡ ኅዳ፲፰) ።

**ዮናን ፤ (ዕብ ፡ ያዋን)** ፤ ፪ኛው ፡ የያፌት ፡ ልጅ ፤ የግሪኮች ፡ አባት ። የሀገርና ፡ የሕዝብ ፡ ስም ፤ ጽርእ ፡ ግሪክ ፤ ፍችው ፡ አስሓቲ ፡ መስሕት ። በያዋን ፡ ፈንታ ፡ ይህያን ፡ ይላል ፤ ስሕተት ፡ ነው ፡ (ዘፍ፲ ፡ ፪) ።

**ዮናናዊ** ፤ የያዋን ፡ ዘር ፡ የግሪክ ፡ አገር ፡ ሰው ።

**ዮናኒ** ፤ ጽርእ ፡ የግሪክ ፡ ቋንቋ ፡ ከቅብጥ ፡ የሚስማማ ፡ የቅብጥ ፡ ጎረ ፡ ቤት ፡ ባለ፳፬ ፡ ፊደል ። ቅብጡ ፡ ፯ ፡ ፊደሎች ፡ ይጨምራል ፤ መለዮው ፡ ይህ ፡ ነው ።

**ያክንት ፤ (ጽር ፡ ኢያኪንቶስ ። ዕብ ፡ ሌሼም)** ፤ ክቡር ፡ ደንጊያ ፤ ዕንቍ ፡ የቀይ ፡ ጥቍር ፡ ደምማ ፤ ቅላቱ ፡ የሮማን ፡ ፍሬ ፡ ደረቅ ፡ በርበሬ ፡ የሚመስል ፤ ደባባ ፡ (ራእ፳፩ ፡ ፳ ። ሔኖ፳፭ ፡ ፪ ። ሕዝ፳፰ ፡ ፲፫) ።

—፤ ቀይ ፡ ቀለም ፤ የደም ፡ ዐይነት ። ዘሚረቱ ፡ ሕብረ ፡ ያክንት ። ወእምሕብረ ፡ ያክንት ፡ ወሜላት ፡ (ዘፀ፳፭ ፡ ፬ ። ፳፯ ፡ ፩) ።

**የካቲት ፤ (ከቲት ፡ ከተ ፤ ከተተ)** ፤ በቁሙ ፤ የወር ፡ ስም ፤ ፮ኛ ፡ ወር ፡ ከመስከረም ። የመከር ፡ ማፍ ፡ መከተቻ ፤ የበልግ ፡ መባቻ ፡ ማለት ፡ ነው ፤ ከተተን ፡ እይ ። አመ ፡ ዐሡሩ ፡ ወሰዱሱ ፡ ለየካቲት ፡ በዘወህበ ፡ ኪዳነ ፡ ምሕረት ፡ (መቅ ፡ ታም) ።

**ዮም ፤—ዛሬ ፤—የውም ።**

**የመመ ፤ (ትግ ፡ ሐበ)** ፤ መላ ፡ ፈጸመ ፡ ቈረጠ ፡ ገደበ ። ዘሩ ፡ ሚመየ ፡ ነው ።

(ጥ) **ያም ፤ (ዕብ)** ፤ ባሕር ፡ ሥሬ ፤ ዐዘቅት ፡ ምንጭ ፤ ጕድጓድ ፤ ታላቅ ፡ የውሃ ፡ ዕቃ ። ምዕራብ ፤ የፀሓይ ፡ መግቢያ ፡ መጥለቂያ ። ባሕርንና ፡ ማርያምን ፡ እይ ።

**ዬም** ፤ ማዎት ፤ ማየ ፡ ሕይወት ፡ ፍል ፡ ውሃ ።

**የሚን ፤ ኖት ፤ (የመነ ፡ ይየምን ፡ ይይምን ። ዕብ ፡ ያሚን ፤ ዐዲመ)** ፤ መቅናት ፤ ቅን ፡ ቀኝ ፡ መኾን ፤ መጽናት ፡ መበርደድ ፤ መብዛት ፡ መፈድፈድ ፤ መክበር ፡ መወደድ ፤ በቀኝ ፡ መቀመጥ ፡ ወደ ፡ ቀኝ ፡ መኼድ ።

**ይሙን ፤ (ናን ፡ ናት ፡ ምንት)** ፤ የማናይ ፤ የቀና ፡ የጠና ፤ ብርቱ ፡ በርዳዳ ።

**ይሙኒ ፤ (ንኢ ፡ አግ)** ፤ እጅግ ፡ በጅግ ፤ ብዙ ፡ በብዙ ፤ አካቶ ፤ ፈጽሞ ፤ ጭራሽ ። እስመ ፡ አኅበርዎሙ ፡ ይሙኒ ። አበስኩ ፡ ይሙኒ ። ይከብደኒ ፡ ይሙኒ ። ብዙኅ ፡ ይሙኒ ፡ (፩ዜና ፡ ፲፱ ፡ ፩ ። ፳፩ ፡ ፰ ፡ ፲፫ ። ፪ዜና ፡ ፱ ፡ ፱) ። አንዳንድ ፡ መጻሕፍት ፡ በይሙኒ ፡ ፈንታ ፡ እሙኒ ፡ ይላሉ ፤ የጣፊ ፡ ስሕተት ፡ ነው ።

**የማን** ፤ (ዕብ፡ ያሚን ። ሱር፡ ያሚና ። ዐረ፡ የሚን) ፤ ቀኝ ፤ የቀኝ፡ እጅ ፤ የቀኝ፡ ጐን፡ ማእዝን ፤ ደቡብ ፤ የግራ፡ ትይዩ፡ የስሜን፡ አንጻር ። ዘትገብር፡ የማንከ፡ ኢታእምር፡ ፀጋምከ ። ልቡ፡ ለጠቢብ፡ ውስተ፡ የማኑ ። ተፈለጥ፡ የማነ፡ አው፡ ፀጋመ ። መንገለ፡ የማነ፡ ምሥዋዕ፡ (ማቴ፳፭፡ ፴፫ ። መክ፲፡ ፪ ። ዘፍ፲፫፡ ፱ ። ሉቃ፡ ፩፡ ፲፩) ። ኀይል፡ ጽንዕ፡ ብዛት፡ እጅግነት ።

**ይምን** ፤ ዝኒ፡ ከማሁ ፤ ቀኝ፡ የቀኝ፡ ክፍል፡ ወገን ፤ በስተቀኝ፡ ያለ፡ ዐቃ፡ ማእዝን ፤ እጅ፡ ሐዋስ ። ኀበ፡ ይምነ፡ ሐመር ። ዘይምኖሙ ። እንዘ፡ ይሰርር፡ ይምነ፡ ወፀግመ ። ይምና፡ ለበድነ፡ ሥጋሁ ። ነዲፍ፡ በይምን፡ ወበፀግም፡ (ዮሐ፳፩፡ ፮ ። ዘካ፲፪፡ ፮ ። ቀሌ ። ስንክ፡ ጥቅ፮ ። ፩ዜና፡ ፲፪፡ ፪) ።

**የማናዊ** ፤ (ዊ ፤ ይ) ፤ የቀኝ ፤ በቀኝ፡ ያለ፡ ቅን ፤ ቀኛም፡ ባለቀኝ ፤ ቀኝ፡ አዝማች ፤ ቀኝ፡ ጌታ፡ በቀኝ፡ የሚቆም ። የማናዌ፡ ፍኖት ። ዐይኑ፡ የማናይ ። ነደፎ፡ የማና(ዌ)የ፡ ገቦሁ ። የማና(ዊ)ይ፡ ወፀጋማይ ። እለ፡ ክልኤሆን፡ ኢደዊሆሙ፡ የማናይ(ው)ያን፡ (ስንክ፡ ታኅ፭ ። ኪዳ ። ስንክ፡ ነሐ፲፮ ። ቀሌ ። መሳ፳፡ ፲፮) ።

**አይመነ** ፤ አቀና ፤ ቀኝ፡ አደረገ ፤ ወደ፡ ቀኝ፡ መራ፡ አስተማረ ። ሀይመኑንና፡ አእመኑን፡ እይ ፤ የዚህ፡ አግዋር፡ ናቸው ።

**የመን** ፤ (ዕብ፡ ቴማን) ፤ ስመ፡ ሀገር ፤ የምድረ፡ እስራኤል፡ ደቡብ ፤ ምድረ፡ ዐረብ ።

**ይንዋርዮስ** ፤ (ሮማይ፡ ዥንዋሪዉስ) ፤ ስመ፡ ወርኅ ፤ ጥር፡ የኤውሮፖች፡ መዠመሪያ፡ ወር ። ዘይንዋርዮስ፡ (ተረ፡ ቄር፳፩) ።

**ያፌስ** ፤ (ዕብ፡ ኤፌስ) ፤ ባዶ፡ ደካማ፡ ልምሾ ። ባለብሉዮች፡ ግን፡ ፋስ፡ ምማር፡ ይሉታል ። ዕብራይስጡ ፤ ውብኤፌስ፡ ያድ፡ ይሻቤር፡ ያለውን፡ ወበድከምት፡ እድ ፤ ወይም፡ ዕብስት ፤ ዕውስት፡ ዘእንበለ፡ ኀይል፡ በማለት፡ ፈንታ ፤ ወበያፌስ፡ ይቀጠቅጥ፡ እደ፡ ይላል ፤ አንዳንዱም፡ መጣፍ፡ ዘእንበለ፡ እድ፡ ይላል፡ (ዳን፰፡ ፳፭) ።

**ዮቅጣን** ፤—የሰው፡ ስም ፤—ቀጠነ ።

**ያቁም** ፤—የዐምድ፡ ስም ፤—ቀዊም፡ ቆመ፡ አቀመ ።

**ያርብሕ** ፤—ዐርበኛ ፤—ረብሐ ።

**ያሬድ** ፤ (ዕብራ) ፤ የሰው፡ ስም ፤ ፮ኛው፡ ትውልድ፡ የሔኖክ፡ አባት ። ወሪድ፡ ርደት፡ ማለት፡ ነው ፤ በርሱ፡ ዘመን ፤ የደቂቀ፡ ሴት፡ ከደቂቀ፡ ቃየል፡ መጋባትና፡ መዋለድ ፤ ከደብር፡ ቅዱስ፡ ወደ፡ ምድረ፡ ፋውድ፡ መውረድ፡ ተዠምሯል ። የወረዱበትም፡ ምክንያት፡ አዋልደ፡ ቃየል፡ እንደ፡ የጁ፡ አርኽ፡ ስለ፡ ኾኑ፡ በመልካቸው፡ ውበት፡ በድምፃቸውና፡ በዘፈናቸው፡ ጣዕም፡ ተመሥጠው፡ ነው ። ወሰደት፡ ሎቱ፡ ዲና፡ ወልደ ፤ ወጸውዐ፡ ስሞ፡ ያሬድሀ ፤ እስመ፡ በመዋዕሊሁ፡ ወረዱ፡ መላእክቲ፡ እግዚ፡ ውስተ፡ ምድር፡ እለ፡ ተሰምዩ፡ ትጉሃነ ። በእማንቱ፡ መዋዕል፡ ተወልደ፡ ሎሙ፡ አዋልድ፡ ሠናያት፡ ወልሑያት ፤ ወርእዩ፡ ኪያሆን፡ መላእክት፡ ውሉደ፡ ሰማያት፡ ወፈተውዎን ፤ ወይቤሉ፡ በበይናቲሆሙ ፤ ንዑ፡ ንኅረይ፡ ለነ፡ አንስቲ፡ እምውሉደ፡ ሰብእ ፤ ወንለድ፡ ለነ፡ ውሉደ፡ (ኩፋ፡ ፬ ። ሔኖ፡ ፮ ። ዘፍ፮፡ ፩፡ ፪) ። በኢትዮጵያም፡ በሳድሳይ፡ ምእት፡ (ሴክል)፡ ተነሥቶ፡ ፩ቱን፡ ጸዋትወ፡ ዜማ፡ የደረሰ፡ የድጓና፡ የማሕሌት፡ አባት ፤ አሮድዮን፡ እንደሚባለው፡ ወፍ፡ ዜማው፡ ልብ፡ የሚመሥጥ፡ እጅግ፡ ድምፀ፡ መልካም፡ ስለ፡ ኾነ ፤ ሰውዮው፡ ያሬድ፡ ወፉም፡ ያፈ፡ ያሬድ፡ ተብሏል ፤ ምስክሩን፡ በአሮድዮን፡ ፍች፡ ተመልከት ። አእመርነኒ፡ ከመ፡ ሀሎ፡ በቀራንዮ፡ ገነት ፤ ያሬድ፡ ዘወለዶ፡ ሔኖክ፡ ማሕሌት፡ (ጕንግማዊ፡ ቅኔ) ።

**ዮርዳኖስ** ፤ (ጽር፡ ዮርዳን ። ዕብ፡ ያርዴን ። ሱር፡ ያርድና) ፤ ስመ፡ ፈለግ ፤ የከነዓን፡ ወንዝ ፤ ታላቅ፡ ዠማ ፤ ከምድረ፡ እስራኤል፡ ዳርቻ፡ ከነገደ፡ ዳን፡ ክፍል፡ እንደ፡ የወልና፡ እንደ፡ ዳሽን፡ ካለው፡ ደብረ፡ ሔርሞን፡ ከሚባለው፡ ከደቡብ፡ ወገን፡ ከተራራው፡ እግር፡ ከሔርሞን፡ ሥር፡ ተነሥቶ፡ ወደ፡ ደቡብ፡ ወደ፡ ባሕረ፡ ጨው፡ የሚፈስ ። ዮር ፤ ወራጅ፡ ፈሳሽ ። ዳን ፤ ደየን፡ ዳኘ፡ ፈረደ ፤ በተገናኝ፡ ፈለገ፡ ዳን፡ ማለት፡ ነው ፤ በዳኖስ፡ ዘይቤ፡ ሲፈቱት፡ ግን፡ ዳናዊ፡ ፈለግ ፤ ወይም፡ በጠቅላላው፡ ዮርዳናዊ፡ ያሰኛል፡ (ኢያ፫፡ ፰) ። ዳን፡ የውነተኛው፡ ዳኛ ፤ የውነተኛው፡ መጥምቅ፡ የመሲሕ፡ ምሳሌ፡ ጸዋሬ፡ ስሙ፡ ስለ፡ ኾነ ፤ የዮርዳኖስ፡ ነቅ፡ ሥሉስ፡ ቅዱስ፡ ምንጩ፡ አውራጁውና፡ ቀበሌው፡ ገና፡ ነገደ፡ ዳን፡ ሳይወርሱት፡ ከሙሴና፡ ከአብርሃም፡ በፊት፡ አስቀድሞ፡ ባምላካዊ፡ ትንቢት፡ ዳን፡ ተብሏል ። ወሐዊርየ፡ ነበርኩ፡ ዲበ፡ ማያተ፡ ዳን፡ በዳን ፤ እንተ፡ ይእቲ፡ እምየማነ፡ ዐረበ፡ ሔርሞን ። ተለዎሙ፡ እስከ፡ ዳን ። ወአርአዮ፡ ኵሎ፡ ምድረ፡ ገለዓድ፡ እስከ፡ ዳን፡ (ሔኖ፡ ፲፫ ። ዘፍ፲፬፡ ፲፬ ። ዘዳ፴፬፡ ፩) ። ትርጓሜ፡ ወንጌልም፡ ዘአምነ፡ ወዘተጠምቀ፡ ይድኅን ፤ ወዘሰ፡ ኢአምነ፡ ይደየን፡ ያለውን፡ ሲፈታ ፤ ዳንን፡ ደያኒ፡ ደያን፡ መደይን፡ ብሎ፡ ዮርዳኖስን፡ ፈለገ፡ ደይን፡ ይላል ፤ ፍርዱን፡ እንደ፡ ውሃው፡ ከሰደምና፡ ከገሞራ፡ ከባሕረ፡ ጨው፡ ጋራ፡ ለማያያዝ፡ (ማር፲፮፡ ፲፮ ። ማቴ፲፩፡ ፳፫፡ ፳፬) ። የዮርዳኖስ፡ ራስ፡ ነቁና፡ ስሙ፡ በሦላሴ፡ አምሳል፡ ሦስት፡ ነው ፤ ያውም፡ አብ፡ ወልድ፡ መንፈስ፡ እንደ፡ ማለት፡ ሐስባኒ ፤ ተለልጋዲ ፤ ቫንያሲ፡ ይባላል ። ጣዕሙና፡ ሕብሩም፡ እንደ፡ ስሙ፡ ልዩ፡ ልዩ፡ ነው ፤ መጠኑም፡ በላይና፡ በታች፡ ትክክል፡ ነው ፤ ርሕቀቱም፡ ካንዱ፡ ነቅ፡ እስካንዱ፡ ሩብ፡ ሩብ፡ ሰዓት፡ ያስኬዳል ፤ ወደ፡ ታች፡ ደግሞ፡ መካከለኛው፡ በቀጥታ፡ ግራና፡ ቀኙ፡ በማስየፍ ፤ ኹሉም፡ በየፊቱ፡ አንዳንድ፡ ሩብ፡ ወይም፡ እኩል፡ ሰዓት፡ ብቻ፡ ብቻውን፡ ይወርድና፡ ሦስቱ፡ ነቅዐ፡ ማይ፡ ካንድ፡ ቦታ፡ ላይ፡ ይገናኛል ። ከተገናኘም፡ በኋላ፡ ፩፡ ወንዝ፡ በመ

ኾን፡ ወደ፡ ታች፡ ፩፡ ሰዓት፡ ወርዶ፤ ማየ፡ ሜሮም፡ ወይም፡ ባሕረ፡ ሖሊ፡ ከሚሏት፡ ከታናሽቱ፡ ሐይቅ፡ ይገባና፡ ርቧን፡ እንደ፡ መርከብ፡ ማኽል፡ ለማኽል፡ ሠንጥቆ፡ ዐልፎ፤ ከርሷ፡ በታች፡ ደግሞ፡ ፪፡ ሰዓት፡ ጐርፎ፡ ኪኔሬትና፡ ጌንሴሬጥ፡ ባሕረ፡ ገሊላ፡ ወይም፡ ጥብርያደስ፡ ከሚባለው፡ ከታላቁ፡ ሐይቅ፡ ይገባል። ጥብርያደስንም፤ አባይ፡ በጣና፡ ላይ፡ እንደሚያልፈው፡ ማኽል፡ ለማኽል፡ ሠንጥቆ፡ ዐልፎ፤ ከግራና፡ ከቀኝ፡ ብዙ፡ አፍላጋት፡ እየጨመረ፤ ሮቤልን፡ ጋድን፡ መንፈቀ፡ ምናሴን፡ ወደ፡ ግራ፤ የቀሩትን፡ ነገድ፡ ወደ፡ ቀኝ፡ ትቶ፤ ማኽል፡ ለማኽል፡ አቅንቶ፡ የሦስት፡ ቀን፡ ጐዳና፡ ተጐትቶ፡ ከባሕረ፡ ጨው፡ አፍ፡ ይገባና፡ ተውጦና፡ ሰምጦ፡ ይቀራል፤ የባሕረ፡ ጨው፡ ዙሪያ፡ ተራራና፡ ገደል፡ የቈላ፡ ቈላ፡ መቀራቅርት፡ መትሕተ፡ ታሕቲት፡ ብለ፡ ኾኖ፡ ከዚያ፡ ሲወጣ፡ አይታይም። የጥምቀትን፡ ውሃ፡ የንዋየ፡ ቅድሳትን፡ ዕጣቢ፡ የተቀደሰን፡ ፈሳሽ፡ ነገር፡ ኹሉ፡ ከመሬት፡ መቅበር፡ የትም፡ አለማፍሰስ፡ የዚህ፡ ምሳሌ፡ ነው፡ ይባላል። ቀድሞ፡ በኢያሱ፡ እስራኤል፡ የተሻገሩበት፡ ኋላም፡ በዮሐንስ፡ ጌታችን፡ የተጠመቀበት፡ ወደቡ፡ ፩፡ ነው፤ ከዚያ፡ በታች፡ እስከ፡ ባሕረ፡ ጨው፡ እኩል፡ ሰዓት፡ ወይም፡ ፫፡ ሩብ፡ ያስኬዳል። «ጌታም፡ በዚህ፡ ወደብ፡ በዮርዳኖስ፡ እግር፡ መጠመቁ፡ ስለ፡ ሦስት፡ ነገር፡ ነው፡ ይባላል። ፩ኛው፤ ግራዝማች፡ ዲያብሎስ፡ ያዳምን፡ ዘር፡ ኹሉ፡ የላሜ፡ ልጅ፡ ያውራዬ፡ ውላጅ፡ ለማለት፡ አዳም፡ ገብሩ፡ ሔዋን፡ አመቱ፡ ብሎ፡ በደንጊያ፡ የጣፈው፡ ደብዳቤ፡ ከዚያ፡ ነበረና፤ ያንን፡ ለማጥፋት፡ ለመደምሰስ። ፪ኛው፤ ጥምቀት፡ የሞቱ፡ አርኣያ፡ የመቃብሩ፡ አምሳል፡ ነውና፤ ከኃጥኣን፡ ጋራ፡ ተቈጥሮ፡ እንዲጠመቅና፡ እንዲሰቀል፡ የተጣፈውን፡ ቃል፡ ንስሐና፡ ጥምቀት፡ የሚሻ፡ ፍጹም፡ ኃጥእ፡ መስሎ፡ በዮሐንስ፡ እጅ፡ ለመፈጸምና፡ ከላይ፡ በዮርዳኖስ፡ ነቅ፡ የተከተተውን፡ የጥምቀት፡ ቀሚስ፡ ሽልማትና፡ ጌጥ፡ ምስጢረ፡ ሥላሴን፡ ለመግለጥ። ፫ኛው፤ የአዳም፡ ኀጢአት፡ ከናት፡ የፈሰሰ፡ እስከ፡ እግር፡ ድረስ፡ እንደሚሉት፡ እንደ፡ ታላቅ፡ ወንዝ፡ ነውና፤ እስራኤል፡ ዘሥጋ፡ ከፈርዖን፡ ባርነት፡ ወጥተው፡ ዮርዳኖስን፡ በዚህ፡ ወደብ፡ ዐልፈው፡ ተሻግረው፡ ምድረ፡ ከነዓን፡ እንደ፡ ገቡ፤ እስራኤል፡ ዘነፍስም፡ ከሰይጣን፡ ባርነት፡ ወጥተው፡ ያዳምን፡ ኀጢአት፡ በርሱ፡ ጥምቀትና፡ በኵርነት፤ በጽድቁና፡ በትሩፋቱ፡ በሕማሙና፡ በሞቱ፡ ዐልፈው፡ ተሻግረው፡ ወደ፡ ሰማያዊት፡ ከነዓን፡ እንዲገቡ፡ መጠን፤ መግባታቸውን፡ ለመስበክ፡ ነው»፡ (ሉቃ፬፡ ፲፮—፳። ፳፬—፳፯። ፩ነገ፡ ፳፡ ፲፱)።

**እምአፍላግሂ፡ ወአብሕርት፡ እንዘ፡ ይእቲ፡ ነኣስ፤ ኢይትከሀል፡ በበ፡ ገጹ፡ ነጊረ፡ ዕበያ፡ ለዮርዳኖስ፤ አምጣነ፡ ዳግማይ፡ አዳም፡ መልክአ፡ ዚኣሃ፡ ክርስቶስ፤ ወከመ፡ ትኩኖ፡ ብእሲተ፡ አልሀቃ፡ መንፈስ፡ ቅዱስ፡ (ቅኔ)።**

**የሱስ፤—መድኅን፤—ኢየሱስ።**

**ዮቶር፤ (ዕብ፡ ዬቴር፤ ይትሮ)፤** የሰው፡ ስም፤ የሙሴ፡ ዐማት። ተረፍ፡ ትራፊ፡ ቅሬታ፤ ወይም፡ ከቍጥር፡ ያልገባ፡ ጭማሪ፡ ማለት፡ ነው፤ ትርፌ፡ እንደ፡ ማለት፡ (ዘፀ፫፡ ፩። ፬፡ ፲፰)።

# ከ

**ከ፤** ፲፩ኛ፡ ፊደል፡ በግእዝ፡ አልፍ፡ ቤት፡ በአበገደ፤ ስሙ፡ ካፍ፡ ቍጥሩ፡ ካያ፤ አኃዝ፡ ሲኾን፡ ከ፡ ፅሥራ፡ ይባላል፤ ካያ፡ ኻያ፤ ወይም፡ ኹለት፡ ዐሥር፡ ማለት፡ ነው፤ ከዕበተ፡ የ፡ እንደ፡ ማለት።

**ከ፤ (ኩ፡ ኪ፡ ክሙ፡ ክን)፤** የአካል፡ ዝርዝር፤ ጠቃሽና፡ አስሚ፤ ወይም፡ ምእላድ። አንተ፡ አንቲ፡ አንትሙ፡ አንትን፡ የሚባሉትን፡ የቅርብ፡ የቅርቦቹን፡ ወንዶችና፡ ሴቶች፡ ፭ቱን፡ ሰራዊት፤ ነበብከ፡ ኩ፡ ኪ፡ ክሙ፡ ክን፡ እያለ፡ ዘርዝሮና፡ ጠቅሶ፡ ለይቶ፡ ያሳያል። አን፡ ለሚለው፡ ግን፡ ከቀዳማይ፡ በቀር፡ በዝርዝር፡ ኹሉ፡ አይገባም፤ ኩ፡ የነበረውን፡ የ፡ ይወርሰዋል፤ ነበብኩ፡ ንባብየ።

**ኬ፤ (አ—መ—ሰ)፤** የአንክሮና፡ የአጋኖ፡ የአብተብቍዖ፡ ቃል፤ በመጨረሻ፡ ቃል፡ እየገባ፡ መድረሻውን፡ ራብዕ፡ በማድረግ፡ ቃል፡ ያገነታል፤ እኮ፡ እንኳን፡ ይኾናል። ብዙ፡ ጊዜም፡ ትርጓሜና፡ ፍች፡ ሳይፈልግ፡ እንደ፡ ከመ፡ አዳማቂና፡ የንባብ፡ ጌጥ፡ ኹኖ፡ ይቀራል። ምንትኬ፡ ሰብእ፡ ዘይጸንሖ፡ እሳት። ምንትኬ፡ ዘአሜሃ፡ ዐውያት፡ (አንክሮ)። ንግባእኬ፡ ኀበ፡ ጥ፡ ነ። ውእቱኬ። አንትሙኬ። ዝኬ፡ ውእቱ፤ ዝኬ፡ እፎ፤ ይህ፡ ነዋ፤ ይህሳ፡ (አጋኖ)። ወይንኬ፡ አልቦሙ፤ የላቸውም፡ እኮ፡ (ምልጃ)። ርእዩ፡ እመ፡ ይዌልጡ፡ አሕዛብ፡ አማልክቲሆሙ፤ እንዘኬ፡ ኢኮኑ፡ አማልክተ፤ እንኳን፡ (ኤር፪፡ ፲፩)። አንዳንድ፡ ጊዜም፡ በዋዌ፡ ፈንታ፤ ኵሉኬ፡ ዕፀ፡ ዘኢይፈሪ። ዝኬ፡ ፈትሐ፡ አሐተ፡ እምላ። ኦሪትሰኬ፡ እያለ፡ አለቦታው፡ ገብቶ፡ ይገኛል። አንዳንድ፡ ጊዜም፡ ማ፡ ይኾናል፤ ይኸውም፡ በነባርና፡ በትእዛዝ፡ አንቀጽ፡ ሲገባ፡ ነው። ነዐኬ፡ በልኬ፤ ናማ፡ በልማ፡ (ዕር፳፡ ቍ፲፱)።

**ከእብ፤**—ኹለተኛ፤—ክዒብ፡ ከዐበ ።
**ከአወ፤**—አፈሰሰ፤—ክዒው፡ ከዐወ ።
**ኵኢስ፤**—ታላቅ ፡ ግንበ ፤—ኵዒስ ፡ ኰዐሰ ።
**ከበ፤**—ኵበት ፤—ከበወ ።
**ከቢብ ፤ ቦት ፤** (ከበበ ፡ ይከብብ ፡ ይክብብ ። ዐረ ፡ ከበ ። ሱር ፡ ከባበ) ፤ መክበብ ፡ ማጠር ፤ መሾም ፡ ማክበር ፤ መጥራት ፡ ማደም ፤ መሰብሰብ ፡ ማከብ ፤ በዓል ፡ ሰርግ ፡ ጉባኤ ፡ ማድረግ ። ከመ ፡ ይቁሙ ፡ ከቢቦሙ ፡ እሳተ ፡ ከመ ፡ አረፍት ። ርእየት ፡ ለዳዊት ፡ ምስለ ፡ ሡሉሙ ፡ ማኅበረ ፡ ነቢያት ፡ ወነፍሳተ ፡ ጻድቃን ፡ ከቢቦሙ ፡ ከመ ፡ አረፍት ። ሐዋርያቲሁ ፡ ከበበ ፤ እግረ ፡ አርዳኢሁ ፡ ኀፀበ ፡ (ገድ ፡ ተክ ። ስንክ ፡ የካ ፲፯ ። ድጓ) ። ማኮብ ፡ ማኳስ ፡ መጠምጠም ፤ የፈትል ። ማንከብከብ ፡ ማንከብለል ፤ ከብ ፡ እንክብል ፡ ማድረግ ፤ የርጥብ ፡ ነገር ፡ የመድኀኒት ።

**ከባቢ ፤** በቁሙ ፤ የሚከብ ፤ ሰብሳቢ ።

**አክበበ ፤** አስከበበ ፤ ጉባኤ ፡ አስደረገ ።

**መክብብ ፤** (ብት ፡ ብን ፡ ብት) ፤ የሚከብ ፡ የሚያስከብብ ፤ ከባቢ ፡ አስከባቢ ፤ ሹም ፡ አለቃ ፡ ሰብሳቢ ። ኵን ፡ መክብበ ፡ አሕዛብ ። በመክብበ ፡ ማኅበሮሙ ፡ ለቅዱሳን ፡ (ኵፉ ፡ ፳፯ ። አርጋ ፡ ፱) ።

—፤ የቍጥር ፡ ድምር ፤ ጅምላ ፡ ጠቅላላ ፡ ቍጥር ። በመንቶ ፡ እልፍ ፡ ወሰብዓ ፡ ምእት ፡ ከነ ፡ መክብበ ፡ ኵሎሙ ። ወከነ ፡ መክብበ ፡ አዳብዒሁ ፡ ዕሥራ ፡ ወአርባዕቱ ፡ (፩ዜና ፡ ፯ ፡ ፩ ። ፳ ፡ ፯) ። ዘመን ፡ መዋዕል ፡ በማለት ፡ ፈንታ ፡ መክብብ ፡ ይላል ፤ ስሕተት ፡ ነው ። ወከነ ፡ መክብበ ፡ ንግሡ ፡ ለዳዊት ፡ አርብዓ ፡ ዓመተ ፡ (፩ዜና ፡ ፳፱ ፡ ፳፯) ።

—፤ ኵሉ ፡ ኵለንታ ፤ መላው ። መክብበ ፡ ሥጋ ። መክብበ ፡ መጻሕፍት ፡ ዘብሉይ ፡ (ፊልክ ፡ ፲፱ ። መጽ ፡ ምስ) ።

—፤ መጨረሻ ፡ መደምደሚያ ፤ ጕልላት ። ዮሐንስ ፡ መክብበ ፡ ነቢያት ። ጴጥሮስ ፡ መክብበ ፡ ለስምዐ ፡ ሃይማኖት ፡ (አዋል ። ስንክ ፡ የካ፩) ።

—፤ ወገን ፡ ዐይነት ። እብነ ፡ ሶም ፡ በበ ፡ መክብቡ ፡ (፩ዜና ፡ ፳፱ ፡ ፪) ።

—፤ የመጽሐፍ ፡ ስም ፤ ከመጻሕፍተ ፡ ሰሎሞን ፡ አንዱ ። ርሱው ፡ ራሱ ፡ ሰሎሞን ፤ ሰባኪ ፡ መምህር ፡ መገሥጽ ፡ ማለት ፡ ነው ፤ ቈህልትን ፡ እይ ። ቃለ ፡ መክብብ ፡ ወልደ ፡ ዳዊት ፡ (መክ፩ ፡ ፩ ፡ ፲፪ ። ፯ ፡ ፳፰ ። ፲፪ ፡ ፰ ፡ ፱) ።

**ተከበ ፤** ተከበበ ፤ ተሰበሰበ ፤ ተኮበ ፡ ተኳሰ ፤ ተንከበከበ ፡ ከብ ፡ እንክብል ፡ ኾነ ።

**ከቡብ ፤** (ብን ፡ ብት ፡ ብብት) ፤ የተከበበ ፤ ክብ ፡ እንክብል ፤ ድንብልብል ። እስመ ፡ ምድር ፡ ክቡብ ፡ ከመ ፡ ኩራ ። ከመ ፡ ዐይነ ፡ ማኅተም ፡ ክቡብ ። እእባን ፡ ክቡባት ፡ ወልሙጻት ፡ (አዋል ። ተረ ፡ ቈርጾ) ። በክቡባት ፡ ፈንታ ፡ ክበብት ፡ ይላል ፤ ስሕተት ፡ ነው ፡ (ጊ ፡ ወ ፡ ሐ ፡ ገ፲፱ ። ሄርማ ፡ ገ፲፫ ። ፹፩) ።

**ክበብ ፤** (ባት) ፤ በቁሙ ፤ ዘውድ ፡ ዙፋያ ፤ ክብነት ። ይቁሙ ፡ ካህናት ፡ ክበቡ ፡ ለምሥዋዕ ። ክበቡ ፡ ከመ ፡ ፀሓይ ፡ (ግንዘ ። ሔኖ፲፱ ፡ ፲፰) ።

—፤ ኩብ ፤ ኳስ ። ክበበ ፡ አፍትልት ፡ (ታሪ ፡ አኵ) ።

—፤ ክበብ ፡ ያለው ፡ ገንዘብ ፡ ብር ፤ የገንዘብ ፡ ቍጥር ። የሐሰብ ፡ ሎቱ ፡ ካህን ፡ ክበበ ፡ ሤጡ ፡ (ዘሌ፳፯ ፡ ፳፫) ። በክበብ ፡ ፈንታ ፡ መክብብ ፡ ይላል ፡ (፩ዜና ፡ ፳ ፡ ፯) ።

**ከብከበ ፤** (ተቀ ፡ ግ) ፤ አኰበኰበ ፤ ኵብ ፤ ኵብ ፡ አለ ፤ ያካኼድ ፡ የዘፈን ፤ የዝላይ ፡ (ትግሬ) ። ኵብ ኵብ ፡ ማለት ፡ ከዚህ ፡ ወጥቷል ። ከበከበ ፤ ተከባከበ ፡ አከበረ ፡ (ዐማርኛ) ።

**ከብካብ ፤** ሰርግ ፤ የመርዓዊና ፡ የመርዓት ፡ ጉባኤ ፤ የዘፈን ፡ የደስታ ፡ በዓል ፡ (ዮሐ፪ ፡ ፩ ። ሉቃ፲፬ ፡ ፴፯ ። ማቴ፳፪ ፡ ፪) ። ገብረ ፡ ከብካበ ። መዋዕለ ፡ ከብካብ ። አመ ፡ ከብካብ ። በከመ ፡ መርዓዊ ፡ ይትፌሣሕ ፡ በውስተ ፡ ከብካቡ ፡ (ዘፍ፳፱ ፡ ፳፪ ። አስቴ፱ ፡ ፳፪ ። ጦቢ፯ ፡ ፲፱ ። ቀሌ) ።

**አንከብከበ ፤** አንከበከበ ፤ ተንከበከበ ፤ የፍትፍት ፡ (ዐማርኛ) ።

**ከቢድ ፤ ዶት ፤** (ከብደ ፡ ይከብድ ፡ ይክበድ ። ዕብ ፡ ካቤድ) ፤ መክበድ ፡ መመንዘል ፤ መብለጥ ፡ መብዛት ፤ በሚዛን ፡ በቍጥር ። ምንት ፡ ይከብድ ፡ እምነ ፡ ዐረር ። ይከብድ ፡ እምኆጻ ፡ ባሕር ፡ (ሢራ፳፪ ፡ ፲፬ ። ኢዮ፮ ፡ ፫) ።

—፤ መጥናት ፤ መበርታት ፤ ማየል ። ክብደ ፡ ልቡ ፡ ለፈርዖን ። ወከብደ ፡ ቀትል ፡ ዲበ ፡ ሳኦል ። ክብደ ፡ ደዌሁ ፡ (ዘፀ፯ ፡ ፲፬ ። ፩ዜና ፡ ፲ ፡ ፫ ። ፫ነገ ፡ ፲፯ ፡ ፲፯) ።

**ክቡድ ፤** (ዳን ፡ ዳት ፡ ብድ) ፤ በቁሙ ፤ የከበደ ፡ ከባድ ፤ ጥኑ ፡ ብርቱ ፤ ክቡር ፡ ታላቅ ፤ ዐያሌ ፡ እጅግ ፡ ብዙ ። ነገሩ ፡ ለአብድ ፡ ከመ ፡ ጾር ፡ ክቡድ ። ሕማም ፡ ክቡድ ። ብዓው ፡ ክቡድ ። ብእሲ ፡ ክቡድ ። ተአምሪሁ ፡ ክቡድ ፡ (ሢራ፳፩ ፡ ፲፮ ። ፀ፱ ፡ ፪ ። መጽ ፡ ምስ ። ፩ነገ ፡ ፱ ፡ ፲፰ ። ስንክ ፡ ኀሐ፲፱) ።

**ክብደ ፡ ሒረት ፤** ዳተኛ ፡ ዝግተኛ ፤ ቀርፋፋ ፡ (ግብ፳፯ ፡ ፯) ።

**ክቡደ ፡ መዝራዕት ፤** ጡንቻም ፡ እጀ ፡ ወፍራም ፤ ክንደ ፡ በርዳዳ ።

**ክቡዳነ ፡ አቅርንት ፤** ቀንዳሞች ፤ ቀንደ ፡ ትልልቆች ፡ (መዝ ፡ ፵፱) ።

**ክቡዳነ ፡ ጾር ፤** ሸክም ፡ የከበዳቸው ፤ ሐማሎች ።

**ክበድ ፤** (ዳት) ፤ መክበድ ፤ አከባበድ ፡ ክብደት ፤ ከባድነት ፤ ብዛት ። ክበደ ፡ ጾርነ ፡ አቅልል ። ክበዱ ፡ ለጸባሕት ። ክበደ ፡ ንዋም ። ክበደ ፡ ቅኔ ። ክበዳ ፡ ለስብሐቲክሙ ። አልቦ ፡ ዘይክል ፡ ጸዊረ ፡ ክበ

ደሙ ፡ ኢአድባር ፡ ወኢአውግር ፡ ወኢቈላት ፡ (መዋሥ ። ስንክ ፡ የካ፳ ። ቅዳ ፡ ያዕ ። ፪ዜና ፡ ፲ ፡ ፱ ። ስንክ ፡ ግን፪ ። ዮዲ፯ ፡ ፱) ። ሸክም ፤ ሐሳብ ፡ ሐዘን ፡ ከባድ ፡ ነገር ። ኢይወዲ ፡ ላዕሌክሙ ፡ ክበደ ። ለምንት ፡ ይከውን ፡ ገብርከ ፡ ክበደ ፡ ላዕለ ፡ እግዚእየ ። ግድፍ ፡ እምላዕሌከ ፡ ክበደ ፡ ዕጓለ ፡ መሕየው ። ከመ ፡ ያቅልል ፡ እምኔሁ ፡ ክበዳተ ፡ (ሉቃ፪ ፡ ፳፱ ። ፪ነገ ፡ ፲፱ ፡ ፴፭ ። ሱቱ ፡ ዕዝ፲፱ ፡ ፲፪ ። ፊልክ ፡ ፻፳፭ ። ዕብ፲፪ ፡ ፩) ።

—፤ ቤት ፡ ግንብ ፤ በቤት ፡ ያለ ፡ ገንዘብ ፤ ብዙ ፡ ብዕል ፡ ክብር ፡ ወርቅ ፡ ብር ፤ ሰባራ ፡ ሥንጥር ፤ ደጃፍ ፡ የመለሰው ፡ ማጀት ፡ የጕረሠው ፡ የቤት ፡ ዕቃ ። እግዚ ፡ የአምር ፡ ክበዳቲሃ ። ወትትካፈልዎ ፡ ለክበዲሃ ። ማኅፈደ ፡ ክበዲከ ። አስጠመ ፡ ሥሎ ፡ ክበዲሃ ፡ (መዝ ፡ ፵፯ ። ፪፳፭ ። ሰቈ፪ ፡ ፮) ። ርጉዝ ፡ ከብት ፤ ላም ፡ ባዝራ ። የሐር ፡ ገመድ ፡ የበቅሎ ፡ ክበድ ፡ እንዲሉ ፡ (ዐማርኛ) ።

**አክበደ** ፤ አከበደ ፤ አስከበደ ፤ አበዛ ፡ አጸና ። አክበድኪ ፡ አርዑተሙ ፡ ፈድፋደ ። በኢያእምሮ ፡ ያከብድ ፡ ነገሮ ። አክበደ ፡ ሙሴ ፡ ተክዞ ፡ ጥቀ ። እለ ፡ ያከብዱ ፡ ዲበ ፡ አግብርቲሆሙ ፡ ቅኔ ፡ እኩየ ። አክበድክሙ ፡ ላዕሌየ ፡ ነገረክሙ ፡ (ኢሳ፵፯ ፡ ፮ ። ኢዮ፴፭ ፡ ፲፮ ። ዘኍ፲፩ ፡ ፲፭ ። ዲድ ፡ ፳፭ ። ሚል፫ ፡ ፲፫) ።

—፤ ጫነ ፡ ጨቈነ ፡ አሸከመ ፤ ምስጢሩ ፡ ያው ፡ ማክበድ ፡ ነው ። ኢታክብድ ፡ ላዕሌሁ ፡ ጾረ ፡ ክቡደ ። ይደሉ ፡ ከመ ፡ ያክብዱ ፡ ቀኖና ፡ ላዕሌሁ ፡ (ቀሌ ። ፈ ፡ መ ፡ ፲፯ ፡ ፱) ። በአክበደ ፡ ፈንታ ፡ አስተከበደ ፡ ይላል ፤ ፍችው ፡ ፩ ፡ ነው ። አስተክብዶ ። ኢያስተክብድ ፡ ላዕሌሆሙ ፡ (ዲድ ፡ ፴፱ ። ፵፩) ።

**አስተካበደ** ፤ አከበደ ፤ አከባበደ ፤ አስተባበለ ፤ የመጥላትና ፡ የመሰቀቅ ። ግስነቱ ፡ ዐጕልና ፡ ሐውልት ፡ ስለ ፡ ኾነ ፡ ፍችው ፡ እንደ ፡ አከበደ ፡ አድራጊ ፡ ነው ። ሰእመ ፡ አስተዐጸበ ፡ ወአስተካበደ ፡ ንስሓሁ ፡ ዘወሀብዎ ፡ ካህናት ፡ (ቀሌ) ። ይቴክዝ ፡ ወያስተካብድ ፡ ፍና ፡ መንሱት ። አስተካበደ ፡ ሐሚመ ፡ (ቄር ፡ ጸላ) ።

**ክብድ** ፤ (ዕብ ፡ ካቤድ ። ሱር ፡ ካብዳ ። ዐረ ፡ ኪብድ) ፤ ጉበት ፤ ከንዋያተ ፡ ውስጥ ፡ አንዱ ፤ የሐሞት ፡ ምንጭ ፡ ዐይነቱ ፡ ዳማ ። ምትሮ ፡ ለዝ ፡ ዓሣ ፡ ወነሣእ ፡ ልቦ ፡ ወክብዶ ፡ ወሐሞቶ ። ሕብረ ፡ ክብድ ፡ (ጦቢ፮ ፡ ፬ ። ዘኍ፬ ፡ ፯) ።

—፤ ሆድ ፡ ማኅደረ ፡ ክብድ ፤ ሸክም ፡ ወይም ፡ ተሸካሚ ፡ ማለት ፡ ነው ። አስከቡኪ ፡ ውስተ ፡ መሬት ፡ በክብድኪ ። ገዚፍ ፡ ዐምድ ፡ ዘአንበሩ ፡ ዲበ ፡ ክብዱ ። በአንተ ፡ ሕማመ ፡ ክብድከ ፡ (ኢሳ፶፩ ፡ ፳፫ ። ስንክ ፡ ጳጕ፩ ። ፩ጢሞ ፡ ፭ ፡ ፳፫) ።

**ከበወ** ፤ (ዕብ ፡ ካባህ) ፤ ጠፋ ፡ ጠለሰ ፤ ፈዘዘ ፤ ዕልም ፡ ድርግም ፡ አለ ፤ የእሳት ፡ የመብራት ፡ የዐይን ።

**ከቦ** ፤ ኵበት ፡ የደረቀ ፡ እበት ፤ ፍሕምና ፡ ብርሃን ፡ የሌለው ። ሐመደ ፡ ከቦ ፡ (ኩፋ ፡ ፳፰) ። ከበተንና ፡ ለከወን ፡ እይ ።

**ከብካብ** ፤—ሰርግ ፤—ከቢብ ፡ ከበበ ፡ ከብከበ ።

**ከበለ** ፤ (ዕብ ፡ ካቤል) ፤ አሰረ ፡ ዘነጀረ ፤ በብረት ። ከንበሎን ፡ እይ ፤ የዚህ ፡ ዘር ፡ ነው ።

**ከበሎ** ፤ (ዕብ ፡ ኬቤል) ፤ ማሰሪያ ፤ የግር ፡ ብረትና ፡ የሰንሰለት ፡ ፍንጅ ፤ የማጥን ፡ ገሮ ፡ ቀለበት ፡ ዙሪያው ፡ ክብ ፡ የኾነ ፡ ምእዙን ፡ ያይደለ ። ወትገብር ፡ ውስተ ፡ አርባዕቱ ፡ መሳምክቲሃ ፡ ለታቦት ፡ አርባዕተ ፡ ከበሎ ፡ (ክብ ፡ ነገ፲፯) ። ዕብንን ፡ እይ ፤ ከዚህ ፡ ጋራ ፡ አንድ ፡ ነው ።

**ከቢር ፤ ሮት ፤ (ከብረ ፡ ይከብር ፡ ይክበር ። ዐረ ፡ ከቡረ ። ዕብ ፡ ካባር ፤ ዱሮ ፡ ቀድሞ)** ፤ መክበር ፡ መከበር ፤ መወደድ ፤ ማደግ ፡ መብለጥ ፤ መግነን ፡ ታላቅ ፡ መኾን ፤ የሀብት ፡ የዋጋ ፤ የማዕርግ ፡ የድግሪ ፤ የወርድ ፡ የቁመት ። ከቢር ፡ እንዲል ፡ ዐረብ ፤ ታላቅ ፤ ሲል ። በከብረ ፡ አቡሁ ፡ ይከብር ፡ ሰብእ ። ቦ ፡ ዘይከብር ፡ በአትሕቶ ፡ ርእሱ ። ዘይውኅድ ፡ ይከብር ፡ ወይቴሐት ፡ ዘይበዝኅ ። ብከሙ ፡ ይክበር ፡ ዘርዐ ፡ አብርሃም ። ውእቱ ፡ ይከብር ፡ እምኔሆሙ ፡ (ሢራ፫ ፡ ፲፩ ። ፳ ፡ ፲፩ ። ሱቱ ፡ ዕዝ፯ ፡ ፴፫ ። ኩፋ ፡ ፴፩ ። ዳን፩ ፡ ፱) ። በከብረ ፡ ፈንታ ፡ ተከበረ ፡ ይላል ፤ ተ ፡ ያማርኛ ፡ ነው ። ወአንስትኒ ፡ ይትከበራ ። ተከባሪ ፡ (ተረ ፡ ቄር፲፰ ። ሲኖዶ) ።

**ክቡር** ፤ (ራን ፡ ራት ፡ ብርት) ፤ በቁሙ ፤ የከበረ ፤ የተከበረ ፤ የተወደደ ፡ ውድ ። ብእሲ ፡ ክቡር ፤ ዕንቍ ፡ ክቡር ። ክቡረ ፡ ስም ፤ ክቡረ ፡ ሤጥ ። ዕደው ፡ ክቡራን ። አልባስ ፡ ክቡራት ። ሀገር ፡ ክብርት ፡ (ሚራ፱ ፡ ፩ ። አርጋ ፡ ፪ ። ሕዝ፳፯ ፡ ፲፯) ።

**ክብረት** ፤ በቁሙ ፤ መክበር ፤ አከባበር ፤ ክበሬታ ። ውድነት ፤ ክቡርነት ።

**ክብር** ፤ (ራት) ፤ በቁሙ ፤ ልዕልና ፡ ላቂያ ፡ ብልጫ ፤ ሹመት ፡ ሽልማት ፤ ታላቅነት ፤ ኀይል ፡ ብዕል ፤ ብዙ ፡ ገንዘብ ። ወድቀት ፡ እምክብራ ፤ ትላሑ ፡ እምክብራ ። በእንተ ፡ ክብረ ፡ ዘመዱ ። ሥሉ ፡ ክብሩ ፡ ለሰብእ ፡ ከመ ፡ ፍሬ ፡ ሣዕር ። መንግሥታተ ፡ ዓለም ፡ ወክብሮሙ ። ዘኔሠ ፡ ድኅሬሆን ፡ ለክብራት ፡ ይጐይዩ ፡ (ቀሌ ። ስንክ ፡ ጳጕ፩ ። ኢሳ፵ ፡ ፯ ። ማቴ፬ ፡ ፰ ። ማር ፡ ይሥ) ።

**ክብርና** ፤ ክቡርነት ። በቁሙ ፤ የቤት ፡ ልጅ ፡ ክብር ፤ ማኅተመ ፡ ድንግልና ።

**ክብረ ፡ ነገሥት** ፤ የመጽሐፍ ፡ ስም ፤ ያኵስሞች ፡ መጣፍ ፤ ንቡረ ፡ እድ ፡ ይሥሐቅ ፡ በላስቶች ፡ ዘመን ፡ የደረሰው ፤ ወይም ፡ ከዐረብ ፡ የመለሰው ፤ የጽላተ ፡ ሙሴን ፡ አመጣጥ ፡ የአኵስምን ፡ ልዕልና ፤ የነገሥታቷን ፡ ክብር ፡ ከሰሎሞን ፡ መወለዳቸውን ፡ አምልቶ ፡ አስፍቶ ፡ የሚናገር ።

**አክበረ** ፤ አከበረ ፤ አላቀ ፡ አበለጠ ፤ አስከበረ ፡ አዕደደ ። አክብር ፡ አባከ ፡ ወእመከ ። አክበረ ፡ እግዚ ፡

ሕበ ፡ ኅዕለ ፡ ውሉዱ ። እግዚ ፡ አክበረከ ፡ (ዘፀ፳ ፡ ፲፪ ። ሚራ፫ ፡ ፪ ። ኢሳ፶፰ ፡ ፭) ።

**አክባሪ ፤ (ሪት ፡ ርያን ፡ ያት) ፤** በቁሙ ፤ የሚያከብር ፡ የሚያስከብር ። እስመ ፡ እሙንቱ ፡ መልክአ ፡ እግዚ ፡ አክባሪት ፡ ለሹሎሙ ፡ ሰብእ ፡ (ፊልክ ፡ ፹፯) ።

**ክብረወ ፤ (ተቀ ፡ ግ ። ዕብ ፡ ቶፌፍ) ፤** ጸፋ ፡ መታ ፡ ኰረኰረ ፤ ጐሰመ ።

**ከበሮ ፤ (ብ ፡ ከባርው) ፤** በቁሙ ፤ ንዋየ ፡ ማሕሌት ፡ አታሞ ፡ ነጋሪት ፤ ከማዕደን ፡ ከንጨት ፡ ከቈርበት ፡ የሚሠራ ፤ ስለ ፡ ክብረ ፡ በዓል ፡ የሚመታ ። ክብራዊ ፡ ትእምርተ ፡ ክብር ፤ ጨኺ ፡ ተሰሚ ፡ ማለት ፡ ነው ። ሰብሕዎ ፡ በከበሮ ። ንሥኢ ፡ ከበሮኪ ። መሰንቆ ፡ ወከበሮ ፡ (መዝ ፡ ፻፶ ። ኤር፴፰ ፡ ፬ ። ዳን፫ ፡ ፲) ።



ከበሮ ፡

**ክብሬት ፤ (ዐረ ፡ ኪብሬት ። ሱር ፡ ካብሬታ ። ዕብ ፡ ጐፍሬት) ፤** በቁሙ ፤ ዲን ፡ የእሳት ፡ ዐፈር ፡ እሳታዊ ፡ ሜቃ ፤ ዐይነቱ ፡ ብጫ ፡ ክርፋታም ፡ (መቃ ፡ ፯፪) ።

**ክብሬታዊ ፤** የዲን ፡ ዐፈር ፡ ሜቃ ፤ የዲን ፡ ውሃ ። ይነግሥ ፡ ሙዳየ ፡ ልሕዙት ፡ ወይደይ ፡ ውስቴቱ ፡ ማየ ፡ መሪረ ፡ ክብሪታዊተ ፡ ወይነግሥ ፡ መሬተ ፡ (ፍ ፡ ነ ፡ ፳፬ ፡ ፯ ። ዘጕ፭ ፡ ፲፯ ፡ ፲፰) ።

**ክብራታን ፤** ስመ ፡ ሀገር ፡ በምድረ ፡ እስራኤል ፡ ያለች ፡ አንዲት ፡ ገጠር ። (ኩፋ ፡ ፴፪) ። አንዳንድ ፡ መጣፍ ፡ በክብራታን ፡ ፈንታ ፡ ኬብሮን ፡ ይላል ፤ ባለብሉዮችም ፡ ክብራታንን ፡ ኬብሮን ፡ ብለው ፡ ይፈቱታል ። በዕብራይስጥ ፡ ግን ፤ ሔብሮንና ፡ ክብራታን ፡ ልዩ ፡ ነው ።

**ከቢስ ፤ ሶት ፤ (ከበሰ ፡ ይከብስ ፡ ይክብስ ። ዕብ ፡ ካባስ ፤ ዐጠበ ፡ አጠራ ፡ ወለወለ ። ካበሽ ፤ ያዘ ፡ ገዛ ፡ ሣቀየ ፡ አጠቃ) ፤** መከበስ ፡ ማክበስበስ ፤ ጠጕርን ፡ ሰብስቦ ፡ ጠምዞ ፡ በማኽል ፡ ራስ ፡ ላይ ፡ መጠቅለል ፡ ማሰር ፤ በወለባና ፡ በሚደ ፡ መያዝ ፡ መቸንከር ። ራስን ፡ ጠጕርን ፡ በሚታሰርና ፡ በሚደፋ ፡ በሚለበስ ፡ ነገር ፡ መሸለም ፡ ማስጌጥ ፡ ማንቈጥቈጥ ።

**ተከብሰ ፤** ተከበሰ ፤ ተከበሰበሰ ፤ በራሱ ፡ ላይ ፡ ጌጥ ፡ ታሸከመ ፤ ታሸለመ ። ፀፈረት ፡ ርእሳ ፡ ወተከብሰት ፡ (ዮዲ፲፮ ፡ ፰) ።

**ክቡስ ፤ (ሳን ፡ ሳት ፡ ብስት) ፤** የተከበሰ ፡ ክብስ ፤ ክብስብስ ፤ ጌጥ ፡ ወዳድ ።

**ክብሶ ፤ (ብ ፡ ከባስው ፤ አው ፡ ክብሳት) ፤** ክብስ ፡ ጠጕር ፤ ክብሳት ። የራስ ፡ የጠጕር ፡ ክባስ ፤ በሰቱ ፡ ላይ ፡ የሚኽን ፡ ጌጥ ፡ ሽልማት ፤ ቀጸላ ፡ ሠርመዲ ፡ ዐይነ ፡ ርግብ ። ውስተ ፡ መካነ ፡ ሰርጐ ፡ ዘክብሶ ፡ ሥዕርታ ፡ ወደየት ፡ ሐመደ ። ክብሶሆን ፡ ወአልባሲሆን ፡ ዘሥጋባት ፡ (አስቴ፬ ፡ ፲፯ ። ኢሳ፫ ፡ ፳) ።



ክብሶ ፡

**ኰብስ ፤ ኮብስ ፤** ኰብሽ ፤ የደዌ ፡ ስም ፤ ገላ ፡ የሚነፋ ፡ የሚያሳብጥ ፤ የሚያፈርስ ፡ የሚቈምጥ ፤ ቍምጥና ፡ ቢስ ፡ ገላ ። አዝልፎ ፡ ስካር ፡ ያመጽእ ፡ ነቀጥቃጠ ፡ ወጥፍአተ ፡ ልብ ፤ ወኰብሰ ፡ ወሞተ ፡ ግብት ፡ ወፈፀንተ ፡ (ፍ ፡ ነ ፡ ፶) ።

**ከቢት ፤ ቶት ፤ (ከበተ ፡ ይከብት ፡ ይክብት ። ኀብአ) ፤** መከበት ፤ መሸሸግ ፡ መሰወር ፡ መደበቅ ፤ እንዳይገኝ ፡ ማድረግ ። ኢትረክበ ፡ እስመ ፡ ከበቶ ፡ እግዚ ። ከበተት ፡ ርእሳ ። ኢንክል ፡ ከቢቶቶ ። ይኄይስ ፡ አብድ ፡ ዘየኀብእ ፡ አበዲሁ ፡ እምጠቢብ ፡ ዘይከብት ፡ ጥበቢሁ ፡ (ዕብ፲፩ ፡ ፳ ። ሉቃ፩ ፡ ፳፬ ። ግብ፬ ፡ ፲፯ ። ሢራ፳ ፡ ፴፩) ።

**—፤** ማሳደር ፤ ከቤት ፡ ከበረት ፡ ማግባት ፤ መጠበቅ ፡ መመልከት ፤ የንግዳ ፡ የከብት ። ከብት ፡ ማለት ፡ ቃሉ ፡ ከዐብትም ፡ ሳይቀር ፡ ዐማርኛው ፡ ከዚህ ፡ የወጣ ፡ ነው ።

**ከባቲ ፤ (ቲት ፡ ትያን ፡ ያት) ፤** የሚከብት ፡ ከባች ፤ ሸሻጊ ፡ ደባቂ ። ከባቲሁ ፡ ለሹሉ ፡ ክሡት ። አምላክ ፡ ከባቴ ፡ አበሳ ፡ (ቅዳ ፡ ሕር ። ግንዘ) ።

**አክበተ ፤** አስከበተ ፤ አስደበቀ ፤ አስጠበቀ ።

**ተከብተ ፤** ተሸሸገ ፡ ተደበቀ ፤ ታባ ፡ ተሰወረ ፤ ከቦታው ፡ ታጣ ። ተከብተ ፡ ሔኖክ ። ከመ ፡ ትትከበት ፡ መንፈስየ ። ስእነ ፡ ተከብቶ ፡ (ሔኖ፲፪ ፡ ፩ ። ፎ፩ ፡ ፩ ። ማር፯ ፡ ፳፬) ።

**ክቡት ፤ (ታን ፡ ታት ፡ ብት) ፤** የተሸሸገ ፡ ሽሽግ ፤ ክብት ፡ ስውር ፡ ድብቅ ። ጥበብሰ ፡ ክቡት ፡ ወመዝገብ ፡ ዘኢያስተርኢ ። ኅቡእ ፡ ወክቡት ። ክቡት ፡ ተአምር ፤ እስመ ፡ ውስተ ፡ ብርሃን ፡ ሀሎከ ፡ (ሢራ፵፩ ፡ ፲፬ ። ፩ቆሮ ፡ ፪ ፡ ፯ ። ቅዳ ፡ ሐዋ) ።

**ክቡታዊ ፤** የውስጥ ፡ የልቡና ፤ ረቂቅ ፡ መንፈሳዊ ። ሥርዐት ፡ ክቡታዊ ፡ (ፊልክ ፡ ፫) ።

**ክብተት ፤** (ላ ፡ ጥ) መሸሸግ ፤ ሽሽጋ ፤ ሽሽግነት ። ክብተት ፡ ዘኢየኀልቅ ፡ (ራእ ፡ ሲኖ) ።

**ከበታ ፤** ስዋሬ ፡ ስወራ ፤ ስውርነት ። በመንክራቲሁ ፡ ያርኢ ፡ ከበታሁ ። ኢይነግር ፡ በእንተ ፡ ከበታየ ፤ አላ ፡ በዘያስተርኢ ፡ (ተረ ፡ ቄር፩ ። ፲) ።

**ኬደ ፤—ረገጠ ፤—ከዪድ ፡ ኬደ ።**

**ከደዋ፤(ዕብ፡ከድከድ)፤** ዕንቍ፡የዕንቍ፡ስም፤ ሕብሩ፡የሮማን፡ዐይነት፡እንደ፡ቦረቦሜ፡ያለ፤ የሚፈልቅ፡የሚብለጨለጭ። ሠለስቱ፡አዕናቍ፡ዘወርቅ፡ወብሩር፡ወከደዋ። ወርቅ፡ወከደዋ፡ወብሩር፡ወካልኣን፡አዕናቍ፡ሀለዉ፡ይትረከቡ፡እስከ፡ዮም፡(ታሪ፡አሆ፡ገ፲፩)።

**ከድከድ፤** ዝኒ፡ከማሁ፤ ከደዋና፡ካድኮድ፡አንድ፡ስም፡ነው። ረአሙት፡ወካድኮድ፡(ሕዝ፳፯፡፲፮)። በካድኮድ፡ፈንታ፡ከርከንድ፡ይላል፤ ከርከዴን፡ማለት፡ነው፤ ፍችውን፡በቦታው፡ተመልከት።

**ከዲን፤ ኖት፤ (ከደነ፡ ይከድን፡ ይከድን። ዕብ፡ካዳን፤አሰረ፡አቈራኘ፡የፈረሰ፡የሠረገላ)፤** መክደን፡መግጠም፤ማልበስ፡መሸፈን፤መሰወር፡መጋረድ፤ እንዳይታይ፡ማድረግ። አምጽኡ፡እብነ፡ወከደኑ፡ዲበ፡አፈ፡ግብ። ከደነት፡ኀፍረታ፡በቈጽል። ፈጺሞሙ፡ከዲነ፡ዘቅድሳት። ዘይከድን፡አበሳሁ። ይከድኑ፡ገጾሙ፡(ዳን፮፡፲፯። ኩፋ፡፫። ዘኍ፬፡፲፭። ምሳ፳፰፡፲፫። ኢሳ፮፡፪)።

**ከዳኒ፤ (ኒት፡ ንያን፡ ያት፤ ደንት)፤** የሚከድን፡የሚያለብስ፡ከዳኝ፤ ሰዋሪ፡ጠባቂ፤ ወባት፡ጠበቃ። ልብስ፡ጽድቅከ፡ይኩነኒ፡ከዳኔ። ለመበለት፡ከዳኒ፡(ስንክ፡መጋ፭። ኪዳ)።

**መክድን፤ መክደኒ፤** ዝኒ፡ከማሁ።

**አክደነ፤** አስከደነ፡አስለበሰ።

**ተከድነ፤** ተከደነ፡ለበሰ፡ተሰወረ፡ተሸፈነ። ትትከደኑ፡ወኢትመውቁ። ከመ፡ትትከደኑ፡በዕለተ፡መዐቱ፡ለእግዚ። ተከድነት፡ገጻ፡(ሐጌ፩፡፮። ሶፎ፪፡፫። ዘፍ፳፬፡፷፭)።

**ከዱን፤(ናን፡ናት፡ ድንት)፤** የተከደነ፡የለበሰ፤ስውር፡ሽፍን። ከዱን፡እብን፡ዲቤሁ። ከዱን፡ብከ፡ዐበይከ። ከዱን፡ትምህርትነ፡(ዮሐ፲፩፡፴፰። ቅዳ፡ዮሐ። ፪ቆሮ፡፬፡፫)።

**ከድነት፤** መከደን፡መከደን፤ አከዳደን፡አለባበስ፤ ከዱንነት። የሌት፡ልብስ፤ ጭን፡ኀፍረት። ኢይከሥት፡ከድነተ፡አቡሁ፡(ኩፋ፡፴፫)።

**ከዳን፤(ናት)፤** በቁሙ፤ መከደኛ፡መግጠሚያ፤ ልብስ፡ቀሚስ፤መጐናጸፊያ፡ለሓፍ፡ምንጣፍ፤ መጋረጃ፡ድንኳን፤ ዳስ፡ጥላ፡ከለላ፤ ቤት፡ጐጆ፤ የሚሰውርና፡የሚሸፍን፡ኹሉ። ከዳነ፡ዐዘቅት። ዘቦ፡ክልኤ፡ከዳናተ። ከዳን፡ዘሕብረ፡ፀሰቅ። ትከድኖሙ፡ከዳነከ። ነሥአ፡ከዳነ፡ወጠምዐ፡ውስተ፡ማይ። ከዳንከ፡ዘታሕተ፡ገቦከ። ከዳን፡በዘይትገለበቡ፡እምጠል፡(፪ነገ፡፲፯፡፲፱። ሉቃ፫፡፲፮። ዘፍ፴፯፡፫። ሕዝ፳፮፡፫። ፬ነገ፡፰፡፲፭። ምሳ፳፪፡፳፯። ኢሳ፬፡፮)።

**መክደን፤(ብ፡መከድን)፤** መከደኛ፡መሸፈኛ፤ ከዳን፡ልብስ። አልቦ፡ዣዕር፡ለመክደኖን። አምሳለ፡መክደን። መክደነ፡አርእስት፡ዘንጹን፤ የራስ፡ቍር፡(ገድ፡ላሊ። ፊልክ፡፺፴፯። ፪ዜና፡፳፯፡፲፯)።

**መክደንት፤(ታት)፤** ዝኒ፡ከማሁ።

**ምክዳን፤** ዝኒ፡ዓዲ፡ከማሁ፤ መከደኛ፡መከደኛ።

**ኪዳን፤—ውል፤—ከዩድ፡ኬደ።**

**ከሂሀ፤ ሆት፤ (ከሀሀ፡ ይከሀሀ፡ ይከሀሀ። ዕብ፡ካሃሀ፡ ይክሄሀ)፤** መድከም፡ማነስ፤ መጨለም፡መፍዘዝ፤ መደንገዝ፤ የኀይል፡የጕልበት፡የዐይን፡የብርሃን። ከበወንና፡ለከወን፡እይ፤ የዚህ፡ኀሮች፡ናቸው። ከሕከሐም፡የዚህ፡ዲቃላ፡ነው።

**ካሂ፤ አካሂ፤ (ብ፡ካሀያት፤አካሀያት)፤** ጊደርና፡ጥገት። ካሂ፡ጊደር፤ እንስት፡ጥጃ። አካሂ፡ጥገት፤ እመጫት፡ላም። ምስጢራቸው፡ማነስና፡መድከም፡ሕጹጽነት፡ነው። በዕብራይስጥ፡ግን፡ካሂ፡ማለት፡ከማሃ፡ከመ፡ዛ፡ማለት፡ነውና፤ በዚህ፡ዘይቤ፡ሲፈቱት፡ካሂ፡የጥጃ፡ጕፍላ፡ወይም፡እንቡጣ፡ስልቻው፡ምስሉ፤ ሲሞት፡ከኹራቱ፡እስከኁ፡ሸልቅቀው፡በሥጋው፡ፈንታ፡ገለባ፡ጐስረው፡ጠቅጥቀው፤ በማሮቹ፡ፈንታ፡፬፡ዕንጨት፡ሰክተው፡ሕያው፡አስመስለው፡የጨው፡ውሃ፡ቀብተው፡የሚያቆሙት፤ አካሂ፡ያንን፡እያየች፡እየላሰች፡ወተቷን፡የምትሰጥ፡ማለት፡ነው። (ሙሾ፤ላምና፡ዐላቢ)፤ ያለ፡እየመሰለኝ፡ልጄ፡ሙቶ፡ሳለ፤ እንቡጣውን፡ባየው፡ልቤ፡ተታለለ። እንኳን፡አንች፡ላሚ፡ቤተ፡እስራኤል፤ ታታለል፡ነበረች፡በጥጃ፡ምስል።



አካሂ፡

**ከሃ፤(ብ፡ከሃት)፤** ወዲያ፡ወደዚያ፤ከዚያ፡በዚያ፤ የቦታን፡ፈቀቅታ፡ጥቂት፡ርሕቀት፡ያሳያል፤ ፍችው፡እንደ፡ሀየ፤ ስልቱ፡እንደ፡ሰፌ፡ነው። እም፡እየተስማማው፡ከሰፌና፡ከዝየ፡ጋራ፤ ሳይስማማውም፡ይነገራል። አሐዱ፡እምሰፌ፡ድንጋገ፡ፈለግ፤ ወአሐዱ፡እምከሃ፡ድንጋገ፡ፈለግ። ፍልስ፡እምዝየ፡ኀበ፡ከሃ። አሐውር፡ከሃ፡ወእጼሊ። ዝርዎ፡ከሃ። ረሐቁ፡ከሃ። በዝ፡ዓለም፡ወበከሃ፡በኀበ፡እግዚ። ከሃ፡ከሃቲሆሙ፡(ዳን፲፪፡፭። ማቴ፲፯፡፳። ፳፮፡፴፮። ዘኍ፲፯፡፪። ፩ነገ፡፲፬፡፱። ዲድ፡፲፬። ሔኖ፴፪፡፫)። ከሃየ፡ከ፡ኪ፡ሁ፡ሃ፤ ከሃነ፡ከሙ፡ከን፡ሆሙ፡ሆን፡እያለ፡ይዘረዝራል። እምሰፌሁ፡ፈለግ፡ወእምከሃሁ፡ዐፀ፡ሕይወት፡(ራእ፳፪፡፪)። (ዕር፳፩፡ቍ፲፲፰)። አንዳንድ፡መጣፍ፡ግን፡በከሃ፡ፈንታ፡ከሃከ፡ከሃከ፡ይላል፤ የጣፊ፡ስሕተት፡ነው። ነዋ፡ዝየ፡ወነዋ፡ከሃከ። እስከ፡እትመየጥ፡ሰፌ፡ወከሃከ። ተኀሥሦት፡እምጥንቃቄ፡ከሃከ። ወዓዲ፡ዘእምዝ፡ከሃከ፡(ሉቃ፲፯፡፳፫። ፫ነገ፡፳፡፵። ቄር)።

ከሂል ፤ ሎት ፤ (ክህለ ፡ ይክል ፡ ይክሀል ። ዕብ ፡ ያከል) ፤ መቻል ፡ መብቃት ፤ ማግመር ፡ መወሰን ፤ በሚሠሩት ፡ ሥራ ፡ ማየል ፡ መበርታት ፤ መብት ፡ ማግኘት ። ገቢረ ፡ ትግብር ፤ ወክሂለኒ ፡ ትክል ። ኵሎ ፡ ዘትክል ፡ እዴከ ፡ ለገቢር ። መኑ ፡ አነ ፡ ከመ ፡ እክህል ፡ ሐኒጸ ፡ ሎቱ ፡ ቤተ ፡ (፩ነገ ፡ ፳፮ ፡ ፳፭ ። መክ፱ ፡ ፲ ። ፪ዜና ፡ ፪ ፡ ፮) ።

—፤ ችሎት ፡ አቻቻል ፤ ኀይል ፡ ብርታት ፤ ዐቅም ፡ ጕልበት ፤ ሥልጣን ፡ መብት ። ሰብሕዎ ፡ በክሂሎቱ ። በከመ ፡ ክሂሎትነ ። አልብየ ፡ ክሂል ፡ ላዕሌሁ ። ከመ ፡ የሀበ ፡ ክሂለ ፡ ላዕሌሁ ፡ ወላዕለ ፡ ንዋዩ ፡ (መዝ ፡ ፻፶ ። ስንክ ፡ ሠኔ፲፪ ። ገድ ፡ ተክ ። ስንክ ፡ ግን፪) ።

ከሃሊ ፤ (ሊት ፡ ልያን ፡ ያት) ፤ የሚችል ፡ ቻይ ፤ ኀይለኛ ፡ ብርቱ ፤ ሥሉጥ ፡ ዕጉሥ ። ከሃሌ ፡ ኵሉ ። ጽኑዕ ፡ ወከሃሊ ። ዘከነ ፡ ከሃሌ ፡ በቃሉ ፡ ወበምግባሩ ። መሥዋዕት ፡ ከሃሊት ፡ ከመ ፡ ታስተስሪ ። ንሕነ ፡ ከሃልያን ፡ ለውላጤሁ ። ከሃሊ ፡ አነ ፡ ተጽናስሂ ፡ ወተደልዎሂ ፡ (ጥበ፯ ፡ ፳፫ ። ሩት፪ ፡ ፩ ። ሉቃ፳፬ ፡ ፲፱ ። አፈ ፡ ድ፲፯ ። ዮሴፍ ። ፊልጵ፬ ፡ ፲፪) ።

አክሀለ ፤ አስቻለ ፡ አበረታ ፤ አበቃ ፡ መብት ፡ ሰጠ ፡ አስናበተ ። ኵሎ ፡ እክል ፡ በዘውእቱ ፡ አክሀለኒ ። እግዚ ፡ አክሀለነ ፡ በኵሉ ፡ ዘንፈቅድ ። ያክህልክሙ ፡ እግዚ ፡ ለገቢረ ፡ ኵሉ ፡ ፈቃዱ ። ወኢያክህሎ ፡ ከመ ፡ ይቅረብ ፡ ኀቤሆሙ ፡ (ፊልጵ፬ ፡ ፲፫ ። ዮሴፍ ። ግንዘ ። ማር ፡ ይሥ፯ ፡ ፪) ።

አክሃሊ ፤ መክህል ፤ የሚያስችል ፤ አስቻይ ።

ተክህለ ፤ ተቻለ ፤ ተመቸ ። ኵሉ ፡ ይትክሀል ። እምእደ ፡ ዚኣሁ ፡ ጕይይ ፡ ኢይትክሀል ፡ ወኢይደሉ ። ኢይትክሀል ፡ ለኈልቆ ። ኢይትክሀል ፡ ከመ ፡ ዝ ፡ ይኩን ። በከመ ፡ ይትክሀለከ ። እስመ ፡ ቅኔ ፡ መዝሙርሰ ፡ ተከሃሊት ፡ በኵሉ ፡ ጊዜ ፡ (ማቴ፲፱ ፡ ፳፮ ። ጥበ፲፮ ፡ ፲፭ ። መክ፫ ፡ ፲፱ ። ዘፀ፰ ፡ ፳፪ ። ሢራ፴፰ ፡ ፲፭ ። ፊልክ ፡ ፪፻፴፰) ።

ተካሀለ ፤ ተቻቻለ ፤ ተስማማ ፡ ተዋደደ ፤ ተዋዋለ ፡ ተቋረጠ ፤ የዋጋ ። ተካሀለ ፡ ምስለ ፡ ገባእት ፡ በበ ፡ ዲናር ፡ ለዕለት ። አኮኑ ፡ በዲናር ፡ ተካሀልኩክ ። መኑ ፡ ውእቱ ፡ ዘተካሀለከ ፡ (ማቴ፳ ፡ ፪ ፡ ፲፫ ። ማር ፡ ይሥ፲፫ ፡ ፪) ።

ከሁል ፤ (ላን ፡ ላት ፡ ሀልት) ፤ የተቻለ ፡ የተቻቻለ ፤ የተስማማ ፡ ስምም ።

አስተካሀለ ፤ አቻቻለ ፤ አስማማ ፡ አዋደደ ።

መስተካህል ፤ (ልት ፡ ላን ፡ ላት) ፤ የሚያቻችል ፡ አቻቻይ ፤ አስማሚ ።

ኳሂላ ፤ (ላት) ፤ የጠፍር ፡ ኳስ ፤ ዕሩር ፡ ጥንግ ፤ የተኰሰ ፡ ዐባማ ፡ ጊጤ ፤ ከሆድ ፡ የሚወጣ ፡ ሐሠር ፡ ጕድፍ ። ጕድ ፡ እብድ ፡ ልብሱን ፡ የጣለ ፤ ወይም ፡ የእብድ ፡ አሸንጉሊት ፤ ከዐቢይ ፡ ጾም ፡ በፊት ፡ ከጾመ ፡ ነነዌ ፡ በኋላ ፡ የእብድ ፡ ዐሙስ ፡ ለት ፡ ርሱን ፡ በየግንባራቸው ፡ ለጥፈው ፡ ሲሥቁ ፡ ሲያሥቁ ፡ የሚውሉበት ። ወከመ ፡ ኳሂላት ፡ ኮነ ፡ ውስተ ፡ ዓለም ። ከመ ፡ ኳሂላ ፡ ኮንክምሙ ፡ ለብዙኃን ፡ (፩ቆሮ ፡ ፬ ፡ ፲፫ ። መዝ ፡ ፳) ።

—፤ መከን ፡ የበረሓ ፡ ዕንጨት ፤ እሾኽም ፡ ፍሬ ፡ ቢስ ። ወይም ፡ ብቸኛ ፡ በረኸኛ ፡ አውሬ ፤ ፋደት ፡ የዱር ፡ ድመት ። ወይከውን ፡ ከመ ፡ ኳሂላ ፡ በውስተ ፡ ገዳም ፡ (ኤር፲፯ ፡ ፮) ።

ከሂን ፤ (ከሀነ ፡ ይክህን ፡ ይክሀን ። ዕብ ፡ ካሄን) ፤ ካህን ፡ መኾን ፤ ክህነት ፡ ተሹሞ ፡ በግዜር ፡ ፊት ፡ ቁሞ ፡ ማገልገል ፡ የአምልኮ ፡ ሥራ ፡ መሥራት ፤ ስለ ፡ ራስና ፡ ስለ ፡ ሕዝብ ፡ መሥዕትና ፡ ጸሎት ፡ ማቅረብ ፤ መባረክ ፡ መቀደስ ፡ ማጥመቅ ፡ ማቍረብ ።

ካህን ፤ (ናት ። ዕብ ፡ ኮሄን ። ሱር ፡ ካህና ። ዐረ ፡ ካሂን) ፤ በቁሙ ፤ ቄስ ፡ ጳጳስ ፡ የግዜር ፡ አገልጋይ ፡ የሕዝብ ፡ መሪ ፡ አስተማሪ ፤ መንፈሳዊ ፡ አባት ። አንተ ፡ ካህኑ ፡ ለዓለም ። ትቀብዖ ፡ ወትቄድሶ ፡ ወይከውነኒ ፡ ካህነ ። ካህናት ፡ ወሊቃነ ፡ ካህናት ። ዐሥሩ ፡ ወአርባዕቱ ፡ ካህናተ ፡ ሰማይ ፡ (መዝ ፡ ፻፱ ። ዘፀ፵ ፡ ፲፭ ። ቅዳ ፡ ሕር ። ስንክ ፡ ኅዳ፳፬) ።

አክሀነ ፤ አስካነ ፤ ክህነት ፡ ሰጠ ፡ ሾመ ፤ ካህን ፡ አደረገ ። ያክህኖሙ ፡ (ቀኖ ፡ ኒቅ ፡ ፳፯) ። ክህነት ፡ አሰጠ ፡ አሾመ ፤ ካህን ፡ አስደረገ ።

ተክህነ ፤ ተካነ ፤ ክህነት ፡ ተሾመ ፡ ተቀበለ ፤ ካህን ፡ ኾነ ፡ ካህን ፡ ተባለ ፤ ለማገልገል ። ክሂን ፡ ክሹመት ፡ በኋላ ፡ ማገልገልን ፤ ተክህኖ ፡ ከማገልገል ፡ በፊት ፡ መሾምን ፡ የሹመትን ፡ ጊዜ ፡ የተቀበሉበትን ፡ ዕለትና ፡ ሰዓት ፡ ያሳያል ። መጽሐፍ ፡ ግን ፡ ኹለቱንም ፡ ጾታ ፡ አንድ ፡ አድርጎ ፡ ተክህነ ፡ ይላል ፤ አያሰኝም ። ይርዐይ ፡ መርዔት ፡ ወይትክህን ። እስመ ፡ አንተ ፡ አዘዝከነ ፡ ንቅም ፡ ቅድሜከ ፡ ወለከ ፡ ንትክሀን ። እፎ ፡ ተንረይከ ፡ ለተክህኖ ፡ (ኪዳ ። ቅዳ ። መጽ ፡ ምስ) ።

ክሁን ፤ (ናን ፡ ናት ፡ ሀንት) ፤ የተካነ ፤ ክህነት ፡ የተሾመ ፡ የተቀበለ ።

ክህነት ፤ መካን ፡ ማስካን ፤ ክህንነት ፤ ተክኖ ፡ ማገልገል ። አገልግሎት ፤ መንፈሳዊ ፡ ሹመት ፤ ፯ ፡ ዕርከኖች ፡ ያሉት ። ፫ቱ ፡ ላይኞች ፤ ጵጵስናና ፡ ቅስና ፡ ዲቁና ። ፬ቱ ፡ ታችኞች ፡ ንፍቀ ፡ ዲያቆንና ፡ አንባቢ ፤ መዘምርና ፡ በረኛ ። ጳጳስንና ፡ ኤጲስቆጶስን ፡ እይ ። ተኀርየ ፡ ዘርዐ ፡ ሌዊ ፡ ለክህነት ። ለክህነት ፡ ቅድስት ፡ ወንጹሕት ። ኢይግበር ፡ ሕዝባዊ ፡ ግብረ ፡ ክህነት ፡ (ኩፋ ፡ ፴ ። ፩ጴጥ ፡ ፪ ፡ ፭ ። ዲድ ፡ ፲፯) ።

ክህነታዊ ፤ የክህነት ፤ ክህነታም ፡ ባለክህነት ። መልእክት ፡ ክህነታዊት ። ሀብት ፡ ክህነታዊት ፡ (ፍ ፡ ነ ፡ ፲ ፡ ፯ ። ፊልክ ፡ ፲፭) ።

ከዊው ፤ ዎት ፤ (ከወ ፤ ከወወ ፡ ይከውው ፡ ይክውው) ፤ መቅለል ፤ መፍጠን ፡ መቀልጠፍ ፡ ያከኼድ ፡ ያነጋገር ። መዋኸት ፡ መቅጠፍ ፤ መለፍለፍ ። ኀወወን ፡ እይ ፤ የዚህ ፡ ዘር ፡ ነው ።

**ከዋው** ፤ (ዋዋን ፡ ት) ፤ ቀላል ፡ ፈጣን ፤ ቀልጣፋ ። እበን ፡ ከዋዋት ። አእጋሪሁ ፡ ከዋዋት ፡ (ኢያ ፴ ፡ ፫ ። ስንክ ፡ ጥቅ ፲፭) ።

**ከዋው** ፤ (ዋት) ፤ ቅለት ፤ ውሸት ፡ ቅጥፈት ። በጠዋይ ፡ ቃል ፡ ወበከዋው ፡ ነገር ፡ (መቃ ፡ ገ፳፫) ።

**ከከወ ፤ ከውከወ** ፤ (ተቀ ፡ ግ) ፤ ዘረ ፡ ዋተተ ፤ ተንከወከወ ። ከውካዋ ፡ እንዲሉ ፤ ዘዋሪ ፡ ሲሉ ።

**አንከከወ** ፤ ነዘረ ፡ አዞረ ፡ አሽከረከረ ፤ ተሽከረከረ ።

**መንከክት** ፤ (ብ ፡ መናኩክት) ፤ እንዝርት ፤ የመንኰራኵር ፡ ብረት ፡ ተጋዳሚው ። ከመ ፡ መንከክት ፡ እንተ ፡ ተዐውድ ፡ (ሚራ፴፯ ፡ ፭) ።

**ኮከብ** ፤ (ብ ፡ ከዋክብት ። ዕብ ፡ ኮካብ ። ሱር ፡ ካውክባ ። ዐረ ፡ ከውከብ) ፤ በቁሙ ፤ የብርሃን ፡ ቅንጣት ፡ የጸዳል ፡ ስሌዳ ፤ ብርሃን ፡ የተሣለበት ፡ የሰማይ ፡ ጌጥ ፡ የጠፈር ፡ ፈርጥ ፤ ሌሊት ፡ እንዳሸዋና ፡ እንደ ፡ ፋና ፡ በዝቶ ፡ የሚታይ ፡ የሚያበራ ፤ የፀሓይ ፡ ሰራዊት ፡ የጨረቃ ፡ ጭፍራ ፤ ዘዋሪ ፡ ከባቢ ። ስምነቱ ፡ ከከወና ፡ ከከበበ ፡ ከኹለቱ ፡ የተደቀለ ፡ ነው ፤ ስለዚህ ፡ በኮከው ፡ ፈንታ ፡ ኮከብ ፡ ይላል ። ኣበዝኅ ፡ ዘርዐከ ፡ ከመ ፡ ኮከበ ፡ ሰማይ ። ኮከብ ፡ እምኮከብ ፡ ይኄይስ ፡ ክብሩ ። አሰርገወ ፡ ሰማየ ፡ በከዋክብት ። ከዋክብተ ፡ ሰማይ ። ለወርኅ ፡ ወለከዋክብት ፡ ዘአኰነኖሙ ፡ ሌሊተ ፡ (ኩፋ ፡ ፳፬ ። ፩ቆሮ ፡ ፲፭ ፡ ፵፩ ። ድጓ ። ኤር፲፱ ፡ ፲፫ ። መዝ ፡ ፻፴፭) ።



ኮከብ ፡

**ከዋክብት ፡ እለ ፡ ጽኑዓን** ፤ የማይኼዱ ፤ የማይናወጡ ፡ (አቡሻ ፡ ፴፯) ።

**ኮከበ ፡ ገዳም** ፤ ቅዱስ ፡ እንጦንዮስ ፡ (ስንክ ፡ ጥር፳፪) ።

**ኮከብ ፡ ዘቦቱ ፡ ዘነብ** ፤ ጅራታም ፤ ባለጅራት ፤ የክፉ ፡ ምልክት ፡ (አዋል) ።

**ኮከበ ፡ ምዕራብ** ፤ የማታ ፡ ኮከብ ፡ አስታርቦሽሽ ፡ (ስንክ ፡ የካ፪) ።

**ከዋክብተ ፡ ናግራን** ፤ ሰማዕታት ፡ (ስንክ ፡ ኅዳ፳፮) ።

**ኮከበ ፡ ጽባሕ** ፤ ያጥቢያ ፡ ኮከብ ፤ ማለዳ ፡ የሚወጣ ፡ (ኢሳ፲፬ ፡ ፲፪) ።

**ከዋክብት ፡ ጽልሙታን** ፤ ሰሑታን ፤ ስተው ፡ የሚያስቱ ፤ ደቂቀ ፡ ሴት ፡ (ይሁ ፡ ፲፫) ።

**ኮክህ** ፤ በቁሙ ፤ ኮክ ፡ የተክል ፡ ዕንጨት ፡ ስም ፤ ፍሬው ፡ የሚጥም ፡ ዐጥንታም ። ኮል ፡ ወኮክህ ። ፍሬሁ ፡ ለኮክህ ፡ (ፍ ፡ ነ ፡ ፲፯ ፡ ፪ ። መ ፡ ፈ) ።



ኮክህ ፡

**ኮክህ** ፤—ንጥፍ ፡ ደንጊያ ፤—ኰኵሕ ።

**ከከወ** ፤—ዘረ ፡ ዋተተ ፤—ከዊው ፡ ከወ ፤ ከወወ ።

**ከዊል ፤ ሎት** ፤ (ከለ ፡ ይከውል ፡ ይኩል) ፤ አው ፡

**ከውሎ ፤ ሎት** ፤ (ከወለ ፡ ይኬውል ፡ ይከውል) ፤ መከወል ፤ ወደ ፡ ኋላ ፡ ማድረግ ፤ የኋሊት ፡ ማስኼድ ፡ ማስፈግፈግ ፤ ወይም ፡ በኋላ ፡ ማስከተል ፤ አስከታይ ፡ መኾን ።

**ተከወለ** ፤ ወደ ፡ ኋላ ፡ አለ ፤ አፈገፈገ ። ደጀን ፡ ኾነ ፤ በኋላ ፡ ኼደ ፡ ተከተለ ፤ የሰልፍ ፡ የጕዞ ። ይትኬወል ፡ እምኔነ ። እለ ፡ ይትኬወሉ ፡ ድኅረ ፡ መስቀል ። ወእለሂ ፡ ይትኬወሉ ፡ ድኅረ ፡ ታቦት ፡ የሐውሩ ፡ እንዘ ፡ ይነፍኁ ፡ ቀርነ ፡ (መጽ ፡ ምስ ። ኢያ፮ ፡ ፱) ። ደንረንና ፡ ተድኅረን ፡ እይ ።

**ከዉል** ፤ (ላን ፡ ላት ፡ ውልት) ፤ በኋላ ፡ ያለ ፤ የተከተለ ፤ ኋለኛ ፡ ደጀን ።

**ከዋላ** ፤ ኋላ ፡ ጀርባ ፤ ድኅር ፡ ዘባን ። ነዐቅብ ፡ ፍጽመ ፡ ወከዋላ ። ዳዊትሰ ፡ ወሰብኡ ፡ የሐውሩ ፡ ከዋላ ። መንገለ ፡ ከዋላ ፡ ሐመር ፡ (ኅሐ፬ ፡ ፲፯ ። ፩ነገ ፡ ፳፱ ፡ ፪ ። ማርቆ፬ ፡ ፴፰) ።

**ኮል** ፤ (ብ ፡ አክዋል) ፤ የተክል ፡ ዕንጨት ፡ ስም ፤ ትፋሕ ፡ ፍሬው ፡ ክብ ፡ እንክብል ፡ ሎጋማ ፤ ሲያዩት ፡ ሲበሉት ፡ ደስ ፡ የሚያሰኝ ፤ ቶሎ ፡ የማይደርስ ፡ የማይበስል ፡ ወደ ፡ ኋላ ፡ የሚል ። ኮል ፡ ዘውስተ ፡ ዕፀወ ፡ ገዳም ። ሰደቁኒ ፡ በአክዋል ። እምነበ ፡ ኮል ፡ አንሣእኩከ ። ቅርፍተ ፡ ኮል ፡ (ማሕ ፡ ፪ ፡ ፫ ፡ ፭ ። ፰ ፡ ፭ ። መ ፡ ፈ) ። ከወሎ ፤ የደጋ ፡ ዕንጨት ፡ ኵሽሽላ ፤ ቅጠሉን ፡ አህዮች ፡ ፍሬውን ፡ እረኞች ፡ አበባዉን ፡ ንቦች ፡ የሚወዱት ፤ ማራም ፡ ማረ ፡ መልካም ።



ኮል ፡

**ኮለ ፡ ወርቅ** ፤ የወርቅ ፡ ትፋሕ ፤ በትፋሕ ፡ አምሳል ፡ የተሣለ ፡ የተቀረጸ ፡ (ምሳ፳፭ ፡ ፲፩) ።

**አክዋል ፡ ዘዐርሞን** ፤ ያርሞን ፡ ፍሬዎች ፤ እንደ ፡ ትፋሕ ፡ ደስ ፡ የሚያሰኙ ፡ (መቃ ፡ ገ፫ ። ድጓ) ።

ዐርሞንንና ፡ ኤጓጤን ፡ እይ ። አክዋል ፡ ዘአርሞን ፡ ተብሎ ፡ በአልፍ ፡ ሲጣፍ ፡ ግን ፡ አርሞን ፡ በዕብራይስጥ ፡ ቃል ፡ ታላቅ ፡ ቤት ፡ ምሽራብ ፡ ነውና ፤ የቤት ፡ ዙሪያ ፡ ጌጥ ፡ የጕልላት ፡ ሻኹራ ፡ መርገፍና ፡ አጫዋች ፡ ያሰኛል ፤ ሕንባብን ፡ እይ ።

**ከለ ፡ ሐቅል** ፤ ዕንጕት ፤ የሽቱ ፡ ቅጠል ፡ በርሻ ፡ ባዝመራ ፡ ውስጥ ፡ የሚበቅል ፤ አበባው ፡ ጥቍር ፤ ፍሬው ፡ ታናናሽ ፤ ዐረቦች ፡ ሱፋሕ ፡ የሚሉት ። ሱፋሕና ፡ ትፋሕ ፡ አንድ ፡ መስሎ ፡ በለ ፡ ታያቸው ፡ መላሾች ፡ ኮል ፡ ብለውታል ፤ ተርጓሞችም ፡ እንኰይ ፡ ይሉታል ፤ ዕንጕትን ፡ እይ ፡ (ዘፍ፴ ፡ ፲፬ ፡ ፲፭) ። ይሰወጥ ፡ በአንፍየ ፡ ጼናከሙ ፡ ኮል ። ቅብዐ ፡ ጽጌ ፡ ለአንፈ ፡ ዙሉ ፡ ዘይጼኑ ፡ ኮለ ፡ (ስንክ ፡ መስ፳፭ ፡ መጋ ፡ ፲፯) ።

**ከለለ ፤ (ተቀ ፡ ግ)** ፤ ተንኳለለ ፤ ኮለል ፡ ኮለል ፡ ዱብ ፡ ዱብ ፡ አለ ፤ የፍሬ ፡ የእንባ ፡ የደም ፡ አወራረድ ፤ ለውሃም ፡ ይኾናል ። የሞፈርንና ፡ ያባለ ፡ ዘርን ፡ ጫፍ ፡ ቋፉን ፡ ከርከሩን ፡ ኮለል ፡ ማለት ፡ ከዚህ ፡ የወጣ ፡ ነው ።

**አንከለለ** ፤ (ኰኰለለ ፤ አንኰለለ) ፤ ዘረ ፤ አዘረ ፡ አሰከረ ። ሐመር ፡ አንተ ፡ ታንከልል ፡ ማእከለ ፡ ዐውሎ ፤ ዘረ ፡ (ሚራ፴፯ ፡ ፱) ። ዘአንከለሎ ፡ ደም ። ብፃው ፡ ከቡድ ፡ ዘያንከልሎ ፡ ሲድማኅ ፡ ከመ ፡ ስቴ ፡ ክርዳድ ፡ (ኢሳ፲፱ ፡ ፲፬ ። መጽ ፡ ምስ) ።

**ንከላል** ፤ የራስ ፡ በሽታ ፤ አዞሪቴ ፤ ስካር ። አንዘኒ ፡ ነከላል ፡ ወአሐምምም ። እምትንታኔ ፡ ዘነከላለ ፡ ጌጋይ ፤ እስመ ፡ በነከላለ ፡ ጌጋይ ፡ ልብየ ፡ አንበዘ ፡ ከመ ፡ ዘሰትየ ፡ ወይነ ፡ መስያዝዘ ፡ (ኤር፳ ፡ ፳፭ ። አርጋ ፡ ፬) ።

—፤ የራስ ፡ ጠጕር ፡ ሥራ ፤ ዙሪያ ፡ ክብ ፡ ጥምጥም ፡ ሥር ። ኢታንኅ ፡ ሥዕርተ ፡ ርእስከ ፡ ወኢትሕፀዮ ፡ ወኢትቅብዖ ፡ ዕፍረተ ፤ ወኢትኅድጎ ፡ ስሩሐ ፡ ወኢፍቱሰ ፡ ወኢፀፉረ ፤ ወኢትረሲ ፡ ለከ ፡ ድንጉዛተ ፡ ወነኮላሰ ፡ አላ ፡ ላጽዮ ፡ (ፍ ፡ ነ ፡ ፶፩) ።

**ከሞል ፤ (ላት)** ፤ ስመ ፡ ዕፅ ፤ ፍሬው ፡ የሚበላ ፡ የኮል ፡ ሱታፍ ፡ የተክል ፡ ዐይነት ፡ ዘፍ ፤ ባለቅኔዎች ፡ ግን ፡ ሲይተው ፡ ሸዬ ፡ ወይም ፡ እሺ ፡ ይሉታል ። ፍችው ፡ ከመ ፡ ኮል ፡ አምሳለ ፡ ኮል ፡ ማለት ፡ ነው ። ቀነውዎ ፡ ውስተ ፡ ሥጋሁ ፡ ምእተ ፡ ወኀምስ ፡ ወሠለስተ ፡ ቅንዋተ ፡ ዲበ ፡ ዕፀ ፡ ከሞል ። ወሀለዉ ፡ ሀየ ፡ ዕፀው ፡ ከሞል ፤ ወስገዱ ፡ ሎቱ ፡ ለእግዚእነ ፡ ኢየሱስ ፡ ክርስቶስ ፤ ወኮኑ ፡ ድኑናነ ፡ እስከ ፡ ዛቲ ፡ ዕለት ፡ (ስንክ ፡ መስ፲፭ ። ጥር፲፭ ። ግንጀ፱) ።

**ከሞስ ፤—ስመ ፡ ጣዖት ፤—ከመወ ።**

**ከዊን ፤ ኖት ፤ (ኮነ ፡ ይከውን ፡ ይኩን ። ዐረ ፡ ካነ ፤ ሀሎ ። ዕብ ፡ ካን ፤ ሀያህ)** ፤ መኾን ፤ መባል ፤ ሳይለወጡ ፡ በሱታፌና ፡ በምሳሌ ፡ በግብር ፡ ሌላ ፡ ስም ፡ መቀበል ። ቃል ፡ ሥጋ ፡ ኮነ ። ውእቱ ፡ አምላክ ፡ ዘኮነ ፡ ሰብአ ፡ ወውእቱ ፡ ሰብእ ፡ ዘኮነ ፡ አምላከ ፡ በተዋሕዶተ ፡ መለኮት ፡ ምስለ ፡ ትስብእት ። ኮንኪ ፡ ዐጽቀ ፡ ንጹሐ ። እግዚአ ፡ ጸወነ ፡ ኮንከነ ፡ ለትውልደ ፡ ትውልድ ። አነ ፡ እከውና ፡ ጥቅመ ፡ እሳት ፡ ዐውዳ ፡ (ዮሐ፩ ፡ ፲፬ ። ሃይ ፡ አበ ። ውዳ ፡ ማርያ ። መዝ ፡ ፹፱ ። ዘካ፪ ፡ ፭) ። ወይም ፡ በጭራሽ ፡ ወደ ፡ ሌላ ፡ ባሕርይ ፡ መለወጥ ፡ ሌላ ፡ ዐይነት ፡ መኾን ፤ ተለውጦና ፡ ተገልብጦ ፡ በሌላ ፡ ባሕርይ ፡ ስም ፡ መጠራት ፤ ያው ፡ ግን ፡ ጭገሬታውና ፡ ምልክቱ ፡ አሠሩ ፡ ቢጋሩ ፡ ህላዌው ፡ ሳይጠፋ ፡ ሳይታጣ ። ነጸረት ፡ ብእሲተ ፡ ሎጥ ፡ ድኅሬሃ ፡ ወኮነት ፡ ሐውልተ ፡ ጼው ። ወኮነት ፡ በትር ፡ አርዌ ፡ ምድር ። ወኮነ ፡ ዙሉ ፡ ማይ ፡ ዘውስተ ፡ ተከዚ ፡ ደመ ። ጥዒም ፡ አንከረ ፡ ሊቀ ፡ ምርፋቅ ፡ ውእተ ፡ ማየ ፡ ዘኮነ ፡ ወይነ ፡ (ዘፍ፲፱ ፡ ፳፮ ። ዘፀ፬ ፡ ፫ ። ፯ ፡ ፳ ። ዮሐ፪ ፡ ፱) ። ቀጥ ፡ ብሎ ፡ መቆም ፡ መገተር ፤ ባሉበት ፡ መጥናት ፡ አለመናወጥ ፡ የምሰሶ ፡ የዐምድ ፡ የሐውልት ፤ ከዋኒትን ፡ እይ ፤ ምሰክሩ ፡ ርሱ ፡ ነው ። በመቆም ፡ አንጻር ፡ መቀመጥንም ፡ ያሳያል ፤ ና ፡ ከዚህ ፡ ኹን ፡ እንዲሉ ፡ ተቀመጥ ፡ ሲሉ ።

**ከዊን** ፤ መፈጠር ፡ መገኘት ፤ መወለድ ፡ ከማሕፀን ፡ መውጣት ፤ ከላይ ፡ ወደ ፡ ታች ፡ መውረድ ፡ መዝነም ፤ መምጣት ፡ መሰማት ፡ መነገር ። እስመ ፡ ውእቱ ፡ ይቤ ፡ ወኮኑ ። ነገር ፡ በእንተ ፡ ከዊነ ፡ ዓለም ። ዙሉ ፡ ኮነ ፡ እመሬት ። ኢይኩን ፡ ፍሬ ፡ እምኔኪ ። ወኮኑ ፡ ሊተ ፡ እምኔሃ ፡ ሠለስቱ ፡ ውሉድ ። ወኮነ ፡ አይኅ ፡ ላዕለ ፡ ምድር ፡ አርብዓ ፡ ዕለተ ። ወኮነ ፡ ቃል ፡ እመልዕልተ ፡ ጠፈር ፡ (መዝ ፡ ፻፵፰ ። ጊ ፡ ወ ፡ ሐ ፡ ገ፪ ። መክ፫ ፡ ፳ ። ማቴ፳፩ ፡ ፲፱ ። ፊልክ ፡ ፫ ። ዘፍ፯ ፡ ፲፪ ። ሕዝ፩ ፡ ፳፭) ።

—፤ መደረግ ፤ መፈጸም ፡ መከናወን ፤ የሥራ ፡ የትንቢት ፡ የትእዛዝ ። ዝ ፡ ዙሉ ፡ ይከውን ፡ ፍጡነ ። በከመ ፡ ነበብኩ ፡ ከማሁ ፡ ይከውን ። እስመ ፡ በግብር ፡ ይከውን ፡ ዘነበበ ፡ ዮናስ ፡ ነቢይ ፡ (ኢሳ፲፬ ፡ ፭ ፡ ፳፬ ። ጦቢ፲፬ ፡ ፰) ።

—፤ ማደር ፡ መኖር ፤ በታ ፡ መያዝ ፤ ምስጢሩ ፡ ከመቆምና ፡ ከመቀመጥ ፡ ጋራ ፡ ይሰማማል ። ኮነ ፡ በማርያም ፡ ድንግል ። ሰይኩን ፡ ብርሃኑ ፡ ለእግዚ ፡ አምላክነ ፡ ላዕሌነ ። ከመ ፡ እኩን ፡ ቦቱ ፡ (ውዳ ፡ ማርያ ። መዝ ፡ ፹፱ ። ፊልጵ፫ ፡ ፱) ።

—፤ መገባት ፡ መመቸት ፤ መስማማት ። ኢይከውነከ ፡ ትዕጥን ። ኢይከውነነ ፡ ንደዮ ፡ ውስተ ፡ ቤተ ፡ መባእ ። ዘኢይከውኖሙ ፡ ለበሊዕ ፡ (፪ዜና ፡ ፳፮ ፡ ፲፰ ። ማቴ፳፯ ፡ ፮ ። ሉቃ፮ ፡ ፬) ።

—፤ መብቃት ፤ ልክ ፡ መኾን ። ከነክሙ ፡ ዐቀይቶ ፡ ለዝንቱ ፡ ደብር ። ከነከ ፡ ወኢትድግም ። ይከውነክሙ ፡ ዐሪግ ፡ ውስተ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ (ዘዳ፪ ፡ ፫ ። ፫ ፡ ፳፮ ። ፫ነገ ፡ ፲፪ ፡ ፳፰) ።

—፤ መጥቀም ፡ መርባት ፤ ማገልገል ። ምንተ ፡ ይከውን ፡ ዕፀ ፡ ወይን ፡ እምዙሉ ፡ ዕፀ ፡ (ሕዝ፲፭ ፡ ፪) ።

—፤ መሼጥ ፤ መለወጥ ፤ መገዛት ። ወኮነ ፡ ርእሰ ፡ አድግ ፡ ለኀምሳ ፡ ሰቅለ ፡ ብሩር ። መስፈርተ ፡ ስንዳሌ ፡ በሰቅል ፡ ትከውን ፡ (፬ነገ ፡ ፮ ፡ ፳፭ ። ፯ ፡ ፩) ።

**ከዊን ፤ (ዘርና ፡ ጥሬ)** ፤ መኾን ፡ ኹነታ ፤ እንት ፤ ባሕርይ ፡ ጠባይ ። እንትና ፡ መኾን ፡ አንድ ፡ ወገን ፡

ናቸው፤ ምስጢራቸውም፡ ባሕርይ፡ ነው። እመሰኬ፡ ከዊነ፡እግዚአብሔር፡ዘኢይትዌለጥ፡በከመ፡ ይት ዌለጥ፡ህላዌሆሙ፡ለፍጡራን፡፡እምከዊነ፡ካህን፡ ይኄይስ፡ከዊነ፡ ኖላዊ፡ (ማር፡ ይሥሐቅ፡ ፫። ቅኔ)።

**ከነ** ፤ ኾነ፤ ነበረ። የነገር፡ ጥንት፡ የንባብ፡ አር እስት፡ እየኾነ፡ እንደ፡ ይቤ፡ አንቀጽ፡ ይሰባል። ወኮነ፡ እምድኅረ፡ ሞተ፡ ሙሴ ፤ ተናገሮ፡ እግዚ፡ ለኢ ያሱ፡፡ ወኮነ፡እምድኅረ፡ሞተ፡ሳኦል፤ተመይጠ፡ ዳዊት፡እምቀትለ፡ዐማሌቅ፡፡ ወኮነ፡በውእቱ፡መ ዋዕል ፤ ወፅአ፡ ትእዛዝ፡ እምኀበ፡ ቄሳር፡ንጉሥ፡ (ኢያ፩፡ ፩። ፪ነገ፡ ፩፡ ፩። ሉቃ፪፡ ፩)። ፪ኛም፡ በትን ቢት፡ አንቀጽ፡ ላይ፡ ሲደረብ ፤ ምስጢሩና፡ ፍችው፡ ጽንዕ፡ ይኾናል። ከነ፡ያፈቅር፤ከነ፡ይጐይይ፤ ከነ፡ ይትመዐዕ፡ ቢል ፤ ይወድ፡ ነበር፡ ወይም፡ ይወዳል፡ ኾነ፡ ያሰኛል። ዐጸደ፡ ወይን፡ከነ፡ ለሰሎሞን፡ ያለ ውም ፤ ኮነ፡ የለ፡ ጽንዕ፡ ይባላል ፤ ኮነም፡ ቢቀር፡ ሎቱ፡ ለሰሎሞን፡ ብሎ ፤ አለው፡ ነበረው፡ ያሰኛል። ፫ኛም፡ ኢ፡ ስቶድቅበት፡ ዘማችንቱን፡ አሉታ፡ በዝብዞት፡ በኢና፡ በአኮ፡ በነባርነት፡ ይፈታል ፤ ምክንያቱም፡ ደራሽና፡ መ ላሽ፡ አለበታው፡ ስላገቡት፡ ነው። አንሰ፡ ኢኮንኩ፡ ኪ ያሁ፡፡ ኢኮነ፡ ሠናየ፡ነሚአ፡ኅብስተ፡ ውሉድ፡ ወወ ሂብ፡ ለከለባት ፡፡ ኢኮነ፡ ለክሙ፡ ታእምሩ፡ መዋ ዕለ፡ ወአዝማነ፡፡ ኢኮንክሙ፡ ነግደ፡ ወፈላሴ፡፡ ኢ፡ወ ናይ ፤ ኢለክሙ ፤ ኢአንትሙ ፤ ወይም፡ አኮ፡ አንትሙ፡ ነግድ፡ ወፈላሲ፡ ማለት፡ ነው ፤ አኮና፡ ኢ፡ አንድ፡ ወ ገን፡ ናቸው። ኮነ፡ ግእዝ፡ መሳቡ፡ ተለዋጭና፡ ኳኝ፡ ቢያገኝ፡ ነው ፤ አንዳንድ፡ ጊዜም፡ በግእዝ፡ ፈንታ፡ ለን፡ ይሰባል። ወይክውን፡ ፍሬሁ፡ ለሲሳይ ፤ ወቈጽሉሂ፡ ለፈውስ፡ (ሕዝ፵፯፡ ፲፪)። የኮነን፡ እፈታት፡ ፴፡ ብ ለው፡ የሚቈጥሩ፡ አሉ ፤ ምስክራቸው፡ አያጠግብም ፤ ብዙው፡ ልብ፡ ወለድ፡ ነው። ኮነና፡ ሀሎ፡ በዐረብና፡ በዕብራይስጥ፡ አንዳንድ፡ ወገን፡ ናቸው ፤ ዐረብ፡ ካን፡ ብሎ፡ ኾነ፡ አለ፡ ነበረ፡ ይላል ፤ ዕብራይስጥም፡ ሀያህ፡ ብሎ፡ ኮነ፡ ሀለወ፡ ይላልና ፤ የኮነ፡ እፈታት፡ ስልቱ፡ መብዛቱ፡ ስለዚህ፡ ነው። ዳግመኛም፡ ኮነኒ፡ ኮነኒ፡ በ ቍዐኒ፡ አከለኒ፡ በማለት፡ ፈንታ፡ ኮንየ፡ ይላል፡ የመ ላሽና፡ የጣፊ፡ ስሕተት፡ ነው። ስእነት፡ ብሂለ፡ ከንየ ፤ እሳት፡ ወማይ፡ ኢይብሉ፡ ኮንየ፡ (ምሳ፴፤፡ ፴)። (ዕር፪፡ ቍ፸፯። ዕር፳፯፡ ቍ፪፻፳)።

**ከዋኒ ፤ (ኒት፡ ንያን፡ ያት)** ፤ የኾነ፡ የሚ ኾን ፤ ኳኝ ፤ ተሰጭ፡ ተለዋጭ።

**ኵነት ፤ (ታት)** ፤ መኾን ፤ አኳኾን፡ ኹነታ ፤ ኣኗኗር። እግዚእ፡የአምር፡ኅሊና፡ ሰብእ፡ እምቅ ድመ፡ኵነታ ፡፡ ኵነተ፡ ብሔር፡ (አፈ፡ ድ፫። ገድ፡ ኪሮ)።

—፤ ፍጥረት ፤ ሥነ፡ ፍጥረት ፤ ለይኩን፡ በማለት፡ የተ ገኘ። ገባሬ፡ኵሉ፡ኵነታት፡(ያዕ፡ ዘእል)።

—፤ የአካል፡ ህላዌ ፤ ወይም፡ ስም። ህላዌ ፤ ወላዲን ትና፡ ተወላዲነት፡ ሠራጺነት። ስም ፤ ወላዲ፡ ተወላዲ፡ ሠራጺ ፤ ወይም፡ አብ፡ ወልድ፡ መንፈስ፡ መባል፡ ነው። እግዚ፡ ዘይሜለስ፡ በኵነታት ፤ ዘውእቱ፡ ሠለስቱ፡ አካላቲሁ፡፡ ዘይሜለስ፡ በአካላት፡ ወበኵነታት፡ (ያዕ፡ ዘእል። ፍ፡ ነ፡ ፩)።

**ከዋን ፤ (ናት። አው፡ ከዋኒት ፤ ንያት)** ፤ የደንጊያ፡ ዐምድ ፤ ሐውልት ፤ ትክል፡ ደንጊያ፡ ቁሞ፡ ተገትሮ፡ የሚኖር። ዘአ ዘዝከ፡ ከዋኒተ፡ ወአእመንከ፡ ሐዋ ርያተ ፤ በመስቀልከ፡ ረከብነ፡ ሕይ ወተ ፡፡ ወርእየ፡ክልኤተ፡ ከዋንያተ፡ አሐተ፡ በየማነ፡ ቤት፡ ወአሐተ፡ በፀ ጋመ፡ ቤት ፤ ወይቤ፡ እግዚእነ፡ ትሬ እዩኑ፡ አርኣያ፡ ..ወተመይጠ፡ ኀበ፡ ከዋኒት፡ ወይቤላ፡ ..በጊዜሃ፡ ቀነጸት፡ ከዋኒት፡ ወነበበት፡ ከመ፡ ሰብእ፡ (ሞ ዋሥ። ስንክ፡ ነሐ፴)።


ከዋኒት፡

**ከንየ** ፤ ኮነኒ ፤ ኾነኝ፡ በቃኝ ፤ በቀ ቶኛል። ከንየ፡ እንከሰ፡ (፩ነገ፡ ፲፱፡ ፬)።

**መከን ፤ (ናት። ዐረ፡ መከን። ዕብ፡ ማ ቆም። ሱር፡ አታር)** ፤ ቦታ፡ ስፍር፡ ስፍራ። መቆ ሚያ፡ መቀመጫ ፤ ቤት፡ መሥሪያ፡ ማደሪያ፡ መኖሪያ ፤ መሰብሰቢያና፡ መከማቻ ፤ ዐጸድ፡ ወሽድ ፤ አገር፡ መን ደር፡ ከተማ፡ ገጠር። ለይትጋባእ፡ ማይ፡ ዘመትሕተ፡ ሰማይ፡ ውስተ፡ አሐዱ፡ መካን፡፡ ከሞ፡ ኢይቁሙ፡ ውስተ፡ መካንከ፡፡ እስመ፡ አልቦሙ ፤ መካን፡፡ መካ ናት፡ ብሩሃን፡፡ መካናት፡ ሠናያት፡፡ ራሕበ፡ መካና ቲሆሙ፡ (ዘፍ፩፡ ፱። ሚራ፲፪፡ ፲፪። ሉቃ፪፡ ፯። ሔኖ ፲፯፡ ፫። ፳፪፡ ፩። ፵፫፡ ፪)።

—፤ ማእዝን ፤ የመጽሐፍ፡ አንቀጽ፡ ምዕራፍ፡ ክፍል። እምአርባዕቱ፡ መካን፡፡ወከሚተ፡ መጽሐፈ፡ ረከበ፡ መካነ፡ ዘይብል፡፡ በዝንቱ፡ ገጸ፡ መካን ፤ ወበገጸ፡ መ ካኒ፡ (ማቴ፳፬፡ ፴፩። ሉቃ፬፡ ፲፯። ሃይ፡ አበ)።

—፤ የቍጥር፡ መደብ ፤ የአኃዝ፡ ጉባኤ፡ በየረድፉና፡ በ የተራው፡ በየተለላው፡ የሚጣፍበት፡ (አቡሻ፡ ፲፩)። ም ስጢሩ፡ ከዚያው፡ ከቦታነት፡ አይወጣም።

(ጥ) **ከውኖ ፤ (ከወነ፡ ይኬውን፡ ይከውን። ዕብ፡ ከዌን)** ፤ መከወን ፤ ማከናወን፡ መፈጸም ፤ ማበ ጀት፡ ማዘጋጀት ፤ ማሳመር፡ ማስጌጥ ፤ ማቅናት፡ ማሳ ከት።

**ተከወነ ፤ (ከነ)** ፤ በቁሙ ፤ ተፈጸመ፡ ሥራው፡ ዐለቀለት።

**ከዋኔ ፤ (ንያት)** ፤ መከወን ፤ (ጥ፡ ክ) መከወን ፤ አከዋወን፡ ከወና።

**ክዋኔ ፤ (ኩነት)** ፤ መኾን ፤ አኳኾን፡ ኹነታ፡ ተፈጥሮ ፤ አኗኗር፡ ኑሮ። ምስጢሩ፡ እንደ፡ ህላዌ፡ ነው ፤ የባሕርይንና፡ የተረከበን፡ ጾታ፡ ያካልን፡ ሦለንታ፡ ያ ሳያል። አኀሥሥ፡ እምጥንተ፡ ክዋኔሃ፡፡ ገባሬ፡ ክዋ

ኔሁ ። ይቤ ፡ ፎጢኖስ፤ ለፌ ፡ እማርያም ፡ ክዋኔሁ ፡ ለወልድ ። ኅሊና ፡ ፍጡራን ፡ ይኄሊ ፡ አእምሮ ፡ ክዋኔሁ፤ ወባሕቱ ፡ ይስእን ። አልቦ ፡ ማኅለቅት ፡ ለክዋኔሁ ፡ (ጥበ፳ ፡ ፳፱ ። ፲፫ ፡ ፩ ። መጽ ፡ ምስ ። ፊልክ ። ቅዳ ፡ ኤጲ) ። የሀላዌን ፡ ፍች ፡ እይ፤ ከዚህ ፡ ጋራ ፡ አንድ ፡ ነው ።

**ተክወነ**፤ ተኳኊነ፤ ተከዋወነ ፡ ተከነዋወነ፤ ተቃና ፡ ተሳካ ።

**ትኳን፤ (ናት ። ዐረ ፡ ተክዊን፤ ፍጥረት)**፤ በቁሙ፤ ትኳን ፡ ያልጋ ፡ ተባይ፤ ሲበላ ፡ የሚያተክን ፡ የሚያትከነክን፤ ግማታም ፡ ከርፋታም ።

**ከዋኒም፤ (ዕብ ፡ አዳርከኒም)**፤ የገንዘብ ፡ ስም፤ ፋርሳዊ ፡ ገንዘብ ። አዳርኮኒም ፡ የብዙ ፡ ነው ። ሳንድ ፡ ሲኾን ፡ አዳርኮን ፡ አዳርከሞን ፡ ይላል ፤ ባለብሉዮች ፡ ግን ፡ ሥንቅ ፡ ልብስ ፡ ተክህኖ ፡ ይሉታል ፡ (ዕዝ፰ ፡ ፳፯) ።

**ከዊር፤ ሮት፤ (ኮረ ፡ ይከውር ፡ ይኩር ። ዐረ ፡ ከረ)**፤ መሸከም ፡ ማሸከም፤ (ላ ፡ ጥ ፡ ጣ) መጣን፤ ማንገት ፡ መቀዳጀት፤ የሸክም ፡ የጌጥ ። ለጥምጥምና ፡ ለቆብም ፡ ይኾናል ። ከረየን ፡ እይ፤ የዚህ ፡ ጎር ፡ ነው ።

**ኮር፤ (ብ ፡ አክዋር ። ዕብ ፡ ካር)**፤ በቁሙ፤ ኮርቻ ፡ ግላስ፤ መከዳ ፡ ትራስ፤ ቀንበር ። ወሀለወት ፡ ሰይፍ ፡ ታሕተ ፡ ኮር፤ ኮርቻ ፡ (ድር ፡ ሚክ) ።

**ከውር፤ (ዕብ ፡ ኩር ። ሱር ፡ ኩራ ። ዐረ ፡ ከውር)**፤ በቁሙ፤ አጕደ ፡ የማዕደናት ፡ ኹሉ ፡ መጥበሻ፤ ማቅለጫ ፡ ማፍሰሻ ። ፀከመ ፡ ይትፌተን ፡ በከውር ፡ ወርቅ ፡ ወብሩር ። ማእከለ ፡ ከውር ። ይትዌለጥ ፡ ወርቅ ፡ ውስተ ፡ ከውር ፡ ኀበ ፡ ብሩር ፡ (ምሳ፲፯ ፡ ፫ ። ሕዝ ፳፪ ፡ ፳ ። ያዕ ፡ ዘእል) ።

(ጥ) **ከወረ፤ (ይኬውር ፡ ይከውር ። ዕብ ፡ ከዌር)**፤ ጠመደ ፡ አጠመደ፤ ጋፈፈ ፡ ያዘ፤ የዓሣ ። ቀዘፈ ፡ ተረከዘ፤ መርከብን ፡ ነዳ ፡ በሥራት ፡ አስኬደ፤ በባሕር ፡ በመርከብ ፡ ሥሉጥ ፡ ኾነ ። መጽሐፍ ፡ ግን ፡ በከወረ ፡ ፈንታ ፡ ተከወረ ፡ ይላል፤ በሕተት ፡ ነው ። ኖትያት ፡ እለ ፡ ይትኬወኑ ፡ ውስተ ፡ ባሕረ ፡ ዓለም ፡ ዐሠርቱ ፡ ወክልኤቱ ፡ ሐዋርያት ። መዋግድ ፡ እለ ፡ ያበጥሙ ፡ ሐመረ ፡ ልቡ ፡ ለዘኢይክል ፡ ጻቢተ ፡ ውስተ ፡ ቀላየ ፡ መጻሕፍት ፡ ወለዘኢይትኬወር ፡ በመቃድፈ ፡ ኦሪት ፡ ወነቢያት ፡ ወበመቃድፈ ፡ ወንጌል ፡ ወሐዋርያት ፡ (መጽ ፡ ምስ ፡ ገ፷፩ ። ፻፷) ።

**ከራ፤ (ራት)**፤ ኵሬ፤ ምዕቃል ፡ የውሃ ፡ መቋሚያ ፡ መጠራቀሚያ ። የውሃ ፡ ዕቃ ፡ ታናሹም ፡ ታላቁም፤ ጽዋ ፡ ጣሳ ፡ ምንዛህ ፡ ኵስኵስት ። ከራየ ፡ ዘብሩር ፡ ደይ ፡ ውስተ ፡ ሐስሉ ፡ ለዘይንእስ ፡ ወሜጠ ፡ እክሉሂ ። ወይከውና ፡ ጻህራት ፡ ዘቤተ ፡ እግዚ ፡ ከመ ፡ ኮራት ፡ (ዘፍ ፵፬ ፡ ፪ ፡ ፱ ። ኩፋ ፡ ፵፪ ። ዘካ፲፬ ፡ ፳) ።

—፤ ጋን ፡ ዝንግሪር፤ ማድጋ ፡ ፊቀን፤ እንስራ ፡ በርሚል፤ የመሰለው ፡ ኹሉ ። ትመልእ ፡ ማየ ፡ በኮራ ፡ ሐዲስ ። ምልአ ፡ ኮራ ፡ ማየ ። ይመልአሙ ፡ በኮራቲሆሙ ፡ ማየ ፡ (ቄድር ፡ ገ፩ ። ስንክ ፡ መስ፳፯ ። ሠኔ፳፱) ።

—፤ ስመ ፡ ሀገር፤ የደብረ ፡ ሊባኖስ ፡ ገጠር ፡ ታችኛው ፡ ገዳም፤ ውሃው ፡ የማያልቅ ፡ የማይደርቅ ፡ ጠበላም ፡ ማለት ፡ ነው፤ ምስጢሩ ፡ ውሃን ፡ አይለቅም ። (የታቦት ፡ ዘፈን)፤ ትምሩኝ ፡ እንደኾን ፡ ልም(ን)ጣ ፡ ወደ ፡ ኮራ፤ ያባ ፡ ጠጋዛብ ፡ ልጅ ፡ የይቶት ፡ እዝጊያራ ።

**ኮራ**፤ ኾራ ፡ አንቦ፤ እንብ ፡ እንብ ፡ የሚል ፡ የጨው ፡ ውሃ፤ ለከብቶች ፡ የሚበጅ፤ የሚያሸርና ፡ የሚያወፍር ። ወይም ፡ ግጦ ፡ ቦረቦር፤ ጨው ፡ ጨው ፡ የሚል ፡ ዐፈር ። ይኸውም ፡ የሚገኝ ፡ በወንዝ ፡ ዳር ፡ ከዚያው ፡ ከውሃው ፡ አጠገብ ፡ ነው ።

**ኮሬ፤ (ጽር ፡ ኾሬ፤ ኾራይ)**፤ ሙራደ ፡ ማይ፤ የስን ፡ የኵስኵስት ፡ ጡት ። የላሕመ ፡ ብርት ፡ አፍ ፡ እንደ ፡ በንቧ ፡ አፍ ፡ ኹኖ ፡ ጡት ፡ ያለው፤ የሚከፈትና ፡ የሚዘጋ ። ባለቅኔዎች ፡ ግን ፡ የብረት ፡ ጋን ፡ ይሉታል፤ ፍችው ፡ አይደለም ። ወእምላዕሉሂ ፡ አናብስት ፡ ወአልሕምት ፡ ግብረ ፡ ኮሬ ፡ ሙራዱ ፡ (፫ነገ ፡ ፯ ፡ ፳፱) ። ሙራድና ፡ ኮሬ ፡ አንድ ፡ ወገን ፡ ነው፤ ዕብራይስጡ ፡ ሞራድ ፡ ያለውን ፡ ጽርኡ ፡ ኾሬ ፡ ብሎታል፤ የግእዝ ፡ መላሽ ፡ ግን ፡ ኮሬን ፡ በከንቱ ፡ አግብቶታል ። ወይም ፡ መላሽ ፡ ግብረ ፡ ኮሬሁ ፡ ያለውን ፡ ትርጓሚ ፡ ሙራዱ ፡ ብሎ ፡ በዳር ፡ አመልክቶት፤ የኋላ ፡ ጣፊ ፡ አግብቶት ፡ ይኾናል ። በብዙ ፡ መጣፍ ፡ ውስጥ ፡ ስንኳን ፡ ትርጓሜው ፡ ጥቅሱና ፡ ሐተታው ፡ ሳይቀር ፡ ገብቶ ፡ እየተጣፈ ፡ ይገኛል፤ ምክንያቱም ፡ ጥፈትና ፡ ትምርት ፡ ተባብረው ፡ ተጫፍረው ፡ ባንድ ፡ ሰው ፡ እጅ ፡ ስላልተገኙ ፡ ነው ።

**ኮሬ ፡ ኤጲስቆጶስ፤ (ጽር ፡ ኾሬፒስኮፖስ)**፤ የኤጲስቆጶስ ፡ ዐርክ ፡ ምክትል፤ እንደራሴ ፡ ወኪል፤ ወራሴ ፡ መንበር ፡ (ፍ ፡ ነ ፡ ፬ ። ፯ ፡ ፫ ። ፱ ፡ ፪) ።

**ከዊስ፤ ሶት፤ (ኮሰ ፡ ይከውስ ፡ ይኩስ ። ሐሰ)**፤ ማካወስ ፡ መበጥበጥ፤ ማወክ ፡ መድረጥ፤ መንቅነቅ ፡ ማናወጥ፤ የባሕር ፡ የኮሶ ፡ የፈሳሽ ፡ ነገር፤ ኮሶም ፡ በምሳሌ ፡ ባሕር ፡ ይባላል ። (ዕንቆቅልኽ)፤ ታናሽ ፡ ባሕር ፡ ዐጤን ፡ ታስፈር) ። ኮሶ ፡ ማለት ፡ ቅሉ ፡ የዚህ ፡ ዘር ፡ ነው ። መጽሐፍ ፡ ግን ፡ በኮስ ፡ ፈንታ ፡ አኮስ ፡ ይላል፤ በሕተት ፡ ነው ። አንተ ፡ እግዚ ፡ ዘአከውሳ ፡ ለባሕር ። አኮስካ ፡ ለባሕር ። ሰይጣናት ፡ ያከውሱ ፡ ውስተ ፡ ልቡ ፡ ብዙኃ ፡ እከያተ ፡ (ኢሳ፶፩ ፡ ፲፭ ። ሱቱ ፡ ዕዝ፩ ፡ ፲፱ ። ፊልክ ፡ ፴ ። ፴፯) ። ኮስና ፡ ሖሰ ፡ ኆሠ ፡ አንድ ፡ ዘር ፡ ናቸው፤ ስልታቸው ፡ ግን ፡ እንደ ፡ ፊደላቸው ፡ ልዩ ፡ ነው፤ ይኸውም ፡ በምስክራቸው ፡ ይታወቃል፤ ፍቻቸውን ፡ በየቦታቸው ፡ ተመልከት ።

**አኮሰ**፤ አስደረጠ፤ አስበጠበጠ ፡ አስነቀነቀ ።

**ተከውሰ**፤ ተካወሰ፤ ተናወጠ ፡ ተነዋወጠ፤ ታወከ ፡ ተደረጠ ።

**ከዉሰ** ፤ (ሳን ፡ ሳት ፡ ውስት) ፤ የተካወሰ ፤ የተናጠ ፡ የተናወጠ ።

**ከውሰ** ፤ (ዕብ ፡ ኮስ ። ሱር ፡ ካሳ ። ዐረ ፡ ካስ) ፤ ጽዋ ፡ ዋንጫ ፤ የመጠጥ ፡ መሣሪያ ፤ መቅጃ ፡ መጠጫ ፤ ማደያ ፡ መስጫ ። ኮሶ ፤ የደጋ ፡ ዛፍ ፤ የሹጥ ፡ መድኀኒት ፤ ፍሬውን ፡ ደቍሶ ፡ በጥብጦ ፡ ሲጠጡት ፡ ሆድ ፡ እያካወሰ ፡ የሚያስቀምጥ ። ድፍርስ ፡ ብጥብጥ ፡ መራራ ፡ መጠጥ ፡ ማለት ፡ ነው ፤ ሹጡም ፡ ኮሶ ፡ የሚያስጠጣ ፡ ስለ ፡ ኾነ ፡ ኮሶ ፡ ይባላል ፤ ኮሶ ፡ ታየኝ ፡ እንዲሉ ።

**ኮፒ** ፤ (ሮማይ ፡ ኮፒያ) ፤ ብዛት ፤ የጥፈት ፡ አበዛዝ ፤ ብዥ ፡ ቅጅ ፤ አንድ ፡ የነበረው ፡ ብዙ ፡ መኾን ። የማይጠፋ ፡ ቀለምና ፡ ርሳስ ፤ የሴቴ ፡ ሬት ፡ ደም ፡ የሚመስል ።

**ከሓ** ፤—**ወዲያ** ፤—**ከሀሀ ፡ ከሃ** ።

**ኵሓ** ፤—**ሓያ ፡ አሓያ** ፤—**በኵሕ ፡ በኰሐ** ።

**ከሒድ** ፤ ዶት ፤ (ክሕደ ፡ ይክሕድ ፡ ይክሐድ ። ዕብ ፡ ካሓድ ፡ ሂከሔድ ፤ ታበ ፡ ተካደ) ፤ መካድ ፤ መክዳት ፤ እምነትን ፡ ውልን ፡ መሐላን ፡ ማፍረስ ፤ መሸፈጥ ፡ ቃልን ፡ መለወጥ ፤ መዋሸት ፡ ዐሎ ፡ ማለት ፤ ማበል ፡ መወንጀል ። ክሒደ ፡ ትክሕዱኒ ። ክሕደ ፡ ሃይማኖቶ ። አምጽኡ ፡ ላዕሌነ ፡ መሐላ ፡ ዘኢንክል ፡ ክሒደ ። አምነ ፡ ወኢክሕደ ። ከመ ፡ ተዐልዎ ፡ ብእሲት ፡ ለምታ ፡ ከማሁ ፡ ክሕዱኒ ፡ ቤተ ፡ እስራኤል ፡ (ኢሳ፵፰ ፡ ፰ ። ፩ጢሞ ፡ ፭ ፡ ፰ ። ዮዲ፰ ፡ ፴ ። ዮሐ፩ ፡ ፰ ። ኤር፫ ፡ ፳) ።

**ከሓዲ** ፤ (ዲት ፤ ድያን ፡ ያት) ፤ በቁሙ ፤ የሚክድ ፡ ከዳተኛ ፡ ሸፋጭ ፤ ዐላዊ ። ይዘለፈክሙ ፡ ሕግ ፡ ከመ ፡ ከሓዲ ። ወልድ ፡ ከሓዲ ። ኢትኩኑ ፡ ከሓድያነ ፡ በእግዚ ። መላእክትኪ ፡ ከሓድያን ፡ (ያዕ፪ ፡ ፱ ። ዘዳ፴፩ ፡ ፳፰ ። ዘኍ፲፬ ፡ ፱ ። ኢሳ፩ ፡ ፳፫) ።

**አክሐደ** ፤ አስካደ ፤ አስከዳ ፡ ዐሎ ፡ አሰኘ ፤ አሳበለ ፤ ከሓዲ ፡ አደረገ ። አኀዊክሙ ፡ አክሐድዎ ፡ ለልብክሙ ። አክሐድዎሙ ፡ ወይቤልዎሙ ፡ ንዑ ፡ ናምልክ ፡ ባዕደ ፡ (ዘዳ፩ ፡ ፳፰ ። ፲፫ ፡ ፲፫) ። በክሕደና ፡ በአርሐቀ ፡ ፈንታ ፡ አክሐደ ፡ ይላል ፤ የመላሽና ፡ የጣፊ ፡ ስሕተት ፡ ነው ። ኢአምንዎን ፡ ወአክሐድዎን ። አይድዐተነ ፡ ወአክሐድናሃ ። ይቤ ፤ መኑ ፡ አክሐደከ ፡ (ሉቃ ፳፱ ፡ ፲፩ ። ኪዳ ። ቄር ፡ ጸላ) ። እስመ ፡ ያክሕዶ ፡ ለወልድከ ፡ እምኔየ ፤ ወያመልክ ፡ ባዕደ ። ትዕቢት ፡ ታክሕዶ ፡ እምነ ፡ ፈጣሪሁ ፡ (ዘዳ፯ ፡ ፬ ። ሢራ፲ ፡ ፲፪) ። በአክሐደ ፡ ፈንታ ፡ አስተክሐደ ፡ አስተክሐደ ፡ ይላል ፤ ፍችው ፡ አንድ ፡ ነው ። ከመ ፡ ያስተክሕዶ ፡ ጸጋ ፤ እግዚ ፡ እንተ ፡ ነበረት ፡ ላዕሌሁ ። ቶማስ ፡ አስተክሐዶሙ ፡ ለአኀዊሁ ፡ (ቀሌ ፡ ገ፭ ። መጽ ፡ ምስ ፡ ገ፰፰) ።

**አክሓዲ** ፤ **መክሐዲ** ፤ **መክሕድ** ፤ የሚያስክድ ፡ አስካጅ ፤ አስከጅ ።

**ተክሕደ** ፤ ተካደ ፡ ተጣለ ፡ ተተወ ፤ ተከዳ ፡ ዐሎ ፡ ተባለ ። እለ ፡ ኵሎሙ ፡ ይትከሐዱ ፡ ወይትሀጐሉ ፡ (ሔኖ፶፪ ፡ ፰) ።

**ተካሐደ** ፤ ተካካደ ፡ ተከራከረ ፤ ተሟገተ ፡ (ግብ፲፰ ፡ ፲፭ ። ፩ቆሮ ፡ ፩ ፡ ፲፭ ። ፪ጴጥ ፡ ፪ ፡ ፫) ። ትፈቅዱኑ ፡ ንትካሐዶሙ ፡ ለቃላቲከ ፡ በነገራቶሙ ፡ ለዐልዋን ፤ እስመ ፡ በተካሕዶ ፡ ይትወሊድ ፡ ለነ ፡ ባቍዕ ። ቦኑ ፡ እንከ ፡ ዘትትካሐደኒ ፡ በዝ ፡ ነገርየ ። ኢትትካሐድ ፡ በእንተ ፡ ጽድቅ ፡ (ቄር ፡ ጸላ ፡ ገ፰፰ ። ፳ ። ሢራ፬ ፡ ፳፭) ።

**ክሑድ** ፤ (ዳን ፡ ዳት ፡ ሕድ) ፤ የተካደ ፤ የተካካደ ።

**ክሕደት** ፤ (ላ ፡ ጥ) መካድ ፤ መካካድ ፡ አካካድ ። በቁሙ ፤ ክዳት ፡ አሉታ ፤ ሸፍጥ ፡ ዐመጥ ፤ በደል ፡ ወንጀል ። ዝንቱሰ ፡ ክሕደት ፤ ወአኮ ፡ ሃይማኖት ። መጽሐፈ ፡ ክሕደት ። ክሕደቶሙ ፡ ዘክሕዱከ ፡ (ታሪ ፡ ነገ ። ስንክ ፡ መስ፲፫ ። ፫ነገ ፡ ፰ ፡ ፶) ።

**ክሕድ** ፤ ጥርጥር ፡ አሉታ ፤ ኑፋቄ ፡ ክሕደት ፤ ክርክር ፡ ሙግት ፤ የነገርና ፡ የትምርት ፡ ዕንቅፋት ፡ መሰናክል ። እለ ፡ ይገብሩ ፡ ካሕደ ፡ በላዕለ ፡ ክርስቶስ ። እስመ ፡ ኵሉ ፡ ካሕድ ፡ ምግባሪሆሙ ። ዘእንበለ ፡ ካሕድ ። አልቦ ፡ ካሕድ ፡ በዝንቱ ። ያመጽኡ ፡ ካሕደ ፡ ላዕለ ፡ ትምህርትክሙ ። እብነ ፡ ካሕድ ፡ (ስንክ ፡ የካ፰ ። ኵፋ ፡ ፳፫ ። ዕብ፯ ፡ ፯ ። ቄር ። ሮሜ፲፯ ፡ ፲፯ ። ፩ጴጥ ፡ ፪ ፡ ፰) ።

**አስተካሐደ** ፤ አካካደ ፤ አሟገተ ፤ አከራከረ ።

**መስተካሕድ** ፤ (ዳን) ፤ የሚያሟግት ፡ የሚያከራክር ፤ ዳኛ ። ተሟጋች ፡ ተከራካሪ ፤ መናፍቅ ፡ ከሓዲ ። ለመስተካሕድ ፡ ብእሲ ፡ (ቲቶ፫ ፡ ፲ ። መጽ ፡ ምስ ። አፈ ፡ ድ፲፫) ።

**ከሕክሐ** ፤ (ክሂሀ ፡ ከሀሀ ። ዐረ ፡ ከዕከዐ) ፤ ቀላቀለ ፡ ደባለቀ ፤ አንድ ፡ አደረገ ፤ ቀምሞ ። ከካ ፡ ፈነከተ ፤ ፈነካከተ ፤ ፈጨ ፡ ደቈሰ ፡ ጨፈለቀ ፤ የወፍጮ ፡ የናዳ ፡ የመርግ ።

**ኰኵሕ** ፤ (ሓት ። ዕብ ፡ ኰሕ ፤ ጥንካሬ ፡ ብርታት) ፤ ጥኑ ፡ ደንጊያ ፤ ንጥፍ ፡ ዐፈር ፡ ለበስ ፤ ቋጥኝ ፡ ገዎቻ ፤ ተራራ ፡ ኰረብታ ፤ ጭንጫ ፡ ደረቅ ፡ ጥብቅ ፡ ጠጠራም ፡ መሬት ። አንቅዐ ፡ ኰኵሐ ፡ ዘሐነጸ ፡ ቤቶ ፡ ዲበ ፡ ኰኵሕ ። እግዚ ፡ ጸወንየ ፡ ወኰኵሕየ ። ጕዩ ፡ ውስተ ፡ ኰኵሐ ፡ ሬሞን ። ቦ ፡ ዘወድቀ ፡ ውስተ ፡ ኰኵሕ ፡ ኀበ ፡ አልቦ ፡ መሬት ፡ ብዙኀ ፡ (መዝ ፡ ፸፯ ። ማቴ፯ ፡ ፳፬ ። ፪ነገ ፡ ፳፪ ፡ ፪ ። መሳ፳ ፡ ፵፯ ። ማቴ፲፫ ፡ ፭ ፡ ፳) ።

**አንከሐክሐ** ፤ ፈተፈተ ፡ ተፈተፈተ ።

**ነክሕካሕ** ፤ **አው ፡ ሰከሕካሕ** ፤ ፍትፍት ። እክሽ ፡ ካካ ፤ ሐሠር ፡ ዐይነ ፡ ምድር ፤ ተቅማጥ ፡ ሻታ ፡ እሕታ ፡ የሆድ ፡ በሽታ ፤ ክብርድ ፡ የተነሣ ፡ (ኵፋ ፡ ፳፫) ።

ክሕለ፤—ቻለ፤—ክሂል፡ ክሀለ ።

ኰሐል፤ ሎት፤ (ኰሐለ፡ ይኰሕል፡ ይኰሐል ። ዕብ፡ ካሐል ። ሱር፡ ክሓል ። ዐረ፡ ከሐለ)፤ መኳል፡ ማስነካት፤ ዐይንን፡ በኵል፡ ደቄት፡ በመድኀኒት፡ መቅባት፤ ለጌጥና፡ ለፈውስ ። በእብነ፡ ፈውስ፡ ኰሐሎኒ፡ ዐይነ ። አንተሰ፡ ኰሐሎ፡ ዝኩ፡ ሐሞተ፡ ውስተ፡ አዕይንቲሁ ። ለዘተወልደ፡ ዕዉር፡ አሕየዎ፡ ክርስቶስ፡ ኰሒሎ፡ አዕይንቲሁ፡ ጽቡረ፡ (ስንክ፡ ታኅሣ፳፱ ። ጦቢ፲፩፡ ፯ ። ሲኖዶ) ።

—፤ መተኰስ፡ አመሳቅሎ፡ መጥበስ፤ የሴባን፡ ግንባር፡ በጋለ፡ ብረት፡ ማመልከት፤ ለክብትም፡ ይኾናል ። እመ፡ ቦ፡ ብእሲ፡ ዘይበውእ፡ ውስተ፡ ምሥዋዕ፡ መዓልተ፡ አው፡ ሌሊተ፡ ወይነሥእ፡ እምውስቴታ፡ ምንተኒ፡ ይኰሕልዎ፡ በንጺን፡ ርሱን ። ወተአዘዙ፡ መገብት፡ አመ፡ ሆሳዕና፡ ተዐርቀ፡ ጽልመተ፡ ይኰሕልዎ፡ ለፀሓይ፡ ዘ(ሠ)በረቀ፡ (ፍ፡ ነ፡ ፵፱ ። ቅኔ) ።

ኰሓሊ፤ (ሊት፡ ልያን፡ ያት፤ ሐልት)፤ የኳለ፡ የሚኵል፤ ኳይ፡ ተኳሽ ።

ተኰሕለ፤ ተኳለ፡ ተቀባ፤ ተተኰሰ ። ተኰሕሎት፡ ወአሠንየ፡ ቀራንብት ። በተኰሕሎትን ። ተኰሕለት፡ አዕይንቲሃ፡ (ሔኖ፰፡ ፩ ። ፈ፡ መ፡ ፴፱፡ ፰ ። ፪ነገ፡ ፱፡ ፴) ።

ኩሑል፤ (ላን፡ ላት፡ ሕልት)፤ የተኳለ፤ የተቀባ፤ ተኰሳም፡ ምልክታም ።

ኰሕል፤ (ላት)፤ በቁሙ፡ ኵል፤ ጥቍር፡ ሰማያዊ፡ የቀለም፡ ደንጊያ፤ ተደቍሶ፡ ዓይን፡ የሚቀባ፡ የሚኳል፤ ጌጥነት፡ ከመድኀኒትነት፡ ስላለው፡ በኹለት፡ ወገን፡ የሚፈለግ ። አዕይንት፡ እለ፡ ስርግዋን፡ በኰሕል ። ብንተ፡ አዕይንቲሁ፡ ከመ፡ ኰሕል፡ ወጸሊም፡ ጽሕሙ ። ተኰሕልኪ፡ ኰሕለ፡ (ግንዘ ። ስንክ፡ ሐምሌ ። ኤር፬፡ ፴) ።

ኰሕሊ፤ (ዐረብ)፤ ኰሕላዊ፤ ኵልማ፡ የኵል፡ ዐይነት፤ ጥቍረቱ፡ ኵል፡ የሚመስል ።

ኰሐስ፤ ሶት፤ (ኰሕሰ፡ ይኰሕስ፡ ይኰሐስ ። ዕብ፡ ካሐሽ)፤ መክሳት፡ መቅጠን፤ ማነስ፡ መኰስሰ፡ ከሻዋ፡ መኾን፤ የገላ ። ማቅበር፡ መለገም፤ ሳይሸር፡ የሻረ፡ መምሰል፤ ወይም፡ መስፋት፡ መግነን፤ የቍስል ። ኰሕሰ፡ ጸልዕኪ ። እምቅድመ፡ ይጺሑ፡ ወይኰሐሱ፡ ቍስላተ፡ ነፍስየ፡ (ናሖ፫፡ ፲፱ ። አረጋ፡ ድ፴፮) ።

ኰሕስ፤ ክሳት፡ ኰሳስነት፤ የቍስል፡ ስፋት ። ኀፍረተ፡ ብእሲት ።

ኬጢኢም፤ (ጽር፡ ኬቲይም ። ዕብ፡ ባቲም)፤ ቤቶች፤ ድንኳኖች፤ ወይም፡ የድንኳን፡ ቁር በቶች፡ በስተላይ፡ ጠፈር፡ መዋቅር፡ የሚኾኑ፡ (፪ነገ፡ ፳፫፡ ፯) ።

ኽጥሜ፤—ሰላጣ፡ ሥንቆ፤—ኀጥሜ ።

ኬጥሮጋውሎስ፤ (ጽር፡ ኪትሮክፍሉስ ። ዕብ፡ ኪዮሮት)፤ የብረት፡ ጋኖች፤ ታላላቅ፡ ድስቶች፤ ለማብሰያ፡ ለመቀቀያ፤ ወይም፡ ውሃ፡ ለመምሊያ፡ ለመታጠቢያ፡ የተሠሩ፤ ለታናናሾችም፡ ይነገራል፡ (፫ነገ፡ ፯፡ ፴፰) ።

ኪያ፤ (ዐረ፡ ኢያ ። ዕብ፡ ኤት፤ አት)፤ የገቢር፡ ዐጸፋና፡ ቅጽል ። ለልን፡ ተመልክት፤ ይህም፡ እንደዚያ፡ ነው፤ አለዝርዝር፡ ብቻውን፡ አይገባም ። ምንጩና፡ ሥሩ፡ አየየ፡ ነው፤ አ፡ በከ፡ ተለውጦ፡ ኢያ፡ በመባል፡ ፈንታ፡ ኪያ፡ ተብሏል፤ ይኸውም፡ ባረቡ፡ ይታወቃል ።

ኪያየ፤ (ከ፡ ኪ፡ ሁ፡ ሃ ። ነ፡ ክሙ፡ ክን፡ ሆሙ፡ ሆን)፤ እኔን፤ ራሴን ። ቦኑ፡ ኪያየ፡ ትፈርሁ ። ኪያከ፡ ንሴብሕ ። እስመ፡ ኪያኪ፡ ሠምረ ። ኪያሁ፡ ኅረየ ። ዘኪያሃ፡ አፍቀረ፡ (ኤር፭፡ ፳፪ ። ኪዳ ። ውዳ፡ ማር፬ ። ሚራ፵፭፡ ፬ ። ፬፡ ፲፪) ። እፎ፡ እንከ፡ ኪያነ፡ ያድኅኑ ። እፎ፡ እንከ፡ ፈድፋደ፡ ኪያክሙ ። ወኪያ ክንሂ ። በእንተ፡ ፈጢሮትየ፡ ኪያሆሙ ። ወኪያሆን፡ (ኢሳ፳፡ ፮ ። ማቴ፮፡ ፴ ። ዘረፋ ። ዘፍ፮፡ ፯ ። ዘሌ፳፡ ፲፬) ። አንዳንድ፡ ጊዜም፡ በተገብሮ፡ ዐጸፋ፡ በለሊሁና፡ በውእቱ፡ በሎቱና፡ በቦቱ፡ ፈንታ፡ ተጥፎ፡ ይገኛል፤ የመላሽ፡ ስሕተት፡ ነው ። እወ፡ ውእቱ፡ ኪያሁ ። ወኰሎሙ፡ ርቱዓነ፡ ልብ፡ እለ፡ ኪያሃ፡ ቦሙ ። እለ፡ ሀለዉ፡ በኪያሆን፡ መዋዕል ። ጸውዖ፡ ኪያሁኒ፡ ውስተ፡ በዓል ። ነዋ፡ አምላክነ፡ ዘኪያሁ፡ ተወከልነ፡ (አፈ፡ ድ፲፩ ። መዝ፡ ፺፫ ። ዮዲ፬፡ ፯ ። ጦቢ፱፡ ፪ ። ኢሳ፳፭፡ ፱) ። ቅጽል፡ መኾኑም፤ በዝኩና፡ በውእቱ፡ ፈንታ፡ ሲገባ፡ ነው ። ኪያሁ፡ መንፈሰ፡ ነሚአሙ ። ይሠውዐ፡ ኪያሃ፡ መሥዋዕተ ። አሬኢኑ፡ እንጋ፡ ኪያሃ፡ ዕለተ፡ ቢል፤ ያንን፡ መንፈስ፡ ያችን፡ መሥዕት፡ ያችን፡ ዕለት፡ ያሰኛል፡ እንጂ፤ ርሱን፡ ርሷን፡ ማለት፡ አይስማማም፡ (ስንክ፡ ግን፲፰ ። ዕብ፲፡ ፲፩ ። ተረ፡ ቄር) ። (ዕር ፲፱፡ ቍ፶፲፱) ።

ከዩድ፤ ዶት፤ (ኬደ፡ ይከይድ፡ ይኪድ ። ረገፀ፡ ኄደ)፤ መኼድ፤ መርገጥ፡ መዳጥ፡ መደፍጠጥ፤ መጠቅጠቅ፡ ማጥቃት፤ በእግር፡ በጫማ፡ በርግጫ፡ መምታት፤ ያውድማ፡ የነደ፡ የወይን፡ የጭቃ፡ የልብስ፡ የሰው ። ይከይድዋ፡ ለሞአብ፡ ከመ፡ ዘይከይዱ፡ እክለ፡ በመንኰራኵር ። ኬዱኒ፡ ከመ፡ ጽቡር ። ነዳይ፡ እመ፡ ወድቀ፡ ይከይድዎ፡ ቢጹ ። ወኬዱኒ፡ ፀርየ ። ከመ፡ ትኪዶሙ፡ (ኢሳ፳፭፡ ፲ ። ኢዮ፴፡ ፲፱ ። ሚራ፲፫፡ ፳፩ ። መዝ፡ ፶፭ ። ኩፋ፡ ፴፩) ።

—፤ መሄድ፡ መራመድ፤ እግሮችን፡ እያፈራረቁ፡ ማንሣትና፡ መጣል፡ መንቀልና፡ መትከል፤ ምስጢሩ፡ ከዚያው፡ ከመርገጥ፡ አይወጣም፤ ሀይድን፡ እይ ። ፍኖተ፡ ረሲዓን፡ ኢትኪድ ። ሰከይደ፡ አሠሮሙ ። ወኀበኒ፡ ኬደ፡ ይደምፅ፡ እግሩ፡ በቃለ፡ ፀዓዐ፡ (ምሳ፬፡ ፲፬ ። ኩፋ፡ ፳፩ ። ሚራ፴፭፡ ፱) ። አንዳንድ፡ መጣፍ፡

በኬደ ፡ ፈንታ ፡ እንዳማርኛው ፡ አኬደ ፡ ይላል ፤ አያስኼም ። ኢያከይዱ ፡ ወይነ ፡ ውስተ ፡ ምክያድ ። ያከይዱ ፡ እክለ ፡ ወወይነ ። ተንሥኢ ፡ አኪዲዮሙ ። ላሕም ፡ ዘያከይድ ፡ (ኢሳ ፲፮ ፡ ፲ ። ነሐ ፲፫ ፡ ፲፭ ። ሚክ ፮ ፡ ፲፫ ። ዘዳ ፳፭ ፡ ፬) ።

**ከያዲ** ፤ (ዲት ፡ ድያን ፡ ያት) ፤ የሚረግጥ ፡ ረጋጭ ፤ አጥቂ ፡ ጠቅጣቂ ።

**አኬደ** ፤ አስረገጠ ፤ አበራየ ። ኢትፍፅሞ ፡ አፉሁ ፡ ለላሕም ፡ ሶበ ፡ ታከይድ ፡ እክለከ ። ወዘኒ ፡ ያከይድ ፡ እክለ ፡ (፩ጢሞ ፡ ፭ ፡ ፲፰ ። ፩ቆሮ ፡ ፱ ፡ ፱ ፡ ፲) ።

—፤ አስኬደ ፤ አስሮጠ ፤ ነዳ ። አኬድከ ፡ ውስተ ፡ ባሕር ፡ አፍራሲከ ። ወያከይዳ ፡ ለሐመሩ ፡ (ዕንባ ፡ ፲፭ ። ማር ፡ ይሥ፳፰) ። በዐጸደ ፡ ፈንታ ፡ አኬደ ፡ ይላል ፤ የመላሽ ፡ ስሕተት ፡ ነው ፤ ለእመ ፡ አኬድከ ፡ እክለ ፡ ገራህትከ ። ያከይድ ፡ ዘርዐ ፡ ሠዊት ፡ (ዘዳ ፳፬ ፡ ፲፱ ። ኢሳ ፲፯ ፡ ፭) ።

**ተከይደ** ፤ ተረገጠ ፡ ተጠቀጠቀ ፤ ተናቀ ፡ ተጠቃ ፡ ተጨቈነ ። ውስተ ፡ መካን ፡ እንተ ፡ ኢተከይደት ። መቅደስ ፡ ወኀይል ፡ ተከይደ ። አርዌ ፡ ተከይደ ፡ ወከይሲ ፡ ተቀትለ ፡ (ጥበ ፲፩ ፡ ፪ ። ዳን ፰ ፡ ፲፫ ። ኪዳ) ።

**ከዩድ** ፤ (ዳን ፡ ዳት ፡ ይድ) ፤ የተረገጠ ፡ የተጠቃ ፡ ጥቁ ። ሕዝብ ፡ ቅቡጻን ፡ ወከዩዳን ፡ (ኢሳ ፲፰ ፡ ፪) ።

**ኪደት** ፤ መርገጥ ፤ መረገጥ ፤ አረጋገጥ ፤ ርግጫ ፤ ጫማ ፡ ሰኰና ፡ (ስንክ ፡ መጋ ፲፩ ። ኢሳ ፳፪ ፡ ፭) ። ወኢታገምር ፡ ፍኖታ ፡ ዘእንበለ ፡ አሐቲ ፡ ኪደተ ፡ እግረ ፡ ብእሲ ፡ (ሱቱ ፡ ዕዝ ፭ ፡ ፯) ።

**ተከየደ** ፤ ተራገጠ ፤ ተረጋገጠ ። እስከ ፡ ይትካየዱ ፡ በበይናቲሆሙ ፡ (ሉቃ ፳፩ ፡ ፩) ። በኬደ ፡ ፈንታ ፡ ተክየደ ፡ ይላል ፤ ስሕተት ፡ ነው ። ይትካየድዋ ፡ አሕዛብ ፡ (ራእ ፲፩ ፡ ፪) ።

**መከየድ** ፤ (ብ ፡ መካይድ) ፤ መርገጫ ፡ መኼጃ ፤ ጫማ ፡ ውስጥ ፡ እግር ፡ ዝርጉ ፡ ጠፍጣፋው ። መካነ ፡ መከየደ ፡ እገርየ ። በማእከለ ፡ መከየደ ፡ እገሪሁ ፡ ወፅአ ፡ ቍስል ። ፍቅርኪ ፡ ሠረጸ ፡ ውስተ ፡ ልብየ ፡ ወከነ ፡ ሥረዊሁ ፡ እስከ ፡ መካይድየ ። ሰላም ፡ ለመካይድኪ ፡ እለ ፡ ረከቦን ፡ መከራ ፤ እንበለ ፡ አሣእን ፡ አመ ፡ ሖራ ፡ (ሕዝ፵፫ ፡ ፯ ። ገድ ፡ ተክ ። አርጋ ፡ ፭ ። ደራሲ) ።

—፤ ድኳ ፡ ግርንቡድ ፤ ሉሕ ፡ ምንጣፍ ፡ የእግር ፡ ድጋፍ ፡ ማረፊያ ። በማይኒ ፡ መንበርየ ፡ ወምድርኒ ፡ መከየደ ፡ እገርየ ። ወኢተዘከረ ፡ መከየደ ፡ እገሪሁ ፡ በዕለተ ፡ መዐቱ ። ኣገብኦሙ ፡ ለጸላእትከ ፡ ታሕተ ፡ መከየደ ፡ እገሪከ ፡ (ኢሳ፷፮ ፡ ፩ ። ሰቈ፪ ፡ ፩ ። መዝ ፡ ፻፱) ።

—፤ የንጨት ፡ ሰገነት ፤ ደርብ ፡ መረባርብ ፡ እንደ ፡ ቈጥና ፡ እንደ ፡ ማማ ፡ ኹኖ ፡ ለመስበኪያና ፡ ለማንበቢያ ፡ ላዋጅ ፡ መንገሪያ ፡ የተሠራ ፤ ዕርከንና ፡ መሰላል ፡ ያለው ። ወቆመ ፡ ዕዝራ ፡ ላዕለ ፡ መከየድ ፡ ዘዕፀ ፡ (ነሐ፰ ፡ ፬) ።

—፤ ጫማ ፡ ወይም ፡ መጫሚያ ፤ የውስጥ ፡ እግር ፡ ቤዛ ። ዲበ ፡ ኤዶምያስ ፡ እሰፍሕ ፡ መከየድየ ፡ (መዝ ፡ ፶፱ ። ፻፯) ።

—፤ የጫማ ፡ ልክ ፡ መጠን ፤ በፍሩ ፡ ወይም ፡ አሠሩ ። ዐሥርቱ ፡ ወክልኤቱ ፡ መከየደ ፡ እግር ፡ (ፍ ፡ ነ ፡ ፴፯) ።

—፤ ስክተት ፤ የዐምድ ፡ ሥር ፡ መሠረት ፤ መብቀያውና ፡ መተከያው ። አዕማደ ፡ ወርቅ ፡ እለ ፡ ይቀውሙ ፡ ዲበ ፡ መከየደ ፡ ብሩር ። ወመካይዲሆን ፡ ኅምስቱ ፡ ዘብርት ፡ (ሢራ ፳፮ ፡ ፲፰ ። ዘፀ ፴፯ ፡ ፯—፱) ። በመከየድ ፡ ፈንታ ፡ ምከያድ ፡ ይላል ፤ አያስኼም ። አሠረ ፡ ምክያደ ፡ ብእሲ ፡ (ስንክ ፡ ታኅ፲) ።

**ምክያድ** ፤ (ዳት) ፤ ዐውድማ ፡ ተረግጦ ፡ የጠበቀ ፡ መሬት ፤ ያዝመራ ፡ መውቂያ ፡ ማበራያ ፤ ፍሬን ፡ ከገለባ ፡ መለያ ፤ ማምረቻ ፡ ማግረጃ ። የወይን ፡ መርገጫ ፤ የዘይት ፡ የሰሊጥ ፡ የቅባኑግ ፡ ማውጫ ። ምክያደ ፡ እክል ። ምክያደ ፡ ወይን ። ትበውኡ ፡ ውስተ ፡ ምክያድ ፡ ትቅድሑ ። ምክያዳቲሆሙ ፡ (፫ነገ ፡ ፳፩ ፡ ፩ ። ዘኍ፲፰ ፡ ፳፯ ። ሐጌ፪ ፡ ፲፯ ። ፍ ፡ ነ ፡ ፲፰) ። መዘግብት ፡ በማለት ፡ ፈንታ ፡ ምክያዳት ፡ ይላል ፤ ስሕተት ፡ ነው ። ተነሥቱ ፡ ምክያዳት ፡ (ዮኤ፩ ፡ ፲፯) ።

**ኬደ** ፤ **ከየደ** ፤ (ዐረ ፡ ዐሂደ ። ዕብ ፡ ዐዌድ ፤ ሄዒድ) ፤ አዋለ ፡ አሰረ ፤ ውል ፡ አደረገ ፤ ነገርን ፡ ቈረጠ ፡ አጠበቀ ፡ አጠና ፤ በቃል ፡ በጥፈት ፤ የሥራ ፡ የንግድ ።

**ተከየደ** ፤ ተዋዋለ ፤ ተጣጣፈ ፤ ቃል ፡ ኪዳን ፡ ተጋባ ፡ ተማማለ ፤ ነገር ፡ ተቋረጠ ። ተካየዶሙ ፡ በእደ ፡ ነቢያት ። ተካየዱ ፡ ዮናታን ፡ ወዳዊት ፡ ኪዳነ ። ተካየድነ ፡ ምስለ ፡ ሞት ። ተካየዶ ፡ ከመ ፡ ያውስብ ፡ ወለቶ ፡ (፪ነገ ፡ ፲፯ ፡ ፲፫ ። ፩ነገ ፡ ፲፰ ፡ ፫ ። ኢሳ፳፰ ፡ ፲፭ ። ስንክ ፡ ሚያ፳፫) ።

**አስተከየደ** ፤ አዋዋለ ፡ አማማለ ፤ ቃል ፡ ኪዳን ፡ አጋባ ። ወአስተካየደ ፡ ዮዳሄ ፡ ኪዳነ ፡ ማእከለ ፡ ቤተ ፡ እግዚ ፡ ወማእከለ ፡ ቤተ ፡ ንጉሥ ፡ ወማእከለ ፡ ሕዝብ ፤ ከመ ፡ ይኩኑ ፡ ሕዝበ ፡ እግዚ ። አስተካየድዎ ፡ ከመ ፡ ኢ ፡ (፬ነገ ፡ ፲፭ ፡ ፲፯ ። ስንክ ፡ ሠኔ፲፪) ።

**ኪዳን** ፤ (ናት ። ዐረ ፡ ዐህድ ። ዕብ ፡ ብሪት ። ሱር ፡ ቅያም) ፤ በቁሙ ፤ ውል ፡ ቁም ፡ ነገር ፤ የፍቅርና ፡ ያንድነት ፡ መሐላ ፤ ሰላማዊ ፡ ሕግ ፡ ኹለቱን ፡ ወገን ፡ አንድ ፡ የሚያደርግ ፤ ስለ ፡ ረብና ፡ ስለ ፡ ጥቅም ፡ በተስፋ ፡ የቆመ ፡ የተጣፈ ፡ ሥርዐት ፤ ቢያፈርሱት ፡ ጉዳትና ፡ ጠብ ፡ የሚያመጣ ፡ ጥቅም ፡ የሚያሳጣ ። ወኵሎ ፡ ኪዳነ ፡ ዘተካየዶሙ ፡ ኢዐቀቡ ። ግበሩ ፡ በከመ ፡ ኪዳንክሙ ። ወኢይፀራዕ ፡ ኪዳነ ፡ ጼው ። ኪዳን ፡ ዘጽኑዕ ። መጽሐፈ ፡ ኪዳን ። ኪዳን ፡ ብሊት ፡ ወሐዳስ ። አይሁድ ፡ እለ ፡ መኑ ፡ ኪዳናት ፡ (፬ነገ ፡ ፲፯ ፡ ፭ ። ስንክ ፡ ጥቅ፲፱ ። ኩፉ ፡ ፳፩ ። ገላ፫ ፡ ፲፭ ። ዮሴፍ ። አርጋ ፡ ፭ ። ዲድ ፡ ፴፫) ።

**ኪዳን** ፤ የመጽሐፍ ፡ ስም ፤ ተረፈ ፡ ወንጌል ፡ የጌታና ፡ የሐዋርያት ፡ ቃል ፤ ከትንሣኤ ፡ እስከ ፡ ዕርገት ፡

ያስተማራቸው፤ እየጠየቁት፡ የመለሰላቸው። ከዕርገት፡ በኋላ፡ ከወንጌል፡ በፊት፡ በጥንተ፡ ስብከት፡ ጥፈውታል፤ እንደ፡ ሔኖክ፡ ፪፡ ክፍል፡ አለው፤ ማስተማሩንም፡ ሉቃስ፡ ይመሰክራል፡ (ግብ፩፡ ፪፡ ፫)። መጽሐፈ፡ ኪዳን፡ ዘእግዚእነ፡ ኢየሱስ፡ ክርስቶስ። ጸሐፍዎ፡ ለዝ፡ ኪዳን፡ ዮሐንስ፡ ወጴጥሮስ፡ ወማቴዎስ፡ እንዘ፡ ያጽሕፎሙ፡ እግዚእነ፤ ወፈነዉ፡ በእርኤዩ፡ ዝ፡ ግጽወ፡ እምኢየሩሳሌም፡ (ክፍል፡ ፩)።

**ኪዳን፡ ዘነግህ፤** ከመጽሐፈ፡ ኪዳን፡ የወጣ፡ የነግህ፡ ጸሎት፤ ቀሳውስት፡ ጧት፡ ጧት፡ የሚያደርሱት። ከዚህ፡ ሌላ፡ ደግሞ፡ ፯፡ ክፍሎች፡ አሉ፤ ኹሉም፡ በቅዳሴ፡ ውስጥ፡ ይገኛሉ፤ ያንድነት፡ ስማቸው፡ ፯ቱ፡ ኪዳናት፡ ይባላል።

**ኪዳነ፡ምሕረት፤** የማርያም፡ ስም፤ ወይም፡ የኪዳኗ፡ በዓል፡ በየካቲትና፡ በናሴ፡ ባ፲፮፡ ቀን፡ የሚውል፤ ትእምርተ፡ ኪዳን፡ ማለት፡ ነው፤ ቀስተ፡ ደመና፡ እንደ፡ ማለት፤ ቀስቱም፡ ቅሉ፡ በሕፃናት፡ አፍ፡ የማሪያም፡ መቀነት፡ ይባላል። (የታቦት፡ ዘፈን)፤ ኪዳነ፡ ምሕረት፡ ዘላለም፡ እመቤት። ሰላም፡ ለኪ፡ ኪዳነ፡ ምሕረት፡ እምነ፡ (ደራሲ)።

**ኪያህክ፤ ኪያክ፤ (ቅብጥ)፤** ስመ፡ ወርኅ፡ ራብዕ፤ ታኅሣሥ። ወኪያህክ፡ ይሰመይ፡ ማኅኑ፤ ወዓዲ፡ ይሰመይ፡ ሰዋዋ፡ (አቡሻ፡ ፰)።

**ኪዮኪሉ፤ (ዕብ፡ ኪ፡ዮክሉ)፤** እስመ፡ ይንእሱ፤ ያንሳሉና፡ (ሕዝ፵፪፡ ፭)።

**ኪማ፤ (ዕብ፡ ኪማህ)፤** የ፯ቱ፡ ከዋክብት፡ ተራ፤ ጸታቸውና፡ ምግብናቸው፡ አክኼዳቸው። ኪማ፡ ወኬሴላ፡ (ዓሞ፭፡ ፰)።

**ከዩን፤ ኖት፤ (ኬነ፤ ከየነ፡ ይከይን፡ ይኪን)፤** መቻል፡ መስላት፤ ቹል፡ ስል፡ መኾን፤ ለመውጋት፡ ለመቍረጥ፡ መዘጋጀት፤ የብረት። ብልኅ፡ መኾን፤ ሥራ፡ ማወቅ፡ በሥራ፡ መራቀቅ፤ ሐዲስ፡ ነገር፡ መፍጠር፤ መኪና፡ ማውጣት። በልኅንና፡ ጠበን፡ ተመልከት፤ የዚህ፡ ጎሮች፡ ናቸው። መጽሐፍ፡ ግን፡ በኬነ፡ ፈንታ፡ ኬነወ፤ ተኬነወ፡ ይላል፤ ተ፡ ከንቱ፡ ነው። ተኬነዉ፡ ሎልክሙ፡ እለ፡ ትስሕቱ። በተኬንዎ፡ ምግባር። ዘዐቢይ፡ በተኬንዎቱ፡ ወኅያል፡ በምግባሩ። ልብሰ፡ ብሩህ፡ ዘኢተኬነዎ፡ እደ፡ ዕጓለ፡ መሕያው፡ (ኢሳ፵፮፡ ፭። ጥበ፲፫፡ ፲። ቅዳ)።

**ከያኒ፤ ኬንያ፤ (ያት)፤** ብልኅ፡ ጠቢብ፤ ብልኅተኛ፡ ጥበበኛ፤ ሥራ፡ ዐዋቂ፡ አንጥረኛ፡ ባለመኪና፤ ፈጣሪ፡ ሐኪም፡ ወጌሻ፤ መሐንድዝ፡ ፈላስፋ፡ በፍጥረት፡ በሥራ፡ የሚራቀቅ፤ ጥሩ፡ ዕውቀት፡ ያለው፡ (ማሕ፯፡ ፪። ዕብ፲፩፡ ፲። ጥበ፯፡ ፳፩)። አንተ፡ ኬንያሁ፡ ለኵሉ፡ ፍጥረት። ኬንያ፡ ፍጥረትነ። ኬንያት፡ (ድጓ። ቅዳ። ስንክ፡ ኅዳ፲፮)።

**ኬናዊ፤ (ዊት፡ ውያን፡ ያት፤ ነውት፤ ኬነወ)፤** ዝኒ፡ ከማሁ። ኬነውት፡ (ስንክ፡ መስ፭)።

እንዳንድ፡ መጽሐፍ፡ ግን፡ በኬንያትና፡ በኬነውት፡ ፈንታ፡ ኪነት፡ ኬነት፡ ይላል፤ የጣፊ፡ ስሕተት፡ ነው። ኪነተ፡ ዕፀ። ኪነተ፡ አሕማር። ያስተጋብሮሙ፡ ለኪነት፡ ወይሁቦሙ፡ ብዙኀ፡ ንዋየ። ወያስተጋብኦሙ፡ ለኵሉ፡ ኬነት። ኤልያብ፡ ሊቀ፡ ኬነት፡ ዘማእነም? (ኩፋ፡ ፲፭። ራእ፲፰፡ ፲፯። ግብ፲፱፡ ፳፬፡ ፳፭። ዘፀ፴፯፡ ፳፮)።

**ኪነት፤ (ታት)፤** መጠበብ፤ መራቀቅ፤ ጥበበኛነት። የእጅ፡ ጥበብ፤ ተግባረ፡ እድ። ኪነተ፡ ንዋየ፡ ጸብእ። ኪነታቲሆሙ፡ (ዮሴፍ። ፊልክ፡ ፫)።

**ኪን፤ (ብ፡ ኪናት)፤** ጥበብ፡ ብልኀት፤ ተንኰል፡ ርቀት። ዘእንበለ፡ ኪን። በሥነ፡ ኪኑ። ኪነ፡ ዕንቍ። ዘቦቱ፡ ኪን፡ በወርቅ። ኪን፡ ዘሕንጻት። ኪነ፡ ሠራዪ። ርእዩ፡ ኪኖ፡ ወምግባሮ፡ ለሰይጣን፡ (ጥበ፲፬፡ ፬። ፲፫፡ ፲፭። ዘፀ፴፭፡ ፴፫። ፩ዜና፡ ፳፫፡ ፲፭። ዮሴፍ። ቀሌ። ዲድ፡ ፴፪)።

—፤ ሥራ፡ ተግባር፡ በየስሙና፡ በያይነቱ፡ ማናቸውም፡ ኹሉ። ኢትትማከር፡ ምስለ፡ አብድ፡ እንበይነ፡ ኪን። ከመ፡ ይጥብቡ፡ በኪኖሙ። ተምህረ፡ ኪነ፡ እድ፡ ለሲሳየ፡ ዕለቱ፡ (ሢራ፴፯፡ ፲፭። ፴፰፡ ፴፬። ፊልክ፡ ፩)።

—፤ መሣሪያ፡ መኪና፤ ወይም፡ ሥራ፤ ተደራጊና፡ ተሠሪ። አውዕዩ፡ ሞግአ፡ ኀጺን፡ ወኵሎ፡ ኪነ፡ ዘንዋየ፡ ጸብእ። ይብሎኑ፡ ኪን፡ ለኬንያሁ። ኵሉ፡ ኬንያ፡ ወኵሉ፡ ኪን፡ ኢይትረከብ፡ (ዮሴፍ። ኢሳ፳፱፡ ፲፮። ራእ፲፰፡ ፳፪)።

**ኬነወ፤ ተኬነወ፤** ከዩን፡ ኬነ፡ ከየነ።

**መኪና፤ (ጽር፡ ሜካኔ)፤** በቁሙ፤ መዘውር፡ የጥበብና፡ የብልኀት፡ መሣሪያ፤ ሥራን፡ ኹሉ፡ በፍጥነት፡ የሚያስኬድ።

**ኩናት፤ (ታት፤ ኵያንው። ዕብ፡ ሐኒት። ዐረ፡ ሐርበት)፤** ጦር፡ ዘገር፤ መውጊያ፡ መዘርከቻ፤ በብልኀት፡ በጥበብ፡ የተሠራ፤ የሰላ፡ የቾለ። ንሣእ፡ ወልታ፡ ወኩናተ። ኩናታተ፡ ወአርማሐ። ወላትው፡ ወኵያንው፡ (መዝ፡ ፴፬። ፪ዜና፡ ፲፩፡ ፲፪። ፳፫፡ ፱)።



ኩናት፡

**ኬፋ፤ ኬፋስ፤—ኰኵሕ፤—ከፊአ፡ ከፍአ።**

**ኬሰ፤ (ይከይስ፡ ይኪስ፤ ከዩስ። ኰዐሰ፤ ለወየ፤ ጠወየ)፤** ዐጠፈ፡ ጠቀለለ፤ ሰበሰበ፤ የልብስ፡ የገመድ፡ የሽቦ። ታጠፈ፡ ተጠቀለለ። ግስነቱ፡ ከኰዐሰና፡ ከለወየ፡ የተዳቀለ፡ ነው፤ የ፡ ከለወየ፡ መጥፋቱ፡ በዐ፡ ፈንታ፡ ገብቷል። የኹሉንም፡ ፍች፡ በየቦታው፡ እይ።

**ከይሲ፤(ብ፡ አክ(ካ)ይስት፤ አኪስት)፤** እባብ፤ ዘንዶ። ከይሲ፡ ተጠብለለ፡ ውስተ፡ ክሣዱ። ስነ፡ አክይስት፡ ዘቦቱ፡ ሕምዝ። ወሀሎ፡ ከይሲ፡ ዐቢይ፡ ዘያመልክዎ፡ ሰብአ፡ ባቢሎን። ወትከይድ፡ አንበሳ፡ ወከይሴ። ወናሁ፡ ክልኤቱ፡ አክይስት፡ ዐበይት፡ (ስንክ፡ ሐምሌ ፳፱። ጥበ ፲፮፡ ፲። ዳን ፲፫፡ ፳፱። መዝ፡ ፺። አስቴ ፩፡ ፭)።



ከይሲ፡

—፤ ዐዞ፡ ደራጎን፤ የባሕር፡ ትመን። ሰበርከ፡ ርእሰ፡ ከይሲ፡ በውስተ፡ ማይ። ይቀትሎ፡ ለከይሲ፡ ዘውስተ፡ ባሕር። አክይስትኒ፡ ወኵሉ፡ ቀላያት፡ (መዝ፡ ፸፫። ኢሳ ፳፯፡ ፩። መዝ፡ ፻፵፰)።

—፤ ዐንበሪ፡ ሌዋታን፤ ዲያብሎስ፡ ሰይጣን። ከይሲ፡ ዘፈጠርከ፡ ይሣለቅ፡ ላዕሌሆሙ፡ በምክረ፡ ከይሲ፡ ርጉም፡ (መዝ፡ ፻፫። ቅዳ፡ አፈ)። ስንን፡ እናብስት፡ በማለት፡ ፈንታ፡ ግርማ፡ አክይስት፡ ይላል፤ የመላሽ፡ ስሕተት፡ ነው። ብሄሞትንና፡ ሌዋታንን፡ እይ፡ (ኢዮ ፵፡ ፲)።

**ኪስ፤ (ብ፡ አክያስ። ዕብ፡ ወዐረ፤ ኪስ። ሱር፡ ኪሳ)፤** በቁሙ፤ ታናሽ፡ ከረጢት፡ ቍናማት፡ የገንዘብ፡ መያዣ፤ ማስሪያና፡ መቈለፊያ፡ ያለው፡ በጀብ፡ የሚያዝ። ፈትሐ፡ ኪሶ፡ ወአውፅአ፡ ወርቀ፡ (ዮሴፍ)። ጅብ፤ በኮት ብክቡት፡ በቀሚስ፡ በሴደርያ፡ ላይ፡ በውስጥ፡ በአፍኣ፡ የሚሰፋ፡ የልብስ፡ ጓዳ። ሐሰል፤ ሠቅ፤ ጆንያ፡ ኬሻ። ጆን፡ ሀንዲ፡ ነው።

**ኳኳ፤ (ጽር፡ ከከስ)፤** ጥሩ፡ ቀይ፡ ቀለም፤ ወይም፡ በቀይ፡ ቀለም፡ የታለለ፡ ልብስ፡ ፈትል። ባለብሉዮች፡ ግን፡ ጥቍር፡ ሱፋላ፡ ለማለት፡ በርኖስ፡ ይሉታል። እመኒ፡ ኮነ፡ ኀጢአትክሙ፡ ከመ፡ ኳኳ፡ ይጻዕዱ፡ ከመ፡ በረድ፤ ወእመኒ፡ ቈሐ፡ ከመ፡ ለይ፡ ይከውን፡ ከመ፡ ፀምር፡ (ኢሳ ፩፡ ፲፰)። ቈሐና፡ ኮን፤ ለይና፡ ኳኳ፤ ይከውንና፡ ይጻዐዱ፤ ከመ፡ ፀምርና፡ ከመ፡ በረድ፡ አንዳንድ፡ ወገን፡ ናቸው።

**ከክሀ፤—ኮክ፡ የኮክ፡ ፍሬ፤—ከወከ።**

**ኰኰሕ፤—ጥኑ፡ ደንጊያ፤—ከሕከሐ።**

**ኰከይ፤ (ዋከየ፡ ውኩይ)፤** ቡሓ፡ ራስ፡ ነጭ፤ በግ፡ ቍራ፡ (ትግሬ)።

**ኰከመ፤** ከከመ፤ የእግር። ኰመኰመ፤ የምግብ፡ የጨዎት። ዐፈስ፡ ዛቀ፤ የምርት።

**ኰከም፤(ማት)፤** የፍም፡ መጫሪያ፡ መተርከሻ፤ ያመድ፡ ማፈሻ። ኢያሚንን፡ እይ፤ ከዚህ፡ ጋራ፡ ፩፡ ነው። ባለብሉዮች፡ ግን፡ እንቅብ፡ ይሉታል፤ አንኮላ፡ ሽክና፡ የሚሉም፡ አሉ። ጽህርታት፡ ወኵከማት፡ (ኤርምያ ፶፪፡ ፲፰)።



ኰከማት፡

**ኬክሮስ፤(ሳት። ጽር፡ ኪርኮስ)፤** የክፍለ፡ ዕለት፡ ስም፤ የዕለት፡ ፳ኛ። ፩ዱ፡ ዕለት፡ ወይም፡ ፳፬ቱ፡ ሰዓት፡ ፷፡ ኬክሮስ፤ አንዱ፡ ኬ፡ ፷፡ ካልኢት፤ አንዱ፡ ካ፡ ፷፡ ሣልሲት፤ አንዱ፡ ሣ፡ ፷፡ ራብዒት፤ አንዱ፡ ራ፡ ፷፡ ኃምሲት፤ አንዱ፡ ኃ፡ ፷፡ ሳድሲት፡ ይኾናል፤ ይህ፡ ሲዘረዘር፡ ነው። ሲጠቀለል፡ ደግሞ፤ ስሳው፡ ሳ፡ ፩፡ ኃምሲት፤ ስሳው፡ ኃ፡ ፩፡ ራብዒት፤ ስሳው፡ ራ፡ ፩፡ ሣልሲት፤ ስሳው፡ ሣ፡ ፩፡ ካልኢት፤ ስሳው፡ ካ፡ ፩፡ ኬክሮስ፤ ስሳው፡ ኬ፡ ፩፡ ዕለት፡ ይኾናል። አኀዘ፡ ዓመተ፡ እልሐ፡ ጅራ፡ በስድስቱ፡ መካናት፤ በመካነ፡ ዕለት፡ ኍልቈ፡ ኬክሮስ፡ ወበመካነ፡ ኬክሮስ፡ ኍልቈ፡ ካልኢት። ዘይኄምሶን፡ ለኬክሮሳተ፡ ሰዓታት፡ ከመ፡ ይኩና፡ መዓርገ፡ ጸሎታት፡ (አቡሻ፡ ፲፩። መጽ፡ ምስ)።

**ከል፤—ቅፉሕ፤—ከወለ።**

**ኵሉ፤—ኹሉ፤—ከልሎ፡ ከለለ።**

(ጥ) **ከልአ፤ አት፤ (ከልአ፡ ይኬልእ፡ ይኩልእ)፤ አው፡ ከሊእ፤ አት፤ (ከልአ፡ ይከልኢ፡ ይክላእ። ዕብ፡ ካላእ። ሱር፡ ክላእ። ዐረ፡ ከለአ)፤** መከልከል፡ መንሣት፤ ማገድ፡ ማስቀረት፤ ማቆም፡ መግታት፤ ከንቢብ፡ ከገቢር፡ ከሐዊር። ከሊአ፡ መንፈስ። ክላእ፡ ልሳነከ፡ እምእኩይ። መኑ፡ ይከልአኒ፡ ተጠምቆ። አንዘ፡ ሰንጉሥ፡ ወከልአ፡ ኢይባእ። ኢይከልእ፡ ምሕረቶ፡ እምግብሩ፡ (መክ ፳፡ ፳። መዝ፡ ፴፫። ግብ ፰፡ ፴፮። ዳን ፲፫፡ ፲፮። ኩፋ፡ ፵፭)።

—፤ መኾለት፤ ኹለት፡ ማድረግ፡ ከኹለት፡ መክፈል።

**ከላኢ፤ መክልኢ፤(ኢት፡ እያን፡ ያት)፤** የሚከለክል፡ ክልካይ፤ በረኛ፡ ዘበኛ፡ አጋፋሪ፤ ጠላት፡ ምቀኛ። ፍና፡ መክልኢት፡ (ፊልክ፡ ፻፷፱)።

**መክልእ፤ መከልእ፤(እት፡ ኣን፡ ኣት)፤** ዝኒ፡ ከማሁ። ይቀውሙ፡ ቅድመ፡ ንጉሥ፡ መክልኣን፡ እለ፡ ኢያበውሑ፡ ከመ፡ ይቅረቡ፡ መኳንንት፡ ወባሕቱ፡ ብዙኃን፡ መክልኣን፡ (መጽ፡ ምስ። ፩ቆሮ፡ ፲፮፡ ፱)።

**ምክላእ፤ (ኣት)፤** መከልከያ፡ ኬላ፡ በር፤ ዐጥር፡ ቅጥር፡ አጕራ።

**ተከልአ፤** ተከለከለ፤ ተገታ፡ ቆመ። ተከልአኒ፡ ገቢር፡ ዘእፈቅድ። ተከልአ፡ ዝናመ፡ ሰማይ። ተከልአ፡ ጸብእ፡ ንስቲተ፡ ዕለተ፡ (ኪዳ። ፫ነገ፡ ፳፡ ፴፭። ዮሴፍ)።

**ክሉእ፤(ኣን፡ ኣት፡ ልእት)፤** የተከለከለ፡ ክልክል። ቀቲልሰ፡ እምኍልቈ፡ ዐበይት፡ ኀጣውእ፡ እለ፡ ክሉኣት፡ ወውጉዛት፡ በልብ፡ ወበሕግ፡ (ፍን፡ ፵፯)።

**ክልአት፤(ታት)፤** መክልክል፡(ጥ፡ክ) መክልክል፡መቅረት፤አከላከል፡ክልከላ። ወሃቢ፡ ዘእንበለ፡ክልአት።አልቦ፡ክልአት፡ በሞትነ። ዘእንበለ፡ ምሕረት፡ ወኢክልአት። ክልአታት፡(ቅዳ፡ ኤጲ። ጥበ፱፡፳። ፲፯፡፲፯። ፊልክ፡ ፶፭)።

**ክልእ፤(ዕብ፡ ኬሌእ)፤** ክልክል፤የግዞት፡ቤት፡ ዘበኛ፡ ክልከይ፡ የሚቆምበት። የቍጥር፡ ስም፤ የጊዜ፡ቅጽል፤ ባንድና፡ በሦስት፡ መካከል፡ ያለ፡ ቍጥር፡ ኹለት። ክልእ፡ክልአ፤ ኹለት፡ ጊዜ። በበ፡አሐዱ፡ወበበ፡ክልእ።

**ክልኤ፤(ዕብ፡ ኪልአዪም)፤** ዝኒ፡ከማሁ፤ ኹለት፤ጥንድ፡ጣምራ፤የተቈራኙ፡የተመሳሰሉ፤እንደ፡ መቀስና፡ እንደ፡ ጕጠት፡ እንደ፡ ሚዛንና፡ እንደ፡ ጡት፡ያሉ፤ቅጽልነቱ፡ ሴትና፡ ወንድ፡ያስተባብራል። ክልኤ፡አጥባትኪ። ምስለ፡ክልኤ፡አዋልዲሃ። ወፀአ፡ክልኤሆን፡ኅቡረ። ተወልዱ፡ሎቱ፡ክልኤ፡ደቂቅ። ወነሥአ፡ ክልኤ፡ ደቂቀ። ይመጽኡ፡ እሉ፡ ክልኤሆሙ፡ላዕሌኪ፡(ማሕ፯፡፬። ዳን፩፡፲፭። ዮዲ፲፫፡፲። ዘፍ፲፡፳፭። ዓ፳፡፩። ኢሳ፵፯፡፱)።

**ክልኤት፤ ክልኤቱ፤(ወንዶች)፤** ኹለት፡ ኹለቱ። ክልኤቱ፡ዐደው፡ዐርጉ፡ቤተ፡መቅደስ።ክልኤቱ፡እምኔክሙ። ትረክብ፡ክልኤተ፡ዐደወ፡(ሉቃ፲፰፡፲። ማቴ፲፰፡፲፱። ፩ነገ፡፲፡፪)።

**ክልኤቲ፤ ክልኤ፤(ሴቶች)፤** ዝኒ፡ከማሁ፤ ኹለት። በገቢር፡ጊዜ፡ ክልኤ፡ ቢል፡ እንጂ፡ ክልኤተ፡ አይልም። ክልኤቲ፡ አንስት። ክልኤቲ፡ ኀጣይእ፡(ዘካ፭፡፱። ሚራ፯፡፰)። ነሥአ፡ክልኤ፡ አንስትየ፤ ወወለዳ፡ሎቱ፡ክልኤ፡አዋልደ።

**ክልእ፤(እት፡ኣን፡ኣት)፤** ሌላ፡ ልዩ፤ ኹለተኛ፡ ተከታይ፤ መሰል፡ እኩያ፡ መንቲያ፤ ጓደኛ፡ ወዳጅ፡ባልንጀራ፤ባለሟል። ካልእ፡ክብሩ፡ለዘበሰማይ፤ ወካልእ፡ክብሩ፡ለዘበምድር። ሕገሙ፡ካልእ፡እምነ፡ዙሉ፡አሕዛብ። ሶበ፡አሐዱ፡ ይድኅር፡ወካልኡ፡ይረግም። ካልኣኒሁ፡አርዳእ። ካልእየ፡ኢገፋዕኩክ። ዙሲ፡ካልኡ፡ለዳዊት፡(፩ቆሮ፡፲፭፡፵። አስቴ፱፡፰። ሚራ፴፬፡፳፱። ዮሐ፳፡፳፭። ማቴ፳፡፲፫። ፪ነገ፡፲፭፡፴፯)።

**ካልኣዊ፡ ዪ፡ ይ፤** ኹለተኛ፤ የኹለተኛ፡ የዳግመኛ።

**ካልኢት፤** ፪ኛ፡ ክፍል፡ የቍጥር፡ ቤት፡ የኬክሮስ፡ ፰ኛ። ኬክሮስን፡ እይ፡(አቡሻ፡ ፲፩)።

**ክልአ፤—ከላ፡ አወለቀ፤—ክልዐ፤ ቀልዐ።**

**ክሊብ፤ ቦት፤(ከለበ፡ ይክልብ፡ ይክልብ። ዕብ፡ ካሌብ፤ ሰፋ፡ ጠቀመ)፤** መክለብ፡ መክለብለብ፤ መቅለል፡ መቻኰል፤ መክልፍለፍ፤ ቀላል፡ ችሎል፡ ክልፍልፍ፡ መኾን፡(ፀማርኛ)።

**ከልብ፤(ብ፡ ከለባት፤ አክላብ፤አክልብት። ዕብ፡ ኬሌብ። ሱር፡ ካልባ። ዐረ፡ ከልብ)፤** ውሻ፤ የቤት፡ አውሬ፡ የኹርብ፡ ወገን፤ የክፉ፡ ሰዎች፡ ምሳሌ። ውሻ፡ ማለት፤ ደግሞ፡ ዋሻም፡ ሳይቀር፡ ወሐሽ፡ ውሕሽ፡ ከማለት፡ ከዐረብ፡ ቃል፡ መጥቷል፤ ይኸውም፡ አውሬ፡ ያራዊት፡ ጕሬ፡ ማለት፡ ነው። ከልብ፡ይገብእ፡ዲበ፡ቅያኡ። ዐገቱኒ፡ ከለባት፡ብብዝኃን። ኅምስቱ፡ አክላብ። አክልብት፡ ወአዝእብት፡(፪ጴጥ፡፪፡፳፪። መዝ፡፳፩። ራእ፳፪፡፲፭። ሚራ፲፫፡፲፰)። ያገዳ፡ ድርቆሽ፡ ደረቅ፡ ሳንፉ፡ ነፋስ፡ የሚያከልበው።


ከልብ፡

**ከልባዊ፤** ገጸ፡ ከልብ፤ ውሻማ፡ የውሻ፡ ፀይነት፤ ውሻ፡ ፊት፤ ጠባየ፡ ውሻ፤ ዘማዊ፡ ወሻሚ፡ ልክስክስ። (ግጥም፡ ስለ፡ ውሽማ)፤ ውሾ፡ ናና፡ ናና፡ ዕንክ፡ ጤፍ፡ እንጀራ፤ ወዳጅ፡ መስሎ፡ ጠላት፡ የሴት፡ ባልንጀራ።

**ከሌብ፤(ዕብ። ዘኍ፲፫፡፯)፤** የሰው፡ ስም፤ ካ፡ ከመ፤ ሌብ፡ ልብ፤ በተገናኝ፡ ከመ፡ ልብ፡ ዘከመ፡ ልብ፡ ማለት፡ ነው። ካሌብን፡ አንቀጽ፡ አድርጎ፡ ሰፋ፡ ጠቀመ፡ ባለው፡ ፀማርኛ፡ ሲፈቱት፡ ግን፡ አንዳርጌ፡ ያሰኛል። አንዳርጌ፡ መባልም፡ ባሕር፡ ተሻግሮ፡ የመንን፡ ይገዛ፡ ለነበረው፡ ለትግሬው፡ ካሌብ፡ ይስማማል። ክርሱም፡ አስቀድሞ፡ ብዙ፡ ያበሻ፡ ነገሥታት፡ ፫፻፯፡ ዓመት፡ ገዝተውታል፡(ታሪክ)።

**ከልበኔ፡(ጽር፡ ኻልባኒ)፤** የሙጫ፡ ሽቱ፤ እንደ፡ ዕጣን፡ ያለ። ባለብሉዮች፡ ግን፡ በልብን፡ ዘይቤ፡ ልባንጃ፡ ይሉታል፡(ሔኖ፵፩፡፩። ሚራ፳፬፡፲፭)።

**ከሊሕ፤ ሖት፤(ክልሐ፡ ይከልሕ፡ ይክላሕ)፤አው፡ክልሖ፤ሖት፤(ክልሐ፡ይኬልሕ፡ ይክልሕ)፤** መክለል፡መጮኽ፤በታላቅ፡ቃል፡መስበክ፡ መንገር፤ ማዜም፡ ማጕረምረም። ቀመ፡ ራፋስቂስ፡ ወከልሐ፡በዐቢይ፡ቃል። ክላሕ፡በኀይልክ።ክልሑ፡ ከመ፡ቀርን፡(ኢሳ፴፮፡፲፫። ፶፰፡፩። ቅዳ፡ ዮሐ)። ሰራሕኩ፡ በክልሖ። ይኬልሕ፡ ላዕሌሆሙ። ይኬልሑ፡ አሐዱ፡ አሐዱ፡ ምስለ፡ ካልኡ። ዙላ፡ ምድር፡ ትኬልሕ። እንዘ፡ ይኬልሓ፡ መጻሕፍት፡(መዝ፡፳፰። ኩፋ፡ ፲፩። ኢሳ፺፡፫። ፲፬፡፯። ቄር)። መብጣት፡ መፍቃት፤ መሠንጠቅ፡(ትግ፡ ሐባ)።

**ከላሒ፤(ሒት፡ ሕያን፡ ያት)፤** የሚክል፡ የሚጮኽ፤ጩኺ፤ቀጡ፡ ደረቅ። ብእሲት፡ከላሒት፡ ወነባቢት፡ ታነሥእ፡ መዋግደ፡ጸብእ። ኢትቅረብ፡

ኀበ ፡ ብእሲት ፡ መስተጋእዝት ፡ ወከላሒት ፡ (ፊላስ ፡ ገ፶፪ ፡ ፳፬) ።

**ከላሐ** ፤ ጮኸት ፤ አጨጨኸ ፡ ዜማ ፤ ፍጅት ፡ ውካታ ። በምዐ ፡ ከላሐ ፡ በብእ ። ከላሖሙ ፡ ለሰይጣናት ። ያፈደፍዱ ፡ ከላሐ ፡ ዘእንበለ ፡ ኅፍረት ፡ (ዮሴፍ ። ስንክ ፡ መስ፲፫ ። አፈ ፡ ድ፬) ።

**ተከልሐ** ፤ ተጨጨኸ ፤ ተፋጀ ፡ ተዋከ ፤ ተዚያዚያመ ።

**አስተከልሐ** ፤ አጨጨኸ ፤ አዳመቀ ፤ ጮኸት ፡ አስተማረ ። ወአስተካልሐ ፡ ደቂቃ ፡ በዜማ ፡ ሐዲስ ፡ ለሀገረ ፡ አዜብ ፡ (ገድ ፡ ዘሚ) ።

**ክልይ** ፤ **ዮት** ፤ **(ከለየ ፡ ይክሊ ፡ ይክሊ ። ዕብ ፡ ክል ። ዐረ ፡ ከለ)** ፤ መስፈር ፤ መመዘን ፡ መለካት ፤ ክልክ ፡ ማግባት ፤ የሥራ ፡ የምግብ ፡ የገንዘብ ።

**ከላዪ** ፤ **መክለዪ ፡ (ዪት ፡ ይያን ፡ ያት)** ፤ የሚሰፍር ፤ ሰፋሪ ፡ መዛኝ ።

**ከሌ** ፤ **(ትግ ። ዕብ ፡ ክሊ ፡ ኬሊ)** ፤ የቤት ፡ ዕቃ ፤ መሣሪያ ፡ ቈሳቍስ ፤ ንዋየ ፡ ሐቅል ፡ ልክና ፡ መልክ ፡ ልዩ ፡ ስም ፡ ያለው ፤ እንትትን ፡ የሚባል ።

**ኪሎ** ፤ የሚዛን ፡ ስም ፤ ፍጹም ፡ ልክ ፡ ባለሺሕ ፡ ክፍል ። ኪሎ ፡ ግራም ፤ ኪሎ ፡ መትር ፡ እንዲሉ ፡ ሺ ፡ ሲሉ ።

**መክልይ** ፤ **መክሊት** ፤ **(ብ ፡ መካልይ ፤ መካልያት ። መክሊታት)** ፤ የሚዛን ፡ ዐዋቂ ፤ ደንጊያ ፡ ወይም ፡ ብረት ፡ ርሳስ ፤ መጠኑ ፡ ፫ ፡ ሺሕ ፡ ሰቀል ፡ የሚያነሣ ። አንዱ ፡ መክሊት ፡ ስሳ ፡ ምናን ፤ አንዱ ፡ ምናን ፡ ኀምሳ ፡ ሰቀል ፡ ይኾናል ። የቤተ ፡ መቅደስ ፡ ሚዛን ፡ ግን ፡ ዕጥፍ ፡ ነው ፤ መክሊቱ ፡ ቀክ—፻፳ ፡ ምናን ፤ ምናኑ ፡ ቀ—፻ ፡ ሰቅል ፡ ይኾናል ። መክሊተ ፡ ወርቅ ፡ ትገብራ ። መክሊተ ፡ ጥጥ ፤ መክሊተ ፡ ኀጺን ። መክሊተ ፡ ዐረር ። ነሥአ ፡ ዐሠርተ ፡ ወክልኤተ ፡ መክሊተ ፡ ብሩር ፡ (ዘፀ፳፭ ፡ ፴፱ ። ፍ ፡ ነ ፡ ፴፮ ። ዘክ፭ ፡ ፯ ። ፬ነገ ፡ ፭ ፡ ፭) ። ኦሉ ፡ ወርቅ ፡ ዘተገብረ ፡ ዕሥራ ፡ ወተስዐቱ ፡ መካልይ ፤ ወብሩርኒ ፡ ዘመባእ ፡ ምእት ፡ መካልይ ። ዘይፈዲ ፡ እልፈ ፡ መካልየ ። በረድ ፡ ዘመጠነ ፡ መካልይ ፡ (ዘፀ፴፱ ፡ ፩ ። ማቴ ፡ ፲፰ ፡ ፳፬ ። ፳፭ ፡ ፲፭—፳፰ ። ራእ፲፮ ፡ ፳፩) ።

**ኵሊት** ፤ **(ብ ፡ ኵልያት ። ዕብ ፡ ኪልያ ። ሱር ፡ ኩሌይታ ። ዐረ ፡ ኩልየት)** ፤ በቁሙ ፤ ኵላሊት ፡ የሆድ ፡ ዕቃ ፡ ንዋየ ፡ ውስጥ ፡ ከጕበትና ፡ ከጣፊያ ፡ በታች ፡ በግራና ፡ በቀኝ ፡ በ፪ ፡ ወገን ፡ የሚገኝ ፤ ክብ ፡ እንክብል ፡ የባሕርይ ፡ ሚዛን ፤ እንደ ፡ ቍላ ፡ ፍሬ ፡ ኹለትንትና ፡ ትክክልነት ፡ ያለው ። የፍትወት ፡ ምንጭ ፡ የፈቃደ ፡ ሥጋ ፡ መነሻ ። ወንድን ፡ በሴት ፡ ላይ ፡ የሚያስገሽ ፡ የሚያቅበጠብጥ ፤ ወገብ ፡ የሚነጥ ፡ የሚያናውጥ ፡ ርሱ ፡ ነው ፡ ይባላል ። ክልኤ ፡ ኵልያቲሁ ፡ ወሥብሐ ፡ ኵሊቱ ። ረገዘኒ ፡ ኵልያትየ ፡ (ዘፀ፳፱ ፡ ፲፫ ፡ ፳፪ ። ኢዮ፲፮ ፡ ፲፫) ።

ኵሊት ፡

—፤ ዕውቀት ፡ ሐሳብ ፤ ረቂቅ ፡ ምክር ፡ ውሳጣዊ ፡ ነገር ፤ ኵላሊት ፡ የሚያጤሰው ፤ ልብ ፡ የሚያመላልሰው ፤ ኅሊና ፡ የሚወርሰው ፤ እነዚህም ፡ ፫ቱ ፡ ባንድ ፡ ሚዛን ፡ ይመስላሉ ። ዘይፈትን ፡ ልበ ፡ ወኵልያተ ። ርሑቅ ፡ አንተ ፡ እምነ ፡ ኵልያቲሆሙ ። ገሠጻኒ ፡ ኵልያትየ ። ይትሀወከ ፡ ኵልያቲሁ ፡ እምዘቲ ፡ ቃል ፡ (ኤር፲፩ ፡ ፳ ። ፲፪ ፡ ፪ ። መዝ ፡ ፲፭ ። ሔኖ፳፰ ፡ ፫) ።

**ክልክለ** ፤ **(ክልአ ። ዕብ ፡ ካልኬል ፤ አበላ ፡ ረኀብን ፡ ከላ)** ፤ ክለከለ ፤ ክላ ፡ ክላ ፡ አለ ፤ አገረ ፡ አስተጓጐለ ። ክልካይ ፡ እንዲሉ ፡ (ዐማርኛ) ።

**ተከልከለ** ፤ ተከለከለ ፤ ክልክል ፡ ኾነ ። ጺሕ ፡ ፍኖቶ ፡ ዘእንበለ ፡ ክልአት ፡ ወኢተከልክሎ ። ኢይትከለከል ፡ (ግንዘ ። ገድ ፡ ኪሮ) ።

**ክልሎ** ፤ **ሎት** ፤ **(ከለለ ፡ ይኬልል ፡ ይክልል ። ዕብ ፡ ካላል ። ሱር ። ክሌል ፡ ዐረ ፡ ክለ)** ፤ መክለል ፡ መጋረድ ፤ ማጠር ፡ መክበብ ፡ ማጀብ ፤ ማክበር ፡ ጮኾ ፡ ማመስገን ። ግሩማን ፡ የዐውድዎ ፡ ወሱራፌል ፡ ይኬልልዎ ። እግዚኦ ፡ ከመ ፡ ወልታ ፡ ሥሙር ፡ ከለልከነ ። ተለውዋ ፡ እንዘ ፡ ይኬልልዋ ፡ ወይሴብሑ ፡ በአፉሆሙ ። ሶበ ፡ ርእይዎ ፡ ተወሊዶ ፡ ከለልዎ ፡ እንዘ ፡ ይብሉ ፤ ስብሐት ፡ በአርያም ፡ (መዋሥ ። መዝ ፡ ፭ ። ዮዲ፲፭ ፡ ፲፫ ። ቄር ፡ ገ፰) ።

—፤ ፈጽሞ ፡ ማስጌጥ ፡ መሸለም ፤ ዘውድ ፡ መድፋት ፡ አክሊል ፡ ማቀዳጀት ፤ ለንጉሥ ፡ ለሙሽራ ። ዘከለሎ ፡ ለሰማይ ፡ በከዋክብት ፤ ምድረ ፡ በጽጌ ፡ ወበፍሬ ፡ ከለልከ ። እምዕበየ ፡ ግርማሁ ፡ ዘከለሎ ። ክብረ ፡ ወስብሐተ ፡ ከለልኮ ፡ (ድጓ ። ቀሌ ። መዝ ፡ ፰) ።

— ፤ መደምለል ፤ መጠቅለል ፡ መሰብሰብ ፤ ብዙውን ፡ ባንድነት ፡ ማሰብ ፤ ኵሉ ፡ ኵለንታ ፡ ማለት ። መፈጸም ፡ መጨረስ ፡ ማከናወን ፤ የሥራ ። መቍረጥ ፡ መክፈል ፤ ያንገት ፡ የመሬት ።

**ከላሊ** ፤ **መክልል** ፤ የሚከልል ፡ ከላይ ፤ ቈራጭ ፡ ከፋይ ።

**አክለለ** ፤ **አስተክለለ** ፤ አስከለለ ፤ ተክሊል ፡ አስደረገ ፤ አክሊል ፡ አሠራ ፤ አስደፋ ።

**አክሊል** ፤ **(ላት ። ዐረ ፡ ኢክሊል ። ሱር ፡ ክሊላ)** ፤ በቁሙ ፤ ዘውድ ፤ የራስ ፡ ጌጥ ፡ ሽልማት ፤ የክብር ፡ ጕልላት ። ወድቀ ፡ አክሊለ ፡ ርእስነ ። አክሊለ ፡ ጽጌ ። አክሊል ፡ ዘሦክ ። ንሣእ ፡ ወርቀ ፡ ወብሩረ ፡ ወግበር ፡ አክሊላተ ። አክሊለ ፡ ክህነት ፡ ወመ

ንግሥት። አክሊል፡ ዘእምዕንቍ፡ ክቡር፡ (ሰቈ፭፡ ፲፯። ደራሲ። ማር፲፭፡ ፲፯። ዘካ፮፡ ፲፩። ሳታት። መዝ፡ ፳)።



አክሊል፡

—፤ ኵፌት፡ ቆብ፡ ጥምጥም፤ የራስ፡ ልብስ፡ ቀጸላ፡ መሸፈኛ፡ ጌጥንት፡ ያለው፡ (ዘሌ፰፡ ፱)። መጽንፍትንና፡ ቈዳርስን፡ እይ፤ ከዚህ፡ ጋራ፡ አንድ፡ ነው።

**ሚክሎል** ፤ (ዕብራ) ፤ ክቡር፡ ልብስ፤ ፍጹም፡ ጌጥ፡ ፍጹም፡ ሽልማት፡ (ሕዝ፳፫፡ ፲፪)።

**ከላል** ፤ ክሎታ፡ ወለባ፤ ሚደ፡ መሥዕርት፡ (ትግ፡ ሐባ)። ከለላ፡ ዐጥር፤ ግርደሽ።

**ተከለለ** ፤ በቊሙ፤ ተጋረደ፡ ለበሰ፤ ተቀዳጀ። ተከለሉ፡ በፍኖቶሙ፡ ደመና። ተከለለ፡ ገጹ፡ ብርሃነ። ክብረ፡ ወስብሐተ፡ ዘተከለለ፡ (ዮሴፍ። ስንክ፡ የካ፳፩። ዕብ፪፡ ፱)።

**ክሉል** ፤ (ላን፡ ላት፡ ልልት) ፤ የተከለለ፡ ክልል፤ የተጌጠ፤ ክቡር፡ ምስጉን፤ ቅድሱ፤ ዝግጁ። ቤት፡ ክሉል፡ በአክዋል። በስብሐት፡ ልዕልት፡ ክሉል፡ ውእቱ። ክሉል፡ በትርሲተ፡ ብርሃን። ክሉል፡ ብጌራ፡ መዊእ፡ (መቃ፡ ገ፫። ቍር። ስንክ፡ ታኅ፳። ጥር፳፫)።

—፤ የተደፋ፡ የተጕለለ፤ ጕልል፡ ንቡር። አክሊሉኒ፡ ይኩን፡ ክሉለ፡ መልዕልተ፡ ርእሱ፡ (ፈ፡ መ፡ ፴፭፡ ፩)።

**ክላሌ** ፤ (ልያት) ፤ መከለል፤ (ጥክ) መከለል፤ መቈረጥ፡ መቀዳጀት። ከለላ፡ ቈረጣ፡ ቅድጅት፤ ምስጋና፡ ፍጻሜ፤ ፍጹም፡ ክብር። ዮም፡ ተጽሕፈ፡ እምነገሥት፡ ክላሌሁ፡ በመጥባሕት፡ ለጊዮርጊስ፡ ሰማዕት። ኀይለ፡ ክላሌሆሙ። ክላሌ፡ ክብር፡ ወስብሐት፡ ይደሉ፡ ለባሕቲቱ፡ (ድጓ። ስንክ፡ ኅዳ፯። አፈ፡ ድ፱)። ክላሌሁ፡ በመጥባሕት፡ ያለው፤ የሰማዕታት፡ ሞት፡ እንደ፡ ጌታ፡ ሞት፡ ስለ፡ ኾነ፡ ነፍሳቸውም፡ ሙሽራው፡ ናትና፤ ሥጋዋ፡ ሲሰየፍ፡ ገድሏ፡ መፈጸሙን፤ የተፋኀሮን፡ ሥራ፡ ጨርሳ፡ አክሊለ፡ ብርሃን፡ መቀበሏንና፡ መቀዳጀቷንም፡ ቢያሳይ፡ እንጂ፤ መቈረጥን፡ ብቻ፡ አያሳይም።

**ተክሊል** ፤ በቊሙ፤ የግቢ፡ ሥርዐት፡ ቃል፡ ኪዳን፤ ክህናት፡ በመርዓዊና፡ በመርዓት፡ ላይ፡ የሚፈጽሙት፤ የሕግ፡ ጋብቻ፡ ሊፈርስ፡ የማይቻል። ቃል፡ ኪዳኑን፡ ተክሊል፡ ያሰኘው፡ የሙሽሮቹ፡ ልብስ፡ ጌጡ፡ ሽልማቱ፡ ፈርጡ፡ ቀለበቱ፡ ያበባው፡ አክሊል፡ ነው። ሶበ፡ ተዋሰቡ፡ በጸሎተ፡ ተክሊል። እምቅድመ፡ ይግበሩ፡ ሎቱ፡ ተክሊለ፤ ወእምድኅረ፡ ተክሊል። አውስቦሰ፡ ዳግሚት፡ ተሐጽጽ፡ እምቀዳሚት፤ ወለዛቲ፡ ትሠርዐ፡ በቀኖናት፡ ከመ፡ ኢይኩን፡ ላቲ፡ በረከተ፡ ተክሊል፤ አላ፡ ይግበሩ፡ ጸሎተ፡ አስተስርዮ፡ (ፈ፡ መ፡ ፳፡ ፲፯። ፲፪፡ ፳። ፍ፡ ነ፡ ፳፬፡ ፩)።

**ኵል** ፤ (ዕብ፡ ከል። ሱር፡ ካል። ዐረ፡ ኩል) ፤ ኹል፤ (ኹል፡ ጊዜ፤ ኹል፡ ቀን)። ምሉእ፡ ፍጹም፡ ነገር፡ ደምላላ፡ ጠቅላላ፡ ውስጠ፡ ብዙ፤ ባንድነት፡ የቆመ፡ የተወሰነ፡ ሥራ፡ ነገር፡ ቍጥር፡ ማኅበር፤ አንድ፡ ያልቀረው፡ ያልጐደለው፡ ድምር፤ ፍጥረት፡ ሕዋሳት፡ እንደ፡ ማለት። ኵልና፡ ኵሉ፡ አሐድ፡ አሐዱ፤ ዐሠርት፡ ዐሠርቱ፡ እንደ፡ ማለት፡ ናቸው፤ ርባታቸውም፡ እንዲህ፡ ነው፤ ኵል፡ ለስድስቱ፡ ቅርቦች፤ ኵሉ፡ ላራቱ፡ ሩቆች፡ ይነገራል። ኵልየ፡ ከ፡ ኪ፤ ኵልነ፡ ክሙ፡ ክን። ኵሉ፡ ላ፡ ሎሙ፡ ሎን። አብርሃም፡ አበ፡ ኵልነ። ኵልክሙ፡ አሕዛብ፡ (ሮሜ፬፡ ፲፮። መዝ፡ ፵፮)። በገቢርም፡ ጊዜ፡ ኵልየ፡ ካለው፡ በቀር፡ ባምስቱ፡ ኹሉ፡ ልን፡ ለ፡ ይወርሰዋል። ዕቀብ፡ ኵለነ። ከመ፡ ትቅትል፡ ኵለነ፡ (ሊጦን። ዘፀ፲፮፡ ፫)።

**ኵሉ** ፤ (ኵላ፡ ኵሎሙ፡ ኵሎን) ፤ ኹሉ፡ መላው፤ ፍጹሙ፡ ጠቅላላው፤ አንድ፡ ሳይቀር። ኵሉ፡ ዓለም፤ ኵላ፡ ምድር፤ ኵሎሙ፡ ዕደው፤ ኵሎን፡ አንስት። ኵሉ፡ ቀባያት፤ ኵሉ፡ ዕፀው፤ ኵሉ፡ አሕዛብ። ሉ፡ የሩቅ፡ ዐጸፋ፡ ስለ፡ ኾነ፡ የኵሉ፡ ርባታ፡ ከሩቆች፡ በቀር፡ ለቅርቦች፡ ሰራዊት፡ አይስማማም፤ በገቢርም፡ ጊዜ፡ ከሉ፡ በቀር፡ ላና፡ ሎ፡ አይለወጡም። ዳግመኛም፤ ኵሉ፡ ላ፡ ሎሙ፡ ሎን፡ በማለት፡ ፈንታ፤ ኵልሁ፡ ልሃ፡ ልሆሙ፡ ሆን፡ እያሉ፡ ኵልን፡ ብቻ፡ እንደ፡ አሐድ፡ እስከ፡ ሥር፡ ማርባት፡ ይቻላል። አሐዱና፡ ኵሉ፡ በምስጢር፡ አንድ፡ ስለ፡ ኾኑ፤ አሐዱ፡ አሐዱ፡ በማለት፡ ፈንታ፤ ኵሉ፡ ኵሉ፤ ወይም፡ እያቀናጀ፡ ኵሉ፡ አሐዱ፡ ይላል፤ አንድ፡ እንኳ፡ ሳይቀር፡ ማለት፡ ነው፡ (ስንክ፡ ሐም፳፯)። ኵሉ፡ ከተጸውዖ፡ ስም፡ በቀር፡ ውስጠ፡ ብዙነት፡ ላለው፡ ለብትን፡ ሰዋስው፡ ኹሉ፡ ቅጽልና፡ ዐጸፋ፡ በቂ፡ ይኾናል፤ ካንድ፡ በላይ፡ ላለ፡ ላንዱም፡ ሳይቀር፡ ከኹለት፡ እስከ፡ ምእልፊት፡ በተከፍሎም፡ ያለተከፍሎም፡ ለብዙም፡ ለጥቂትም፡ ይነገራል። ኵሉ፡ ሕዝብ፤ ኵሉ፡ ፍጥረት፤ ኵሉ፡ ነፍስ፡ ይሴብሖ፤ ቅጽል። ኵልክሙ፡ ተዐልዉኒ፤ እመሂ፡ ኵሎሙ፡ ዐለዉከ፤ ወኵሎሙ፡ ሰማዕት፡ ኮኑ፤ ዐጸፋ። ኵሉ፡ ዐረየ፤ እግዚአ፡ ኵሉ፤ ወኵሉ፡ ከመ፡ ልብስ፡ ይበሊ፤ በቂ። ኵሉ፡ ላንድ፡ መነገሩ፡ ባንድነቱ፡ ውስጥ፡ ብዙ፡ ክፍላት፡ ብዙ፡ ሕዋሳት፡ ስላሉ፡ ነው፤ ኵሉ፡ ሕንጻ፤ ኵሉ፡ መሌሊት፤ ኵሉ፡ ሥጋሁ፤ የመሰለው፡ ኹሉ። የግእዝ፡ መጽሐፍ፡ ግን፡ በመላሽ፡ ስሕተት፤ ዘላዕሌሁ፡ ኀደረ፡ ኵሉ፡ መለኮቱ፡ በሥጋ፡ ሰብእ፡ ይላል፡ (ቆላ፪፡ ፱)። የጽርኡ፡ አብነት፤ ከጽርእም፡ የተቀዳው፡ ኹሉ፤ እስመ፡ ኵሉ፡ ምልአ፡ መለኮት፡ ኀደረ፡ ቦቱ፡ በሥጋሁ፡ ይላል፡ እንጂ፤ ኵሉ፡ መለኮቱ፡ አይልም። ኵሉ፡ በማንም፡ ቋንቋ፡ ውስጠ፡ ብዙነት፡ ለሌለውና፡ መክፈል፡ ለማይስማማው፡ ላንድ፡ ብቻ፡ አይነገርም፤ ምልአ፡ መለኮት፡ ያለውም፡ ፍጹም፡ ጸጋ፡ ነው። ይህም፡ ንባብ፡ ምሉእ፡ ጸጋ፡ ወጽድቅ፡ ካለው፡ ጋራ፡ እንጂ፤ ቃል፡ ሥጋ፡ ኮነ፡ ወኀደረ፡ ላዕሌነ፡ ካለው፡ ጋራ፡ አይገጥምም፤ በጣም፡ ሩቅ፡ ነው፡ (ዮሐ፩፡ ፲፬)።

**ኵልሄ፤ ኵለሄ፤ (ኵል ፡ ሄ)፤** ኹል ፡ ጊዜ፤ ኹለግዜ፤ ኹለዬ፤ ዘወትር ። በታ ፡ ኹሉ፤ አገር ፡ ኹሉ፤ አራቱ ፡ ማእዝን፤ ዐውድ ፡ ዘውድ ። ል ፡ ከተገብሮ ፡ ለ ፡ ከገቢር ፡ ይስማማል ። ምሉእ፡እምኔሁ፡ዦልሄ። አዐቅብከ፡በዦልሄ። አንሶሰወ፡ውስተ፡ዦልሄ። መሐወኒ፡እንተ፡ዦልሄ፡(አዋል ። ኩፋ ፡ ፳፯ ። ስንክ ፡ ግንጃ፯ ፡ ኢዮ፲፱ ፡ ፲) ። ተሐውር፡ዦለሄ፡ ኀበ፡ ፈነውኩከ። ኀበ፡ ታንሶሱ፡ ዦለሄ። መላእክት፡ ወሰብእ፡ ዘይነብሩ፡ዦለሄ፡(ኤር፩ ፡ ፯ ። ስንክ ፡ ሐምጃ፯ ። ደራሲ) ። ብዙው ፡ መጽሐፍ ፡ ገቢር ፡ ተገብሮ ፡ ሳይለይ፤ በኵለሄ፡ እንተ ፡ ኵለሄ፡ ውስተ ፡ ኵለሄ ፡ ይላል፤ አንዳንድ ፡ ጊዜም፡ ላዕለ ፡ ምድር ፡ ኵልሄ ፡ እያለ ፡ አለቦታም ፡ ገብቶ ፡ ይገኛል፤ የሄን ፡ አፈታት ፡ ተመልከት ።

**ኵላዊ፤** የኹሉ ፡ የመላው ፡ (ፊልክ ፡ ፻፴፬) ።

**ኵለንታ፤** ኹለንተና፡ ኹለመና፤ መላው ፡ ጠቅላላው፡ ዙሪያ ፡ ገባው፡ አራቱ ፡ ማእዝን፤ የገላ ፡ የቦታ ። እንተ፡ ዦለንታሆሙ፡ ምሉኣነ፡ አዕይንት። ዦለንታኪ፡ ሠናይት። ዦለንታየ፡ ተመስወ። ወዦለንታሁ፡ ብወርቅ፡ ወበዕንቍ። ተቋመ፡ ማኅቶት፡ ዘዦለንታሃ፡ ወርቅ። ዦለንታሃ፡ ለዛቲ፡ ምድር፡ (ራእ፬ ፡ ፰ ። ማሕ፬ ፡ ፯ ። ሔኖ፰ ፡ ፫ ። አስቴ ፡ ፭ ። ዘካ፬ ፡ ፪ ። ዘፍ፲፫ ፡ ፲፭) ።

**ኵለንታዊ፤ (ዊት)፤** የውስጥ ፡ የአፍኣ ፡ የነፍስ ፡ የሥጋ ፡ ፍጹም ፡ ሰብእና ፡ ፍጹም ፡ ልቡና ፡ ፍጹም ፡ ኀሊና ። ኀደገት ፡ ግብራቲሁ ፡ ለዝ፡ ዓለም፡ ወመጽአት፡ ምስለ፡ ዦለንታዊታ ፡ ለኀበ፡ ዓለም፡ ኻልእ፤ ልብ፡ ሳይቀራት ፡ (ፊልክ ፡ ፫) ።

**ኵላ፤ (ጽር ፡ ከሊ)፤** ቀለም፤ መጣብቅ ፡ ሙጫ፤ ለሚታነጥ ፡ ዕንጨት ፡ መልክና ፡ ውበት ፡ አንድነት ፡ የሚሰጥ ። ወያስተጣግዖ፡ በዦላ፡ (ኢሳ፵፬ ፡ ፲፫) ።

**ከለሚዳ፤ (ዳት ። ጽር ፡ ክላሚዳ)፤** ሠጋር ፡ ካባ፤ የክብርና ፡ የማዕርግ ፡ ልብስ ፡ ካንገት ፡ እስከ ፡ ወገብ ፡ ወይም ፡ እስከ ፡ ጕልበት ፡ የሚደርስ፤ ነገሥታት ፡ መኳንንት ፡ ልጆቻቸውም ፡ የሚለብሱት ። ለምድ ፡ ለምደኛ፤ ያርበኞች ፡ ሽልማት ፡ (ማቴጃ፯ ፡ ጃ፰ ፡ ፴፩) ። ፀምር ፡ መንጸፍ ፡ በማለት ፡ ፈንታ ፡ ከለሜዳ ፡ ይላል፤ የመላሽ ፡ ስሕተት ፡ ነው ። ክዑበ፡ ከለሜደ፡ (ምሳ፴፩ ፡ ጃ፪ ። ዲድ ፡ ፫) ። ዘርቤትን ፡ እይ፤ ከዚህ ፡ ጋራ ፡ ፩ ፡ ነው ። በያክንትም ፡ ፈንታ ፡ ቀይ ፡ ለማለት ፡ ከለሜዳ ፡ ይላል፤ ፍችው ፡ አይደለም ። ያለብስዎ ፡ ከለሜዳተ ፡ ወደርክዮ፡ (ኤር፲ ፡ ፱) ።

**ኵለንታ፤—ኹለንተና፤—ከልሎ ፡ ከለለ፤ ኵል ፡ ኵሉ ።**

**ከልዐ፤—ከለከለ፤—ከሊእ ፡ ከልአ ።**

**ከልዐ፤ (ቀልዐ)፤** ከላ ፡ አወለቀ፤ አወጣ ፡ አሰለበ፤ የልብስ ፡ የቀሚስ ፡ የጫማ ። ቀልዐን ፡ እይ፤ የዚህ ፡ መንቲያ ፡ ነው ። ኢትክልዑ፡ አልባስየ። ከላዕኩ፡ ክዳንየ፡ ዘእትዐጸፍ፡ ወወገርኩ። ክልዐ፡ አልባሲሁ፡ ወለብሰ፡ ሠቀ፡ (ገድ ፡ ዳን) ። ክላዕ፡ አሣእኒከ፡ እምእገሪከ፡ (ቀሌ) ።

**ኬልቄዶን፤ (ጽር ፡ ኻልኪዶን ። ዕብ ፡ ሽበ)፤** ነጭ ፡ ዕንቍ፤ በንጣቱ ፡ ስማያዊነት ፡ ያለበት ። አካጥስን ፡ እይ፤ ከዚህ ፡ ጋራ ፡ አንድ ፡ ነው ። ወሣልስት፡ በኬልቄዶን፡ (ራእ፳፩ ፡ ፲፱) ።

—፤ የመዲና ፡ ስም፤ በታናሽ ፡ እስያ ፡ በቱርክ ፡ አገር ፡ ውስጥ ፡ ያለ፤ የቍስጥንጥንያ ፡ ቅርብ ፡ አጠገብ፤ ክልደት ፡ በኋላ ፡ ባ፬፻፶፩ ፡ የግሪክ ፡ ንጉሥ ፡ መርቅያኖስና ፡ ሚስቱ ፡ ብርክልያ ፡ ስለ ፡ መንግሥታቸው ፡ ልዕልና ፡ በሠለስቱ ፡ ምእት ፡ ዕጥፍ ፡ ፮፻፴፯ ፡ ጳጳሳት ፡ ሰብሰበው ፡ ከጉባኤ ፡ ኹሉ ፡ የሚበልጥ ፡ ታላቅ ፡ ጉባኤ ፡ ያቆሙበት፤ ቀድሞ ፡ በኤፌሶን ፡ ከንስጥሮስ ፡ ጋራ ፡ ዐብረው ፡ ተወግዘው ፡ የነበሩ ፡ ኋላም ፡ እንደ ፡ ገና ፡ ከሞቱ ፡ በኋላ ፡ በቍስጥንጥንያ ፡ ጉባኤ ፡ ቢጊሊዮስ ፡ ዘሮም ፡ ከነመጽሐፋቸው ፡ ረግሞ ፡ አውግዞ ፡ የለያቸው ፡ እንኤባስ ፡ እንታዎድሬጦስ ፡ የገቡበት፤ የእስክንድርያው ፡ ሊቀ ፡ ጳጳስ ፡ ዲዮስቆሮስና ፡ መቃርዮስ፤ ሌሎችም ፡ መምህራን ፡ ከሶርያና ፡ ከአርመን ፡ የመጡ ፡ አራት ፡ ጳጳሳት ፡ ተጨምረው ፡ እነዚህ ፡ ፮ቱ ፡ የተለዩበት ። ምክንያቱን ፡ በቤተ ፡ ክሲያን ፡ ታሪክ ፡ ተመልከት፤ ታሪኩ ፡ ግን ፡ ፪ ፡ ወገን ፡ ነው፤ ፩ኛው ፡ የግብጽ ፡ የሶርያ ፡ የአርማንያ፤ ፪ኛው ፡ የግሬክና ፡ የሮምያ ። የግሬኮች ፡ ታሪክ ፡ በዲዮስቆሮስ ፡ እጅ ፡ ከተጣፈው ፡ ከቅዳሴውና ፡ ከድርሳኑ ፡ ቃል ፡ አይስማማም ፡ ዐይንና ፡ ዐፈር ፡ ነው፤ ይኸውም ፡ ሊታወቅ ፡ ፍሬ ፡ ቅዳሴውን ፡ የኢትዮጵያ ፡ ካቶሊኮች ፡ ከሮማ ፡ ሊቃውንት ፡ አስመርምረው ፡ ከፓፓ ፡ አስፈቅደው ፡ ሐሰትና ፡ ስሕተት ፡ ጸያፍ ፡ የሌለበት ፡ ስለ ፡ ኾነ ፡ ይቀድሱበታል ። ስሙን ፡ ብቻ ፡ በአርእስቱ ፡ አኰቴተ ፡ ቍርባን ፡ ዘቅዱስ ፡ ዲዮስቆሮስ ፡ በማለት ፡ ፈንታ ፡ ዲዮናስዮስ ፡ ብለውታል፤ ይህም ፡ ቅዳሴ ፡ የተደረሰና ፡ የተጣፈ ፡ በጋግራ ፡ ሳለ ፡ ነው፤ በግእዝ ፡ ተጥፎ ፡ እንደሚገኝ ፡ በሌሎችም ፡ ቋንቋ ፡ በሶርያና ፡ በአርመን ፡ በጽርእ ፡ በላቲን ፡ ይገኛል ። ከመስማት ፡ ማየት ፡ ይበልጣልና፤ ቅዳሴዉን ፡ ከሥር ፡ እስከ ፡ ጫፍ ፡ ተመልከት፤ ፩ ፡ አካል ፡ ፪ ፡ ባሕርይ ፡ ሲል ፡ ታገኘዋለኽ ። ፪ኛም ፡ ሃይማኖተ ፡ አበው ፡ ዲዮስቆሮስ ፡ የተለየበትን ፡ ለማስረዳት ፡ ከገዛ ፡ መጽሐፉ ፡ ባሮር ፡ ቃል ፡ ጠቅሶ ፡ ያመጣው ፡ የድርሳኑ ፡ ቍርጭኝ ፡ ወይም ፡ መልእክቱ ፡ ስላካልና ፡ ስለ ፡ ባሕርይ ፡ ስለ ፡ ህላዌም ፡ ፍች ፡ የሚለውን ፡ ባባ ፡ ብንያሚ ፡ ድርሳን ፡ ውስጥ ፡ ወካዕበ፡ ይቤ፤ ዲዮስቆሮስ፡ ተአማኒ፡ ርእሰ፡ ኤጲስቆጶሳት፡ ዘእለእስክንድርያ፡ በመልእክቱ፡ ዘጸሐፋ፡ ኀበ፡ በርጢር፡ እንዘ፡ ሀሎ፡ በጋግራ። ይቤ፤ አንሰ፡ ረከብኩ፡ ነገረ፡ እንዘ፡ ኣነብብ፡ መጻሕፍቲከ፡ ዘፈኖከ፡ ሊተ፡ ምስለ፡ ሰብእ፡ መትሕላን፡ እለ፡ ኢኮኑ፡ ፍጹማነ፡ ወአልቦሙ ፡ አእምሮ ፡ ጥዩቀ፤ ካለው ፡ ዠምረኽ ፡ እስከ ፡ መጨረሻው ፡ ተመልከት ። መልእክቱም ፡ የተጣፈበት ፡ ምክንያት ፡ ግብጦች ፡ በኦርቶደክስ ፡ ባህል ፡ ተጣልተው ፡ ፪ ፡ ወገን ፡ ኹነው ፡ የጣፉትን ፡ ከታብ፤ በርጢር ፡ የተባለው ፡ ሰውዬ ፡ የርሱንም ፡ ከታብ ፡ ጨምሮ ፡ ፪ ፡ መነኮሳት ፡ አሲዞ ፡ ስለ ፡ ላከለት ፡ ነው ፡ ይባላል ።

**ክልስሶ ፤ ሶት ፤** (ከልሰሰ ፡ ይከለስስ ፡ ይ ክልስስ ። ዐረ ፡ ከለደ ፡ ከለዘ) ፤ መሰብሰብ ፤ መላ ስስ ፡ መንቀል ፤ የሽት ፡ የሽንብራ ። እያጨዱ ፡ ማሰር ፡ የ ታጨደውን ፡ መሰንደቅ ፤ መጐቸት ፡ መከመር ፤ የነደ ፡ የማር ። አስደንና ፡ ቈለዘን ፡ እይ ፤ የዚህ ፡ ጎሮች ፡ ናቸው ።

**ከልሳሲ ፤** (ሲት ፡ ስያን ፡ ያት ፤ ሰስት) ፤ የሚላስስ ፤ ፀማጅ ፡ አባሪ ፤ ሰብሳቢ ፡ ከማሪ ።

**ተከልሰሰ ፤** ተላሰሰ ፤ ታጨደ ፡ ታሰረ ፤ ተሰበሰበ ።

**ክልሱስ ፤** (ሳን ፡ ሳት ፡ ስስት) ፤ የተላሰሰ ፤ የታጨደ ፡ የተሰበሰበ ።

**ከልሰስ ፤ ክልስስት ፤** (ብ ፡ ከላስስት) ፤ ነደ ፡ ቋጨራ ፤ ሰንድቅ ፡ ድንከን ፤ የታሰረና ፡ ያልታሰረ ። ታበውኡ ፡ ክልስስተ ፡ እምቀዳሚ ፡ ማእረርክሙ ። እለ ፡ የአስሩ ፡ ከላስስተ ። ዘወድቀ ፡ እምነ ፡ ከላስስት ፡ ወጾሩ ፡ ከላስስቲሆሙ ፡ (ዘሌ፳፫ ፡ ፲—፲፪ ። ዮዲ፰ ፡ ፫ ። ሩት፪ ፡ ፯ ። መዝ ፡ ፻፳፭) ።



ክልስስ ፡

**ኬልቲ ፤** (ጽር ፡ ኬሬቲ ። ዕብ ፡ ክሬቲ) ፤ የጭፍራ ፡ ስም ። ቀርጤሳዊ ፡ የቀርጤስ ፡ ሕዝብ ፡ ማለት ፡ ነው ፤ ጕንደፌ ፡ እንደ ፡ ማለት ፡ (፫ነገ ፡ ፩ ፡ ፴፰) ። ል ፡ በጣፊ ፡ ስሕተት ፡ ወይም ፡ በጸያፍ ፡ አንደበት ፡ የገባ ፡ ነው ። በሐረረ ፡ ፈንታ ፡ ሐለለ ፡ እንዲል ።

**ከልተፈ ፤** (ከተፈ) ፤ ኰለተፈ ፡ ተኰላተፈ ፤ ኰ ልትፍትፍ ፡ አለ ፡ ታሰረ ፤ ጕለደፈ ፤ ያንደበት ፡ የስለት ። ል ፡ ሰሯጽ ፡ ነው ፤ ከተፈን ፡ እይ ።

**ኪማ ፤**—፯ ፡ ከዋክብት ፤—ከየመ ።

**ከመ ፤**—መቼም ፡ መች ፤—ከመመ ።

**ከሚው ፤ ዎት ፤** (ከመወ ፡ ይከሙ ፡ ይ ክሙ ። ዕብ ፡ ከማህ) ፤ አጥብቆ ፡ መውደድ ፤ መሳብ ፡ ማቅረብ ፤ እኩያ ፡ አምሳያ ፡ ማድረግ ፤ እንደ ፡ ራስ ፡ ማ የት ። መመዘን ፡ ማስተካከል ፡ አንዱን ፡ ባንዱ ፡ ልክ ፡ መወሰን ።

**ከመ ፤** (ዕብ ፡ ክሞ ። ሱር ፡ ክማእ ። ዐረ ፡ ከማ) ፤ ዐቢይና ፡ ደቂቅ ፡ አገባብ ፤ እንደ ። በ ፡ ዘ ፡ እያ ዳመቁት ፡ ሳያዳምቁትም ፡ ይነገራል ፤ በአንጻር ፡ በውጥን ፡ ይገባል ፤ ምስጢሩ ፡ መጠንና ፡ ልክ ፡ አምሳል ፡ ነው ። በከመ ፡ ፈነወኒ ፡ አቡየ ፡ ከማሁ ፡ አነሂ ፡ እፌንወክሙ ። ዐገቱኒ ፡ ከመ ፡ ንህብ ፡ መዓረ ። ፪ኛም ፤ እንተ ፡ እለ ፡ ዘ ፡ ባሉበት ፡ አንቀጽና ፡ ጥሬ ፡ ሲገባ ፡ መሰለ ፡ ይኾናል ። ከመ ፡ ዘበንይልነ ፡ ወከመ ፡ ዘበጽድቅነ ፡ ረሰይናሁ ፤ ያደረግነው ፡ ይመስል ፤ ወይም ፡ እንዳደረግነው ፡ ኹሉ ። ፫ኛም ፤ መሰለ ፡ ሲቀድመውና ፡ ሲከተለው ፡ ን ፡ ይኾ ናል ። ሱብዐተ ፡ ዓመተ ፡ ዘኵነንዎ ፡ ኢመሰሎ ፡ ከመ ፡ አሐቲ ፡ ዕለት ። ወከመ ፡ ገሞራ ፡ እመሰልነ ። ፬ኛም ፤ በዘንድ ፡ ላይ ፡ ሲወድቅ ፡ አዳማቂ ፡ ኹኖ ፡ ይቀራል ። መኑ ፡ ውእቱ ፡ እግዚእ ፡ ከመ ፡ እእመን ፡ ቦቱ ። ፭ ኛም ፤ አንቀጽ ፡ እያስቀረ ፡ ባንቀጽ ፡ ሲሳብ ፡ ገቢር ፡ ተ ገብሮ ፡ ይኾናል ። ተዘከር ፡ እግዚኦ ፡ ከመ ፡ መሬት ፡ ንሕነ ። ርእየ ፡ ከመ ፡ በዝኀ ። ሰምዐ ፡ ከመ ፡ ተዔ ወወ ። ደቂቅ ፡ አገባብም ፡ ሲኾን ፡ በጥሬና ፡ በስም ፡ እየገባ ፡ አንጻር ፡ ይኾናል ። ተሰብረ ፡ ከመ ፡ ዕፀ ፤ ተክ ዕወ ፡ ከመ ፡ ማይ ። ፮ኛም ፤ እም ፡ ሲወድቅበት ፡ እ ንደ ፡ ዘ ፡ በር ፡ ከፋች ፡ ኹኖ ፡ በእምና ፡ በእመ ፡ በሶበ ፡ በድኅረ ፡ ዘይቤ ፡ ይፈታል ፤ ምክንያቱም ፡ መላሾች ፡ በ ነዚህ ፡ ቦታ ፡ ስላገቡት ፡ ነው ። እምከመ ፡ ገሰስኩ ፡ ጽ ንፈ ፡ ልብሱ ፡ አሐዩ ፤ ከዳሰስኹ ፡ ብዳስስ ፡ የዳሰስኹ ። እንደኾን ፡ ነ ። እምከመ ፡ ርእዩኪ ፡ ሰብአ ፡ ግብጽ ፤ ቢያዩሽ ፡ ካዩሽ ፡ ያዩሽ ፡ እንደ ፡ ኾነ ። እምከመ ፡ ቦአ ፡ ሙሴ ፡ ውስተ ፡ ደብተራ ፤ በገባ ፡ ጊዜ ፡ ሲገባ ። ወእ ምከመ ፡ ወፅአ ፡ መንፈስ ፡ ርኩስ ፡ እምሰብእ ፤ ከ ወጣ ፡ በኋላ ፡ በወጣ ፡ ጊዜ ፡ እያስኘ ፡ በየግንዘቡ ፡ በያወ ራረዱ ፡ ይፈታል ፤ እምን ፡ ተመልከት ፡ (ዕር፲፱ ፡ ቀ፳፫) ።

**ከማሁ ፤** (ሃ ፡ ሆሙ ፡ ሆን ፤ ከማየ ፡ ከ ኪ ፤ ነ ፡ ከሙ ፡ ክን) ፤ እንዲሁ ፤ እንደ ፡ ርሱ ።

**ከሙ ፤** (ክምው ፡ ከ) ፤ የቅርብ ፡ ወንዶች ፡ ጠቃሽ ፤ ዝርዝር ፤ ከን ፡ ተመልከት ።

**ከሙን ፤** (ዕብ ፡ ካሞን ። ሱር ፡ ካሙና ። ዐረ ፡ ከሙን ። ጽር ፡ ኪሚኖን) ፤ በቁሙ ፤ የቅ መም ፡ ስም ፤ ፍሬው ፡ ታናናሽ ፡ ያንሰላል ፡ ዐይነት ፤ ጣ ዕምና ፡ መዐዛ ፡ ስላለው ፡ ከንጀራና ፡ ከወጥ ፡ የሚገባ ። ባለቅኔዎች ፡ ግን ፡ ተልባ ፡ ሬጠ ፡ ይሉታል ፡ (ማቴ፳፫ ፡ ፳፫ ። ኢሳ፳፰ ፡ ፳፭ ፡ ፳፯) ። ወከነ ፡ ኢይበልዕ ፡ ዘእን በለ ፡ ኅብስት ፡ ወጼው ፡ ምስለ ፡ ከሙን ፡ ወሐምል ፡ ዘኢያብሰልዎ ፡ በእሳት ፡ (ስንክ ፡ ሐም፳፱) ። በከሙን ፡ ፈንታ ፡ ከሜን ፡ ከሚን ፡ ክሚን ፡ ይላል ፤ የጣፊ ፡ ስሕ ተት ፡ ነው ። ስንድሪስ ፡ ወከሜን ። እመ ፡ ዘራዕከ ፡ ከሚነ ፡ (ስንክ ፡ ሐም፰ ። መቃ ፡ ገ፭) ።



ከሙን ፡

**ከመዝ ፤** (ከመ ፡ ዝ) ፤ እንዲህ ፤ እንደዚህ ። ዘከመ ፡ ዝ ፤ እንደዚህ ፡ ያለ ፡ ይህን ፡ የመሰለ ፤ የዝን ፡ አፈታት ፡ እይ ። ከመ ፡ ዝ ፡ ይቤ ። ዘከመ ፡ ዝ ፡ ብሥራት ።

**ከመዝ፤** (ዝን ፡ አትማን) ፤ የውሃ ፡ እናት ፤ ጥቍር ፡ ጠቋራ ፡ እንዝዝ ፡ የምትመስል ፤ በቋሚ ፡ ውሃ ፡ ላይ ፡ እንደ ፡ እንዝርት ፡ ራስ ፡ የምትዞር ፡ የምትሽከረ ከር ፤ ፊክትምን ፡ እይ ። ዝ ፡ ከእንዝዝ ፡ ከእንዝርት ፡ መጥቶ ፡ ከከመ ፡ ጋራ ፡ ተቈራኝቷል ፤ ዘይቤው ፡ ከመ ፡ እንዝዝ ፤ ወይም ፡ ከመ ፡ እንዝርት ፡ ማለት ፡ ነው ። አር ኣያ ፡ ከመዝ ፡ ሰረረ ፡ በዘባነ ፡ ዐባይ ፡ ተርሴስ ፤ ሐመ ርኑ ፡ እንተ ፡ ይነድአ ፡ ነፋስ ፡ (ደራሲ) ።



ከመዝ ፡

**ክሞስ፤ ከሞስ፤ (ዕብ ፡ ክሞሽ ። ጽር ፡ ኻሞስ)** ፤ ስመ ፡ ጣዖት ፡ ሞአባዊ ፤ ከመ ፡ ሰብእ ፡ ከመ ፡ ብእሲ ፤ ሰው ፡ የሚመስል ፡ (ዘኍ፳፩ ፡ ፳፱ ። መሳ፲፩ ፡ ፳፬ ። ፫ነገ ፡ ፲፩ ፡ ፯) ።

**ከሚዎን፤ ከሚዮን፤ (ሮማይ)** ፤ የእሳት ፡ ቦታ ፤ እሳታዊ ፡ ማኅፈድ ፤ በእሳት ፡ የሚኼድ ፡ ማለት ፡ ነው ፤ ሠረገላ ፡ እሳት ፡ እንደ ፡ ማለት ። የከመወ ፡ ዘር ፡ አድርጎ ፡ በከመ ፡ ዘይቤ ፡ ሲፈቱት ፡ ግን ፤ ከሚዎን ፤ ከመ ፡ ኀሰር ። ከሚዮን ፤ (ከመ ፡ ዮን) ፡ ከመ ፡ ርግብ ፡ አምሳለ ፡ ርግብ ፡ ያሰኛል ፤ ዮንን ፡ እይ ፡ (ራእ፲፪ ፡ ፲፱ ። መዝ ፡ ፶፱) ።

**ከሞል ፤—ስመ ፡ ዕፅ ፤—ከወሞል ።**

**ከሜሌዎን፤ (ጽር ፡ ኻሜሌዎን)** ፤ ኅሥ ሥት ፤ ዕሥሥት ፡ የንሽላሊት ፡ ዐይነት ፡ (ዘሌ፲፩ ፡ ፴) ። ባለብሉዮች ፡ ግን ፡ እንቃቅላ ፡ ይሉታል ። ከሜሌዎን ፡ በማለት ፡ ፈንታ ፡ ገላሜዎስ ፡ ይላል ፤ ስሕተት ፡ ነው ።

**ክሚም ፤ ሞት ፤ (ከመ ፤ ከመመ ፡ ይከ ምም ፡ ይክምም)** ፤ መከምከም ፤ ማስተካከል ። መ ሸፈን ፤ ማልበስ ።

**ከመ ፡ (ንኡስ ፡ አገ)** ፤ መቼም ፤ መቼም ፡ መቸ ፡ ዘወትር ፡ ድንት ፡ ዘላለም ። እመሂ ፡ ትልህቁ ፡ አነ ፡ ክመ ፡ ውእቱ ። ወአንተሰ ፡ አንተ ፡ ክመ ። ወክመ ፡ ውእቱ ፡ እስከ ፡ ለዓለም ፡ (ኢሳ፵፮ ፡ ፬ ። ዕብ፩ ፡ ፲፪ ። ፲፫ ፡ ፰) ። ፪ኛም ፡ እንደ ፡ ዳእሙ ፡ ብቻ ፡ ይኾናል ። አነ ፡ ክመ ፡ ወአልቦ ፡ እንተ ፡ ከማየ ። ሕቀ ፡ ክመ ፡ ዘእ ምትንትና ፡ እገርየ ። ሕያዋን ፡ ክመ ፡ ይባርኩከ ፡ (ሶፎ፪ ፡ ፲፭ ። መዝ ፡ ፸፪ ። ቀሌ) ። ፫ኛም ፡ ባወራረድ ፡ ፍቾ ፡ ከቶ ፡ ፈጽሞ ፡ ይኾናል ፤ ምስጢሩ ፡ መቼም ፡ መቸ ፡ ካለው ፡ ይገባል ፡ (ዕርገ ፡ ቍ፺፯) ።

**ክማም ፤ (ብ ፡ አክማም ። ዐረብ)** ፤ በቁሙ ፤ የክንድ ፡ ልብስ ፡ እንደ ፡ እጅ ፡ ቤዛ ፡ ያለ ፡ ባለ መሸቀቅ ፡ ዐጭር ፡ ቍምጣ ፡ እጅጌ ፤ ቀዳሽ ፡ ቄስ ፡ በቅ ዳሴ ፡ ጊዜ ፡ ሲለብሰው ፡ እጁ ፡ ስፊውን ፡ ሰብስቦ ፡ ክም ክሞ ፡ እጁ ፡ ጠባብ ፡ ቀሚስ ፡ የሚያስመስል ። ወእምዝ ፡ ይልበስ ፡ አክማመ ፤ ወይእስሮ ፡ በዝናር ፡ (ሥር ፡ ቅዳ) ።

**ከሙን ፤—በቁሙ ፤ ከመወ ።**

**ከመሠ ፤—ቀመሰ ፤—ከመሰ ።**

(ላ) **ከመረ ፤ (ቀመረ ። አለደ)** ፤ በቁሙ ፤ ቈ ለለ ፡ አንድ ፡ ላይ ፡ አከበ ፤ ሰበሰበ ።

**ክምር ፤ (ብ ፡ ክምራት ፤ አክማር)** ፤ በቁሙ ፤ ቍልል ። ከመ ፡ ክምረ ፡ እክል ። ከመ ፡ ክ ምረ ፡ ሐሠር ። በእትወተ ፡ አክማሪሁ ፡ (ሶፎ፪ ፡ ፱ ። ሚራ፳፩ ፡ ፱ ። መቃ ፡ ገ፱) ። ያገዳ ፡ እኽል ፡ ሲኾን ፡ ክ ምሩ ፡ ዝራማ ፡ እንደ ፡ ማለት ፡ ዲራማ ፡ ይባላል ፤ ልዑል ፡ ማለት ፡ ነው ።



ክምር ፡

**ከማርም ፤ (ዕብ ፡ ክማሪም)** ፡ ካህናተ ፡ ጣዖት ፤ ጥምጥማቸው ፡ ክምር ፡ የሚያካክል ፤ አንዱን ፡ ካማር ፡ ኮሜር ፡ ይላል ። አውፅዮሙ ፡ ለክማርም ፡ (፬ነገ ፡ ፳፫ ፡ ፭) ።

**ከሚስ ፤ (ከመሰ ፤ ዐረ ። ትግ ፡ ከምሽ ። ዕብ ፡ ክማሽ ፤ መጽለወ ፡ የብሰ)** ፤ መቀመስ ፤ ቀምሶ ፡ መተው ፡ ልጥገብለት ፡ አለማለት ፤ ሰውነትን ፡ በራብና ፡ በጥም ፡ በችጋር ፡ መቅጣት ።

**ከምሰሰ** ፤ ዐፈረ ፡ ተሰቀጠጠ ፤ ኵምሽሽ ፡ አለ ። **አክሞሰሰ** ፤ በጥቂቱ ፡ ሣቀ ፤ ከንፈሩን ፡ ገለጠ ፤ ጥር ሱን ፡ ፍግግ ፡ ፊቱን ፡ ወገግ ፡ አደረገ ። ሶበ ፡ ይሥሕቅ ፡ አብድ ፡ ያዐቢ ፡ ቃሎ ፤ ጠቢብሰ ፡ እምዕጹብ ፡ ያክሞ ስስ ፡ ክናፍሪሁ ። ወያክሞስሶሙ ፡ በየውሀት ፡ ለአብ ዳን ። አክሞስስ ፡ በኅቡእ ፡ (ሚራ፳፩ ፡ ፳ ። ክብ ፡ ነገ ፳፪ ። አፈ ፡ ድ፳፪) ።

**ክሙሳስ ፤ ከሞሳስ** ፤ ታናሽ ፡ ሣቅ ፤ ፍግግታ ፡ የሠሐቅ ፡ ምልክት ፤ ወይም ፡ ቅምሻ ፡ መፍካትና ፡ መን ከትከት ፡ ሳይኖር ፡ (ዲድ) ።

**ክን ፤-የቅርብ ፡ ሴቶች ፡ ዝርዝር ፤-(ከ ፡ ኪ ፡ ክሙ) ፤ ክን ።**

**ከንበሎ ፤ (ከበለ)** ፤ ወለባ ፤ የራስ ፡ ማከኪያ ፡ የጠጕር ፡ ችንካር ፡ እንደ ፡ ሚደ ፡ ያለ ። ወወሀበተ ፡ ለዐ ጻዌ ፡ ቤታ ፡ ከንበሎሃ ፡ ዘወርቅ ፡ (ስንክ ፡ መስ፳፯) ።

**ከንበለ ፤ (ተቀ ፡ ግ)** ፤ ከነበለ ፤ ደፋ ፡ አፈ ሰሰ ። ክንበሌ ፡ ሆይ ፡ ክንበል ፡ ያርገኝ ፡ አክንባሎ ፡ (ሞ ግድ) ፡ ማለት ፡ የዚህ ፡ ዘር ፡ ነው ።

**ከንይ ፤ ዮት ፤ (ከነየ ፡ ይከኒ ፡ ይክኒ ። ዕብ ፡ ከናህ ፤ ሰመየ)** ፤ መጋረድ ፡ መመከት ፤ እን ዲህ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ እንዲህ ፡ አይደለም ፡ ማለት ፤ በው ነት ፡ ወይም ፡ በሐሰት ። ከየነን ፡ ተመልከት ፤ የዚህ ፡ ጎር ፡ ነው ።

—፤ ላይ ፤ በላይ ። ላዕልና ፡ ዲበን ፡ እይ ፤ ከዚህ ፡ ጋራ ፡ አንድ ፡ ነው ። ወጽልመት ፡ መልዕልተ ፡ ቀላይ ። ለዘ ወረደ ፡ እመልዕልት ። አልቦ ፡ ዘይትማሰለነ ፤ እስመ ፡ መልዕልተ ፡ አምሳል ፡ ንሕነ ፡ (ዘፍ፩ ፡ ፪ ። ድጓ ፡ ቀሌ) ።

**ተልዕለ ፤ ተለዐለ ፤** ልዒል ፤ ልዒሎት ፤ ለ ዐለ ።

**ተላዐለ ፤** ተናሣ ፡ ተነሣሣ ፤ ተከባበረ ፤ ተበላ ለጠ ፤ እኔ ፡ እበልጥ ፤ እኔ ፡ እበልጥ ፡ ተባባለ ። ማእዝና ፡ ራብዕ ፡ ከለመለየት ፡ የተነሣ ፡ በተላዐለና ፡ በለዐለ ፡ ፈንታ ፡ ተለዐለ ፡ ይላል ፤ የመምርና ፡ የጣፊ ፡ ስሕተት ፡ ነው ።

**አስተላዐለ ፤** አናሣ ፡ አጣጣን ፤ ከፍ ፡ ከፍ ፡ አ ዳረገ ። አስተላዕል ፡ ምስሌሁ ፡ (ዘዳ፳፪ ፡ ፩) ።

**ለዓለም ፤—ድንት ፤—ለ ፡ ዓለም ፤ ዐ ልሞ ፡ ዐለመ ።**

**ላዕልዐ ፤ (ላኀልኀ) ፤** ለነበደ ፤ ኰለተፈ ፡ ድዳ ፡ ኾነ ። (ተረት) ፤ አፈ ፡ ድዳ ፡ ቀንደ ፡ ጐዳ ። መጽሐፍ ፡ ግን ፡ ተላዕልዐ ፡ ይላል ፤ ስሕተት ፡ ነው ። እንዘ ፡ ይትላዐላዕ ፡ በልሳን ፡ ወይድሕክ ፡ በነቢብ ፡ ፊደላት ፡ (አፈ ፡ ተ፳፯ ። ያዕ ፡ ዘእል) ።

**ላዕላዕ ፤ (ዓን ፡ ዓት) ፤** ድዳ ፡ ለፍዳዳ ፡ ለንባዳ ፡ ኰልታፋ ፤ ክቡደ ፡ ልሳን ። ጸያፍ ፡ ወላዕላዐ ፡ ልሳን ፡ አነ ። ለበሃማን ፡ ወለጸያፋን ፡ ወለላዕላዓን ፡ ረሰዮሙ ፡ ይትናገሩ ፡ ርቱዐ ፡ (ዘፀ፬ ፡ ፲ ። ቀሌ ። ኪዳ ። ያዕ ፡ ዘ እል) ።

**ልዒት ፤ ቶት ፤ (ለዐተ ፡ ይልዕት ፡ ይል ዐት) ፤** መላት ፤ ላት ፡ ማውጣት ። መትከል ፡ ማግባት ፤ ማዋደድ ፡ መስካት ፤ ማስማማት ፤ ዕንጨትን ፡ ከብረት ፤ ብረትን ፡ ከንጨት ።

**ለዐት ፤ እው ፡ ላዓት ፤** በቁሙ ፡ ላት ፤ የበግ ፡ ኸራት ። ቅጠል ፡ የበግ ፡ ላት ፡ የሚባል ። ውላጋ ፡ እጀታ ፤ የሰይፍ ፡ የካራ ፡ የንፍጥ ። ወአብአ ፡ ሎቱ ፡ እስከ ፡ ላዓታ ፡ (መሳ፫ ፡ ፳፪) ።



ለዐት ፡

**ለፈየ ፤ (ፈለየ ፡ ጠ ፤ ሴለየ) ፤** ለየ ፡ ከፈለ ፤ ኹለት ፡ አደረገ ። ኢትልፍይዎ ፡ ለአሐዱ ፡ ክርስቶስ ፤ ወኢትረስይዎ ፡ ለወልድ ፡ ለፌ ፡ ወለሥጋ ፡ ዘነሥአ ፡ ለፌ ፡ (ሃይ ፡ አበ) ። ወዲያ ፡ ወዲህ ፡ አለ ፤ ተገላመጠ ።

**ለፌ ፤ (ጽር ፡ ፖዬ) ፤** ወዲህ ፡ ወደዚህ ፤ ወ ዲያ ፡ ወደዚያ ፤ የጊዜ ፡ የቦታ ። ለፌ ፡ እማርያም ። ለፌ ፡ እምጥምቀት ፤ የጊዜ ። እምለፌሂ ፡ ወእምለ ፌሂ ። ነጸረ ፡ ለፌ ፡ ወለፌ ፤ የቦታ ፡ (አፈ ፡ ተ፮ ። መጽ ፡ ምስ ። ፩ነገ ፡ ፲፬ ፡ ፲፯ ። ዘፀ፪ ፡ ፲፪) ። ዝየንና ፡ ከሣን ፡ ተመልከት ።

**ለፈፍ ፤ ፎት ፤ (ለፈ ፤ ለፈፈ ፡ ይለፍፍ ፡ ይልፍፍ ። ዕብ ፡ ላፌፍ ። ሱር ፡ ላፍ ። ዐረ ፡ ለፈ) ፤** መለፈፍ ፤ መሸፈን ፤ መጠቅለል ። መልፈፍ ፡ መ ለፍለፍ ፤ መስበክ ፡ ዐዋጅ ፡ መንገር ። (ተረት) ፤ የሹም ፡ ስነፍ ፡ አይለፍ ፡ አይለፈልፍ ። ባፍ ፡ ይጠፋ ፡ በለፈለፉ ። መልፋት ፡ መድከም ፤ የቈርበት ፡ የጕልበት ።

**ለፋፊ ፤ (ፊት ፡ ፍያን ፡ ያት ፤ ፈፍት) ፤** በቁሙ ፤ የሚለፍ ፡ የሚለፈልፍ ፡ ሰባኪ ፤ ጠቅላይ ። ባለ ቅኔዎች ፡ ግን ፡ ለፈፈ ፡ ጻፈ ፤ ለፋፊ ፡ ጣፊ ፡ ይላሉ ።

**ልፋፍ ፤ (ዐረ ፡ ሊፋፈት) ፤** መለፈፊያ ፤ መ ሸፈኛ ፡ ሠርመዲ ። አምጽአ ፡ ልፋፈ ፡ ከመ ፡ ይክድን ፡ አዕይንቲሁ ፡ (ስንክ ፡ መጋ፯) ።

—፤ የጠንቋይ ፡ ክታብ ፤ ጠልሰም ፡ ዐይነ ፡ ጥላ ፤ እንደ ፡ ፊደል ፡ የሚጠቀለል ። የጠንቋይም ፡ ባይኾን ፡ የሚጠቀ ለል ፡ ክኾነ ፡ ማናቸውም ፡ ጥፈት ፡ ልፋፍ ፡ ይባላል ፤ ል ፋፈ ፡ ጽድቅ ፡ እንዲሉ ።

**ልፋፈ ፡ ጽድቅ ፤** መንፈሳዊ ፡ ክታብ ፤ የደ ረት ፡ መጣፍ ፤ ማንበቡና ፡ መሸከሙ ፡ ብቻ ፡ የሚያጸ ድቅ ፤ ኋላም ፡ ሲሞቱ ፡ ዐብሮ ፡ የሚቀበር ። መንፈሳዊ ነቱ ፡ በአፍኣ ፡ ነው ፡ እንጂ ፤ በውስጡ ፡ ብዙ ፡ ጸያፍ ፡ ቃል ፡ ሐሰትና ፡ ስሕተት ፡ አለበት ። ከሐሰቱም ፡ አንዱ ፤ እግዜር ፡ እንዳሠርቱ ፡ ቃላት ፡ በጁ ፡ ጣፈኝ ፡ ይላል ። ሌላም ፡ ይህን ፡ የመሰለ ፡ ግብዞችና ፡ አታላዮች ፡ ፈልሰ ፈው ፡ ያወጡት ፤ አርድእት ፤ ባርቶስ ፤ ኅቡእ ፡ ስም ፡ የሚ ሉት ፡ ልፋፍ ፡ አለ ።

**መልፋፍ ፤ (ዐረ) ፤** የተሸፈነ ፡ የተጠቀለለ ፤ ሽፍን ፡ ጐመን ፡ ኰርንባ ፤ ጭብጠና ፡ ኰብ ፡ ራስ ፡ የሚ መስል ፤ ቶሎ ፡ የሚበስል ።

**ለፍለፈ ፤** በቁሙ ፤ ለፈለፈ ፡ ቀባጠረ ፤ ነገር ፡ አበዛ ፡ (ዐማርኛ) ።

**ለፈጸ ፤ (ፈለጸ ። ሎሰ) ፤** ለፈጠ ፡ ለወሰ ፤ ዐሸ ፡ አበቀ ፡ አበሰበሰ ፤ የደቄት ፡ የበሶ ። ከፈለጸና ፡ ከሎሰ ፡ ከኹለቱ ፡ ሥር ፡ የወጣ ፡ ነው ።

**ተለፍጸ ፤** ተለፈጠ ፤ ታሸ ፡ ታበቀ ፡ ተለወሰ ። ሊጥ ፡ ማለት ፡ የዚህ ፡ ዘር ፡ ነው ።

**ልፋጽ ፤** የተለፈጠ ፡ ልፍጥ ፤ የታሸ ፡ የታበቀ ፡ ልዉስ ፤ ፍጹም ፡ ሊጥ ፡ ቀጭን ፡ ብጥብጥ ፡ ያይደለ ፡ እን ፍርፍር ። ልፋጽ ፡ በቅብዕ ፡ (ዘፀ፳፱ ፡ ፱) ።

**ልፍጸት ፤** ልፋጽነት ፤ እንፍርፍርነት ፡ (መ፡ፈ) ።

**ለፈቀ ፤ (ትግ ፡ ሐባ ፡ ለፍቀ ፤ ሰፋ ፡ ጠ ቀመ) ፤** ነበዘ ፤ አጥብቆ ፡ ያዘ ፤ ቀለመ ፡ ቢያጥቡ ፡ አይ ጠራ ፡ ኾነ ፤ የደም ፡ የቀለም ፡ የርስሐት ። በተነስሖቱኒ ፡ ኢተሰርየ ፡ ሎቱ ፡ ንጢአቱ ፤ እስመ ፡ ደመ ፡ መለኮት ፡ ዘለፈቀ ፡ (መጽ ፡ ምስ) ።

**ላጽዮ ፤ ዮት ፤ (ላጸየ ፡ ይላጺ ። ዕብ ፡ ወሱር ፡ ጋላሕ ። ዐረ ፡ ማሰ) ፤** መላጨት ፡ መለጣ ጨት ፤ ጠጕርን ፡ ከሥጋ ፡ መለየት ፤ ከሥሩ ፡ መቍረጥ ፡

መጋጠጥ፤ ቈርበቱ፡ እስኪታይ፡ እስኪገለጥ። ላጸየ፡ ሥዕርተ፡ ርእሱ። ላጸዮሙ፡ መንፈቀ፡ ጽሕሞሙ። ርእሰ፡ ኢይላጺ፡ (ኢዮ፩፡፳። ፩ዜና፡ ፲፱፡፬። ዘሌ፳፩፡፲)።

**አላጸየ፤ አስተላጸየ፤** አስላጨ።

**ተላጸየ፤** ተላጨ፤ ተለማጨ፡ (ዘሌ፲፫፡ ፴፫። ፲፬፡ ፳፡ ፱። ሚክ፩፡ ፲፮)። ተላጸየ፡ ርእሶ። ለትትላጸይ፡ ወእመ፡ አኮ፡ ለትትቀረፅ፡ (ግብ፲፰፡ ፲፰። ፩ቆሮ፡ ፲፩፡ ፮)።

**ሉጺይ፤ ልጺይ፤ (ያን፡ ያት፡ ጺት)፤** የተላጨ፡ ልጩ። ልጺያን፡ አጽሓሚሆሙ። እስመ፡ ከመ፡ ሉጺት፡ ይእቲ፡ (ኤር፵፰፡ ፴። ፩ቆሮ፡ ፲፩፡ ፭)።

**መላጺ፤ (ጽያት)፤** መላጫ፡ መቍረጫ፤ ምላጭ፡ ሰንጢ፤ ሰይፍ፡ ካራ፤ ስለታም፡ ብረት፡ (ኢሳ፯፡ ፳። መዝ፡ ፶፩። ዘኍ፮፡ ፭)። መላጺ፡ ኢሰከፈኒ፡ ርእስየ፤ እስመ፡ ናዝራዊ፡ አነ። ከመ፡ ጠቢብ፡ ዐቃቤ፡ ሥራይ፡ ዘይጠብሕ፡ በመላጺ። ከመ፡ መላጺ፡ በሊኅ፡ ዘክልኤ፡ አፉሁ፡ (መሳ፲፮፡ ፲፯። ዲድ፡ ፲። ሚራ፳፩፡ ፫)።



መላጺ፡

**ለጽለጸ፤ (ዐረብ)፤** ተናወጠ፡ ተውለበለበ፤ ወዲያ፡ ወዲህ፡ ላይ፡ ታች፡ ደፋ፡ ቀና፡ አለ፤ ተቅመደመደ፤ የሚዛን፡ የልሳኑና፡ የስሓኑ፤ ለከይሲም፡ ይኾናል። ባለቅኔዎች፡ ግን፡ መዘነ፡ ብለው፡ ይፈታሉ። ለጠለጠ፡ ልጥልጥ፡ አደረገ፤ በልክ፡ በሚዛን፡ (ዐማርኛ)። ዘሩ፡ ለጺጽ፡ ነው።

**ለጽሊጽ፤** የሚዛን፡ ምላስ፤ ውልብልቢት፡ ላንሴታ፤ ማእከል፡ ኹኖ፡ ግራና፡ ቀኙን፡ የሚያስተካክል። ከመ፡ ለጽሊጸ፡ መዳልው፡ ፍትሐ፡ እግዚ፡ (ምሳ፲፮፡ ፲፩። ጥበ፲፩፡ ፳፫)። አንዳንዱ፡ መጽሐፍ፡ በለጽሊጽ፡ ፈንታ፡ ለጽላጺ፡ እንደ፡ ማለት፡ ልጽላጼ፡ ይላል፤ የጣፊ፡ ስሕተት፡ ነው።



ለጽሊጽ፡

**ለጺጽ፤ (ለጸ፤ ለጸጸ)፤** መለጠጥ፤ (ጥለ) መለጠጥ፤ ለጣጭ፡ ተለጣጭ፡ ልጥጥ፡ መኾን።

**ለጺቅ፤ ቆት፤ (ለጸቀ፡ ይለጽቅ፡ ይልጽቅ። ዐረ፡ ለጺቀ፤ ለዚቀ፤ ለሲቀ)፤** መለጠቅ፡ መጣበቅ፡ መጠጋት፤ ልክክ፡ ልስቅ፡ ማለት፡ መስማማት። እንዘ፡ ይለጽቅ። እስከ፡ ለጸቀ፡ ማእሰ፡ ሥጋሁ፡ ዲበ፡ ዐፅሙ። ጠግዐ፡ ወለጸቀ፡ ምስለ፡ መንበሩ፡ (ዘፀ፳፯፡ ፳፰። ስንክ፡ መስ፲፱። ግን፮)።

—፤ መቅረብ፡ መድረስ፤ ለመያዝ፡ ለመንካት። እስከ፡ እሙንቱ፡ ይለጽቁ፡ ኀበ፡ ቀቢጸ፡ ተስፋ፡ (ማር፡ ይሥ፬፡ ፩)። ብዙው፡ መጽሐፍ፡ ግን፡ በጽሐ፡ ቀርበ፡ በማለት፡ ፈንታ፡ ለጸቀ፡ እንደ፡ ማለት፡ አልጸቀ፡ ይላል፤ የመላሽና፡ የጣፊ፡ ስሕተት፡ ነው። አልጸቀት፡ ለወሊድ። አልጸቀት፡ ሖሳዕክሙ። አልጸቀ፡ ዘያጸድቀኒ። አልጸቀት፡ ነፍሱ፡ ለመዊት። አልጸቀት፡ ዕለተ፡ እግዚ። አልጺቆ፡ ኢየሩሳሌም፡ (ኢሳ፶፯፡ ፲፯። ፵፩፡ ፳፩። ፱፡ ፳። ኢዮ፴፫፡ ፳፪። ዮኤ፩፡ ፲፭። ማር፲፩፡ ፩)።

**አልጸቀ፤** አለጠቀ፤ አስለጠቀ። አስጠጋ፤ አቀረበ። ታለጽቆሙ፡ ለርሑቃን፡ (ቅዳ፡ ዮሐ)። ዳግመኛም፡ አብጽሐ፡ አቅረበ፡ በማለት፡ ፈንታ፡ አልጸቀ፡ አስተልጸቀ፡ እንደ፡ ማለት፡ ኹሉ፤ ባደራራጊ፡ አስተላጸቀ፡ ይላል፤ ስሕተት፡ ነው። በተቃርቦ፡ አስተላጸቀ፡ ለርእሱ፡ ካልአ፡ ብእሴ። ተዓርከ፡ ከመ፡ ዝ፡ ውእቱ፤ ዘየአምኖ፡ ለፍቁሩ፡ ወያስተላጽቆ፡ በፍሥሓ፡ ወኢይትዔበይ፡ ላዕሌሁ። እለ፡ ያስተላጽቁ፡ ሰንበታተ፡ ሐሰት። እመ፡ አስተላጸቅሙ፡ ወአዝለፍክሙ፡ ኀልዮ፡ (ቄር፡ ጸላ። ፈላስ፡ ገ፲፭። ዓሞ፮፡ ፫። አፈ፡ ድ፴፫)።

**ተላጸቀ፤** ተላጠቀ፡ ተለጣጠፈ፤ ተጣጋ፡ ተያያዘ፤ ተጣመረ፤ ተቃረበ። እለ፡ ይትላጸቃ፡ በበይናቲሆን። ነፍስ፡ እንተ፡ ትትላጸቅ፡ ምስለ፡ እግዚ። እመ፡ ቦ፡ ብእሲ፡ ዘተላጸቀ፡ ወሰከበ፡ ምስለ፡ ብእሲቱ፡ በእሎን፡ መዋዕል። ተላጽቆተ፡ ስኢል፡ (ዘፀ፳፰፡ ፯። አፈ፡ ተ፳፰። ፈ፡ መ፡ ፲፡ ፫። አፈ፡ ተ፳፯)። በቀርበና፡ በለጸቀም፡ ፈንታ፡ ተላጸቀ፡ ይላል። ሶበ፡ ይትላጸቆ፡ ብእሲ፡ ወየሐውር፡ በገቦሁ፡ ይረግዞ። ይትላጸቅ፡ ረድእ፡ ለመምህሩ። ጎኑ፡ ዘይትላጸቅ፡ (ዮሴፍ። ቄር፡ ጸላ። ፍ፡ ነ፡ ፴፯)።

**ልጹቅ፤ (ቃን፡ ቃት፡ ጽቅት)፤** የለጠቀ፡ የቀረበ፤ የተጠጋ፡ የገጠመ፤ የተያያዘ፡ ፅሙር። አዘዘ፡ ጡጦስ፡ ያንኅሉ፡ መካነ፡ ልጹቀ፡ ቍድስ። አግዋር፡ እለ፡ ልጹቃን። እመ፡ ኮነት፡ ነፍስ፡ ልጽቅተ፡ ምስለ፡ እግዚአብሔር፡ (ዮሴፍ። ፍ፡ ነ፡ ፴፯። አፈ፡ ተ፳፯)።

**ልጽቀት፤** መለጠቅ፡ መጣበቅ፤ ልጥቅ፡ ማለት፡ እንደ፡ ድጕስ። ቅርበት፡ አው፡ ልጽቀት፡ (ቄር፡ ጸላ)።

**ለጽቅ፤** ማጣበቂያ፡ መጣብቅ፤ ሙጫ፡ ሙቅ።

**ልጽቅ፤ (ብ፡ ልጸቅ)፤** ሳንቃ፡ መዝጊያ፤ ወይም፡ የቤት፡ ታዛይ፡ ጕርጅ፡ ጓዳ። ሞኀት፡ ውሳጥያት፡ እለ፡ ያበውኣ፡ ውስተ፡ ልጽቀ፡ ቤት፡ (፪ዜና፡ ፬፡ ፳፪)።

**ላጽቂት፤ (ዕብ፡ ልጣአ)፤** ሸለሊት፤ እንሽላሊት፤ የገበሎ፡ ዐይነት። ወይም፡ ሣሬት፡ ሸረሪት። ላጽቂት፡ ዘበእደዊሁ፡ የሐውር፡ (ምሳ፴፡ ፳፰)።



ላጽቂት፡

አስተላጸቀ፤ አላጠቀ፤ አጣጋ፥ አቃረበ። ዛቲ፥ መጽሐፍ፥ አስተላጸቂት፥ ርሑቃን። በአስተላጽቆ፥ (ፈላስ። ስንክ፥ ሠኔ፲፪)።

ሊቅ፤—በቁሙ፥ አሮጌ፤—ልሂቅ፥ ልህቀ።

ሊቃአንስጢ፤ (ጽር፥ ሊከዎኒስቲ)፤ ስመ፥ ሀገር፤ በቱርክ፥ አገር፥ ውስጥ፥ ከዚያውም፥ በፍርግያ፥ ክፍል፥ ያለች፥ ታላቅ፥ መዲና፥ (ግብ፲፬፥ ፲፩)።

ለቂድ፤ ዶት፤ (ለቀደ፥ ይለቅድ፥ ይልቅድ። ዕብ፥ ላከድ)፤ መያዝ፥ እጅ፥ ማድረግ፤ ፈልጎ፥ ማግኘት፤ ይዞ፥ ማሳየት። ዘይሌቅድ፥ ብዕለ፥ እንበለ፥ ንዋይ፤ ወግርማ፥ እንበለ፥ ሚመት፤ ወኀይለ፥ እንበለ፥ ዐደው፥ (ፈላስ፥ ገ፹፮)።

ለቀደ፤ ለቈደ፥ አሰረ፤ የምላስ። ለገደ፥ ዘጋ፤ የጕረሮ።

ለቅዳ፤ በቁሙ፤ ቅምሖ፥ ያንቃር፥ የጕረሮ፥ የምላስ፥ በሽታ፤ ሕበጥ። ቅምሖ፥ የቀምሖ፥ ዘር፥ ነው።

ለቅሀ፤—አለቃ፥ አበደረ፤—ለቅሐ፥ ለቅሐ።

ለቀወ፤ ለቀየ፤ (በቂው፥ በቀወ)፤ ለቀቀ፥ አላቀቀ፤ አዛጋ፥ አፋሸገ፤ ከፈተ፥ ፈታ፤ የአፍ፥ የቍልፍ። መኑ፥ ክልአክሙ፥ አርምሞ፤ መኑ፥ ለቀዎ፥ ለአፋክሙ፥ ከመ፥ ትንብቡ፥ ዘንተ፤ መኑ፥ አገበረክሙ፥ ለተናግሮ፥ (መጽ፥ ምስ)። ወና፥ የ፥ ተወራራሾች፥ ስለ፥ ኸኑ፥ በዘረወ፥ ፈንታ፥ ዘረየ፥ እንዲል፤ በለቀወም፥ ፈንታ፥ ለቀየ፥ ይላል፤ ሥሩና፥ ምንጩ፥ በቀወ፥ ነው። ጕድጕደ፤ ወሶበ፥ አልቦ፥ ዘያወሥእ፥ ለቀየ፥ ወቦአ፥ ውስተ፥ ጽርሕ፥ (ዮዲ፲፬፥ ፲፭)።

ለቀወ፤ አቀጠለ፥ ቅጥይ፥ አወጣ፤ የማር፥ የቅጠል፥ የማሽላ።

ለቆ፤ (ዕብ፥ ሌቄሽ)፤ በቁሙ፥ ደኃራዊ፥ ማር፤ ዳግማይ፥ ቡቃያ፥ ቅጥይ፤ ከቈረጣና፥ ከጨዳ፥ በኋላ፥ በገፍና፥ በብላጊ፥ ዝናም፥ የሚበቅል፥ (ዐማርኛ)።

ለቆታ፤ (ትግሬኛ)፤ አቅማዳ፥ ስልቻ፤ አፋም፥ አፈ፥ ስፊ፥ ማለት፥ ነው። አቅማዳፍ፥ ስልቻፍ፥ እንዲሉ።

ለቅሐ፤ ሐት፤ (ለቅሐ፥ ይሌቅሕ፥ ይለቅሕ። ዕብ፥ ላቃሕ፤ ወሰደ)፤ ማለቃት፤ ማበደር፥ መስጠት፤ ማስተማር፤ ትርፍ፥ ለማግኘት፤ ኋላ፥ ለመቀበል። በደረንና፥ ተበድረን፥ እይ። እመ፥ ለቃሕከ፥ ብሩረ፥ ለነዳይ። ኢትለቅሖ፥ ለዘይብዕለከ። ብዙኃን፥ እለ፥ ኢይሌቅሑ። ወዘኢለቅሐ፥ ወርቀ፥ በርደ፥ (ዘፀ፳፪፥ ፳፬። ሢራ፰፥ ፳፪። ፳፱፥ ፯። መዝ፥ ፲፬)።

ለቃሒ፤ (ሒት፥ ሕያን፥ ያት)፤ የሚያለቃ፥ አለቂ፤ አበዳሪ። ወለእመ፥ ንለፈ፥ ይደልዎ፥ ለለቃሒ፥ ከመ፥ ይምልክ፥ ዘአኀዘ። በቍዔተ፥ ለቃሒ፥ (ፍ፥ ነ፥ ፳፯)።

አለቅሐ፤ አስለቃ፥ አስበደረ፤ ከልቆ፥ ከብድር፥ አገባ።

ተለቅሐ፤ ተለቃ፥ ተበደረ፤ ወሰደ፥ ተቀበለ፤ የገንዘብ፥ የትምርት። እፈዲ፥ እሎንተ፥ ዘተለቃሕኩ፤ ትምርት፥ (አረጋ፥ መልፀ፰)። ዘይትሌቃሕ፥ ከመ፥ ዘይሌቅሕ። ኢትትለቃሕ፥ እንዘ፥ ነዳይ፥ አንተ። ዘይትሌቃሕ፥ ሥርናየ፥ ውስተ፥ ክምሩ፥ (ኢሳ፳፬፥ ፪። ሢራ፲፰፥ ፴፫። ምሳ፳፥ ፬)። ዐለፈ፥ ተሰጠ፤ ተሰሜ፥ ኾነ፥ ገንዘቡ፥ ከበዳሪ፥ ወደ፥ ተበዳሪ።

ተለቃሒ፤ ልቆኛ፤ ተማሪ፥ ተበዳሪ። ለቃሒ፥ ወተለቃሒ፥ (ምሳ፳፱፥ ፲፫)።

ልቁሕ፤ (ሓን፥ ሓት፥ ቅሕት)፤ የተለቃ፥ የተበደረ፥ ተቀባይ፤ ወይም፥ ተሰሜ።

ልቃሕ፤ (ሓት)፤ ልቆ፥ ብድር፥ ዕዳ። ዘየሐንጽ፥ ቤቶ፥ በንዋየ፥ ልቃሕ። ምጽዋትሰ፥ ልቃሕ፥ አምላካዊት። ወልቃሕሰ፥ ይደሉ፥ ከመ፥ ይኩን፥ በአኀዝ፥ አው፥ በትሕቢት፥ (ሢራ፳፩፥ ፰። ፍ፥ ነ፥ ፲፮። ፳፯)።

ልቃሔ፤ (ሕያት)፤ ማበደር፤ መበደር፤ አበዳደር፥ ብድሩ፤ ልቆ፥ የብድር፥ ሥራ። እስመ፥ አፍቅሮቱ፥ በላዕሌከ፥ ልቃሔ። ፍትሐ፥ ልቃሕያት፥ (ማር፥ ይሥ፴፫፥ ፫። ፍ፥ ነ፥ ፴፱)።

ለቀየ፤—ለቀቀ፥ ከፈተ፤—ለቀወ።

ለቅለቀ፤ (ለቂቅ፤ ለቀ)፤ ለቀለቀ፥ ቀባ፤ መረገ፥ ዘጋ፥ ደፈነ፤ የቤት፥ የዐዘቅት፥ ያውድማ፥ የጉቅ፥ የሥንጥቅ። ኢገብአ፥ ውስቴቶሙ፥ ማይ፥ ወለቅለቅ ዎሙ፥ በዐረር፥ (አዋል፥ ትርጓሜ። ኤር፪፥ ፲፫)። ዐጠበ፥ አጠራ፤ የልብስ።

ልቅላቄ፤ መለቅለቅ፤ አለቃለቅ፥ ልቅለቃ፤ ልቅልቃት፤ መጨረሻ፥ ዕጥበት።

ለቀመ፤ (ዐረ፥ ለቀጠ። ዕብ፥ ላቃጥ)፤ በቁሙ፤ ሰበሰበ፥ አከማቸ፥ (ዐማርኛ)።

ለቀሠ፤—ዐዘነ፥ አለቀሰ፤—ለቀሰ።

ለቂቅ፤ ቆት፤ (ለቀ፤ ለቀቀ፥ ይለቅቅ፥ ይልቅቅ። ለቀወ፥ በቀወ። ዕብ፥ ላቃቅ፤ ላቅሌቅ፤ ላሰ፥ ሞለቀቀ)፤ መልቀቅ፤ መክፈት። መተው፥ መስደድ፥ (ዐማርኛ)።

ለቀቀ፤ (ዐረ፥ ለቀ። ዕብ፥ ላቃሀ)፤ መታ፥ ጸፋ፤ ገረፈ። አዘዘ፥ ይልቅቅዎ፥ ወይኅምይዎ፥ ውስተ፥ ዘነበ፥ ፈረስ፥ ወያዑድዎ፥ ውስተ፥ ሀገር፥ (ስንክ፥ ሠኔ፲፱)። ፪ኛም፥ አስረው፥ ይተዉት፥ ዘንድ፥ ያስኛል።

ለቀሰ፤ (ትግ፥ ለቅሰ። ዐረ፥ ለቂሰ)፤ ዐዘነ፥ ተጨነቀ፤ አለቀሰ፥ እንባ፥ አፈሰሰ። ዕብራይስጡ፥ ግን፥ ላቂሽ፥ ብሎ፥ ለቀመ፥ ቃረመ፥ ሰበሰበ፥ ይላልና፤ በዚህ፥ ዘይቤ፥ ሲፈቱት፥ ልቅሶኛ፥ መጥራትን፥ አልቃሹኝ፥ ማለትን፥ ያሳያል፤ በከየን፥ እይ።

አልቀሰ፤ አስለቀሰ፤ አሳዘነ። ባማርኛ፥ ግን፥ አድራጊ፥ ነው።

**ተለቅሰ**፤ ተለቀሰ፤ ልቅሶው፡ ሐዘንተኛው ፡ ተለቀሰለት፤ ሟቹ ።

**ተላቀሰ**፤ በቁሙ፤ ተለቃቀሰ፡ ተዛዘነ ።

**አስተላቀሰ**፤ አላቀሰ፤ አለቃቀሰ፡ አስተዛዘነ ። ስሕልት፡ ሰይፍከ፡ ብእሲ፡ ልዑል፤ (የተሳለች፡ ሰይፍኽ፡ ታላቅሰው)፡ ለሰብአ፡ ሞረት፡ ወመርሕ፡ ቤቴ፡ ለምኃ፡ ኢየሱስ፡ መስተጋድል፡ (ቀጠፋ፡ ቅኔ) ። መጽሐፍ፡ ግን፡ በናዘዘ፡ ፈንታ፡ አስተላቀሰ፡ እንደ፡ ማለት፡ አላቀሰ፡ ይላል፤ ስሕተት፡ ነው ። ወብዙኃን፡ እምነ፡ አይሁድ፡ እለ፡ ሖሩ፡ ኀበ፡ ማርያ፡ ወማርታ፡ ከመ፡ ያላቅስዎን፡ በእንተ፡ እኁሆን፡ (ዮሐ ፲፩፡ ፲፱) ።

**ለሮን**፤ (ጽር፡ ላሮስ ። ሮማይ፡ ላሩስ ። ዕብ፡ ሻሓፍ)፤ የወፍ፡ ስም፤ ድምፁና፡ መልኩ፡ ደስ፡ የሚያሰኝ፤ ደረቱ፡ ብጫቴ፡ ወርቅማ፡ (ዘሌ፲፩፡ ፲፯ ። ዘዳ፲፬፡ ፲፭)፡ ባለብሉዮች፡ ግን፡ ይብራ፡ የባሕር፡ አሞራ፡ ይሉታል ።



ለሮን፡

**ለሮስ**፡ (ዕብ፡ ላሮስ)፤ ለማራስ፡ ለማረስረስ፤ ለማበቅ፡ ለማበስበስ፤ ለማርጠብ፡ ለመለወስ፤ ለማፈርፈር፡ ለመለፈጥ ። ዘሩ፡ ራሰሰ፡ ራሰ፡ ያሩስ፡ ነውና፤ ርሕሰንና፡ አርሐሰን፡ ለፈጸን፡ እይ፡ (ሕዝ፵፯፡ ፲፱) ። ዳግመኛም፤ ለሮስ፡ በማለት፡ ፈንታ፡ ለለዊስ፡ ይላል፤ ፍችው፡ አንድ፡ ነው ።

**ሎሰ**፤—ለወሰ፡ አበካ፤—ለዊስ ።

**ለሰደ**፤ (ዐረ፡ ለሰደ)፤ ጠባ፡ መጠጠ፤ ጨመቀ፡ አፈረጠ፤ የጡት፡ የፍሬ ። ረጋ፡ ጸና፤ የወተት፡ የማር፡ የፈሳሽ ።

**ለስድ**፤ (ዕብ፡ ልሳድ)፤ ጭማቂ፡ ውጤት፡ (ደም፡ ወተት)፤ ዕትብት፡ አሰድ፡ እንግዴ፡ ልጅ ። ለስታ፡ ለጋ፡ ትኵስ፡ ቅቤ፤ ከረጋ፡ ወተት፡ የሚወጣ፤ ዝብድን፡ እይ ። ሕልብ፡ ሐሊበ፡ ወይከውነከ፡ ለስደ፡ (ምሳ፴፡ ፴፫) ።

**ለስሐ**፤ (ለትሐ)፤ ለፈጨቀ፤ አፋን፡ ምላሱን፡ አጮኸ፤ እንጯ፡ እንጯ፡ አለ ። ኢትልሳሕ፡ እንዘ፡ ትሜጽር፡ (ሚራ፵፱፡ ፲፯) ። ለስሐና፡ ለትሐ፡ የልሒስ፡ ዘር፡ ናቸው ።

—፤ ላሸ፡ ዐለጠ፤ ዐልጫ፡ ኾነ፡ ጣዕም፡ ዐጣ፤ ከዚህ፡ የተነሣ፡ ተናቀ፡ ተጠላ፡ ተንቀፈ፤ የምግብ፡ ያንደበት፡ የነገር ። ወእመሰ፡ ጼው፡ ለስሐ፡ በምንት፡ ይቄስም፡፡ ውስተ፡ አፉሁ፡ ለአብድ፡ ይለስሕ፡ አምሳል፡፡ ከመ፡ ኢትልሳሕ፡ በእበድከ፡፡ ለስሐ፡ ኀይልየ፡ ወደከመ፡ በጸሎትከ፡ (ማቴ፭፡ ፲፫ ። ሚራ፳፡ ፳ ። ፳፫፡ ፲፱ ። ገድ፡ ተክ) ።

**ልሱሕ**፤ (ሓን፡ ሓት፡ ስሕት)፤ የላሸ፡ ያለጠ፡ ዐልጫ፤ ሕጹጽ፡ ምኑን ። ልሱሕ፡ ነገሮሙ፡ ለአብዳን ። ጼው፡ ዘአጥዐም፡ ለልሱሕ ። ልሱሐ፡ ኀይል፡ (ሚራ፳፡ ፳፱ ። ቅዳ፡ ዮሐ ። ገድ፡ ኪሮ) ።

**ልስሐት**፤ መላሸት፡ ማለጥ፤ ዐልጫ፡ መኾን፡ ዐልጫነት፤ አለመጣፈጥ ። ልስሐት፡ ጼው፡ ግዱፍ ። ልስሐተ፡ ልሳንየ፡ (ስንክ፡ ጥቅ፲፱ ። ደራሲ) ።

**አልስሐ**፤ አላሸ፡ ዐልጫ፡ አደረገ፤ አደከመ፡ አስነፈ፤ አሰናቀ፡ አስነቀፈ ። አልስሐ፡ ሕምዘ፡ ዘከዐወ፡ ቀታሊ፡፡ በሃይማኖተ፡ ዚኣሁ፡ አልስሐ፡ ዙሉ፡ መዋቅሕቲሁ፡፡ ወዘሰ፡ ይኑብብ፡ በከመ፡ ረከበ፡ ያለስሕ፡ ርእሶ፤ ወአልቦ፡ ሞገስ፡ ለቃሉ፡፡ ያለስሓ፡ ለምክሮሙ፡ (ግንዘ ። ድጓ ። ሚራ፳፱ ። ኢሳ፵፱፡ ፳፭) ።

**ለስኖ**፤ ኖት፤ (ለሰነ፡ ይሌስን፡ ይለስን)፤ መለሰን፡ መምረግ፤ ምርግን፡ ማስተካከል፤ ምላስ፡ የላሰው፡ ማስመሰል፤ የጭቃ ። ገብስሰን፡ እይ፡ (ዐማርኛ) ።

**ለሰነ**፤ (ዕብ፡ ላሼን)፤ ለፈለፈ፡ ቀባጠረ፤ አፈቸለ፡ ተናገረ፤ ፊት፡ ለፊት ። ነገር፡ ሠራ፡ አሳበቀ፤ ባንደበት፡ ወይም፡ በወረቀት ። መጽሐፍ፡ ግን፡ በለሰነ፡ ፈንታ፡ ተለሰነ፡ ይላል፤ ስሕተት፡ ነው ። ዘእንበለ፡ ጥበብ፡ ይትሌሰኑ፡ (ቄር፡ ጸላ) ። ለዐለን፡ እይ፤ ይህም፡ እንደዚያ፡ ነው ።

**ለሳኒ**፤ መለስን፤ ለፍላፊ፡ አሳባቂ፡ ምላሰኛ፤ ለሳኝ ።

**ተለሰነ**፤ በቁሙ፤ ተመረገ፤ ጭቃው፡ ቤቱ ።

**ልሱን**፤ (ናን፡ ናት፡ ስንት)፤ የተለሰነ፡ ልስን፤ ምርግ ።

**ልሳን**፤ (ናት ። ዕብ፡ ላሾን ። ሱር፡ ሊሽና ። ዐረ፡ ሊሳን)፤ በቁሙ፤ ምላስ፡ አንደበት፤ የአፍ፡ ውስጥ፡ ሕዋስ፡ የመብል፡ የነገር፡ መሣሪያ፡ (ያዕ፫፡ ፩፡ ፯ ። ሚራ፳፰፡ ፲፭፡ ፲፱፡ ፳፯ ። መዝ፡ ፩ ። ፲፭) ። በርሱ፡ መሣሪያነት፡ የሚነገር፡ ቃልና፡ ቋንቋም፡ ክርሱ፡ ስም፡ ነሥቶ፡ ልሳን፡ ይባላል ። ዘክልኤ፡ ልሳኑ፡፡ ልሳነ፡ ጥዑም፡፡ ጥዑመ፡ ልሳን፤ ቃል፡ ነገር፡ (ሚራ፮፡ ፩ ። ፵፡ ፳፩ ። ድጓ) ። ሕዝብ፡ ዘኢተአምር፡ ልሳኖሙ፡፡ እለ፡ ካልእ፡ ልሳኖሙ፡፡ በካልእ፡ ልሳን፡ ይትናገሩ፡፡ ሰብዓ፡ ወክልኤቱ፡ ልሳናት፤ ዘሴም፡ ዕሥርቱ፡ ወሰብዐቱ፤ ዘካም፡ ሠላሳ፤ ዘያፌት፡ ዕሥራ፡ ወኀምስቱ፡ (ኤር፭፡ ፲፭ ። ሕዝ፫፡ ፯ ። ማር፲፮፡ ፲፯ ። ትርጓ፡ ፊደ) ።



ልሳን፡

**ልሳን፡ እንተ፡ ወርቅ**፤ የወርቅ፡ ገንዘብ፡ በልሳን፡ አምሳል፡ የተሠራ፡ (ኢያ፯፡ ፳፩) ።

**ልሳን፡ እሳት**፤ የእሳት፡ ላንቃ፡ ነበልባል፡ (ሐዋ፲፱፡ ፱) ።

**ልሳነ ፡ ባሕር ፤** የባሕር ፡ ጫፍ ፤ ሾለቅ ፡ አምጥሙጦ ፡ ወደ ፡ የብስ ፡ ማኸል ፡ የሚገባ ፡ (ኩፋ ፡ ፯) ። ወደ ፡ ባሕርም ፡ የሚገባ ፡ ወንዝ ፡ ልሳን ፡ ይባላል ፡ (ኢሳ፲፩ ፡ ፲፭) ።

**ልሳናዊ ፤** ነዊን ፡ ልሳን ፤ ምላሰኛ ፡ ለፍላፊ ፡ አሳባቂ ፤ ወይም ፡ ቋንቋ ፡ ዐዋቂ ።

**ልሳነ ፡ ወርቅ ፤** ጽሩየ ፡ ቃል ፤ ነባቤ ፡ ቃል ፡ ጽሩይ ፤ እንደበተ ፡ ጥሩ ፡ (ፊ ፡ መ ፡ ፪ ፡ ፱) ።

**ልሳነ ፡ መድሎት ፤** የሚዛን ፡ ቀንበር ፡ ጋድሙ ፤ ወይም ፡ ላንቤታው ፡ (ጥበ፲፩ ፡ ፳፫) ።

**ልሳነ ፡ ዕፍረት ፤** ምዑዝ ፡ ቃል ፤ ነገሩ ፡ እንደ ፡ ሽቱ ፡ ደስ ፡ የሚያሰኝ ፡ (ስንክ ፡ ጥቅ፲፫) ።

**ልሳነ ፡ ሰብእ ፤** የድርሰት ፡ ስም ፤ መልክአ ፡ ልሳን ፤ የልሳንን ፡ ጠባይ ፡ የሚናገር ።

**ሊተ ፤—ለኔ ፡ የኔ ፡ እኔን ፤—ለ ።**

**ለትሐ ፤ (ለስሐ) ፤** ጐረሠ ፡ አላመጠ ፤ ተጐነጨ ፡ ትጕመጠመጠ ፤ ጕንጩን ፡ ነፋ ፡ አሳበጠ ። ከተተ ፡ አገባ ፤ ልብስን ፡ በማጥን ፡ ወይም ፡ ሰውነትን ፡ በልብስ ፡ በቀሚስ ። መክተትና ፡ ማግባት ፡ ከመጕረሥና ፡ ከመጐንጨት ፡ ጋራ ፡ ይሰማማል ፤ ምስጢሩ ፡ አንድ ፡ ነው ። ለትሐና ፡ ለስሐም ፡ አንው ፡ ናቸው ።

**ለታሒ ፤ መልትሒ ፡ ሒ ፤** የሚጐርሥ ፡ የሚጐነጭ ፤ ከታች ፡ አላማጭ ።

**አልትሐ ፤** አጐረሠ ፤ አስጐረሠ ፡ አስጐነጨ ፤ አስከተተ ፡ አስገባ ።

**እልታሕ ፤ (ሓት ። ዕብ ፡ ሜልታሓ) ፤** የልብስ ፡ ማጥን ፤ ወይም ፡ የክት ፡ ልብስ ፡ የጋን ፡ ሸማ ፡ በማጥን ፡ በጋን ፡ የሚከትት ። ሥረ ፡ ወጥ ፡ ልብስ ፡ ያልተሰፋ ፡ ትት ፡ ጥልፍ ፤ መርፌና ፡ መቀስ ፤ ያልዘረበት ፡ የሴቶች ፡ ሥራ ። እልታሐ ፡ መንፈስ ፡ ተዐጽፈ ። ወክዳኑሂ ፡ እልታሕ ፡ (ስንክ ፡ ጥቅ፲፱ ። ዮሐ፲፱ ፡ ፳፫) ።

**መልታሕት ፤ (ብ ፡ መላትሕ ። ዕብ ፡ ማልታዓ ፤ ብ ፡ ማልታዖት) ፤** መንጋጋ ፡ ጕንጭ ፡ ፊት ፡ የግራ ፡ የቀኝ ፡ (ማቴ፭ ፡ ፴፱ ። ኢሳ፶ ፡ ፮ ። ፫ነገ ፡ ፳፪ ፡ ፳፬) ። ሰላም ፡ ለመላትሒከ ፡ ተጸፍዖ ፡ ዘኢነፈራ ፡ (ደራሲ) ።

**መልትሐ ፤ (ዲ ቃ ፡ ግ) ፤** መለታ ፤ እጁን ፡ ባፉና ፡ በጕንጩ ፡ አኖረ ። መጽሐፍ ፡ ግን ፡ በመልትሐ ፡ ፈንታ ፡ ተመላትሖ ፡ ይላል ። ትኔጽሩኒ ፡ ወታነክሩ ፡ ወትትመላተሑ ፡ በእደዊክሙ ፡ (ኢዮ፳፩ ፡ ፭) ።

**አመልትሐ ፤** ፊት ፡ አስመለሰ ፤ አሳፈረ ፤ ወይም ፡ በጥፊ ፡ አስመታ ።

**ተመላትሐ ፤** ጕንጮቹን ፡ ያዘ ፤ ፊቶቹን ፡ ጸፋ ፡ በ፪ ፡ እጁ ፤ የሐዘን ፡ የአንክሮ ። ባለቅኔዎች ፡ ግን ፡ አገና ፡ ተጣፋ ፡ ይሉታል ፤ በጥፊ ፡ ተማታ ፡ ቢያሰኝ ፡ እንጂ ፡ አገና ፡ አያሰኝም ፤ እውነተኛ ፡ ፍችው ፡ ጕንጭንና ፡ ፊትን ፡ አይለቅም ።

**ለተመ ፤ (ዐረ ፡ ለተመ ፤ ቀጠቀጠ) ፤** በቁሙ ፤ መታ ፡ ገጨ ፤ ወገጠ ፡ ፈተገ ፤ ጎፅበ ፡ ጕርደ ፡ አወጣ ፤ ዐሸ ፡ አበቀ ፤ የቈሎ ፡ የሽት ፤ ለደቄትም ፡ ይኾናል ፤ ስፈጸን ፡ እይ ። መለትም ፡ ከበግና ፡ ከፍየል ፡ ውጊያ ፡ የመጣ ፡ ነው ።

**ተለትመ ፤** ተለተመ ፤ ጎፅበ ፡ ጕርደ ፡ ወጣ ፤ ታሸ ፡ ታበቀ ።

**ልቱም ፤** የተለተመ ፤ ውግጥ ፡ ፍትግ ፡ (ዘፀ፳፱ ፡ ፵ ። ዘሌ፪ ፡ ፲፬) ። ሐሪጽ ፡ ልቱም ፤ ታጥቦ ፡ ተፈትጎ ፡ የተፈጨ ፤ ስንዳሌ ፡ (፫ነገ ፡ ፬ ፡ ፳፪) ።

**ሊቶስጥሮስ ፤ (ጽር ፡ ሊቶስትሮቶስ) ፤** የቦታ ፡ ስም ፤ ጸፍጸፍ ፡ ማለት ፡ ነው ። መካን ፡ ዘስሙ ፡ ሊትስጥሮስ ፡ (ዮሐ፲፫ ፡ ፲፫) ። ፪ኛም ፤ ሊቶሶርቶን ፤ ሊቶስትሮቶን ፡ ይላል ፤ ፍችው ፡ አንድ ፡ ነው ፡ (፪ዜና ፡ ፯ ፡ ፫) ።

**ለትቶ ፤ ቶት ፤ (ለተተ ፡ ይሌትት ፡ ይለትት ። ላዕልዐ ። ዐረ ፡ ለትለተ) ፤** መለተት ፤ መኰልተፍ ፡ መኰላተፍ ፤ ለታታ ፡ መኾን ፤ ያንደበት ። ለትቶ ፡ የሕፃናት ፡ ነው ፤ ከልተፈንና ፡ ላዕልዐን ፡ እይ ፤ መጽሐፍ ፡ ግን ፡ በለተተ ፡ ፈንታ ፡ ተለተተ ፡ ይላል ፤ ስሕተት ፡ ነው ። ወዝንቱ ፡ ሕፃን ፡ ቦ ፡ አመ ፡ ይትሌተት ፡ በገዐዘ ፡ ሕፃናት ፤ ወቦ ፡ አመ ፡ ይነብብ ፡ በነገር ፡ ጽኑዕ ፡ ከመ ፡ ወሬዛ ፡ ዘዕሥራ ፡ ዓመት ። እንዘ ፡ ይትሌተት ፡ ልሳኑ ፡ በሥርዐተ ፡ ደቂቅ ፡ (ገድ ፡ ተክ ። መጽ ፡ ምስ) ።

—፤ መለክለክ ፡ ማለክለክ ፤ ምላስን ፡ መጕልጐል ፤ ውሃን ፡ በምላስ ፡ ማንካ ፡ መጨለፍ ፡ መጠጣት ፤ የውሻ ፡ የድመት ፡ የአራዊት ፡ (ገድ ፡ አዳ) ። መድከም ፡ መልፋት ፡ መታከት ፤ የኀይል ፡ የጕልበት ፡ (ዐማርኛ) ።

**ለታት ፤ (ለታቲ ፡ ቲት ፡ ትያን ፡ ያት) ፤** በቁሙ ፤ ለታታ ፡ ኰልታፋ ፤ ክቡደ ፡ ልሳን ፡ አፈ ፡ ድዳ ፤ አጥርቶ ፡ የማይናገር ። ወለታት ፡ ውእቱ ፡ ሙሴ ፡ (ተረ ፡ ቄር፪) ።

—፤ ለክላኪ ፤ አለክላኪ ፤ በምላሱ ፡ ውሃ ፡ የሚልስ ፡ የሚጠጣ ፡ (ገድ ፡ አዳ) ።

**ልቱት ፤ (ታን ፡ ታት ፡ ትት) ፤** የለተተ ፤ ድኩመ ፡ ልሳን ፡ ድዳ ፡ ለንባዳ ፤ ወይም ፡ በጭራሽ ፡ መናገር ፡ የማይችል ፡ በሃም ። አስተርአየ ፡ መድኅኒነ ፡ ከመ ፡ ያርትዕ ፡ ልሳነ ፡ ልቱተ ፡ ወያኑጽ ፡ ሐንካሰ ፡ (መዋሥ) ።

**ልታቴ ፤ ልተት ፤** ልቱትነት ፤ ድካም ፡ ልስላሴ ።

**ልት ፤** በቁሙ ፤ የቅጠል ፡ ስም ፡ የደጋን ፡ መሻገሪ ፡ ደካማ ፡ ለስላሳ ፡ የወጥ ፡ ቅጠል ። (ግጥም) ፤ የዚህ ፡ ቤት ፡ ሴቶች ፡ አትቅበጡ ፤ ልቶጡ ፡ ናችኹ ፡ ልቶጡ ፡ (ልት ፡ ወጡ) ። ቍስልም ፡ ሲለግምና ፡ ሲያቀብር ፡ ልት ፡ ቀጥቅጦ ፡ ቢያስሩበት ፡ ቶሎ ፡ ነፍርቆ ፡ ይሽራል ።



**መ** ፤ ፲፫ኛ ፡ ፊደል ፡ በግእዝ ፡ አልፍ ፡ ቤት ፡ በ አበገደ ፤ ስሙ ፡ ማይ ፤ ቍጥሩ ፡ አርባ ፤ አኃዝ ፡ ሲኾን ፡ (መ—፵) አርብዓ ፡ ይባላል ።

**መ** ፤ የቃል ፡ አጕላማሽ ፤ አጋናኝና ፡ አዳማቂ ። መድረሻ ፡ እየኾነ ፡ በአንቀጽ ፡ ሳይቀር ፡ በኹሉ ፡ ይገባል ። መኑመ ፤ ምንትኑመ ፤ እስኩመ ፤ እፎመ ። ውእቱመ ፡ (ርሑማ) ፤ ካልእመ ፤ ባዕድመ ። መጽአመ ፡ ዘይመጽእ ። ፍችው ፡ ራብዕ ፡ ማድረግ ፤ ወይም ፡ ራብዕ ፡ መኾን ፡ ነው ፤ ሳይፈታም ፡ አዳማቂ ፡ ኹኖ ፡ ይቀራል ። (ዕርጅ ፡ ቍ፲፩) ።

**መ** ፤ ባዕድ ፡ ዘር ። በዘመድ ፡ ዘር ፡ ላይ ፡ እየተ ጨመረ ፡ መነሻ ፡ ይኾናል ፤ ግእዙ ፡ ብቻ ፡ ስለ ፡ ተነገረ ፡ ካዕቡ ፡ ራብዑ ፤ ሳድሱ ፡ ሳብዑ ፡ አይቀሩም ። ይህም ፡ ሰፈነ ፡ መስፍን ፤ ወደየ ፡ ሙዳይ ፤ ሐበ ፡ ማሕየብ ፤ ኀለፈ ፡ ምኅላፍ ፤ ወፀፈ ፡ ሞፀፍ ፡ እያለ ፡ መኼዱን ፡ ያሳያል ። ሙና ፡ ሞ ፡ ጕራጆች ፡ ናቸው ፤ በወ ፡ ከሚ ነሣ ፡ ከወ ፡ ግስ ፡ በቀር ፡ በሌላ ፡ አይገኙም ።

**ሙ** ፤ የወንዶች ፡ አብዢ ፡ ምእላድ ፤ በሩቆችና ፡ በቅርቦች ፡ ዝርዝር ፡ የሚገባ ። ለሊሆሙ ፡ ለሊክሙ ፤ ሎሙ ፡ ለክሙ ፤ ጸውዖሙ ፡ ጸውዐክሙ ።

**ሚ** ፤ (ዕብ ፡ ሚ ፤ ማ ፤ ሜ) ፤ የጥያቄና ፡ የ ምርመራ ፤ የአንክሮ ፡ አገባብ ። ማ ፡ ማን ፤ ምን ፡ ምን ድር ። ሚ ፡ የዐቢ ፡ እምረኀብ ፡ ወሚ ፡ ያሐምም ፡ እምነ ፡ ቍር ። ምንት ፡ አነ ፡ ወሚ ፡ ዘመድየ ። ሚ ፡ ትርጓሜሁ ፡ ለቃል ፡ (አፈ ፡ ተ፹፰ ። ዮዲ፲፪ ፡ ፲፬ ። ፊ ልክ ፡ ፷፩) ።

—፤ ምንኛ ፤ ምን ፡ ያኽል ፤ ስንት ። ሚ ፡ አዳም ። ሚ ፡ ብዝኁ ። ሚ ፡ መጠን ፡ (ማሕ፬ ፡ ፲ ። መዝ ፡ ፫ ። ቅዳ) ። ሚ ፡ ወሚ ፡ ቢል ፤ ምንና ፡ ምን ፤ ማንና ፡ ማን ፡ ያሰ ኛል ። በጠጠትና ፡ በምኞት ፡ ላይ ፡ ሲወድቅ ፡ ምነው ፡ ይኾናል ። ሚ ፡ እሞትነ ፡ በግብጽ ። መጽሐፍ ፡ ግን ፡ ሶበ ፡ ሞትነ ፡ ይላል ፤ አያስኝም ፡ (ዘፀ፲፮ ፡ ፫) ። (ዕርጅ ፡ ቍ፲፩) ።

## ሞአ፤—አሸነፈ፤—መዊእ፤ መዊአት ።

## መአደ፤—መከረ፤—ምዒድ ፡ መዐደ ።

**መአደ** ፤ (ዐረ ፡ ማድ ። ዕብ ፡ ማዳድ) ፤ ሰፈረ ፡ ከነዳ ፤ አስተካከለ ፤ ወርዱን ፡ ቁመቱን ፤ የሕንጻ ፡ የንጨት ፡ የቦታ ፡ የመሬት ።

**ማእድ** ፤ (ዳት ። ዐረ ፡ ማይዳ ፤ ማይ ደት) ፤ በቁሙ ፤ ማድ ፡ ገበታ ፤ ሰደቃ ፡ አውራጅ ፤ የም ግብ ፡ ማቅረቢያ ፤ መብሊያ ፡ መጠጫ ፤ ወይም ፡ መሼጫ ፡ መለወጫ ፤ ሰፊ ፡ ዝርግ ፡ ሞላላ ፤ ወርዳም ፡ ቁመታም ፤ ወይም ፡ ክብ ፡ እንዳውድማ ፡ ያለ ፡ እግራም ። አስተዳ ለወት ፡ ዘዚአሃ ፡ ማእደ ። ማእደ ፡ መኳንንት ። ኢበ ልዐት ፡ አመትከ ፡ እማእደ ፡ ሐማ ። ወገፍትዐ ፡ ማ እዳቲሆሙ ፡ ለመወልጣን ፡ (ምሳ፱ ፡ ፪ ። ፳፫ ፡ ፩ ። አስቴ፬ ፡ ፲፯ ። ማቴ፳፩ ፡ ፲፪ ። ፳፭ ፡ ፳፯) ።

—፤ ምሥዋዕ ፡ መንበር ፤ የግዜር ፡ ማእድ ፡ ዕጣንና ፡ ቍር ባን ፡ ማቅረቢያ ። ማእደ ፡ ክህነት ፡ ዘሥሩዕ ፡ ቅድ ሜከ ፡ (ቅዳ ፡ ያዕ) ። ማእዳት ፡ ዘምሥያም ፡ (፩ዜና ፡ ፳፰ ፡ ፲፮ ። ኩፋ ፡ ፴፩ ። ሚል፩ ፡ ፯) ።

—፤ ምሳ ፤ ድግስ ፤ መብልና ፡ መጠጥ ፡ እንጀራና ፡ ወጥ ። ወገብረ ፡ ማእደ ፡ ዐቢየ ። ባርክ ፡ ማእድ ። ጸሎተ ፡ ማእድ ፡ (ዘፍ፳፩ ፡ ፰ ። ግብ፳ ፡ ፯ ። ሥር ፡ ጳኵ) ።

**ማእዜ** ፤ (ዕብ ፡ ማታይ ። ሱር ፡ ኤም ታይ ። ዐረ ፡ መተ) ፤ የጊዜና ፡ የጥያቄ ፡ አገባብ ፤ መቼ ፡ ምን ፡ ጊዜ ፤ በምን ፡ ሰዓት ። ለ ፡ እም ፡ እስከ ፡ ይስማሙታል ። ኖሎቄኑ ፡ አውራኒሁ ፡ ማእዜ ፡ ይት ወለድ ። ማእዜ ፡ እበጽሕ ። ለአይ ፡ ወለማእዜ ፡ መዋዕል ። ዘኢይብልዎ ፡ እማእዜ ። እስከ ፡ ማእ ዜኑ ፡ ትላሕዎ ፡ (ኢዮ፴፱ ፡ ፪ ። መዝ ፡ ፵ ። ፩ጴጥ ፡ ፩ ፡ ፲፩ ። ቅዳ ፡ ኤጺ ። ፩ነገ ፡ ፲፯) ። ኢ ፡ ወኢ ፡ ትርጓሜ ፤ ኢ ፡ ትርአስ ፡ ሲኾኑት ፡ መቼም ፡ መች ፡ ከቶ ፡ ይኾናል ። ኢማ እዜ ፡ ኢኮኑ ፡ ሕያዋነ ። ወኢማእዜ ። ኢለከፎን ፡ ፀ ሓይ ፡ ማእዜኒ ፡ (መቃ ፡ ገ፩ ። ቄር ። ስንክ ፡ ኅዳ፳፮) ።

## ማእዝን ፤—በቁሙ ፤—አዚን ፡ አዘነ ።

**መአከ** ፤ (የመሀከ ፡ ዋርሳ) ፤ ተቈጣ ፤ ዛተ ፡ ገላመጠ ፤ ቃጣ ፡ ሰነዘረ ፤ አስፈራራ ፤ በቃል ፡ በበትር ። መጽሐፍ ፡ ግን ፡ በመአከ ፡ ፈንታ ፡ ተምእከ ፡ ተመአከ ፡ ይላል ፤ ስሕተት ፡ ነው ። ወዓዲ ፡ አፍርሆ ፡ እንዘ ፡ ይት ሜአክ ። ኢኮነ ፡ ከመ ፡ ሰብእ ፡ እግዚ ፡ ዘይትሜአክ ፡ ወኢኮነ ፡ ከመ ፡ ዕጓለ ፡ መሕያው ፡ ዘይትቈየም ። ወ ይትሜአክ ፡ ጼሳው ፡ ያዕቆብሀ ፡ በእንተ ፡ በረከት ፡ ዘባ ረከ ፡ አቡሁ ፡ (ዮሴፍ ። ዮዲ፰ ፡ ፲፯ ። ኩፋ ፡ ፳፯) ።

**ምኡክ** ፤ (ክን ፡ ክት ፡ እክት) ፤ ቍጡ ፤ ዐ ይነ ፡ ደረቅ ፤ አፍጣጭ ፡ ገላማጭ ። ርኩስ ፡ በኀበ ፡ እግዚ ፡ ምኡክ ፡ ዐይን ። ኅብአኒ ፡ እምልሳን ፡ ድሩክ ፡ ወእ ምዐይን ፡ ምኡክ ፡ (ምሳ፳፯ ፡ ፳ ። ስንክ ፡ ኅዳ፩) ።

**ምእከት** ፤ መቈጣት ፡ መዛት ፤ መቃጣት ፡ ማስ ፈራራት ።

**ትምእከት** ፤ ቍጣ ፡ ዛቻ ፤ ፍጥጫ ፡ ግልምጫ ፤ ጕራ ፡ ፍከራ ፤ በትር ፡ ሰንዘራ ። ያሐዝን ፡ ትምእከት ፡ ልበ ፡ ጠቢባን ። ኢያደንገፃ ፡ ትምእክቱ ፡ (ምሳ፲፯ ፡ ፲ ። ዮሴፍ) ።

**መአክዋ፤—ምግብ፡ ቀለብ፤—አኪል፡ አከለ ።**

**ማእከል ፤—መካከል ፤—አኪል ፡ አ ከለ ።**

**መአነ፤ (ዐረ ፡ መአ ። ዕብ ፡ ማኤን፤ እ ንቢ ፡ አለ)፤** ዘረጋ ፡ አሰፋ ፤ ሰፌ ፡ አደረገ ፤ የቦታ ፡ የሕ ንጻ ። እንደ ፡ ዕብራይስጡ ፡ ሲፈቱት ፡ ግን ፡ ዘጋ ፡ ከለከለ ፡ ያሰኛል ።

**ማእን ፤** ስፋት ፤ ወርድ ። ባለብሉዮች ፡ ግን ፡ መማቻ ፡ መታኰሻ ፡ ቅጥር ፡ ይሉታል ። ወገብረ ፡ ቆመ ፡ አረፍቱ ፡ ሰብዓ ፡ በእመት ፤ ወማእኖ ፡ ዘኍምሳ ፡ በእ መት ፡ (ዮዲ፩ ፡ ፪) ።

**ምእኖ ፤ አው ፡ ማእኖ ፤** ዐዘባ ፡ ጫቃ ፤ ማጥ ፡ ረግረግ ። አሕርው ፡ ዘውስተ ፡ ጽቡረ ፡ ማእኖ ፡ ያንገረግሩ ፡ (መጽ ፡ ምስ) ።

**ሜኤፌሳይም ፤ (ዕብ ፡ ሜይ ፡ አፍሳ ይም ፤** ጥቂት ፡ ውሆች ፡ ጫማ ፡ የሚያስብሱ ፡ እስከ ፡ ቍርጭምጭሚት ፡ የሚደርሱ ፡ ወንዙ ፡ ባይ ፡ ኙና ፡ ከ ማነሳቸው ፡ የተነሣ ፡ እያሉ ፡ የሉም ፡ የሚባሉ ፡ (ሕዝ ፵፯ ፡ ፫) ።

**ምእር ፤—አንድ ፡ ጊዜ ፤—ምዕር ።**

**መአሰ ፤ (ዕብ ፡ ማኣስ ፤ ናቀ ፡ ነቀፈ) ፤** ገፈፈ ፡ አስራቈተ ፤ ቈርበት ፡ አወጣ ። ማሰ ፡ ቈፈረ ፤ አጐ ደጐደ ። ማሳ ፡ ማሽ ፡ ማለት ፡ ከዚህ ፡ ወጥቷል ።

**ማእስ ፤ (ብ ፡ አምእስት) ፤** በቁሙ ፤ ማስ ፡ ቈርበት ፤ ጠፍር ፡ ቈዳ ፡ አጎዛ ። ማእሰ ፡ በግዕ ፡ ሐሩይ ። ማእሰ ፡ ዘባኑ ። ኢይቅንቱ ፡ ማእሰ ፡ (ዘፀ፳፭ ፡ ፭ ። ኢዮ፵ ፡ ፳፩ ። ሕዝ፵፬ ፡ ፲፰) ። ትመሥጥዎሙ ፡ አም እስቲሆሙ ፡ እምላዕሌሆሙ ። በልዑ ፡ አምእስተ ፡ ሠረገላቲሆሙ ፡ ወማእሰ ፡ ቀቀበ ፡ አስይፍቲሆሙ ፡ (ሚክ፫ ፡ ፪ ። ዮሴፍ ። ዘፍ፳፯ ፡ ፲፯) ።

**መአተ ፤ (መዐት ፡ ብዛት ፤ ምኢዕ ፡ መዕዐ) ፤** በዛ ፡ ፈደፈደ ፤ ዐሥር ፡ ዕጥፍ ፡ ወይም ፡ መቶ ፡ ኾነ ፡ መቶ ፡ ተባለ ።

**አምአተ ፤** አበዛ ፤ ዐሥሩን ፡ መቶ ፤ ወይም ፡ መቶውን ፡ ሺሕ ፡ አደረገ ። አምአተ ፡ ወአመክዐበ ፡ (ድጓ ። ሉቃ፰ ፡ ፰) ።

**ምእት ፤ (ዕብ ፡ ሜአ ። ሱር ፡ ማአ ። ዐረ ፡ ሚአት) ፤** የቍጥር ፡ ስም ፡ መቶ ፤ ዐሥር ፡ ጊዜ ፡ ዐሥር ፤ ወይም ፡ መቶ ፡ ጊዜ ፡ አንድ ። ምእት ፡ ክረምት ። ምእት ፡ አባግዕ ። ኀረዩ ፡ ምእተ ፡ ብእሴ ፡ (ሚራ፲፰ ፡ ፱ ። ዘፍ፴፫ ፡ ፲፱ ። ዮዲ፲ ፡ ፲፯) ። ከክልኤቱ ፡ እስከ ፡ እ ልፍ ፡ ተስዓ ፡ ወተስዐቱ ፡ ምእት ፡ እያለ ፡ በቅጽል ፡ ይ ዘምታል ።

**አምአት ፤ (ታት) ፤** መቶዎች ፤ ዐሥር ፡ መቶ ፡ ወይም ፡ መቶ ፡ ጊዜ ፡ ዐሥር ፤ አንድ ፡ ሺሕ ። ይ ገብር ፡ ማህሰ ፡ ለአምአት ፡ ወለአእላፍ ። መላእክተ ፡ አምአት ፡ (ኩፋ ፡ ፳፫ ። ፩ዜና ፡ ፳፰ ፡ ፩) ።

**አምኢታት ፤** መቶ ፡ ጊዜ ፡ መቶ ፤ ዐሥር ፡ ሺሕ ፡ ወይም ፡ አንድ ፡ እልፍ ።

**መብእስ ፤—ወጥ ፡ ገብ ፡ ድንጕር ፤—ብ ኢስ ፡ ብእሰ ።**

**ሚበዝኁ ፤** የቅኔ ፡ ስም ፤ በ፫ኛው ፡ መዝሙር ፡ የሚገባ ፡ ፫ ፡ ቤት ፡ ያለው ።

**መበለ ፤ (ዐበለ ፤ ማዕበል) ፤** ጌታየ ፡ ሠለ ጠነ ፤ ደፈረ ። በሐዘ ፡ እንዘ ፡ ይሜብል ፡ ላዕለ ፡ መር ዒት ። ገብር ፡ ጠቢብ ፡ ይሜብል ፡ አጋዕዝተ ፡ አብዳነ ። ወብእሲትሰ ፡ ትምህር ፡ ኢናበውሕ ፤ ወኢትመብል ፡ ላዕለ ፡ ብእሲ ፡ (ምሳ፳፱ ፡ ፳፯ ። ፲፯ ፡ ፪ ። ፩ጢሞ ፡ ፪ ፡ ፲፪) ።

**አመበለ ፤** አሠለጠነ ፤ ሾመ ፡ ወከለ ። ወአመ በሎ ፡ ዲበ ፡ ኵሉ ፡ ቤቱ ፡ (ኩፋ ፡ ፵) ።

**መብልዕ ፤—መብል ፡ ምግብ ፤—በ ሊዕ ፡ በልዐ ።**

**መበለት ፤—በቁሙ ፡ ድኻ ፡ ሴት ፤—በ ልቶ ፡ በለተ ።**

**ሙባኒም ፤-ቅዉማን ፡ ርቱዓን ፤-መው ።**

**መብዐል ፤—መክደኛ ፤—ብዒል ፡ ብ ዕለ ።**

**መግ ፤** የመጽሐፍ ፡ ስም ፤ ፬ኛው ፡ ክፍል ፡ ፍ ትሐ ፡ ነገሥት ። መግ ፡ ዘውእቱ ፡ ነገሥት ፡ ራብዕ ፡ (ፍ ፡ ነ ፡ መቅ) ።

**መግበ ፤ ቦት ፤ (መገበ ፡ ይሜግብ ፡ ይ መግብ) ፤** መመገብ ፡ መቀለብ ፤ ማብላት ፡ ማጠጣት ፤ ምግብ ፡ መስጠት ፡ (ዐማርኛ) ። መጠበቅ ፡ መከናከን ፤ መከበብ ፡ ስመጠበቅ ። ይሜግቡ ፡ በጽድቅ ፡ መንበሮ ። ኢይክል ፡ ሠሪዐ ፡ መንግሥት ፡ ወመግቦታ ። ዘይሜ ግብ ፡ ንዋዬ ፡ ለድኅትምት ። ይሜግብዋ ፡ ወየዐው ድዋ ። ማህል ፡ ይሜግቦሙ ። ይሜግብ ፡ ሕዝቦ ፡ (ም ሳ፳ ፡ ፳፰ ። ዮሴፍ ። ፍ ፡ ነ ፡ ፳፱ ፡ ፫ ። ፪ዜና ፡ ፱ ፡ ፫ ። መዝ ፡ ፴፭ ። ፪፳፱ ። ዘዳ፴፪ ፡ ፲) ።

—**፤** መምራት ፡ ማስተማር ፤ በሥራት ፡ ማስኬድ ። ም ስጢሩ ፡ ከዚያው ፡ ከመጠበቅ ፡ ይገባል ። ነፍስ ፡ እስ ርት ፡ በሥጋ ፡ ከመ ፡ ትመግቦ ፡ ወትሥራዕ ፡ ሕይወቶ ። ይሜግባ ፡ ለሐመር ፡ (ዮሴፍ ። መጽ ፡ ምስ) ።

**መጋቢ ፤ (ቢት ፡ ብያን ፡ ያት ፤ ገብት ፤** በቁሙ ፤ የሚመግብ ፡ የሚጠብቅ ፤ ጠባቂ ፡ ሹም ፤ አዛዥ ፡ ቤታባት ፤ ምስለኔ ፡ እንደራሴ ፤ ወኪል ፡ ሞግዚት ፤ መሪ ፡ አስተማሪ ። መጋቤ ፡ ቤተ ፡ ንጉሥ ። መጋቤ ፡ ሀገር ። መጋብያነ ፡ ሕግ ። መጋቤ ፡ ኵሉ ። መጋቢት ፡ (ኢሳ ፳፪ ፡ ፲፭ ። ሮሜ፲፯ ፡ ፳፫ ። ዳን፲፩ ፡ ፳፪ ። ቅዳ ። ስንክ ፡ መጋ፳፯) ። መገብተ ፡ አብያተ ፡ ንጉሥ ። ተሠይሙ ፡ መገብተ ፡ ላዕለ ፡ ኵሉ ፡ ጥሪቱ ። መገብተ ፡ ምኵራብ ፡ (ዕዝ፰ ፡ ፳፱ ። ፩ዜና ፡ ፳፯ ፡ ፴፱ ። ግብ፱ ፡ ፩) ።

**ምግብ**፤ በቁሙ፤ ቀለብ፡ መብል፡ መጠጥ፡ እንጀራና፡ ወጥ። ማርያም፡ ሀብኒ፡ ምግበ፡ ዕለት፤ እስመ፡ ተማሕፀንኩ፡ አንሰ፡ በዘዚአኪ፡ ስደት፡ (ቅኔ)።
—፤ ጥበቃ፡ ሹመት፡ የሹመት፡ ሥራ፡ አስተዳደር። መገቦሙ፡ ምግበ፡ እኩየ። ዘሀለወት፡ ታሕተ፡ ምግቡ። ከመ፡ ይፈጽም፡ ምግቦ። ትሰዐር፡ እምግብከ። በምግቡ፡ ለቈስጠንጢኖስ፡ (አፈ፡ ድ፴፱። ፍ፡ ነ፡ ፳፱፡ ፫። ተረ፡ ባሮ። ኢሳ፳፪፡ ፲፱። ስንክ፡ መስ፳፩። ሉቃ ፲፮፡ ፪—፱)።

**አመገበ**፤ አስመገበ፤ አስጠበቀ፡ ዐደራ፡ ሰጠ፤ ሾመ፡ አሠለጠነ፤ መጋቢ፡ አደረገ። መጋቢ፡ ዘአመገብዎ። እግዚ፡ አመገበከ፡ ትቅትል፡ ወታሕዩ። አሜግቦ፡ ምግበከ። ኢታመግብ፡ ነኪረ፡ ላዕለ፡ ቤትከ፡ (ፈ፡ መ፡ ፭፡ ፲፱። መቃ፡ ገ፫። ኢሳ፳፪፡ ፳፩። ሚራ፳፡ ፳፫)።

**ተመገበ**፤ በቁሙ፤ በላ፡ ጠጣ፡ ተቀለበ፤ ተጠበቀ፤ ተሾመ። ነፍስ፡ እንተ፡ ትትሜገብ፡ በመንፈስ፡ አምላካዊት። ተመገበ፡ ቦቱ። እለ፡ ይትሜገብዎ፡ ግብረ፡ መወልጣን፡ (አፈ፡ ተ፴፱። ፍ፡ ነ፡ ፵። ፈ፡ መ፡ ፲፱)።

**ምጉብ**፤ (ባን፡ ባት፡ ግብት)፤ የተመገበ፤ የተጠበቀ፤ የተሾመ። ወውእቱሰ፡ ምጉብ፡ በኀይለ፡ አምላኩ፡ (ገድ፡ ኪሮ)።

**ምግብና**፤ መጋቢነት፤ ጥበቃ፡ ሹመት። በእንተ፡ ምግብና፡ (ፍ፡ ነ፡ ፴)። ምግብ፡ ምግብና፡ ወይም፡ ምጋቤ፡ በማለት፡ ፈንታ፡ ምግበት፡ ይላል፤ ቤቱ፡ የቀደሰ፡ ነውና፡ አያሰኝም። ሥልጣነ፡ ምግበትነ፡ (ፍ፡ ነ፡ ፳፱፡ ፫)።

**መጋቢት**፤ በቁሙ፤ ስመ፡ ወርኅ፡ ሳብዕት፡ እመስከረም፤ የመዓልትና፡ የሌሊት፡ ምግብና፡ እንደ፡ መስከረም፡ ትክክል፡ የሚኾንባት፡ ወርኅ፡ ዕሪና፡ ማለት፡ ነው። እስመ፡ ይዔሪ፡ መዓልት፡ ወሌሊት፡ አመ፡ ዕሥራ፡ ወኀሙሱ፡ ለወርኃ፡ መጋቢት፡ (ዲድ፡ ፴)። ክያ፡ ዐምበት፡ ያለው፡ የዱሮውን፡ ነው፤ ዛሬ፡ ግን፡ በደቃይቅ፡ ቊጥር፡ ፱፡ ቀን፡ ወደ፡ ታች፡ ወርዷ፡ አመ፡ ዕሥራ፡ ወአሚሩ፡ ኹኗል። በኛም፡ ብተት፡ አመ፡ ዐሡሩ፡ ወሠሉሱ፤ ወይም፡ ወረቡዑ፡ ይኾናል።

**ሞገድ**፤—በቁሙ፡ ማዕበል፤—ወጊድ፡ ወገደ።

**መግዌ**፤—ጥራዝ፡ የመጣፍ፡ ነዶ፤—ጎግዎ፡ ጎገወ።

**መግዝእ**፤—ገኛ፡ ፍሪዳ፤—ገዚእ፡ ገዝአ።

**ምጕሕያ**፤—ዐረም፡ ቋያ፤—ጎሐየ።

**ምጕጣይ**፤—መኳጐጫ፤—ጎጥይ፡ ጎጠየ።

**ምጕያይ**፤—መሸሻ፡ መጠጊያ፤—ጎይይ፡ ጎየ።

**መግለ**፤ አው፡ መገለ፤ (ዐረ፡ መጀለ። ዕብ፡ ማጌል)፤ መግል፡ ያዘ፤ ዐበጠ። መገለ፤ ፈረጠ። ጸልዐ፡ ዘይመግል፡ (ኢሳ፩፡ ፮)።

**አምገለ**፤ አመገለ፡ አፈረጠ። ያመግል፡ (መ፡ ፈ)።

**መግል**፤ (ብ፡ አምግልት)፤ በቁሙ፤ ክበጠ፡ ከቍስለ፡ ገላ፡ የሚፈስ፡ ነጭ፡ እድፍ። ለእመ፡ ኮነ፡ ቍስል፡ ዕሙቀ፡ ወምሉአ፡ መግል፡ (ፍ፡ ነ፡ ፭። ስንክ፡ ኅሐ፫)። ቍስለ፡ መቅሠፍት፡ ይገብር፡ አምግልተ፡ (ሚራ፳፰፡ ፲፯)።

**መገን**፤ (ብ፡ አምጋን። ዕብ፡ ማጌን)፤ ጋሻ፡ አግሬ። በዳዊት፡ ጋሻ፡ አምሳል፡ የተሠራ፡ የአይሁድ፡ ንሻን፤ ማኅተመ፡ ሰሎሞን። የኢትዮጵያም፡ ሽልማትና፡ ትእምርተ፡ መንግሥት፡ ከዚህ፡ ጋራ፡ አንድ፡ ነው።

**ምጕንጻ**፤—ጎረንጎሬ፤—ገነጸ።

**መጐጸ**፤ (ደጐጸ፡ መድጐጽ)፤ ተቈጣ፡ ዘለፈ፤ ነጠበ፡ ነቀፈ። መጽሐፍ፡ ግን፡ በመጕጸ፡ ፈንታ፡ አመጕጸ፡ ይላል፤ አያሰኝም። ሊቃናተ፡ ኢታመጕጽ። ዘይመጕጽ፡ ሊቃናተ፡ (፩ጢሞ፡ ፭፡ ፩። ቀሌ)።

**አመጐጸ**፤ (ያሜጕጽ፡ ያመጕጽ)፤ አስቈጣ፤ አስነቀፈ። አስደራጊ፡ ነው፤ ቦኛ፡ አካል፡ ያሳያል።

**መጕረጽ**፤—ማጕርጥ፤—ጎሪጽ፡ ጎረጸ።

**ሞገስ**፤—በለሟልነት፤—ወጊስ፡ ወገሰ።

**ሞገት**፤—ሞገድ፤—ወጊድ፡ ወገደ።

**መድ**፤ ቦኛ፡ ክፍል፡ ፍትሐ፡ ነገሥት። መድ፡ ዘውእቱ፡ ነገሥት፡ ሣልስ፡ (ፍ፡ ነ፡ መቅ)። በቁሙ፡ የወፍጮ፡ ግልገል፡ (ዐማርኛ)።

**መደብ**፤—በቁሙ፡ ዕርከን፤—ደይቦ፡ ደየበ።

**መድበል**፤—ክምቹ፤—ደቢል፡ ደበለ።

**መድበራ**፤—ዱር፡ በረሓ፤—ደቢር፡ ደበረ+ደብር።

**ማድጋ**፤—በቁሙ፡ እንስራ፤—ደጊግ፡ ደገ።

**መደደ**፤ መደ፤ (ትግ፡ ወዐረ)፤ ዘረጋ፤ መደመደ፡ አስተካከለ፤ ያውድማ፡ የቤት። ሜዳ፡ መደዳ፡ ማለት፡ ከዚህ፡ ወጥቷል። መአደን፡ እይ፤ የዚህ፡ ጎር፡ ነው።

**ማድዮ**፤ (ዕብ፡ ማድ፤ ማድያው። ጽር፡ ማንዲያስ)፤ የላይ፡ ልብስ፤ የክብር፡ ልብስ፤ ነገሥታት፡ መኳንንት፡ እጀጠባቦውም፡ የሚለብሱት። ዮና፡ ው፡ ዝርዝሮች፡ የቀሙ፤ ልብሰ፡ ዕበዩ፡ እንደ፡

ማለት ። ወሀቦ ፡ ዐጽፈ ፡ ዘላዕሌሁ ፡ ወማድዮሂ ፡ (፩ነገ ፡ ፲፰ ፡ ፭) ። ባለብሉዮች ፡ ማን ፡ ጩፋ ፡ ይሉታል ። ፪ኛ ፡ ደግሞ ፡ እንደ ፡ ጽርኡ ፡ ቃል ፡ በማድዮ ፡ ፈንታ ፡ መንድያ ፡ ይላል ፤ ይህንንም ፡ የጦር ፡ ልብስ ፡ እንደ ፡ ፀሐየ ፡ ፊሳ ፡ ያለ ፤ ዘየሀይድ ፡ ዐይን ፡ ብለው ፡ ይፈቱታል ።

**ማዳይ ። ምድያም** ፤ ስመ ፡ ነገድ ፡ (ዘፍ ፲ ፡ ፪ ። ፳፭ ፡ ፪) ።

**መዲና ፤—በቁሙ ፡ ከተማ ፤—ደይኖ ፡ ደየነ ።**

**ምዳቀ ፤—ምዳቋ ፤—ደቂሕ ፡ ደቅሐ ።**

**መደረ ፤ (ይመድር ፡ ይምድር ። ዐረ ፡ መዲረ)** ፤ ሰፋ ፤ ረዘመ ፤ ወፈረ ። ስፋት ፡ የወርድ ፡ ርዝማን ፡ የቁመት ፡ ወፍር ፡ የወል ፡ የመካከል ። ብሕረን ፡ ተመልከት ፡ የዚህ ፡ መንቲያ ፡ ነው ፤ ብሕረ ፡ የባሕር ፡ መደረ ፡ የየብስ ።

**መደረ ፤ (ዐረ ፡ ረከዘ)** ፤ በቁሙ ፤ ወጋ ፡ ቸከለ ፤ ምድር ፡ ያዘ ፡ ተመረኰዘ ፤ ከምድር ፡ ወረደ ፡ ተጠጋ ፤ የብስ ፡ ረገጠ ፤ የቀዛፊና ፡ የመርከብ ፡ የባለታንኳ ።

**ምድር ፤ (ብ ፡ ምድራት ፤ አምዳር ፤ አምዳራት ፥ ሮት)** ፤ በቁሙ ፤ ሰፊ ፡ ዝርግ ፤ ረዥም ፡ ወርዳም ፡ ቁመታም ፤ ደንዳና ፡ ወፍራም ፤ ከነባሕሩና ፡ ከነየብሱ ፡ ከነጕተናው ፡ ከነልብሱ ፡ ባንድነት ። ዘገብረ ፡ ሰማየ ፡ ወምድረ ። ገባሬ ፡ ሰማያት ፡ ወምድር ። በማይ ፡ ወምድር ፡ የኀልፍ ፡ (ቅዳ) ።

—፤ የብስ ፡ የባሕር ፡ ርቦ ፤ ከየብስ ፡ የተፈጠሩ ፡ የዐርብ ፡ ፍጥረቶች ፡ የሚኖሩበት ። ወሰመየ ፡ ለየብስ ፡ ምድረ ፡ ወለምእላደ ፡ ማይ ፡ ባሕረ ። ለታብቍል ፡ ምድር ፡ ሐመልማለ ፡ ሣዕር ። ለታውፅእ ፡ ምድር ፡ ዘመደ ፡ እንስሳ ፡ ወአራዊት ፡ (ዘፍ ፩ ፡ ፲ ፡ ፲፩ ። ፳፬) ።

—፤ የቦታ ፡ የርስት ፡ የመንግሥት ፡ ክፍል ፤ ሀገር ፡ ብሔር ፡ አውራጃ ፡ መንደር ፡ ከተማ ፡ ገጠር ፡ በሕዝብ ፡ በነገድ ፡ በገመድ ፡ በቀላድ ፡ የተለየ ፤ ከነሕዝቡ ፡ ከነባለቤቱ ። ዡሉ ፡ ምድር ። ምድራት ፡ ርሒባት ። አድባር ፡ ወአምዳር ። ውሳንያተ ፡ አምዳር ። ይበውእ ፡ ውስተ ፡ አምዳራት ። ወዘረውክዎሙ ፡ በአምዳሮት ፡ (ዮዲ ፲፩ ፡ ፲፯ ። ፩ዜና ፡ ፬ ፡ ፵ ። ዘዳ፲፩ ፡ ፲፩ ። ፍ ፡ ነ ፡ ፳፯ ። ዳን፲፩ ፡ ፵ ። ሕዝ፲፩ ፡ ፲፯) ።

—፤ የሰው ፡ ባሕርይ ፤ ሥጋ ፡ ዐፈር ፡ መሬት ። ዘምድረ ፡ ለብሰ ፡ (ኪዳ) ። ምድረ ፡ ግብ ፡ ምድረ ፡ ባሕር ፡ ቢል ፤ ታሕት ፡ ውስጥ ፡ ልብ ፡ ማለት ፡ ነው ፡ (ዳን፯ ፡ ፳፬ ። ኢዮ ፴፰ ፡ ፲፯) ።

**ምድራዊ ፤ (ዊት ፡ ውያን ፡ ያት)** ፤ በቁሙ ፤ የምድር ፡ ከምድር ፡ የተገኘ ፡ በምድር ፡ የሚኖር ። ወልደ ፡ ምድራዊ ። ሥጋ ፡ መሬት ፡ ምድራዊ ። ንጉሥ ፡ ምድራዊ ። ሕይወት ፡ ኀላፊት ፡ ምድራዊት ፡ (ጥበ፯ ፡ ፩ ። ዮሐ፫ ። ፊልክ ፡ ፻፺፪ ። መቃ) ።

**መድረወ** ፤ ከምድር ፡ አገባ ፤ ከተተ ፡ ቀበረ ፤ ፈጸመ ፡ ጨረሰ ፤ አከናወነ ፤ ያዝመራ ፡ የሥራ ። ገመረን ፡ እይ ፤ የዚህ ፡ ጎር ፡ ነው ።

**አመድረወ** ፤ ከምድር ፡ አስገባ ፤ አስከተተ ።

**እምድሩ** ፤ አከቶ ፡ ፈጽሞ ፡ ጭራሽ ፤ ከንዱ ፡ ዘንዱ ። ገሙራን ፡ እይ ። አመ ፡ እምድሩ ፡ ትኩሲ ፡ ሐማማት ፡ ትክሕድ ፡ ትስብእት ፡ (ተረ ፡ ቄር፩) ።

**ምህወ ፤ (ይምሁ ፡ ይምህው ፤ ምሂው ። መስወ ፤ መሰወ)** ፤ ቀሓ ፡ ቀለጠ ፤ ውሃ ፡ ኾነ ፤ ዛለ ፡ ደከመ ፡ ወዛ ፡ (ዘፀ፲፯ ፡ ፳፩) ። ሥጋሁ ፡ ከመ ፡ ማይ ፡ ምህወ ። ባሕር ፡ እንተ ፡ ኢተዐዱ ፡ እምወሰና ፡ ወምድርኒ ፡ እንተ ፡ ኢትምሁ ፡ እምዝብጠተ ፡ መዋግዲሃ ። ይምሁ ፡ ወይትመሰው ፡ ሡሉ ፡ አባል ፡ (ስንክ ። አትና ። ግንዘ) ። ማይ ፡ ውሃ ፡ ማለት ፡ ኹለቱም ፡ ከዚህ ፡ የወጣ ፡ ነው ። በምህወ ፡ ፈንታ ፡ ተምህወ ፡ ይላል ፤ ስሕተት ፡ ነው ። ትትመሀው ፡ አባሉ ፡ (ግንዘ) ።

**አምህወ** ፤ አቃቃ ፡ አቀለጠ ፤ ውሃ ፡ አደረገ ፡ (ስንክ ፡ ሐም፭) ።

**ማህው ፤ (ብ ፡ ማህዋት ፤ አምሃው ። ዐረ ፡ መሃት)** ፤ የብርሌና ፡ የብርጭቆ ፡ የቅዛዝ ፡ የመስታዮት ፡ ጭቃ ፡ ዐፈሩ ፡ ደንጊያው ፡ እንደ ፡ ኖራ ፡ ፈልቶና ፡ ቀልጦ ፡ የሚሠራ ፤ ወይም ፡ የተሠራው ። መስተገብራነ ፡ ማህው ። አምጽኡ ፡ ሎሙ ፡ እምህየ ፡ ሕምዘ ፡ በማህው ። ጽዋዐ ፡ ማህው ። እለ ፡ ይሰትዩ ፡ ወይነ ፡ በማህው ፡ ወቢረሌ ። ማህው ፡ ለእመ ፡ ተሰብረ ፡ አልቦ ፡ ዘያስተጣግዖ ፡ ዘእንበለ ፡ ገባዕሁ ። ስባራተ ፡ ማህው ፡ በሊኃት ፡ (ስንክ ፡ ኅዳ፳፩ ። ዮሴፍ ። አርጋ ። ዓሞ፮ ፡ ፮ ። ያዕ ፡ ዘእል ። ሚራ፵፫ ፡ ፲፱) ።

ማህው ፡

**መሀከ ፤ ምህከ ፤ (መሐረ ፤ ምሕረ)** ፤ ራራ ፡ ዐዘነ ፡ ማረ ፤ ይቅር ፡ አለ ። ኢመሀከተኪ ፡ ዐይን ። ወልደ ፡ ጥቀ ፡ ኢምህከ ፡ እምኔነ ። አንተሰ ፡ ትምህክ ፡ ሐምሐመ ። መሀክ ፡ ሕዝበከ ። መሀኩ ፡ ሊተ ፡ ወልድየ ። ዘእንበለ ፡ ምሂክ ። ምሂኮትየ ፡ (ሕዝ፲፯ ፡ ፭ ። ሮሜ፰ ፡ ፴፪ ። ዮና፬ ፡ ፲ ። ዮኤ፪ ፡ ፲፯ ። ፪ነገ ፡ ፲፰ ፡ ፭ ። ስንክ ። አርጋ) ።

—፤ ገመገመ ፡ ሣሣ ፡ ቈጠበ ። ዘይምህክ ፡ በትሮ ። ዘይምህክ ፡ ነገረ ። ኢትምሀኩ ፡ ገሥጸቶሙ ፡ (ምሳ፲፫ ፡ ፳፬ ። ኢዮ፵፪ ፡ ፫ ። ዲድ ፡ ፳፪) ።

—፤ አዳነ ፡ ተቤዠ ፤ ጠበቀ ። ይምህክ ፡ ነፍሰ ፡ እሞት ። እምእደ ፡ ሳኦል ፡ መሀከ ። ወእምነኪር ፡ መሀክ ፡ ለገብርከ ፡ (ኢዮ፴፫ ፡ ፲፰ ። አርጋ ፡ ፬ ። መዝ ፡ ፲፰) ።

**መሃኪ፤**(ኪት፡ ክያን፡ ያት)፤ የሚራራ፤ መሐሪ፡ ዐዛኝ፤ ይቅር፡ ባይ፤ አዳኝ፡ ፈዋሽ ። ሕብ፡ መሃኪ፡ ዘይምህክ፡ ወልዶ ። እግዚ፡ መሃኪክ፡ (አፈ፡ ተ፱ ። ዘፀ፲፩፡ ፳፯) ።

**ተምህከ፤** ተማረ፡ ይቅር፡ ተባለ፤ ይቅርታ፡ አገኘ ።

**ምሁክ፤**(ከን፡ ካት፡ ህክት)፤ የተማረ፤ ይቅርታ፡ ያገኘ ።

**ምህከት፤** መራራት፤ ይቅር፡ ማለት ። ይቅር፡ መባል፤ ይቅርታ፡ ማግኘት ። ይቅርታ፡ ስርየት፤ ርኅራኄ ። ምህከት፡ ወምሕረት፡ (ዮሴፍ) ።

**ማህከወ፤**(ተቀ፡ ግ ። መህክ)፤ አስፈራ፤ አስደነገጠ ።

**ተማህከወ፤** ፈራ፡ ደነገጠ፤ ከው፡ ክቶ፡ አለ ። ወሶበ፡ ይወዲ፡ ዲቤክሙ፡ ቃሉ፡ እኩኑ፡ ትትማህከዉ፡ ወትፈርሁ፤ ወዘሉሙ፡ ብርሃናት፡ ይትሀወኩ፡ በፍርሀት፡ ዐቢይ ። ወምድር፡ ዙላ፡ ትትማሀከው፡ ወትርዕድ፡ ወትጌጉእ፡ (ሔኖ፻፪፡ ፩፡ ፪) ።

**ምህላ፤—ልመና፡ ምልጃ፤—ምሒል፡ መሐለ ።**

**ማሄለክ፤**(ዕብ፡ ማሃላኽ)፤ መኼጃ፡ መመላለሻ፤ መንገድ፡ ወልወል፡ (ሕዝ፵፪፡ ፬) ።

**መህን፤—ፈገፈገ፤—ምሒን፡ መሐነ ።**

**መህና፤—እጅ፡ መንሻ፤—መሐና ።**

**ሜሄኑህ፤**(ዕብ፡ ሜሄናህ)፤ እምኔሆን፡ (ሕዝ፵፪፡ ፩) ።

**ምሂር፤ሮት፤**(መሀረ፡ ይሜህር፡ ይምህር ። ዕብ፡ ማህር፤ ፈጠነ፡ ቸኰለ)፤ መማር፤ መምህር፡ መኾን፡ መምራት፡ ማሳየት፤ መምከር፡ ማስተማር፤ ማልመድ፡ ማስለመድ ። መሀሮ፡ አቡሁ፡ መጽሐፈ ። ዘሰ፡ ይሜህር፡ ወይገብር ። ትሜህር፡ እገሪሃ፡ ሐዊረ፡ (ኩፋ፡ ፯ ። ማቴ፭፡ ፲፱ ። ዘዳ፳፰፡ ፶፯) ።
—፤ መቅጣት፡ መገረፍ፤ መቁጣት፡ መገለፍ ። መሀሮ፡ ወልደከ ። መሀረኒ፡ እግዚእ ። ገሥጸ፡ ወመሀረ፡ (ምሳ፳፱፡ ፲፯ ። ኤር፲፡ ፳፬ ። ሚራ፯፡ ፳፫) ። መርሐን፡ እይ፤ የዚህ፡ መንቲያ፡ ነው ።

**መሃሪ፤**(ሪት፡ ርያን፡ ያት፤ ሀርት)፤ በቁሙ፡ ማሪ፡ መሪ፤ መካሪ፡ አስተማሪ ።

**መምህር፤**(ርት፡ ራን፡ ራት)፤ ዝኒ፡ ከማሁ፤ በቁሙ፡ መምር፡ የትምርት፡ አባት ። ሊሕዱ፡ ውእቱ፡ መምህርክሙ ። መምህርት፡ ይእቲ ። መምህራነ፡ ቤተ፡ ክርስቲያን፡ (ማቴ፳፫፡ ፰ ። ስንክ፡ ሐምሌ፳፭ ። ጎዳ፳፱) ። ውርወት፡ ድቀት፡ ፍርሀት፡ በማለት፡ ፈንታ፡ መምሀረ፡ ሕግ፡ ይላል፤ የመላሽ፡ ስሕተት፡ ነው፡ (መዝ፱፡ ፳፩) ።

**ማህር፤**(ብ፡ አምሀርት)፤ ዝኒ፡ ዓዲ፡ ከማሁ ። አእላፍ፡ አምህርት፡ (፩ቆሮ፡ ፬፡ ፲፭) ።

**አምህረ፤** አስማረ፡ አስተማረ፤ ለመምህር፡ ሰጠ፡ ከተማሪ፡ ቤት፡ አገባ ።

**ተምህረ፤** ተማረ፤ ለመደ ። ተምህረ፡ መጽሐፈ ። ተምህረ፡ መሚጠ ። እስከ፡ ይትሜሀሩ፡ ብዙኃን፡ (ኩፋ፡ ፱ ። ሕዝ፲፱፡ ፫ ። ዳን፲፪፡ ፬) ። ነበበ፡ ኀለየ፡ በማለት፡ ፈንታ፡ ተምህረ፡ ይላል፤ የመላሽ፡ ስሕተት፡ ነው ። ኢትትመሀር፡ ነፍስየ፡ ኀጢአተ ። ልበ፡ ጻድቃን፡ ይትሜሀር፡ ሃይማኖተ ። እስመ፡ ሐሰተ፡ ይትሜሀር፡ ልቦሙ፡ (ኢዮ፳፯፡ ፬ ። ምሳ፲፭፡ ፳፰ ። ፳፬፡ ፪) ።

**ተመሃሪ፤** ተማሪ፡ ረድእ፡ ደቀ፡ መዝሙር ። ተመሃርያን፡ (ፍ፡ ነ፡ ፲) ።

**ምሁር፤**(ራን፡ ራት፡ ሀርት)፤ በቁሙ፤ የተማረ፡ ትምርት፡ የጠገበ፤ ዐዋቂ፡ ሊቅ፤ ልባም፡ አስተዋይ ። ምሁር፡ በሡሉ፡ ጥበብ ። ምሁራን፡ በኀበ፡ እግዚ ። ነገሩ፡ ኢኮነ፡ ከመ፡ ምሁር ። ብእሲ፡ ምሁር፡ (ቀሌ ። ኢሳ፶፬፡ ፲፫ ። ኢዮ፴፬፡ ፴፭ ። ሚራ፴፭፡ ፬) ።

**ተምሃር፤** ትምርት፤ ልማድ ። ሕግክ፡ ተምሃርየ፡ ውእቱ ። እስመ፡ እኩይ፡ ተምሃሩ፡ (መዝ፡ ፻፲፰ ። ሄርማ፡ ገ፴፬) ።

**ትምህርት፤**(ታት)፤ ዝኒ፡ ከማሁ፤ በቁሙ፡ ትምርት፤ ዕውቀት፤ ድርሳን፡ ምዕዳን ። ወልድ፡ ዘእንበለ፡ ትምህርት ። ነፍሳት፡ እለ፡ አልቦን፡ ትምህርት ። በትምህርታቲሁ ። ትምህርታት፡ ወተግሣጻት፡ (ምሳ፲፯፡ ፳፩ ። ጥበ፲፯፡ ፩ ። ቄር ። ስንክ፡ መስ፳) ። ልማድና፡ ባህል፡ ይኾናል፤ ምስጢሩ፡ ያው፡ ትምርት፡ ነው ።

**ማህረከ፤**(ይማህርክ፡ ይማህርክ፤ ተቀ፡ ግ፤ ወይም፡ የመህክ፡ ስረጅ)፤ ማረከ፡ ዘረፈ፡ ወሰደ፡ ነዳ፤ ወደ፡ ርሱ፡ ሳበ፡ አቀረበ፤ በትምርት፡ በታምራት፤ ወይም፡ በጦርነት ። ይማህርክሙ፡ ለጽኑዓን ። ማህረኩ፡ ወቀተሉ፡ ደቀከ ። ወማህረከ፡ እንስሳሆሙ ። ማህረክዎሙ፡ ምህርካ፡ ብዙኀ፡ (ኢሳ፶፫፡ ፲፪ ። ኢዮ፩፡ ፲፯ ። ዮዲ፪፡ ፳፫ ። ፪ዜና፡ ፲፬፡ ፲፫) ።

**አማህረከ፤**(ያማህርክ)፤ አስማረከ፤ አዘረፈ ።

**ተማህረከ፤**(ይትማህረክ)፤ ተማረከ፤ ተዘረፈ፡ (ወይም፡ ተመራረከ፤ ተዛረፈ) ። አስዋር፡ እለ፡ ተማህረኩ ። እስመ፡ ተማህረከ፡ አባግዕየ፡ (ኢሳ፭፡ ፲፯ ። ሕዝ፴፬፡ ፰) ።

**ምህርክ፤**(ካት)፤ ምህሩክ፤ የተማረከ፡ ምርኮ፤ ምርኮኛ ። ዴዋ፡ ወምህርካ ። ተካፈልኒ፡ ምህርካ ። እንዘ፡ ትሰመይ፡ መምህረ፡ ወካቶሊካ፤ አባእክ፡ ሉቀ፡ ለክርስቶስ፡ ምህርካ፡ (ዘጉ፴፩፡ ፲፩ ። መዝ፡ ፳፯ ። ስንክ፡ ግንቦ፳) ።

**ምህርክና፤** ምርኮኝነት፤ ምርኮ፡ መኾን ። በምህርክ፡ ፈንታ፡ ምህርክና፡ ይላል፤ ስሕተት፡ ነው፡ (፪ዜና፡ ፳፰፡ ፭፡ ፰፡ ፲፫) ።

**አስተማህረከ፤** አማረከ፤ አመራረከ ። እንደ፡ አማህረከም፡ ባስደራጊነት፡ ይፈታል ።

**መዊእ ፤ አት ፤ (ሞአ ፡ ይመውእ ፡ ይማእ)** ፤ ማሸነፍ ፤ መርታት ፤ ድል ፡ መንሣት ። ትእምርተ ፡ መዊእ ። ወይን ፡ ይመውእ ፤ አንበሳ ፡ ይመውኣ ። ሞአ ፡ ለሞት ፡ ወተንሥአ ። ሞእክምዎ ፡ ለእኩይ ፡ (ኢፌ ፡ ተ፳ ። ዕገዞ ፡ ፲ ። ድጓ ። ፩ዮሐ ፡ ፪ ፡ ፲፫) ።

**መዋኢ ፤ (ኢት ፡ እያን ፡ ያት)** ፤ ያሸነፈ ፡ የሚያሸንፍ ፤ አሸናፊ ። ሰላም ፡ ለከ ፡ አባዲር ፡ መዋኢ ። ወኢሞአ ፡ በኀይሉ ፡ መዋኢት ። በእንተ ፡ በማዕፃት ፡ መዋእያን ፡ (ስንክ ፡ መስ፳፰ ። መቅ ፡ ወን ። ቅዳ) ።

**አሞአ** ፤ ድል ፡ አስነሣ ፤ አጸና ፡ አበረታ ፤ አሠለጠነ ። ኢያመውአ ፡ ሶበ ፡ ይትዋቀሥ ፡ (አርጋ ፡ ፩) ። ዘአሞአ ፡ እግዚ ፡ ላዕለ ፡ ካልኡ ። ከመ ፡ ታሙአ ፡ ለዘፈቀድከ ። ውእቱ ፡ ያመውአከ ፡ በጸራ ፡ ወበመንግሥቱ ፡ (ዮሴፍ) ።

**ተሞአ ፤ (ይትመዋእ)** ፤ ተሸነፈ ፤ ድል ፡ ኾነ ፤ ተረታ ። ሞት ፡ ተሞአ ። ወሶበሂ ፡ ይትዋቀሥ ፡ ይፀእ ፡ ተመዊአ ፡ (ድጓ ። መገ ፡ ፶፰) ። በተሞአ ፡ ፈንታ ፡ ተመውአ ፡ ይላል ፤ በስብሐና ፡ በቀደሰ ፡ መንገድ ፡ ካልኾነ ፡ በቀር ፡ በቀተለ ፡ ቤት ፡ አያስኬም ። ተመውአ ፡ ቀትል ፡ በይእቲ ፡ ዕለት ፡ (፪ዜና ፡ ፲፰ ፡ ፴፬) ።

**ምዉእ ፤ (ኣን ፡ ኣት ፡ ውእት)** ፤ የተሸነፈ ፤ ድል ፡ የኾነ ፤ የተረታ ። ትከውን ፡ ምዉአ ፡ ሎቱ ። ሕገ ፡ ጸብእ ፡ ወመዊእ ፡ ትሬስዮሙ ፡ ለምዉኣን ፡ አግብርተ ፡ ለመዋእያን ፡ (ፈላስ ፡ ገ፴፱ ። ፍ ፡ ነ ፡ ፴፩) ።

**ሙአት** ፤ ማሸነፍ ፤ መሸነፍ ፤ አሸናፊነት ፤ ድል ፡ ርታታ ። እፎ ፡ ትኄልዩ ፡ አንትሙ ፡ ሙአቶሙ ። እምድኅረ ፡ ሙአተ ፡ ሖሎሙ ፡ በይጠናኖት ። እምኀቤከ ፡ ሙአት ። ተሰጥመ ፡ ሞት ፡ ውስተ ፡ ሙአት ፡ (ዮሴፍ ። ፊልክ ፡ ፴፱ ። ዕገ፱ ፡ ፶፱ ። ፩ቆሮ ፡ ፲፭ ፡ ፶፬) ።

**ምዋኤ** ፤ ዝኒ ፡ ከማሁ ። ብጡል ፡ እምዋኤክሙ ፡ (አዋል) ።

**ምሕማእ ፤ (ኣት)** ፤ ማሸነፊያ ፡ ድል ፡ መንሻ ፤ መርቻ ፡ መረቻ ።

**ሙብኒም ፤ (ዕብ ፡ ሙክኒም)** ፤ ቅዉማን ፤ ርቱዓን ፤ ወይም ፡ ቅልብሶች ፡ ቅንፎች ፡ ማለት ፡ ነው ። በዕብራይስጡ ፡ በና ፡ ከ ፡ (ቤት ፡ ካፍ) ፡ ይማስላሉና ፡ በዚሁ ፡ ምክንያት ፡ ተሳስቶ ፡ ሙከ ፡ በማለት ፡ ፈንታ ፡ ሙብ ፡ ብሎታል ። ወከናፍሪሆሙ ፡ አሐዱ ፡ ጥፍሐ ፡ ሙብ(ከ)ኒም ፡ እንተ ፡ ውስጥ ፡ (ሕዝ፵ ፡ ፵፫) ።

**ሞገስ ፤—ውድ ፡ ውዴታ ፤—ወጊስ ፡ ወገሰ ።**

**ሙዝ ፤ (ብ ፡ አሕማዝ ፤ አምዋዝ ። ፀረ ፡ መውዝ ። ሱር ፡ ሙዛ)** ፤ በቁሙ ፤ የታወቀ ፡ ተክል ፡ የንሰትና ፡ የኮባ ፡ የጉናጉና ፡ ወገን ፤ ፍሬው ፡ ጥፍጥ ፡ (አዋል) ።



ሙዝ ፡

**ሞጣሕት ፤—በቁሙ ፤—ወጥሐ ፡ ወጥሐ ።**

**ሕማል ፤ (ዕብ ፡ ሙል)** ፤ ትይዩ ፡ አንጻር ፡ ፊት ፡ ለፊት ፤ አኳያ ፡ እኩያ ፡ አምሳያ ። ወዳጅን ፡ ባለሕማል ፡ እንዲሉ ፤ በዐረብ ፡ ግን ፡ ማል ፡ ብሎ ፡ ገንዘብ ፡ ይላል ።

**መዊጽ ፤ ጸት ፤ (ሞጸ ፡ ይመውጽ ፡ ይሙጽ ። ዐረ ፡ ማጸ)** ፤ መሕጠጥ ፡ መፋቅ ፤ የጥርስ ። መፈግፈግ ፡ መወልወል ፤ መጥረግ ፡ ማጥራት ፤ የድፍ ፡ የጕድፍ ። መካስ ፡ ካሳ ፡ መስጠት ፤ ቂምን ፡ በቀልን ፡ በካሳ ፡ ማጥፋት ። (ተረት) ፤ ሲታረቁ ፡ ከሶ ፤ ሲጸድቁ ፡ መንሾሶ ።

**መዋጺ ፤ (ጺት ፡ ጽያን ፡ ያት)** ፤ የሚሕጭ ፡ ሕጪ ፤ ካሽ ፡ ካሳ ፡ ሰጪ ።

**አሞጸ** ፤ አስካሰ ፤ ካሳ ፡ አሰጠ ።

**ተሞጸ ፤ ተመውጸ** ፤ ተሕጨ ፤ ተካሰ ።

**ምዉጽ ፤ (ጻን ፡ ጻት ፡ ውጽት)** ፤ የተሕጨ ፡ የተካሰ ።

**ተማወጸ** ፤ ተካካሰ ፤ ተራረቀ ።

**አስተማወጸ** ፤ አካካሰ ፤ አስተራረቀ ። ለዘተጻዐለ ፡ ያስተማውጽዎ ፡ (ሢራ፳፯ ፡ ፳፩) ።

**ሞጻ ፤ (ጻት)** ፤ ካሳ ፤ የበደል ፡ ዋጋ ፤ ሜጠ ፡ ደም ፡ መሥዕተ ፡ ኀጢአት ፡ (፩ነገ ፡ ፮ ፡ ፫ ፡ ፬ ፡ ፰ ፡ ፲፯) ። መሕጫ ፡ መፋቂያ ፤ ርጥብ ፡ ዕንጨት ፡ ወይም ፡ ጭራ ።

**ሞጽ ፤ (ዕብ)** ፤ ትቢዮ ፡ እብቅ ፤ ቂንድ ፡ እድፍ ፡ ጕድፍ ፡ ደቃቅ ፡ ነገር ።

**ሙጽ** ፤ ሙጭ ፤ ቂላፋ ፡ በትር ፡ የጤፍና ፡ የግሽላ ፡ መውቂያ ። ቂላፋም ፡ ባይኾን ፡ ማናቸውም ፡ የራቻ ፡ መውቂያ ፡ ሙጭ ፡ ይባላል ።



ሙጽ ፡

**ሙጻእ ፤—መውጫ ፡ ቀዳዳ ፤—ወፂአ ፡ ወፅአ ።**

**መዊቅ ፤ ቆት ፤ (ሞቀ ፡ ይመውቅ ፡ ይሙቅ ። ሐመ ፤ ረስን)** ፤ መሞቅ ፤ መተኰስ ፡ መቃጠል ፡ መንሣት ፡ ማግኘት ፤ ከፀሐይ ፡ ከእሳት ፤ ከልብስ ።

ከደዌ፤ ማቅ፡ ማለት፡ ከዚህ፡ ወጥቷል፤ ደመቀን፡ እ.ዩ። ሰበ፡ ሞቀ፡ ፀሓይ። ወእምከመ፡ ሞቀ፡ ፀሓይ፡ ይ ምሁ። ሐወዘኒ፡ እስመ፡ ሞቁ። ትትከደኑ፡ ወኢ ትመውቁ። እምፀምረ፡ አባግዐየ፡ ሞቀ፡ መታክፍ ቲሆሙ፡ (፩ነገ፡ ፲፩፡ ፱። ዘፀ፲፮፡ ፳፩። ኢሳ፵፬፡ ፲፮። ሐጌ፩፡ ፮። ኢዮ፴፩፡ ፳)። በሞቀ፡ ፈንታ፡ ተማወቀ፡ ይላል፤ አያሰኝም፡ (ኢሳ፵፬፡ ፲፮)።

**ምዉቅ**፤ (ቃን፡ ቃት፡ ውቅት)፤ የሞቀ፤ ሙቅ፡ ትኩስ። ለከሰ፡ ምዉቅ፡ ውእቱ፡ አልባሲከ። ምዉቅ፡ ከመ፡ እሳት። ኅብስት፡ ምዉቅ። ማይ፡ ምዉቅ። ዐዚዝ፡ ወምዉቅ፡ በመንፈስ፡ ቅዱስ፡ (ኢዮ፴፯፡ ፲፯። ሔኖ፲፱፡ ፲፫። ፩ነገ፡ ፳፩፡ ፮። ስንክ፡ የካ፲፩። ራእ፫፡ ፲፭። ቀሌ)።

**ሙቀት**፤ በቁሙ፤ መሞቅ፡ አሻሻቅ፤ ትኩሳት፡ ትኩስነት። እስከ፡ ሙቀተ፡ ፀሓይ። ሙቀተ፡ ሐሩር። እንዘ፡ ሀሎ፡ ሙቀት፡ ላዕሌሁ። አስሐትያ፡ ዘአልቦ፡ ሙቀት፡ (ነሐ፯፡ ፫። ሔኖ፡ ፬። ቅዳ። ቀሌ)።

**ሞቅ**፤ ሙቀት፤ ትኩሳት፡ (ሔኖ፸፭፡ ፬፡ ፯)። ነፋስ፡ ሞቅ። እሳተ፡ መለኮት፡ ዘይቈድስ፡ ነፍስ፡ ወያጥዒ፡ ሞቀ፡ (ሔኖ፸፯፡ ፭፡ ፯። ደራሲ)።

**አሞቀ**፤ በቁሙ፤ አተኰሰ። (አስሞቀ፡ አስተ ኰሰ)። እሳት፡ ያመውቅ፡ ለኀጺን። አሐቲ፡ ኖኅት፡ ታመውቅ፡ ሞቀ። ያመውቆ፡ ፀሓይ፡ ለውእቱ፡ ዕፄ፡ ወይከውን፡ ያፌ። አሙቅ፡ ላሕምቶ፡ (ቁር፡ ጸላ። ሔኖ፸፭፡ ፯። ዲድ፡ ፳፭። ሚራ፴፰፡ ፲፯)። በአሞቀ፡ ፈንታ፡ አስተማወቀ፡ ይላል፤ አድራጊነት፡ ካደራራጊነት፡ ያሳያል። ተሐቅፎ፡ ወታስተማውቆ። አስተማወቅዎ፡ እስትንፋስ፡ አድግ፡ ወላሕም፡ (፫ነገ፡ ፩፡ ፪። ቅዳ፡ ሕር)።

**ተማወቀ**፤ ተሞሞቀ። እስመ፡ እመ፡ ኖሙ፡ ክልኤሆሙ፡ ይትማወቁ፤ ወአሐዱሰ፡ እፎ፡ ይት ማወቅ፡ (መክ፬፡ ፲፩)።

**አስተማወቀ**፤ አሞቀ፤ አሞሞቀ። በዝየ፡ ያስተማውቅ፡ እደሁ፡ ካህን፡ ላዕለ፡ ማዕጠንት። እንዘ፡ ያስተማውቆሙ፡ በሠሉ፡ ምዕዳን፡ (ቅዳ። ገድ፡ ኪሮ)።

**መዊት**፤ ቶት፤ (ሞተ፡ ይመውት፡ ይ ሙት። ዕብ፡ ሜት። ሱር፡ ሚት። ዐረ፡ ማተ)፤ መሞት፡ መለየት፤ በነፍስ፡ ከሥጋ፡ በሥጋ፡ ከነፍስ፡ መራቅ፤ እየብቻ፡ መኾን፤ መድረቅ፡ መፍረስ፡ መበስበስ፤ መነቀል፡ መፍለስ፤ መጥፋት፡ መታጣት። ሐዩውኒ፡ ወመዊትኒ። ሞተ፡ ዐማኑኤል፡ ከመ፡ ሞተ፡ ዚኣነ፡ ዘውእቱ፡ ተፈልጦተ፡ ነፍስ፡ እምሥጋ። ሞትነ፡ እምኀጢአት። ወሙት፡ እምፍትወታቲሁ፡ ለዝ፡ ዓለም። እመ፡ ሞተ፡ አዕጹቂሁ። እለ፡ ካዕበ፡ ሞታ፡ ወተሠረዋ። ሞተት፡ ኅሊና፡ እምኔሁ፡ (ሚራ ፲፩፡ ፲፱። ሃይ፡ አበ። ሮሜ፯፡ ፱። ፊልክ፡ ፫። ኢዮ፲፱፡ ፳። ይሁ፡ ፲፪። ቄድር)።

**መዋቲ**፤ (ቲት፡ ትያን፡ ያት)፤ በቁሙ፤ የሞተ፡ የሚሞት፡ ሟች፤ ሥጋዊ፡ ሰው። አንተ፡ መዋቲ፡ ዘከመ፡ ዕፅናከ፡ ምስሌነ፤ ወአንተ፡ ኢመዋቲ፡ ዘ ከመ፡ ዕፅናከ፡ ምስለ፡ አብ። እመ፡ ኮነ፡ መዋቲ፡ ካህነ። ተናገሮ፡ በልሳነ፡ መዋቲ፡ (ሃይ፡ አበ። ፍ፡ ነ፡ ፳፱። ቀሉ)።

**ምዉት**፤ ሙት፤ (ታን፡ ታት፡ ውት)፤ በቁሙ፤ የሞተ፡ የተለየ፤ ሬሳ፡ በድን፡ አስከሬን። ምዉተ፡ ትካት። ምዉታን፡ በኀጢአት። በእንተ፡ ሙታን። ምውት፡ ይእቲ፡ ለሊሃ። (ሰቈ፫፡ ፯። ኤፌ፪፡ ፩። ፍ፡ ነ፡ ፳፪። ያዕ፪፡ ፲፯)።

**ሙተት**፤ መሞት፤ አማወት። ይሬእዩ፡ ሙ ተተ፡ ጻድቅ። ወሙተቶሂ፡ ምኑነ። በእንተ፡ ሙተቱ፡ ለብልጣሶር፡ (ጥበ፬፡ ፲፯። ፭፡ ፬። ዮሴፍ)።

**ሞት**፤ በቁሙ፤ የሥጋዊና፡ የደማዊ፡ ሕይ ወት፡ ፍጻሜ፤ በአዳም፡ ኀጢአት፡ የመጣ፡ ጠባይዓዊ፡ ፅዳ፤ ባሕርያዊ፡ ፍዳ። (ግጥም)፤ ከጕዣምና፡ ከዳሞት፡ ማን፡ ይበልጣለ፡ በስፋት፤ ተዉት፡ አየነው፡ ለየነው፡ ታላቁ፡ ዳሞት፡ ነው። መኑ፡ ሰብእ፡ ዘየሐዩ፡ ወኢይ ሬእዮ፡ ለሞት። ወሞተ፡ መብዝኅቶሙኒ፡ እስመ፡ ይከውን፡ በፍናው፡ ብዙኃት። ሞተ፡ ግብት። ሞት፡ ጠባይዓዊ፤ ሞተ፡ ፈቃድ። እግዚአብሔርሰ፡ ኢገ ብረ፡ ሞተ፡ ወኢይሔድሞ፡ ህጕሎሙ፡ ለሕያዋን። ኮ ነኖሙ፡ ሞት፡ እምአዳም፡ እስከ፡ ሙሴ፡ ለእለሂ፡ ኢአበሱ፡ ከመ፡ አበሳሁ፡ ለአዳም፡ (መዝ፡ ፹፰። ፊ ልክ። ፍ፡ ነ፡ ፶። ፊላስ። ጥበ፩፡ ፲፫። ሮሜ፭፡ ፲፬)።

**ማውታ**፤ ሙት፡ በከት፡ ሳያርዱት፡ ታሞ፡ ወይም፡ ገደል፡ ገብቶ፡ የሞተ፡ የከብት፡ ሬሳ። ማውታ፡ ወደም፡ ወብትክ። ዘረሠሰ፡ በበሊዐ፡ ማውታ። ጽ ዩእ፡ ሥጋ፡ ማውታ፡ (ቀሌ። ፈ፡ መ፡ ፮፡ ፬። ዲድ፡ ፮)። ለሰው፡ ሬሳም፡ ይኾናል። ዕጓለ፡ ማውታ፤ የሙት፡ ልድ። በደከታም፡ ፈንታ፡ ዕጓለ፡ ማውታ፡ ይላል፤ የት ርጓሜ፡ ቃል፡ ነው። አብ፡ ለዕጓለ፡ ማውታ። ኅደ ገኒ፡ አቡየ፡ ዕጓለ፡ ማውታ። ኢየኀድገክሙ፡ ዕጓለ፡ ማውታ፡ ትኩኑ፡ (መዝ፡ ፷፯። ጦቢ፩፡ ፰። ዮሐ፲፬፡ ፲፰)። ማውቻ፡ ደካማ፡ ኵሳሳ፡ ዐቅመ፡ ቢስ፡ (ዐማርኛ)።

**ማውትና**፤ ሙትነት፡ በከትነት፤ ደካምነት። በእንተ፡ ዕጓለ፡ ማውትናሆሙ፡ ወድክትምናሆሙ፡ (ዮሴፍ)።

**ምሟት**፤ ምምዋት፤ መሞቻ፤ በታ። ምሟቲሁ፡ ለዖዝ፡ (፪ነገ፡ ፮፡ ፰)።

**አሞተ**፤ ገደለ፤ አጠፋ፤ ለየ። አሙተኒ፡ ወኢ ታሙቶ። ለአሙቶቱ፡ ወለቀቲሎቱ። አሙትዋ፡ ለነ ፍስክሙ፡ እምሠሉ፡ ምግባረ፡ እኩይ፡ (ዮሴፍ። ኵፋ፡ ፴፫። ቀሌ)።

**መዝበር**፤—ፍራሽ፤—ዘቢር፡ ዘበረ።

**መዘገ**፤ (ዐረ፡ መዘጀ፤ አጋጨ። ዕብ፡ ማዘግ፤ ቀዳ፡ ቀላቀለ)፤ አስቀና፤ አፈካከረ። በማ ሕዘ፡ ዚአክሙ፡ ምዝጉ፡ ሠልክሙ፡ (፪ቆሮ፡ ፱፡ ፪)።

—፤ ነጠቀ፡ መነጠቀ፤ ነቀለ፡ ሳበ፤ በኀይል፡ ወሰደ። ጸሎቱ፡ ለኤልያስ፡ ሰማየ፡ መዘገ። ረድኤትከ፡ ወለተ፡ ከለባት፡ መዘገ፡ (ድጓ። ስንክ፡ ታኅ፲፪)። መሠጠንና፡ መጠቀን፡ እይ፤ የዚህ፡ ጎሮች፡ ናቸው።

**መዝጐል፤—ዘጐልማ፤—ዘጐል፡ ዘጐለ።**

**መዝገን፤ ምዝጋና፤—ዘጌን፡ ዘገነ።**

**መዚዝ፤ ዘት፤ (መዘ፤ መዘዘ፡ ይመዝዝ፡ ይምዝዝ)፤** መምዘዝ፡ መንቀል፤ መንጠቅ፤ የሰይፍ፡ የዱላ፤ ለሥርም፡ ይኸናል፤ መልጎን፡ እይ፤ ከዚህ፡ ጋራ፡ አንድ፡ ነው። መዝመዘም፡ ከዚህ፡ ወጥቷል።

**መዘዝ፤** ክፉ፡ ነገር፡ ያንደሰት፡ መርዝ፡ ሰይፍና፡ ዱላ፡ የሚያማዝዝ፡ (በማርኛ)።

**ምዙዛት፤ (ዕብራ)፤** ራግዛት፤ የግራና፡ የቀኝ፡ መቃኖች። አንዲቱን፡ ምዙዛ፡ ይላታል፤ ኹሉም፡ የቤት፡ አንቀጽ፡ ነው፡ (ሕዝ፵፭፡ ፳፩)።

**መዝሐ፤ (ዐረ፡ መዘሐ)፤** ተላፈ፡ ተዳፈ፤ ተቃበጠ፡ ተቀማጠለ። መሐዘንና፡ ሕንቀቀን፡ እይ፤ የዚህ፡ ጎሮች፡ ናቸው። መጽሐፍ፡ ግን፡ በመዝሐ፡ ፈንታ፡ አስተማዝሐ፡ ይላል፤ አያሰኝም። እምከመ፡ አስተማዘሕከ፡ ለወልድከ፡ (ሢራ፴፡ ፱)።

**ምዙሕ፤ (ሓን፡ ሓት፡ ዝሕት)፤** ድል ድል፡ ቅምጥል፤ ቀለጤ፡ ቀበጥ፤ ቅብጥብጥ። ከረየ፡ ጽጋብ፡ ለምዙሕ፡ (ዘዳ፴፪፡ ፲፭)። መጽሐፍ፡ ግን፡ በምዙሕ፡ ፈንታ፡ ምንዙሕ፡ ይላል፤ ባለቅኔዎችም፡ መንዝሐ፡ ብለው፡ ይገሳሉ፤ ነዝሀና፡ መዝሐ፡ ተዛንቆን፡ ከነዝሀ፡ መስም፡ ከምንዝህ፡ መጥቷል።

**መዛሕም፤ (ዐረ፡ መዛሒም)፤** ጽፉቅ፡ ጽፍቀት፡ ማለት፡ ነው፤ የሰውን፡ ብዛት፡ የበታን፡ ጥበት፡ መላፋትንና፡ መፋተግንም፡ ያሳያል፡ (ስንክ፡ ሠኔ፲፱)።

**ምዝላል፤—መሎጊያ፤—ዘሊል፡ ዘለ።**

**መዝመዘ፤ (መዚዝ፡ መዘ። ዕብ፡ ማዝሜዝ)፤** መዘመዘ፤ ዐሸ፡ አለፋ፡ አለሰለሰ፤ ዐደፈ፡ ወለወለ፡ (ዮሐ፲፭፡ ፪። ፲፪፡ ፫። ፲፫፡ ፭)። ይመዝምዝዎሙ፡ እምጸበለ፡ ቤት። መዝመዙ፡ ሥጋሆሙ፡ በአጽርቅት፡ (ተረ፡ ኤር፲፪። ስንክ፡ ኅዳ፩። ታኅ፲፱)።

**ተመዝመዘ፤** ተመዘመዘ፤ ታሸ፡ ተወለወለ። በከመ፡ ይትመዘመዝ፡ ጻሕል። እለ፡ ተመዝመዙ፡ በዐጌ፡ (፱ነገ፡ ፳፩፡ ፲፫። ኪዳ። አርጋ)።

**ምዝሙዝ፤** የተመዘመዘ፡ ምዝምዝ፤ የታሸ፡ የተወለወለ፤ ጥሩ፡ ደረቅ።

**መዝሙር፤—ምስጋና፡ በገና፤—ዘምሮ፡ ዘመረ።**

**መዝኖ፤ ኖት፤ (መዘነ፡ ይሜዝን፡ ይመዝን። ዐረ፡ ወዘነ። ዕብ፡ አዜን)፤** መመዘን፡ መለካት፤ ነገርን፡ መምከር፤ በሚዛን፡ ዕውቀት፡ ማንጸጸር፤ ደለወን፡ እይ። መዝኖት፡ (ፍ፡ ነ፡ ፴፫)።

**ተመዝነ፤** በቁሙ፤ ተለካ፡ ከሚዛን፡ ገባ። ዘይሰፈር፡ ወዘይትሜዘን፡ (ፍ፡ ነ፡ ፳፰)።

**ምዙን፤ (ናን፡ ናት፡ ዝንት)፤** የተመዘነ፡ የተለካ፤ ምዝን፡ ምእዙን። እዝንና፡ ማእዘንን፡ በአዘነ፡ ተራ፡ ተመልከት፤ ከዚህ፡ ጋራ፡ አንድ፡ ነው።

**ሚዛን፤ (ዐረ፡ አልሚዛን)፤** በቁሙ፤ መድሎት፡ መመዘኛ፡ ልክ። ዘይሰርቅ፡ በሚዛን። እለ፡ ይዒምፁ፡ በሚዛን፡ (ፈ፡ መ፡ ፲፯፡ ፯። ፳፯፡ ፫። መቃ፡ ፯፲)።



ሚዛን።

—፤ የኮከብ፡ ስም፤ መልኩ፡ ሚዛን፡ የሚመስል፡ የመስከረም፡ ኮከብ። ከፀሐይ፡ ጋራ፡ ፴፡ ዕለት፡ ፲፡ ኬክሮስ፡ ይመግባል፡ (አቡሻ፡ ፱)። ሚዛን፡ ያሰኘው፡ መልኩ፡ ብቻ፡ አይደለም፤ ግብሩም፡ ተጨምሯል፤ በርሱ፡ ምግብና፡ ውስጥ፡ በመስከረም፡ ባ፲፭ኛ፡ ቀን፡ መዓልትና፡ ሌሊት፡ ይተካከላሉ።

**መዘረ፤ (መዚር፤ ሚሰ፤ ዐጸረ)፤** ጠመቀ፡ ዘለለ፤ ዐሸ፡ አማሰለ፤ በጠበጠ፡ ጣለ፤ የድፍድፍ፡ የማር። መጸረን፡ እይ፤ የዚህ፡ መንቲያ፡ ነው፤ መዘረ፡ የጅ፡ የመጻፍ፡ መጸረ፡ ያፍ።

**መዛሬ፤ (ሬት፡ ርያን፡ ያት፤ ዘርት)፤** የጠመቀ፡ የሚጠምቅ፡ ጠማቂ፡ ጠላ፡ ቤት፡ ጠጅ፡ ቤት፤ መሸት፡ መሸተኛ፤ ቀጅ፡ ጂ፡ አሳላፊ። መዛርያን፡ ወመዛርያት። ሊቀ፡ መዘርት፡ (መክ፪፡ ፰። ኩፋ፡ ፴፱)።

**ምዝር፤ (ዐረ፡ ሚዝር፡ መዘር)፤** ዝልል፡ ጥሩ፡ ጠላ፡ ከእኸል፡ ከጌሾ፡ የሚሠራ፤ ዐረቂ፡ ጠጅ፡ የሚያሰክር፡ መጠጥ፡ (ገድ፡ ተክ)።

**መዝራዕት፤—ክንድ፡ ጡንቻ፤—ዘሪዕ፡ ዘርዐ።**

**ማዙሮት፤ (ጽር። ዕብ፡ ማዛሎት)፤** መናዝል፤ ከዋክብት፡ መገብተ፡ አውራኀ፤ የቀድሞ፡ ሰዎች፡ በየወሩ፡ የሚያመልኳቸው፡ ዛሬም፡ ጠንቋዮች፡ ለየሰዉ፡ የሚያድሏቸው፤ ነዛለን፡ እይ፡ (፬ነገ፡ ፳፫፡ ፭)።

**መዝስጢ፤ (ጽር፡ ሜጊስቲ)፤** የልዕልና፡ የክበሬታ፡ ስም፤ ልዑል፡ ዐቢይ፡ ክቡር፡ ራስ፡ ቢቶደድ፡ ይህን፡ የመሰለ፡ (አቡሻ፡ ፰)። ሦሜጋ፡ እንዲል፡ ታላቅ፡ ያ፡ ሲል።

**ምሕወ፤—ሜሜ፡ ቀለጠ፤—ምህወ።**

**መሐወ፤ (ዕብ፡ መሓህ። ዐረ፡ መሓ)፤** አጠፋ፡ ደመሰሰ፡ በውሃ፡ በምራቅ፤ የርስሐት፡ የጥፋት።

ምህወና ፡ መሐወ ፡ መሰወ ፡ እነዚህ ፡ ሦስቱ ፡ ፩ ፡ ዘር ፡ ናቸው ።

**መሐወ** ፤ ነቀለ ፡ መዘዘ ፤ ከሥሩ ፡ አፈለሰ ፤ ቀጨ ፡ ዐሸ ፤ ያታከልት ፡ የሸት ። እግዚ ፡ ይተክል ፡ ወይምሑ ። መሐወኒ ፡ እንተ ፡ ዙሰሄ ። ይየብስ ፡ ዘእንበለ ፡ ይምሐውዎ ። እኀዘ ፡ ይምሐዉ ፡ ሠዊተ ። ወመሐዋ ፡ በእዴሁ ፤ (ቀሌ ። ኢዮ ፲፱ ፡ ፲ ። መዝ ፡ ፶፳፰ ። ማቴ ፲፱ ፡ ፩ ። ስንክ) ።

**መሓዊ** ፤ (ዊት ፡ ውያን ፡ ያት ፤ ሐውት) ፤ የሚያጠፋ ፤ ነቃይ ፡ አጥፊ ።

**ተምሕወ** ፤ ጠፋ ፡ ተደመሰሰ ፤ ተነቀለ ። ወይትመሐዉ ፡ ምግባራቲከሙ ። ሥርወ ፡ ጻድቃን ፡ ኢይትመሐው ። ማዕር ፡ ዘተምሕወ ። ይቀድም ፡ ተምሒዎ ፡ እምነ ፡ ዙሉ ፡ ማዕር ፤ (ሕዝ፯ ፡ ፯ ። ምሳ ፲፪ ፡ ፫ ። ሄርማ ፡ ገ፶፱ ። ሢራ፵ ፡ ፲፯) ።

**ምሕው** ፤ (ዋን ፡ ዋት ፡ ሒት) ፤ የጠፋ ፡ የተነቀለ ፤ ጥፉ ፡ ንቁል ።

**መሐዘ** ፤ (ምዒዝ ፡ ምዕዘ) ፤ ጕለመሰ ፤ ጐበዘ ፡ አደገ ፤ ሚዝት ፡ ፈለገ ፤ ወሸመ ፡ ውሽማ ፡ ያዘ ። ሚዜ ፡ ሚዝ(ስ)ት ፤ ሚያገዝያ ፡ ማለት ፡ ከዚህ ፡ ወጥቷል ።

**መሓዝ** ፤ (ዛን ፡ ዛት) ፤ ደጕባ ፡ ጕልማሳ ፡ ጐበዝ ፤ ውሽማ ፡ የሰው ፡ ሴት ፡ የሚሰርቅ ፡ የሚያማግጥ ። ሊቃናትኒ ፡ ወመሓዛት ። ተንሥኡ ፡ መሓዛት ። ወመሓዝሰ ፡ በንዴተ ፡ አእምሮ ፡ ሀጕለ ፡ ነፍሱ ፡ ይገብር ። ብእሲት ፡ እንተ ፡ ተኀድግ ፡ ምታ ፡ ወትወልድ ፡ ወራሴ ፡ እምዲበ ፡ መሓዛ ። መሓዛንኪ ፡ እለ ፡ ይሰክቡ ፡ ምስሌኪ ፤ (መዝ ፡ ፻፵፰ ። ግብ፭ ፡ ፮ ። ምሳ፮ ፡ ፴፪ ። ሢራ፳፫ ፡ ፳፪ ። ኢሳ፶፯ ፡ ፫) ።

**መሓዝ** ፤ ጕልማስነት ፡ ልጅነት ፤ ዐፍላ ፡ ጕብዝና ፡ ቍንጅና ። ተሐራሚት ፡ እምወይን ፡ መሓዛ ፡ ወእምእክለ ፡ ውርዙት ፤ (ስንክ ፡ ጥቅ፳፱) ።

**ተማሐዘ** ፤ (ይትማሐዝ) ፤ ተጕላመሰ ፤ ተጻራ ፡ ተቃበጠ ፤ ተዋዛ ፡ ተጫወተ ። ይትማሐዛ ፡ መራዕዊከሙ ፤ (ሆሴ፱ ፡ ፲፫ ፡ ፲፬) ። ኢትትማሐዝ ፡ ምስለ ፡ ብእሲት ። ኢትትማሐዝ ፡ ምስለ ፡ መኳንንት ። ዘይትማሐዝ ፡ ምስለ ፡ ጸላእቱ ፡ ይፈቅድ ፡ ከሚተ ፡ ኀጢአቱ ፤ እስመ ፡ ተማሕዞሰ ፡ መራኍት ፡ ተጻልኦ ፡ ለጸላእቱ ፤ (ፈላስ ፡ ገ፶፭ ። ፳፫ ። ፳) ። ዋዛ ፡ ለቁም ፡ ነገር ፡ ብላቴን ፡ ጌታው ፡ ማለት ፡ ከዚህ ፡ የወጣ ፡ ነው ።

**ማሕየብ** ፤—መቅጃ ፤—ሐዩብ ፡ ሔበ ።

**መሐከ** ፤—ራራ ፡ ዐዘነ ፤—ምሂክ ፡ መሀከ ።

**መሐለ** ፤ (ብሂል ፡ ብህለ ። ዐረ ፡ በሀለ) ፤ ማለ ፡ ተረገመ ፤ ተፈጠመ ፤ ነገርን ፡ ለማጽደቅ ፡ ለማጽናት ። ኢትምሐሉ ፡ ግሙራ ። እለ ፡ ይምሕሉ ፡ በጽድቅ ፡ አው ፡ በሐሰት ። መሐልኩ ፡ ሰርእስየ ። ዘብዙኀ ፡ ይምሕል ፤ (ማቴ፭ ፡ ፴፫ ። ፈ ፡ መ ፡ ፳፪ ። ኤር ፳፪ ፡ ፭ ። ሢራ፳፯ ፡ ፲፬) ። ተሳለ ፤ ብፅዐት ፡ ገባ ፤ ውል ፡ አደረገ ። በፅዐንና ፡ ኪደን ፡ ብህለን ፡ ተመልከት ።

**መሓሊ** ፤ (ሊት ፡ ልያን ፡ ያት) ፤ የማለ ፤ የሚምል ፤ ማይ ፡ ማለኛ ። ብእሲ ፡ መሓሊ ። ለእመ ፡ አእመረ ፡ መሓሊ ። ሐሳዊ ፡ ወመሓሊ ፡ በሐሰት ፤ (ሢራ፳፫ ፡ ፲፩ ። ፍ ፡ ነ ፡ ፵፫ ፡ ፭ ። ቀሌ) ።

**መሐላ** ፤ በቁሙ ፡ ማላ ፤ ፍጥም ፤ የውል ፡ ነገር ፡ ማጽደቂያ ፤ በፈጣሪ ፡ ወይም ፡ በፍጡር ፡ ስም ፡ በሚወዱትና ፡ በሚያከብሩት ፡ ነገር ፡ የሚደረግ ። መሐላ ፡ በሐሰት ። መሐላ ፡ ጽድቅ ። ከመ ፡ አቅም ፡ መሐላየ ፤ (ቀሌ ። ኩፋ ፡ ፴፭ ። ኤር፲፩ ፡ ፭) ።

—፤ ስለት ፡ ብፅዐት ፤ ወይም ፡ የስለትና ፡ የብፅዐት ፡ ቃል ፤ ውል ፡ ኪዳን ። በመሐላሆሙ ፡ ለማርደያም ፡ ወለወልዳ ፤ (ስንክ ፡ ጥቅ፱) ።

**አምሐለ** ፤ አማለ ፤ አስማለ ፤ አማጠነ ። አምሐሎ ፡ በደመ ፡ አቤል ፡ ከመ ። አምሐሎሙ ፡ በእንተ ፡ አዕፅምቲሁ ። አምሕለከ ፡ በእግዚ ፡ ከመ ፡ ኢትማቅየኒ ። ይከውን ፡ ጌጋዩ ፡ ላዕለ ፡ ዘአምሐሎ ፤ (ቀሌ ። ኩፋ ፡ ፵፯ ። ማርቆ ፡ ፭ ። ፍ ፡ ነ ፡ ፵፫) ።

**ተምሕለ** ፤ ተማለ ፤ ተማለበት ።

**ተማሐለ** ፤ ተማማለ ፤ ተፈጣጠመ ፤ ቃል ፡ ኪዳን ፡ ተጋባ ። ተማሐልነ ፡ ክልኤነ ። ተማሐልነ ፡ ምስለ ፡ ሲኦል ። ዐደው ፡ እለ ፡ ተማሐልከ ፤ (፩ነገ ፡ ፳ ፡ ፵፪ ። ኢሳ፳፰ ፡ ፲፭ ። ዓብድ ፡ ፯) ።

**ተማሕለለ** ፤ (ተቀ ፡ ግ) ፤ ተማለለ ፤ ለመነ ፡ ማለደ ፤ አቤት ፡ አቤት ፡ አለ ፤ መሐላና ፡ ኪዳን ፡ በማሳሰብ ። ይትማሐለል ፡ አሮን ፡ በደበ ፡ አቅርንቲሁ ። እንዘ ፡ ይትማሐለል ፡ ቅድመ ፡ እግዚ ፡ በእንተ ፡ አበሳ ። ወሰገደ ፡ ሎቱ ፡ እንዘ ፡ ይትማሐለል ። ኀበ ፡ መኑ ፡ እትማሐለል ፤ (ዘፀ፴ ፡ ፲ ። ኩፋ ፡ ፵፩ ። ማቴ፲፯ ፡ ፲፬ ። አርጋ) ።

**ምሕላ** ፤ **ምሕላል** ፤ በቁሙ ፤ ልመና ፡ ምልጃ ፤ የማኅበር ፡ የሕዝብ ፡ ጸሎት ፡ እግዚኦታ ። እመኒ ፡ አብዛኅከሙ ፡ ምሕላከሙ ። ቀድሱ ፡ ጾመ ፡ ወሰብኩ ፡ ምሕላ ። በዙሉ ፡ ምሕላ ፡ ወበዙሉ ፡ ጸሎት ። ተወከፍ ፡ ምሕላነ ፤ (ኢሳ፩ ፡ ፲፭ ። ዮኤ፩ ፡ ፲፬ ። ፫ነገ ፡ ፰ ፡ ፴፰ ። ድጓ) ። መሐለ ፡ ከብህለ ፡ የወጣ ፡ ስለ ፡ ኾነ ፡ ተማህለለ ፡ ምህላ ፡ እያለ ፡ በሆይ ፡ ፀ ፡ ይጥፋል ፤ ገንዘቡ ፡ አይደለም ።

**ማሕሌት** ፤—በቁሙ ፡ ምስጋና ፤—ሐልይ ፡ ሐለየ ።

**ምሒን** ፤ ኖት ፤ (መሐኑ ፡ ይምሕን ፡ ይምሐን ። ዐረ ፡ መሐነ) ፤ መፈግፈግ ፤ ማሸት ፡ ማልፋት ፤ ማለስለስ ፤ የቈርበት ፤ ለልብስና ፡ ለፈትልም ፡ ይኾናል ። መስጠት ፡ ማስረከብ ፡ እንሆ ፡ ማለት ።

**መሓን** ፤ ማሻ ፡ ማልፊያ ፤ ወይም ፡ አልፊ ፡ ዐሻታ ፤ ዐራቢ ። ማእሰ ፡ በግዕ ፡ ሐሩይ ፡ ግቡረ ፡ መሓን ፤ (ዘፀ፴፭ ፡ ፯ ፡ ፳፫) ።

**ምሕን** ፤ በቁሙ ፤ መን ፡ የሽማ ፡ መሥሪያ ፤ ርስ ፡ በርሱ ፡ የሚፋተግ ፡ የሚፈጋፈግ ። አነመን ፡ እይ ።

ወምሕኑሂ ፡ ዘእምላዕሉ ፡ ጽላሎተ ፡ እግዚ ፡ (ቅዳ ፡ ሕር ። ተረ ፡ ቈር) ።

ምሕን ፡

**መሐና ፤(ዕብ ፡ ሚንሓህ)** ፤ እጅ ፡ መንሻ ፡ በረከት ፤ የፍቅር ፡ ስጦታ ። ንሣእ ፡ መሐና ። ወአብአ ፡ ሎቱ ፡ መሐና ፡ (፩ነገ ፡ ፰ ፡ ፰ ። ፲፯ ፡ ፫ ፡ ፬ ። ፰ ፡ ፲፪) ።

**ማሕፈድ ፤—ግንብ ፤—ኀፌድ ፡ ኀፈደ ።**

**ማሕፈር ፤—ወዳጅ ፤—ኀፌር ፡ ኀፍረ ።**

**መሐጸ ፤(ምሒጽ ። ዐረ ፡ መሐጸ ። ዕብ ፡ ማሐጽ)** ፤ መታ ፤ ፈለጠ ፡ ቈረጠ ፤ ሰበረ ፡ አደቀቀ ፤ ገደለ ፡ አጠፋ ። የይፋት ፡ እስላም ፡ መታ ፡ አስመታ ፡ ሲል ፡ ማጠ ፡ አስማጠ ፡ ይላል ። ፪ኛም ፡ ግእዙ ፡ አሐርጸሙ ፡ ከመ ፡ ጸበል ፡ ባለው ፤ ዕብራይስጡ ፡ ኤምሐጼም ፡ ከዓፋር ፡ እንዲል ፡ (መዝ ፲፯) ። ከመ ፡ ይምሐጸሙ ፡ በሰይፍ ። መሐጸሙ ፡ ወቀተሎሙ ፡ (ኩፋ ፡ ፳ና ፡ ፵፰) ።

**መሓጺ ፤(ጺት ፡ ጽያን ፡ ያት)** ፤ የሚመታ ፡ ተማች ፤ ፈላጭ ፡ ቈራጭ ፤ ገዳይ ፡ አጥፊ ። ለሆሎፎርኒስ ፡ ግብተ ፡ በሰይፈ ፡ ዮዲት ፡ መሓጺሁ ፡ (ደራሲ) ።

**ማሕጼ** ፤ ማጤ ፡ ምሣር ፡ መቍረጫ ፡ መፍለጫ ፤ መምቻ ፡ መከትከቻ ፡ (መዝ ፡ ፸፫ ፡ ፮ ። ማቴ ፫ ፡ ፲ ። ፩ነገ ፡ ፮ ፡ ፳ ፡ ፯) ።

ማሕጼ ፡

**ተምሕጸ** ፤ ተመታ ፡ ተቈረጠ ፤ ሞተ ፡ ጠፋ ።

**ምሑጽ ፤(ጻን ፡ ጻት ፡ ሕጽት)** ፤ የተመታ ፡ የተቈረጠ ፤ የሞተ ፡ የጠፋ ። ወትከውን ፡ ምሑጸ ፡ በምርዓየ ፡ አዕይንቲከ ፡ (ዘዳ፳፰ ፡ ፴፬) ። ዕብራይስጡ ፡ ማን ፡ ምሹጋዕ ፡ ይላል ፤ እብድ ፡ እንቡዝ ፡ ቅብዝብዝ ፡ ማለት ፡ ነው ። ባለብሉዮችም ፡ ዐይንን ፡ ተከትለው ፤ ዕውር ፡ ጨምጫማ ፡ ይሉታል ፤ ፪ኛም ፡ ምሕጸ ፡ ሸሸ ፡ ብለው ፡ ምሑጽ ፡ የሸሸ ፡ ይላሉ ። ዘይቤው ፡ አይደለም ። ፫ኛም ፡ በምሑጽ ፡ ፈንታ ፡ ምሑስ ፡ ይላል ፤ ስሕተት ፡ ነው ። ከመ ፡ አይሁድ ፡ ምሑሳን ፡ (ሲኖዶ) ።

**ምሕጻት** ፤ መምታት ፡ መቍረጥ ፤ መመታት ፡ መቈረጥ ፤ ሞት ፡ ጥፋት ። ኢመጽአሙ ፡ መቅሠፍት ፡ ለቀቲል ፡ ወለምሕጻት ፡ (ኩፋ ፡ ፵፬) ።

**ምሕጸ ፤ መሐጸ ፤—አማጠ ፡ ተጨነቀ ፤—ምኂዕ ፡ መኀፀ ።**

**ማሕጸን ፤ – በቁሙ ፡ ማጠን ፤—ሐፂን ፡ ሐፀነ ።**

**መሐረ ፤—አስተማረ ፤—ምሂር ፡ መሀረ ።**

**ምሒር ፤ ሮት ፤ (ምሕረ ፤ መሐረ ፡ ይምሕር ፡ ይምሐር ። ዕብ ፡ ማሐል ፤ ራሐም ። ሱር ፡ ርሔም ። ዐረ ፡ ረሒመ)** ፤ መማር ፡ ይቅር ፡ ማለት ፤ ዕዳን ፡ በደልን ፡ መተው ። ለዘሂ ፡ መሐርክዎ ፡ እምሕሮ ። መፍትው ፡ አንተሂ ፡ ትምሐር ፡ ቢጸከ ፡ በከመ ፡ አነ ፡ መሐርኩከ ። አሐዱ ፡ ዘመሐሮ ፡ መንፈቀ ፡ ዕዳሁ ፡ (ሮሜ፱ ፡ ፲፭ ። ማቴ፲፰ ፡ ፴፫ ። ሉ ፡ መ ፡ ፯ ፡ ፲፩) ።

—፤ መውደድ ፡ ማፍቀር ፤ ከፍቅር ፡ የተነሣ ፡ ማዘን ፡ መራራት ፤ መስጠት ፡ መመጽወት ። በከመ ፡ ይምሕር ፡ አብ ፡ ውሉዶ ፡ ከማሁ ፡ ይምሕሮሙ ፡ እግዚ ፡ ለእለ ፡ ይፈርህዎ ። ሶበ ፡ መጽወትነ ፡ ወመሐርነ ። ርእዮ ፡ ወምሕሮ ። ደቂቅ ፡ ዘምሕሮ ፡ እግዚ ፡ ለገብርከ ። በምሒረ ፡ ነዳይ ፡ (መዝ ፡ ፻፪ ። አፈ ፡ ተ፴፬ ። ሉቃ፲ ፡ ፴፫ ። ዘፍ፴፫ ፡ ፭ ። ዳን፬ ፡ ፳፬) ። በምሕረ ፡ ፈንታ ፡ አስተምሐረ ፡ ይላል ፤ ስሕተት ፡ ነው ። ነጽር ፡ ላዕሌየ ፡ ወአስተምሕረኒ ። አስተምሕር ፡ ሕማሞሙ ፡ ለዘመድነ ፡ (ጦቢ፫ ፡ ፲፭ ። ዮዲ፯ ፡ ፲፱) ።

**መሓሪ ፤ (ሪት ፡ ርያን ፡ ያት)** ፤ በቁሙ ፤ የሚምር ፡ ማሪ ፤ ይቅር ፡ ባይ ፡ ዐዛኝ ፡ ርኅሩኅ ፤ ሰጭ ፡ መጺች ፤ ለጋስ ፡ ሰው ፡ ወዳጅ ። መሓሬ ፡ ብዙኃን ፡ እምዕዳ ። መሓሪ ፡ ለዕጓለ ፡ መሕያው ። ዐይንከ ፡ መሓሪት ። ወኩኑ ፡ መሓርያነ ፡ ቢጽክሙ ። አንስት ፡ መሓርያት ፡ (ስንክ ፡ ጥቅ፱ ። ኀዳ፲፬ ። አርጋ ። ኤፌ፬ ፡ ፴፪ ። ሰቈ፬ ፡ ፲) ። መሐርና ፡ መዓር ፡ ባማርኛ ፡ ይተባበራሉ ። (ግጥም ፤ ልጅ ፡ ኢያሱ ፡ በተያዙ ፡ ጊዜ ፡ ታስረው ፡ ከነበሩት ፡ ሰዎቻቸው ፡ አንዱ) ፤ ጠጅም ፡ አልቀመስነ ፡ ከተለየናችኹ ፤ አውራው ፡ ከተያዘ ፡ ማሩን ፡ እባካችኹ ።

**አምሐረ** ፤ አስማረ ፤ ይቅር ፡ አሰኘ ። አራራ ፤ አሳዘነ ። ያምሕሩኒ ፡ እሉ ፡ አሕዛብ ። ወአምሐርዎ ፡ ለኢየሱስ ፡ (ማቴ፲፭ ፡ ፴፪ ። ፰ ፡ ፴፬ ። ማር፰ ፡ ፪) ።

**ተምሕረ** ፤ ተማረ ፡ ይቅር ፡ ተባለ ፤ ይቅርታ ፡ አገኘ ። ዘይምሕር ፡ ይትመሐር ። ብፁዓን ፡ መሓርያን ፤ እስመ ፡ እሙንቱ ፡ ይትመሐሩ ፡ (ምሳ፲፯ ፡ ፭ ። ማቴ፭ ፡ ፯) ።

**ምሑር ፤(ራን ፡ ራት ፡ ሕርት)** ፤ የተማረ ፤ ይቅር ፡ የተባለ ። ኢኮንክሙ ፡ ምሑራነ ፡ (፩ጴጥ ፡ ፪ ፡ ፲) ።

**ምሕረት ፤(ታት)** ፤ በቁሙ ፤ ይቅር ፡ ማለት ፡ መባል ። ይቅርታ ፡ ቸርነት ፤ ርኅራኄ ፡ ፍቅር ፡ ምጺት ። እለ ፡ ትፈርህዎ ፡ ለእግዚ ፡ ጽንሕዋ ፡ ለምሕረቱ ፤ እስመ ፡ በከመ ፡ ዕበዩ ፡ ከማሁ ፡ ዕበየ ፡ ምሕረቱ ። አበ ፡ ምሕረታት ። የዐጹ ፡ ምሕረቶ ። እለ ፡ አልቦሙ ፡ ምሕረት ። ምሕረተ ፡ ነዳያን ፡ (ሢራ፪ ፡ ፯ ፡ ፳፫ ። ኪዳ ። ፪ጢሞ ፡ ፫ ፡ ፫ ። ሮሜ ፡ ፩ ፡ ፴፩ ። ፍ ፡ ነ ፡ ፲፪) ።

—፤ ልብ ፡ ሆድ ፡ አንዠት ፤ የርኅራኄ ፡ ምንጭ ። ተፈሥሐ ፡ ምሕረቱ ፡ ወልቡ ፡ ላዕሌሁ ። ምሕረትየ ፡ ይ

ባርከከ። አሕዘኑ፡ ምሕረተ፡ አቡሆሙ፡ (ኩፋ፡ ፳፪። ፳፭። ፴፬)።

**ምሕረት፤ (ዕብ፡ ሬሔም፤ ራሓም)፤** ማሕፀን፡ እፊ፡ ማሕፀን፤ የፅንስ፡ የሽል፡ ቦታ። ምስ ጢሩ፡ ከሆድ፡ ይገባል። ኅቡረ፡ ተዘራዕነ፡ በውስተ፡ ከርሥኪ፡ ወኅቡረ፡ ወፃእነ፡ እምሕረትኪ፡ (ኩፋ፡ ፳፭)።

**አስተምሐረ፤** ለመነ፡ ማለደ፤ አማለደ፡ አስ ማረ፤ ማረኝ፡ ማርልኝ፡ አለ። አስተምሕር፡ ለነ፡ ሚ ካኤል። ሰአሉ፡ ለነ፡ አስተምሕሩ፡ ለነ፡ (መሥዋ። ድጓ)።

**አስተማሐረ፤** አማማረ፡ አላመነ፤ አመላለደ፡ አስተዛዘነ። ተፋቅሮ፡ ያስተማሕር፡ (፩ቆሮ፡ ፲፫፡ ፬)።

**መስተምሕር፤ ማሕር፤ (ርት፡ ራን፡ ራት)፤** የሚያስምር፡ የሚያማልድ፡ አማላጅ፤ አስተዛ ዛኝ። ኦ፡ መስተምሕርት፡ አስተምሕሪ፡ ኀበ፡ ወል ድኪ፡ (ቅዳ)።

**ማሕረከ፤—ማረከ፤—ምሂር፡ መሀረ፡ ማሀረከ።**

**መሐረም፤—ያረበች፡ መዠመሪያ፡ ወር፤—ሐረመ።**

**መሐስዕ፤—ጠቦት፤—ሐሲዕ፡ ሐስዐ።**

**ማኅደፍ፤—ማደፊያ፡ መወልወያ፤—ኅ ድፎ፡ ኅደፈ።**

**ማኅፈድ፤—ማንብ፤—ኀፊድ፡ ኀፈደ።**

**ማኅፈር፤—እሙን፡ ወዳጅ፤—ኀፊር፡ ኀፍረ።**

**ምኂፅ፤ ፆት፤ (መኀፀ፡ ይምኅፅ፤ ይም ኅፅ። ዐረ፡ መኂፀ)፤** ማማጥ፡ መጨነቅ፤ በምጥ፡ መያዝ፤ ለመውለድ፤ የሆድን፡ ለማውጣት። መጽሐፍ፡ ግን፡ በምኅፀ፡ ፈንታ፡ እንዳማርኛው፡ አምኀፀ፡ ይላል፤ ስሕተት፡ ነው። ጊዜ፡ ታምኅፀ፡ ትኬልሕ፡ (አዋል)።

**ምኅፅ፤** ምጥ፡ ጭንቅ፤ እሕታ። ሐመመን፡ እይ፤ የዚህ፡ ጎር፡ ነው። (ተረት)፤ ምጡን፡ ርሺው፤ ልጁን፡ አንሺው። የልጅ፡ ደፋር፡ ምጥ፡ ለናቷ፡ ታስተምር።

**አምኀፀ፤** አስማጠ፡ አስጨነቀ፤ እሕ፡ አሰኘ።

**ማኅፅ፤** ማጥ፡ ረግረግ፤ አረንቋ፡ የሚያሰ(ስ) ምጥ፡ የሚያስጨንቅ።

**ማጣ፤ (ዕብ፡ ሚጣ)፤** ዐልጋ፡ ዙፋን። እ ግረ፡ ማጣ፡ (ድጓ። መዋሥ)።

**መጥበስ፤—መጥበሻ፤—ጠቢስ፡ ጠ በሰ።**

**መጥዎ፤ ዎት፤ (መጠወ፡ ይሜጡ፡ ይ መጡ። ሰጠወ፤ ወሀበ፡ ወከፈ፡ ወፈየ። ዐረ፡ አዕጣ)፤** መመጥወት፤ ምጽዋት፡ መስጠት፡ ማደል፤ ማ ጉረሥ፡ ማቀበል፤ ማሳለፍ፡ ማቅረብ፤ ማሲያዝ፡ ማስ ጨበጥ፡ ማስረከብ። ዘመጠወ፡ ርእሶ፡ በእንቲአነ። መ ጠዎ፡ ቍርባነ። ከመ፡ ይመጥውዋ፡ ጽዋዐ። መጥ ወኒ፡ እሜጥወከ፡ (ቲቶ፪፡ ፲፬። ቀሌ። ራእ፲፯፡ ፲፱። አዋል)።

**መጣዊ፤ (ዊት፡ ውያን፡ ያት)፤** የሚሰጥ፡ የሚያድል፡ የሚያቀብል፤ በአፍ፡ በእጅ። መጣዌ፡ አ ፊት፡ (መጽ፡ ምስ)።

**ተመጠወ፤** ተሰጠ፤ ተሰጠው፤ ተቀበለ፤ ተመጠ ወተ፡ ምጺተኛ፡ ኾነ። ተመጠዋ፡ እምነ፡ ያማኑ፤ ወ ሰበ፡ ተመጠዋ። ዘይትሜጠ፡ ቍርባነ፡ ምዕረ፡ በበ፡ ዓመት። ተመጠው፡ እምኃየ፡ እምእዴየ፡ (ራእ፭፡ ፯፡ ፰። እፌ፡ ተ፲፯። ዘፍ፴፫፡ ፲)።

**ተመጣዊ፤** የሚሰጥ፡ ተሰጭ። ተቀባይ፡ ተመጥ ዋች። ሙሴ፡ ተመጣዌ፡ አሪት። ተመጣዌ፡ ቍር ባን። ተመጣዌ፡ ኅብስት፡ ወማይ፡ (መጽ፡ ምስ። ፈ፡ መ፡ ፳፮፡ ፰። ደራሲ)።

**ምጥው፤ (ውት፡ ጡት፤ ዋን፡ ዋት)፤** የተሰጠ፤ የተሰጠው፤ ተሰጭ፡ ገንዘብ፡ ወይም፡ ተቀባይ፡ ሰው። ሶበ፡ ነጸረ፡ ርእሶ፡ ምጥወ፡ ለሐሱ፡ መከራ፡ (ፈ፡ መ፡ ፬፡ ፩)።

**ምጣዌ፤** አሰጣጥ፤ አቀባበል፤ ስጦታ፡ ምጺት።

**መጥለውዝ፤—መጥረቢያ፤—ጸለወ፡ መጽለውዝ።**

**መጢማ፤—ጢቆሽ፤—ጠሚዕ፡ ጠ ምዐ።**

**መጥኖ፤ ኖት፤ (መጠነ፡ ይሜጥን፡ ይ መጥን። መአደ)፤** መመጠን፡ መለካት፤ መስፈር፡ መከንዳት፤ ልክ፡ ማወቅ፡ መገመት፤ ይኽን፡ ያኽል፡ ማለት፤ መወሰን፡ ማስተካከል። ዐቀመንና፡ ወሰነን፡ እይ፤ የዚህ፡ መንደር፡ ናቸው። ይሜጥንዋ፡ በሐብለ፡ መስፈርት። ወመጠነ፡ ርሕበ፡ ሕንጻ፡ አሐደ፡ ኅ ለተ። አሜሃ፡ ይሜጥን፡ ድካመ፡ ዚኣሁ። ይፈቅድ፡ ይትአመንዎ፡ ወአከ፡ ከመ፡ ይመጥንዎ፤ ወእስመ፡ ኢይትከሀሎ፡ ለኅሊና፡ ይመጥን፡ ባሕርየ፡ ዚኣሁ፡ (ኢሳ፵፱፡ ፲፭። ሕዝ፵፡ ፭። ማር፡ ይሥ፯፡ ፭። እፌ፡ ድ፳፪)።

**መጣኒ፤ (ኒት፡ ንያን፡ ያት)፤** የሚመጥን፡ መጣኝ፤ ሰፋሪ፡ ልክ፡ ዐዋቂ። ወኢኅሊና፡ መጣንያን፡ (ያዕ፡ ዘእል)።

**መጠን፤ (ብ፡ አምጣን፤ ናት)፤** በቍሙ፤ ልክ፡ ስፍር፡ ቍጥር፤ ሚዛን፡ ገመድ፤ ዐቅም፡ ማዕርግ። መጠኑ፡ ለረድእ፡ ከመ፡ ሊቁ። ለእሳትሰ፡ ቦቱ፡ መ ጠን። ወዙሉ፡ ክብር፡ ኢመጠና። ክቡራተ፡ መጠን፡ (ማቴ፲፡ ፳፭። ቅዳ። ምሳ፰፡ ፲፭። ማር፡ ይሥ፮፡ ፬)። መኑ፡ ሠርዐ፡ አምጣኒሃ። በከመ፡ አምጣኒሁ፡ ለ ዝኩ። ወእሉ፡ አምጣናተ፡ ምሥዋዕ፡ በእመታት፡ (ኢዮ፴፰፡ ፭። ሕዝ፵፡ ፳፱። ፵፫፡ ፲፫)። ፈትል፡ ሐብል፡

በማለት ፡ ፈንታ ፡ አምጣን ፡ ይላል ፤ ምስጢሩ ፡ እንጂ ፡ ዘይቤው ፡ አይደለም ። ሰሐበ ፡ አምጣነ ። አምጣን ፡ ዘየዐውዶ ፡ (ሰቈ፪ ፡ ፷ ። ኤር፶፪ ፡ ፳፩) ።

**መጠን ፤ አምጣን ፤** ዐቢይ ፡ አገባብ ፤ የ ፡ እንደ ፡ ያኽል ፤ ጊዜ ፡ ዘመን ፤ ሳ ፡ ይኾናል ፤ ጊዜና ፡ ሳ ፡ ፩ ፡ ወገን ፡ ነው ። መጠነ ፡ ገብረ ፡ ላቲ ፡ ለነፍስየ ። ተአምር ፡ መጠነ ፡ ተልእከኒ ። መጠነ ፡ ብክ ፡ የ ፡ (መዝ ፡ ፳፭) ። ፈለግየ ፡ ከነኒ ፡ መጠነ ፡ ባሕር ። ሊትሬሊኑ ፡ መጠነ ፡ ይበልዕ ፡ ወይሰቲ ። ወአምጣነ ፡ ገፍዐት ፡ ወሣቀየት ፤ ኸማሁ ፤ እንደ ፡ (ሚራ፳፬ ፡ ፴፩ ። ዳን፲፫ ፡ ፯ ። ራእ፲፰ ፡ ፯) ። ሚ ፡ መጠን ፡ ኑኃ ፡ ወሚ ፡ መጠን ፡ ርሕባ ። መጠነ ፡ አሐቲ ፡ ሰዓት ። መጠነ ፡ ዝ ፡ መዋዕል ፤ ያኽል ፡ (ዘካ፪ ፡ ፪ ። ዳን፱ ፡ ፲፯ ። አስቴ፪ ፡ ፲፪) ። አምጣነ ፡ ትበልዕዎ ፡ ለዝንቱ ፡ ኅብስት ። አምጣነ ፡ ሕያው ፡ ውእቱ ። አምጣነሰ ፡ ሕፃን ፡ ውእቱ ፡ ወራሲ ። አምጣነ ፡ ሀሎ ፡ መርዓዊ ፡ ምስሌሆሙ ፤ ጊዜ ፡ ሳለ ፡ (፩ቆሮ ፡ ፲፩ ፡ ፳፮ ። ሮሜ፯ ፡ ፩ ። ገላ፬ ፡ ፩ ። ማቴ፱ ፡ ፲፭) ። አምጣን ፡ ለብቻው ፡ ተለይቶ ፡ እንደ ፡ እስመ ፡ ና ፡ ስለ ፡ ይኾናል ። እፈርህ ፡ ሞተ ፤ አምጣነ ፡ ደወይኩ ፤ ታምሚያለኹና ፡ ስለ ። መጠንና ፡ አምጣን ፡ ስፍር ፡ ቍጥር ፡ ሲኾኑ ፡ ውስጠ ፡ ብዙኀት ፡ ባለው ፡ ነገር ፡ ይገባሉ ፤ ልክና ፡ ሚዛን ፡ ሲኾኑ ፡ ግን ፡ ውስጠ ፡ ብዙኀት ፡ አያሳዩም ። አምጣን ፡ የመጠን ፡ ብዝኅ ፡ ነው ፤ አምሳል ፡ የምስል ፡ ብዝኅ ፡ እንደ ፡ ኾነ ። አምጣንና ፡ አምሳል ፡ ላንድ ፡ መንገሩ ፡ በልማድ ፡ እንጂ ፡ በሰዋስው ፡ ሕግ ፡ አይደለም ፡ (ዕር፲፱ ፡ ቍ፸፪) ።

**ተመጠነ ፤** በቍሙ ፤ ተለካ ፡ ተመዘነ ፤ ከልክ ፡ ገባ ። ዘይትሜጠን ፡ በእመት ። ክቡደ ፡ ብዕሉ ፡ ዘኢይትሜጠን ፡ (ፍ ፡ ነ ፡ ፴፫ ። መጽ ፡ ምስ) ።

**ምጡን ፤ (ናን ፡ ናት ፡ ጥንት) ፤** የተመጠነ ፡ የተለካ ፤ ምጥን ፡ ልከኛ ፡ (መጽ ፡ ምስ) ።

**ምጣኔ ፤ (ገቢር ፡ ወተገ) ፤** መመጠን ፡ መለካት ፤ አመጣጠን ፡ አለካክ ፤ ምጠና ፡ ግምገማ ፤ ልክ ፡ መጠን ፡ ስፍር ፡ ቍጥር ፤ የወርድ ፡ የቁመት ፡ የስፋት ። ወእምነ ፡ ምጣኔ ፡ ልቡና ። አምጽአ ፡ ሥርዐተ ፡ ምጣኔ ፡ እምርሑቅ ። ሄሮድስ ፡ አስተናደፈ ፡ መሠረታቲሁ ፤ ኑኆ ፡ ወግድሞ ፡ በምጣኔ ፡ ቀዳማዊ ። ይሬስዩ ፡ ዐድሜ ፡ ወርኆሙ ፡ በምጣኔ ፡ ምሕዋረ ፡ ፀሓይ ፡ ውስተ ፡ አሐቲ ፡ ኖኅት ። ውፁኣን ፡ እምጣኔ ፡ (ፊልክ ፡ ፺ ። አፈ ፡ ድ፰ ። ዮሴፍ ። አቡሻ ፡ ፲፪ ። አዋል) ።

**መጠንጢን ፤** መጠንኛ ፤ ታናሽ ፡ ልክ ፡ መተንተኛ ፤ ወይም ፡ ጢንጦ ፡ የክፍል ፡ ክፍል ፡ ሚሶ ፡ ርቢት ፡ ዐምሾ ፡ ትሙን ፤ ይህን ፡ የመሰለ ፡ (ሄርማ) ።

**መጠቀ ፤ (መጢቅ ። ዐርገ ፡ ለዐለ ፤ ኖኀ) ፤** በቍሙ ፤ ምድር ፡ ለቀቀ ፡ ከምድር ፡ ራቀ ፤ ረዘመ ። ምድር ፡ መልቀቅ ፡ ያሞራ ፡ የወፍ ፤ መርዘም ፡ የሕንጻ ፡ የዛፍ ።

**መጠቀ ፤ (መዘገ ፤ መሠጠ) ፤** ነጠቀ ፡ መንጠቀ ፤ ከፍ ፡ አደረገ ፡ አነሣ ፤ ሳበ ፡ ጐተተ ፤ አዳኝ ፡ አወጣ ፤ ራሱን ፡ ወይም ፡ ሌላውን ። ምስጢሩ ፡ ከዚያው ፡ ከፊተኛው ፡ ይገባል ። ከመ ፡ ኢይረድ ፡ ታሕቲተ ፡ ምጥቅኒ ፡ ላዕለ ። እምግበ ፡ ሙስና ፡ ምጥቀኒ ፡ (ደራሲ) ። እግዚ ፡ መጠቀኒ ። ዘይመጥቃ ፡ ወያሌዕላ ። ይመጥቅ ፡ እምነ ፡ ዝንቱ ፡ መከራ ፡ (ዘፍ፴ ፡ ፰ ። ፫ነገ ፡ ፯ ፡ ፳፱ ። ማር ፡ ይሥ፲፪ ፡ ፪) ።

**መጣቂ ፤ መምጠቂ ፤ (ቂት ፡ ቅያን ፡ ያት) ፤** የሚነጥቅ ፤ ነጣቂ ።

**አምጠቀ ፤** አመጠቀ ፡ አረዘመ ፤ አስመጠቀ ፡ አስረዘመ ፤ ምጡቅ ፡ ረዥም ፡ አደረገ ፤ ወይም ፡ አስደረገ ። አብድ ፡ ሶበ ፡ የሐንጽ ፡ ቤቶ ፡ ያመጥቅ ፡ ሕንጻሁ ፡ እምእግዋሪሁ ፡ ከመ ፡ ይትመካሕ ፡ ላዕሌሆሙ ፡ (ፈላስ ፡ ገ፵፬) ።

**ተመጥቀ ፤** ተነጠቀ ፡ ተመነጠቀ ፤ ወደ ፡ ላይ ፡ ተሳበ ፤ ከፍ ፡ ከፍ ፡ አለ ። ዘተመጥቀ ፡ በደመና ፡ ሰማይ ፡ (ስንክ ፡ ጥቅ፲፪) ።

**ምጡቅ ፤ (ቃን ፡ ቃት ፡ ጥቅት) ፤** በቍሙ ፤ የመጠቀ ፡ ከምድር ፡ የራቀ ፤ ከፍተኛ ፡ ረዥም ፤ ሩቅ ፡ ረቂቅ ። እግዚ ፡ ዘዲበ ፡ ልዑል ፡ ወምጡቅ ፡ የኀድር ። መንበር ፡ ልዑል ፡ ወምጡቅ ። ሰማይ ፡ ምጡቅ ፤ ደመና ፡ ምጡቅ ። ምጡቃነ ፡ ስረት ፡ (ቄድር ። ቁር ። አዋል) ።

**ምጥቀት ፤** ምጡቅነት ፡ ርዝማን ፡ ርዝመት ፤ ዘለግታ ፡ ቁመት ።

**ምጥቅ ፤** ርቀት ፡ አራራቅ ፤ ልዕልና ፡ ከፍታ ። ምጥቆሙ ፡ ለአየራት ፡ (አርጋ) ።

**መምጠቅ ፤ (ቅት) ፤** ኵረጀ ፡ ቍናማት ፡ የግልገል ፡ ስልቻ ፤ ወይም ፡ ከነት ፡ ከቈርበት ፡ የሚሠራ ፡ የረኞች ፡ ኰረዳ ፤ ወንጭፍና ፡ ደንጊያ ፡ ሌላም ፡ ነገር ፡ የሚከቱበት ። ኀረየ ፡ ኃምስተ ፡ አእባነ ፡ እምውስተ ፡ ፈለግ ፡ ወወደየ ፡ ውስተ ፡ መምጠቂሁ ፡ (፩ነገ ፡ ፲፯ ፡ ፵) ።

**መጠቀ ፤—ጣፈጠ ፡ ጥፍጥ ፡ ኾነ ፤—መተቀ ።**

**መጠራ ፤ (ዕብ ፡ ማጣራ) ፤** ማንጠሪያ ፡ ማንጣጠሪያ ፡ የቀስተኛና ፡ የነፍጠኛ ፡ ዐላማ ፡ ወይም ፡ ይላማ ፤ ፍላጻው ፡ ዐረሩ ፡ ሲነድፍ ፡ ሲተኰስ ፡ የሚያርፍበት ፤ እንደ ፡ ጊጤ ፡ ያለ ፡ በሩቅ ፡ በአንጻር ፡ ፊት ፡ ለፊት ፡ የቆመ ፡ የተተከለ ። ባለብሉዮች ፡ ግን ፡ ለይተው ፡ ትክሻ ፡ ብራኳ ፡ መጋፊያ ፡ ይሉታል ። እነድፍ ፡ አሕጻ ፡ ኀበ ፡ መጠራ ፡ (፩ነገ ፡ ፳ ፡ ፳ ። ሰቈ፫ ፡ ፲፪ ። ኢዮ፲፯ ፡ ፲፪) ።


መጠራ ።



ዕጕትማር ፡

**ዕግተት ፤** መክበብ ፤ መከበብ ፤ አከባበብ ፤ ከበባ ። ወሶበ ፡ ጸንዐ ፡ ላዕሌሆሙ ፡ ዕግተት ፡ ወፀኡ ፡ በሌሊት ። ሰእመ ፡ አእመረ ፡ ገብር ፡ ዕግተተ ፡ በእንተ ፡ ሀዩደተ ፡ እግዝእቱ ፡ ወኢረድኣ ፡ ያውዕይዎ ፡ (ዮሴፍ ። ፍ ፡ ነ ፡ ፵፰) ።

**ዐድ ፤ (ዕብራ) ፤** ዘልፈ ፤ ለዓለም ፤ ፍጻሜ ፡ የሌለው ፡ ጊዜ ፡ ዘመን ። ይነግሥ ፡ እግዚ ፡ ለዓለመ ፡ ዓለም ፡ ወዐድ ። አንዳንድ ፡ መጽሐፍ ፡ ግን ፡ ወዓዲ ፡ ይላል ፤ ስሕተት ፡ ነው ፡ (ዘፀ፲፭ ፡ ፲፰) ።

**ዓዲ ፤—ዳግመኛ ፤—ዐድይ ፡ ዐደየ ።**

**ዕዳ ፤—በቁሙ ፤—ዐድይ ፡ ዐደየ ።**

**ዕድ ፤—እጅ ፤—አዲው ፡ አደወ ።**

**ዕድ ፤—ወንድ ፤—ዐዲው ፡ ዐደወ ፤**

**ዐዲድ ፤ (ዐደ ፤ ዐደደ ፡ የዐድድ ፡ ይዕድድ ። ዐረ ፡ ዐደ ፤ ቈጠረ) ፤** ማራቅ ፡ ማሶገድ ፡ ማዋረድ ፤ በፊትና ፡ በቀኝ ፡ የነበረውን ፡ ወደ ፡ ጐን ፡ ወደ ፡ ኋላ ፡ ወደ ፡ ግራ ፡ ማድረግ ። ብርሃን ፡ ዘዐ(ሰ)ደዶ ፡ ለጽልመት ፡ (ቅዳ ፡ ዮሐ) ። ያዐደደ ፡ ፍች ፡ ስለ ፡ ታጣ ፡ ዐደደ ፡ ወደ ፡ ሰደደ ፡ ተለውጧል ፤ ይህን ፡ የመሰለ ፡ ብዙ ፡ አለ ።

**ዕደድ ፤** ኅሳር ፡ ውርደት ፤ ጕስቍልና ፡ ኀዴት ። ለውእቱ ፡ ብእሲ ፡ እንተ ፡ አፍቀረ ፡ ዕደደ ፤ እምኅየሶ ፡ ሶበ ፡ ኢተወልደ ፤ ያግብእከ ፡ ጊዜ ፡ ፈቀደ ፡ (ደራሲ) ። ብዙው ፡ መጣፍ ፡ ግን ፡ በዕደድ ፡ ፈንታ ፡ እበድ ፡ ይላል ፤ የተሳሳተ ፡ ነው ። ዐደዳ ፡ ዲደን ፡ ማለት ፡ ከዚህ ፡ ወጥቷል ፤ ዐደዳ ፡ ንዝንዝ ፡ ውዝግብ ፡ ጭቅጭቅ ፤ ዲደን ፡ ኀይለኛ ፡ ነፋስ ፡ ነው ።

**ዐዲው ፤ ዎት ፤ (ዐደወ ፡ የዐዱ ፡ ይዕዱ ። ዕብ ፡ ዐዳህ ። ሱር ፡ ዐዳእ ። ዐረ ፡ ዐደአ) ፤** መሻገር ፤ ማለፍ ፤ መዝለል ፡ መራመድ ፤ ዐልፎ ፡ ዘሎ ፡ ተራምዶ ፡ መኼድ ። መብዛት ፡ መትረፍ ፤ ከልክ ፡ ማለፍ ፤ መተላለፍ ። እመኒ ፡ ዐዶከ ፡ ማየ ። ዐድዊ ፡ ፈለገ ። ዐደወ ፡ እሞት ፡ ውስተ ፡ ሕይወት ። ወዐዲዎን ፡ እምተዓይን ። እስከ ፡ ዐደዉ ፡ እምደማስቆ ። ዘብዙኅ ፡ እመስፈርት ፡ የዐዱ ፡ (ኢሳ፵፫ ፡ ፪ ። ፵፯ ፡ ፪ ። ዮሐ፭ ፡ ፳፬ ። ዮዲ፲፫ ፡ ፲ ። ፲፭ ፡ ፭ ። ስንክ ፡ መስ፳፰) ። በዐደወ ፡ ፈንታ ፡ ተዐደወ ፡ ይላል ፤ አድራጊውን ፡ በተደራጊ ፤ የስሕተት ፡ መንገድ ፡ ነው ፤ አያሰኝም ። እትዐደዋ ፡ ለአረፍት ። ዘይትዐዶ ፡ ወሰነ ። ድንጊ ፡ ወንትዐዶኪ ። ጸሎተ ፡ ነዳይ ፡ ትትዐዶ ፡ እምደመና ። ኢትዐደዊ ፡ እምወሰንኪ ፡ (መዝ ፡ ፲፯ ። ሆሴ፭ ፡ ፲ ። ኢሳ፶፩ ፡ ፳፫ ። ሢራ፴፫ ፡ ፳፭ ። ቅዳ) ። ቃዕደወንና ፡ አንቃዕደወን ፡ እይ ፤ የዚህ ፡ ዘር ፡ ነው ፤ ስንቀወ ፡ የንቀወ ፡ ዘር ፡ እንደ ፡ ኾነ ።

**ዐዳዊ ፤ (ዊት ፡ ውያን ፡ ያት) ፤** የሚሻገር ፤ ተሻጋሪ ፤ ዐላፊ ፡ ተላላፊ ። በዐዳዊ ፡ ፈንታ ፡ ተዐዳዊ ፡ ይላል ፤ ተ ፡ ያማርኛ ፡ ነው ፤ የግእዝ ፡ አይደለም ። ተዐዳዌ ፡ ትእዛዝ ። ተዐዳዌ ፡ ሕግ ። ተዐዳዊተ ፡ ሕግ ፡ (መቃ ። ጥበ፫ ፡ ፲፯ ። ፍ ፡ ነ ፡ ፳፱ ፡ ፭) ።

**ምዕዳው ፤ (ዋት) ፤** መሻገሪያ ፤ ሜዳ ፡ መልክ ፤ ድልድይ ፤ ታንኳ ። ሕልብየ ፡ ምዕዳው ፡ ዘእንበለ ፡ በተንከተመ ፡ ሃይማኖት ። ማርያም ፡ ምዕዳው ፡ እምሠርም ፤ ዘጽድቅ ፡ ተንከተም ፡ (መጽ ፡ ምስ ። ደራሲ) ።

**አዕደወ ፤** አሻገረ ፤ አሳለፈ ። አዕድዎ ፡ አዕደዎሙ ፡ ገብርከ ። አዕደዎቶሙ ፡ ባሕረ ፡ መፍርሀ ። ወአዕደወኒ ፡ ውስተ ፡ ማይ ፡ (ኢያ፯ ፡ ፯ ። ጥበ፲ ፡ ፲፰ ። ሕዝ፵፯ ፡ ፫) ።

**ማዕዶ ፤ ማዕዶት) ፤** ማዶ ፤ አሻገር ፡ ከወንዝ ፡ ወዲያ ፡ ወይም ፡ ወዲህ ፡ ያለ ፡ ቦታ ፤ ትይዩ ፡ አንጻር ፤ ፊት ፡ ለፊት ፤ አቅጣጫ ፡ አፍዛዥ ። የፋሲካ ፡ ስም ። ማዕዶተ ፡ ዮርዳኖስ ። ነገሥት ፡ እለ ፡ ማዕዶተ ፡ ባሕር ። ወበጺሖ ፡ ማዕዶተ ። ዋዜማ ፡ ዘማዕዶት ፡ (ኢሳ፰ ፡ ፳፫ ። ኤር፴፪ ፡ ፳ ። ማቴ፰ ፡ ፳፰ ። ድጓ) ።

**መዓድው ፤** ማዶዎች ፤ አሻገሮች ፤ ወንዝና ፡ ባሕር ፡ የለያቸው ፤ የከፈላቸው ።

**ተዐድወ ፤** ታለፈ ፤ ተዘለለ ፤ ወንዙ ፡ ሕጉ ፡ ትእዛዙ ።

**ዕድው ፤ (ዋን ፡ ዋት ፡ ዱት) ፤** የታለፈ ፡ የተዘለለ ፤ ሌሎች ፡ ያለፉት ፤ የተሻገሩት ።

**ዕድው ፤** ያለፈ ፤ የተሻገረ ፤ ወንዝን ፡ ሕግን ፡ ዐልፎ ፡ ተሻግሮ ፡ የኼደ ።

**ዕድው ፤ (ጥሬ ። ዐረ ፡ ዐዱው) ፤** ወደረኛ ፤ ባለጋራ ፤ ደመኛ ፤ ጠላት ። ይከውነከ ፡ ዕድወ ። ዘኢከነ ፡ ምስሌየ ፡ ዕድውየ ፡ ውእቱ ። ሰእመ ፡ ረከብኩ ፡ ዕድዋኒሃ ፡ ለሃይማኖት ። ዕድዋኒነ ፡ (ሢራ፮ ፡ ፲፪ ። ማቴ፲፪ ፡ ፴ ። ተረ ፡ ኤር ። ቈር) ።

**ዕድወት ፤** መሻገር ፤ ማለፍ ፤ መታለፍ ፤ መተላለፍ ፤ ዕልፈት ፡ ዐለፈታ ፤ እልፍ ፡ ትርፍ ። ዕድወተ ፡ ቀዳማይ ፡ ብእሲ ፤ ዕድወቱ ፡ ለአዳም ፡ (ቄር ፡ ጸላ) ።

**ዕድ ፤ (ብ ፡ ዕደው) ፤** ወንድ ፡ ተባት ፤ ብእሲ ። ዕድ ፡ ወአንስት ። ዕደው ፡ ጠቢባን ። ዕደወ ፡ ስም ፡ (ቅዳ ። ሢራ፴፮ ፡ ፳፰ ። ዘፍ፮ ፡ ፬) ።

**ዕዳው ፤ (ዋት) ፤** መንታ ፡ መንገድ ፤ ምስቅል ፡ መንገድ ። ኀበ ፡ ዕዳዎት ፡ (ማር፲፩ ፡ ፬) ።

**ተዓደወ ፤ (ተደራራጊ) ፤** ተሸጋገረ ፤ ተላለፈ ፤ ርስ ፡ በርሱ ።

**አስተዓደወ**፤ አሸጋገረ፤ አስተላለፈ።

**ምስትዕዳው**፤ መሸጋገሪያ፡ መተላለፊያ፤ ማሸጋገሪያ፡ ማስተላለፊያ።

**ዕዳው፤—ጕድፍ፤—አዲው፡ አደወ።**

**ዐድይ፤ዮት፤(ዐደየ፡ የዐዲ፡ ይዕዲ። ዐረ፡ ዐደይ)**፤ መክፈል፤ ብድርን፡ መመለስ፤ የክፉ፡ የበጎ።

**ዐዳዪ፤ (ዪት፡ ይያን፡ ያት)**፤የሚከፍል፤ ከፋይ።

**ዕዳ**፤ በቁሙ፤ ብድር፤ ልቅ፤የብድር፡ ገንዘብ። ኀደገ፡ ሎቱ፡ ዕዳሁ። ለመኑ፡ እፈዲ፡ ዕዳ። አግብአ፡ አኀዘ፡ ዕዳሁ። ንቅንዮ፡ ለነዳይ፡ በዕዳነ፡ (ማቴ፲፰፡ ፳፯። ኢሳ፶፡ ፮። ሕዝ፲፰፡ ፯። ዓሞ፰፡ ፮)።

**ዕዳ**፤ በደል፤ኀጢአት፡ ክፋት፤ መቀጮ፡ ቅጣት። አልቦ፡ ላዕሌሁ፡ ዕዳ። ዳእሙ፡ ይጸንዕ፡ ዕዳሃ፡ ለዘቲ፡ ኀጢአት። ሶበ፡ ኢስተይክሙ፡ ዝናመ፡ ትምህርት፡ እምኢኮነክሙ፡ ዕዳ፡ (ፈ፡ መ፡ ፳፱፡ ፬ና፡ ፲፫። አፈ፡ ድ፲)።

**ዕዳዊ**፤ ባለዳ፤ አበዳሪ፤ ወይም፡ ተበዳሪ። ነገረ፡ ዕዳውያን፡ (ፍ፡ ነ፡ ፳፯)።

**ዐደይ፤ (ትግ፡ ሐበ)**፤ ሹጥ፡ የሆድ፡ ትል፤ ኮሶ፡ የሚባል። በቁሙ፡ ብሟቴ፡ አበባ። (ግጥም)፤ ዐደይ፡ ዐደይ፡ የመስከረም፤ ሱስንዮስ፡ ንጉሠ፡ ሮም።

**ዓዲ፤ (ዕብ፡ ዖድ)**፤ ንኡስ፡ አገባብ፤ ገና፤ ደግሞ፤ ዳግመኛ፤ አኹን፤ እንጂ፤ ዋዌ፡ ም፡ ይኾናል። እንጂ፡ ም፡ ሲኾን፡ ዐቢይ፡ አገባብ፡ ነው፤ ዳግመኛነቱን፡ ግን፡ አይለቅም። ዓዲ፡ ኢበጽሐ፡ ጊዜሁ። ተዐገሡ፡ ዓዲ፡ ኅሙስ፡ መዋዕለ። እስከ፡ ዓዲሁ። ዓዲ፡ ሊተኒ፡ (ዮሐ፯፡ ፰። ዮዲ፰፡ ፴። አፈ፡ ድ፬። ፊልጵ፪፡ ፳፯)። ዓዲየ፤ከ፡ ኪ፡ ሁ፡ ሃ፤ዓዲነ፡ እያለ፡ እስካሥር፡ ይዘረዝራል። ዋዌ፡ ሲኾን፤ ሄሮድስ፡ ወጲላጦስ፡ ተንሥኡ፡ ቅድመ፡ እንበለ፡ ፍትሕ፡ ላዕለ፡ አቡሁ፡ ቀባዒ፡ ወላዕለ፡ ወልዱ፡ ቅቡዕ፤ከማሆሙ፡ ዓዲ፡ ተንሥኡ፡ በግፍዕ። ዓዲ፡ ኢታንክርዋ፡ ለዘትመጽእ፡ ኀቤነ፤ መከራ፡ ዘሃይማኖት፡ እስመ፡ ፍዳ፡ ዕሴት፡ አንዊነ፡ (ቅኔ)። (ዕር፲፱፡ ቍ፹፪)።

**ዓዶት፤ (ትግ፡ ሐበ። ዕብ፡ ዳት)**፤ ሕግ፡ ሥርዐት፤ የአበው፡ ትውፊት፤ ልማደ፡ ሀገር፡ (ማር፯፡ ፫)። ሐማሴኖች፡ እናቴ፡ ሲሉ፡ ዓደይ፤ ጋሎችም፡ ዓደቶ፡ የሚሉት፡ ከዚህ፡ ይስማማል።

**ዐደለ**፤ በቁሙ፤ ሰጠ፡ አሳለፈ፡ (ዐማርኛ)። ከፈለን፡ ተመልከት።

**ዐድል፤(ዐረ፡ ፍርድ። ዕብ፡ ኵቶኔት)**፤ ኪታ፤ ጥብቆ፤ ለስላሳ፡ የውስጥ፡ ልብስ፤ ዐጭር፡ የገላ፡ ቀሚስ፤ ኰታ፡ መጐናጠፊያ፤ ልግም፡ በገላ፤ የክት፡ ሸማ፤ ኮት፤ ጀባ፡ ካባ፤ የሚደረብ።

**አዕዳል፤ (ዕብ፡ ካትኖት። ጽር፡ ኺቶኔስ)**፤ ኪቶች፤ ቀሚሶች፤ ኮቶች፤ ኰታዎች። ወገብረ፡ ሎሙ፡ አዕዳለ፡ ማእስ፤ ወአልበሶሙ፡ (ዘፍ፫፡ ፳፩)። ማእስ፡ የሚያሞቅ፡ የሚለሰልስ፤ ጠጕራም፡ የደበሎ፡ ቀሚስ፡ ማለት፡ ነው፤ ትርጓሜ፡ ኦሪት፡ የጥንቸል፡ ቈርበት፡ ነው፡ ይላል። አልበሶሙ፡ ማለት፤ ልብሱ፡ ሳይቀር፡ ፍርዱንም፡ ያሳያል፤ ፍርድ፡ ልበስ፡ እንዲሉ።

**ዐደመ፤—ቀላ፡ አማረ፤—አዲም፡ አደመ።**

(ጥ) **ዐድሞ፤ሞት፤(ዐደመ፡ ይዔድም፡ የዐድም። ዐረ፡ ዐደ። ዕብ፡ ያዓድ)**፤ ማደም፤ መቅጠር፤ ጊዜ፡ መወሰን፤ ቀን፡ መስጠት፤ ለሰርግ፡ ለጉባኤ፤ ለኹሉ። ሰብዓ፡ ሰንበታተ፡ ዐድሞሙ፡ ለሕዝብከ። አኮኑ፡ ዐደምኩ፡ ዕድሜ። ወአስተብቍዖ፡ ከመ፡ የዐድሞ፡ እስከ፡ ሠሉስ፡ ዕለት። እዔድመክሙ፡ ኅዳጠ፡ መዋዕለ፡ (ዳን፱፡ ፳፬። ፯፡ ፲፪። ፪፡ ፲፮። ታሪ)።

**ተዐደመ**፤ ታደመ፤ ተቀጠረ፤ ተወሰነ። በመዋዕል፡ ዘተዐደመ። ዐስብ፡ ዘተዐደመት፡ (ፍ፡ ነ፡ ፳፱፡ ፪። ፴፮)።

**ዕዱም፤(ማን፡ ማት፡ ድምት)**፤የታደመ፤ የተቀጠረ፤ ዕድመኛ።

**ዕድሜ፤(ያት)**፤ በቁሙ፤ ቀጠሮ፤ የተወሰነ፡ ጊዜ፤ ዘመን፡ ወራት፤ የሳምንት፡ የወር፡ ያመት፡ በዓል። ሄሮድያኖስ፡ የአምር፡ ዕድሜሁ። ኢንልቀ፡ ዕድሜሁ፡ ለራእይ። ዕድሜ፡ ሐዘን። በበዓላት፡ ወበዕድሜያት፡ (ኤር፰፡ ፯። ዳን፰፡ ፲፱። ፍ፡ ነ፡ ፳፱፡ ፪። ሕዝ፵፮፡ ፲፩)።

**ተዓደመ**፤ ተቃጠረ፤ ተቀጣጠረ፤ ተዋዋለ፤ ተስማማ። ተዓደሙ፡ እስከ፡ ሠርቀ፡ ወርኅ፤ ይግበሩ፡ ከመ፡ ዝ። በከመ፡ ተደመርከ፡ ወተዓደምከ፡ ምስለ፡ አካዝያስ፡ (፩ዕዝ፡ ፱፡ ፲፯። ፪ዜና፡ ፳፡ ፴፯)።

**ዐደነ**፤ በቁሙ፤ ሻ፡ ፈለገ፡ (ዐማርኛ)።

**ዔዴን፤ (ዕብራ)**፤ ምቹ፡ ቦታ፤ ወፍራም፡ ሥብ፡ መሬት፤ አሻል፡ ፋልማ። ከቦታው፡ የሚገኝ፡ ፍጹም፡ ተድላ፤ ጣዕም፡ ሥን፡ መዐዛ፤ ቈጽል፡ ልምላሜ። ወተከለ፡ እግዚ፡ አምላክ፡ ገነተ፡ በዔዴን፡ እምቅድም፤ ወሤሞ፡ ህየ፡ ለአዳም፡ ዘለሐኮ፡ (ዘፍ፪፡ ፰)። አንዳንድ፡ መጽሐፍ፡ ኤድም፡ ኤደም፡ ይላል፤ የተሳሳተ፡ ነው። ኤደምን፡ ተመልከት። ባለብሉዮች፡ ግን፡ ምሥራቅ፡ ይሉታል። ምሥራቅ፡ የሚባል፡ ቅድም፡ ነው፡ እንጂ፡ ዔዴን፡ አይደለም።

**ዐሀ፤—አዩ፤—አሀ።**

**ዓው**፤ ጭን፤ የጭን፡ ራስ፤ መብቀያው፤ ከሆድ፡ ጋራ፡ የተያያዘው፤ ማጠፊያው፡ ማውዱ። ሥርው፡ ዘሀሎ፡ ውስተ፡ ዓወ፡ እግሩ፡ (ዘፍ፴፪፡ ፴፪)።

**ዐዊግ፤ጎት፤(ዖገ፡ የዐውግ፡ ይዑግ። ዐረ፡ ዐዊገ)**፤ መጥመም፤ መጕበጥ፤ መወላገድ፤ ጠማማ፡ ቈልማማ፤ ዐንካሳ፡ ወንካራ፤ ጠንባሳ፡ ሸውራራ፡ መኾን፤ አለመተካከል፤ የሕዋስ።

**ተዐወገ፤(ይትዔወግ)**፤አላገጠ፤አለመጠ፤ ተማለቀ፤አፉን፡ ከንፈሩን፡ በማጣመም፤ ዐይኑን፡ በማ

ጨንቈር ፡ በማሳወር ፤ ይህን ፡ በመሰለ ፡ ነገር ። ወተዐዊ ኆሙ ፡ አይሁድ ፡ በክርስቶስ ። ተዐዊኆሙ ፡ ይነግሩ ፡ (ቄር ፡ እስት ። ጳላ) ።

**ዖገ** ፤ (**ዕብ ፡ ዓግ ፡ ያዑግ**) ፤ ጋገረ ፤ ዐነኰተ ፤ ክብ ፡ አደረገ ፤ የሊጡን ፡ ቅርጥ ።

**ተዐውገ** ፤ ተጋገረ ፤ ተነኰተ ፤ ተጠቤተ ።

**ዑጋት** ፤ ዕንኰቻ ፤ ሥሥ ፤ ክብ ፤ የጣቢታ ፡ ዐይነት ። ዑጋተ ፡ ሰገም ፡ (ሕዝ፬ ፡ ፲፪) ።

**ዐዊድ** ፤ **ዶት** ፤ (**ዖደ ፡ የዐውድ ፡ ይዑድ ። ዕብ ፡ ዒዌድ ። ዐረ ፡ ዓደ**) ፤ መዞር ፤ መሽከርከር ፤ መገላበጥ ፤ ለራሱ ። ማወድ ፤ በዙሪያ ፡ መኼድ ፤ መመላለስ ፤ ማጠር ፡ መከበብ ፤ ዙሮ ፡ መግጠም ። አገር ፡ ላገር ፡ መንደር ፡ ለመንደር ፡ መዞር ፤ ለማየት ፤ ለመስማት ፤ የሹትን ፡ ለማግኘት ። ማወጅ ፤ እየዞሩ ፡ መልፈፍ ፤ ዐዋጅ ፡ መንገር ፤ ስማ ፡ ስማ ፡ ማለት ። ባዩት ፡ በሰሙት ፡ ምስክር ፡ መኾን ፤ ተጠርቶ ፡ መመስከር ፤ ወይም ፡ ታሪክ ፡ ጥፎ ፡ ማኖር ። ከመ ፡ መንኮክት ፡ እንተ ፡ ተዐውድ ። ወለለ ፡ ዖድዎ ፡ ለውእቱ ፡ መንበር ። ከመ ፡ ቀስተ ፡ ደመና ፡ የዐውዶ ፡ ሡራኄ ። ዖድኩ ፡ እንዘ ፡ እኄሥሣ ። ዖደ ፡ ዐዋዲ ። የዐውድ ፡ ይንግር ፡ ለከ ፡ ዘወሀበከ ፡ (ሚራ፳፯ ፡ ፭ ። መክ፳፯ ፡ ፲፬ ። ቅዳ ። ሳታ ። ጥበ፰ ፡ ፲፰ ። መክ፯ ፡ ፳፭ ። ዘፍ፵፩ ፡ ፵፫ ። ሚራ፰ ፡ ፲፭) ።

**ዐዋዲ** ፤ (**ዲት ፡ ድያን ፡ ያት**) ፤ የሚዞር ፡ ዘዋሪ ፤ ለፋፊ ፡ ዐዋጅ ፡ ነጋሪ ። ብእሲት ፡ ዐዋዲት ፡ ዘኢትከይድን ፡ ኀፍረታ ። ቃለ ፡ ዐዋዲ ። ሐዋርያ ፡ ወዐዋዲ ፡ (ፈላስ ። ዮሐ፭ ፡ ፳፫ ። ፩ጢሞ ፡ ፪ ፡ ፯) ።

**ዐዋድ** ፤ ዐዋጅ ፤ ለሕዝብ ፡ የሚነገር ፡ የንጉሥ ፡ ሕግና ፡ ደንብ ፡ ውሳኔ ። መጽሐፍ ፡ ግን ፡ በዐዋድ ፡ ፈንታ ፡ ዐዋጅ ፡ ይላል ። ወአንገረ ፡ ዐዋጀ ፡ (ታሪ ፡ ነገ) ።

**አዖደ** ፤ አዞረ ፤ አሳወደ ፤ ዐዋጅ ፡ አስነገረ ። ያዐውድ ፡ መንኰራኵሪሁ ። ከመ ፡ ያዑድ ፡ ዐዋዴ ፡ ቅድሜሁ ። አዖደ ፡ ውስተ ፡ መርሕበ ፡ ሀገር ፡ (ሚራ፴፰ ፡ ፳፱ ። ዮሴፍ ። አስቴ፯ ፡ ፲፭) ።

**ተዐውደ** ፤ ታወደ ፤ ተዞረ ፤ ዐዋጅ ፡ ተነገረ ። በዖደ ፡ ፈንታ ፡ ተዐውደ ፡ ይላል ፤ የተሳሳተ ፡ ነው ። አከኑ ፡ ፍጡነ ፡ ይረውጽ ፡ ፀሓይ ፤ ተዐዊዶ ፡ ሰማየ ፡ (፭ዕዝ ፡ ፬ ፡ ፴፬) ።

**ዕዉድ** ፤ **ዕውድ** ፤ የታወደ ፤ የተከበበ ፤ ክብ ፤ የታሰረ ፡ የተጠመጠመ ፤ ጥምጥም ። ጽጌ ፡ ደንጐላ ፡ ዘዕዉድ ፡ በአሥዋክ ። ይኩን ፡ ቀሚስ ፡ ስፉየ ፡ ወዕዉደ ፤ መዝርዐ ፡ ቀሚስ ፡ ይኩኑ ፡ ዕውዳነ ። ፈቃድ ፡ ዕውድ ፡ በምግባር ። ዕውድ ፡ በሜላት ፡ ውስተ ፡ አሕባለ ፡ ቢሶስ ፡ (አዋል ። ፈ ፡ መ ፡ ፴፭ ፡ ፭ ። አፈ ፡ ተ፲፯ ። አስቴ፩ ፡ ፮) ።

**ዑደት** ፤ (**ታት**) ፤ በቁሙ ፤ መዞር ፤ አዟዟር ፤ ዙረት ። ዑደተ ፡ ሆሳዕና ። ዑደተ ፡ ፀሓይ ። ዘእንበለ ፡ ይግበር ፡ ዑደታተ ፡ ከዋክብት ፡ ለአዝማን ፡ (ቅዳ ። አቡሻ ፡ ፴፯ ። መቃ) ። በዑደት ፡ ፈንታ ፡ ዕዋዴ ፡ ይላል ፤ አንድ ፡ ነው ። ሶበ ፡ ፈጸመ ፡ ዕዋዴሁ ፡ (አቡሻ ፡ ፲፫) ።

**ዐውድ** ፤ ዙሪያ ፤ ክበብ ፤ ከበር ፡ እስከ ፡ በር ፤ ከመት ፡ እስከመት ፡ ያለ ። ለታጠረ ፡ ለተወሰነ ፡ ክበብ ፡ ላለው ፡ ኹሉ ፡ ይነገራል ። ወበዐውዱ ፡ ለውእቱ ፡ መንበር ። ይቀውሙ ፡ ዐውዶ ። ዐውደ ፡ ፀሓይ ፤ ዐውደ ፡ ወርኅ ። ዐውደ ፡ ዓመት ፡ (ራእ፬ ፡ ፬ ። ኢሳ፯ ፡ ፪ ። አቡሻ ፡ ፳፫ ። ድጓ) ።

**ዐውደ ፡ አበቅቴ** ፤ ፲፱ ፡ ዓመት ፤ በዚህ ፡ ጨረቃና ፡ ፀሓይ ፡ መንገዳቸውን ፡ እየፈጸሙ ፡ ተራክበ ፡ ያደርጉበታል ።

**ዐውደ ፡ ወርኅ** ፤ ሠላሳ ፡ ቀን ፤ ከ(ልደታ)መባቻ ፡ እስከ ፡ መባቻ ።

**ዐውደ ፡ ወርኅ** ፤ የጨረቃ ፡ ዐውዳመት ፡ ፫፻፶፬ ፡ ቀን ።

**ዐውደ ፡ ማኅተም** ፤ ፹፬ ፡ ዓመት ። ማኅተምን ፡ ተመልከት ።

**ዐውደ ፡ ነገሥት** ፤ የጥንቈላ ፡ መጽሐፍ ፤ ፲፬ ፡ ክብ ፡ ሰንጠረዥ ፡ ያለው ፤ ያቡሻህርና ፡ የመርሐ ፡ ዕዉር ፡ ወደረኛ ። በየሰንጠረዡ ፡ ፲፬ ፡ ነገር ፡ አለበት ፤ ትምርቱን ፡ ግን ፡ ከጥቂት ፡ ሰዎች ፡ በቀር ፡ ኹሉ ፡ አያውቀውም ፤ መጣፉም ፡ በጠንቋይ ፡ ኹሉ ፡ ዘንድ ፡ አይገኝም ።

**ዐውደ ፡ ዕለት** ፤ ሰባት ፡ ቀን ፤ ከእሑድ ፡ እስከ ፡ ቀዳም ።

**ዐውደ ፡ ዓመት** ፤ የፀሓይ ፡ ዐውዳመት ፤ ፫፻፷፭ ፡ ዕለት ፤ ከሩብ ።

**ዐውደ ፡ ፀሓይ** ፤ ፳፰ ፡ ዓመት ፤ በዚህ ፡ ዕለት ፡ ወንጌላዊ ፡ ይገናኙበታል ፤ ዕለቱ ፡ ረቡዕ ፤ ወንጌላዊው ፡ ማቴዎስ ።

**ዐውደ ፡ ቀመር** ፤ ፭፻፴፪ ፡ ዓመት ፤ በዚህ ፡ ዕለት ፡ ወንጌላዊ ፡ አበቅቴ ፡ ይገናኙበታል ፤ ዕለቱ ፡ ሠሉስ ፤ ወንጌላዊው ፡ ማቴዎስ ፤ አበቅቴው ፡ አልቦ ፡ ነው ። ይህ ፡ ኹሉ ፡ ቃል ፡ የመርሐ ፡ ዕዉር ፡ ነው ።

**ዐውድ** ፤ ዐውድማ ፤ ሸንጎ ፤ ጉባኤ ፤ አደባባይ ። ዐውደ ፡ እክል ። ዐውደ ፡ ማእረር ። አምጽእዎ ፡ ኀበ ፡ ዐውድ ። ንጉሥት ፡ ዐውደ ፡ (ሩትር ፡ ፪ ። ዳን፪ ፡ ፴፭ ። ግብ፲፰ ፡ ፲፪ ። ፲፱ ፡ ፴፱) ።

**አዕዋድ** ፤ (**ዳት**) ፤ ዙሪያዎች ፤ ዐውድሞች ፤ ሸንጎዎች ። አውራጆች ፤ ቀበሌዎች ። ያገብኡክሙ ፡ ውስተ ፡ አዕዋድ ። ነቢረ ፡ ፍጽም ፡ በውስተ ፡ አዕዋዳት ። ምኔታት ፡ ዘአዕዋደ ፡ እለእስክንድርያ ፡ (ማቴ ፲ ፡ ፲፯ ። ፳፫ ፡ ፯ ። ፊልክ ፡ ፲፰) ።

**ምዕዋድ** ፤ (**ዳት**) ፤ ዝኒ ፡ ከማሁ ፤ ዙሪያ ፡ ክበብ ። መክበቢያ ፤ መከበቢያ ፤ መዞሪያ ፡ ማወጃ ፡ በታ ፤ ወይም ፡ መዝሙር ፡ እያወዱ ፡ የሚዘምሩት ። ምዕዋደ ፡ ቅጽራ ፡ እምአንቀጽ ፡ ለአንቀጽ ። ሠናይ ፡ ምዕዋደ ፡ ቀስት ። ወአዖደኒ ፡ ውስቴቶሙ ፡ ምዕዋዳተ ። መዝ

ሙር ፡ ዘምዕዋድ ፡ (ዮናፎ ፡ ፫ ። ጥበ፳ ፡ ፳፪ ። ሕዝ፴፯ ፡ ፪ ። ድጓ) ።

**ዑድ** ፤ (ዐረብ) ፤ የሬት ፡ ዕንጨት ፤ ሽታው ፡ የሚያውድ ፤ ከሩቅ ፡ የሚሸት ። ቀናንሞስ ፡ ወሰሊኖት ፡ ወዑድ ፡ (ዲድ ፡ ፳፭ ። መጽ ፡ አዳር ፡ ፭ ፡ ፯) ። ዐልውን ፡ ተመልከት ።

**ዑድር** ፤ (ዐረብ) ፤ ምክንያት ፤ ሰበብ ፤ ሐሳብ ፤ የነገር ፡ ማፍረሻ ፤ ራስን ፡ ከበደል ፡ ለማንጻት ። ነገሮ ፡ ዑድሮ ፡ ወተወክፎ ፡ ፍምፍምዮስ ። አልብክሙ ፡ ዑድር ። ኢሊተ ፡ ዑድር ፡ ለሕይወትክሙ ፡ (ዮሴፍ) ።

**ዐውየወ** ፤ (ዐረ ፡ ዐወይ ። ሱር ፡ ዐዋአ) ፤ ጮኸ ፤ ቡታ ፡ ሰደደ ፤ ዋይ ፡ ዋይ ፡ አለ ። ዐውየወ ፡ በሕቁ ። የዐወይዉ ፡ እምብዝኅ ፡ መስተዐግላን ። ወዐውየወት ፡ በሕማማ ። አንዘኩ ፡ እብኪ ፡ ወአዐውዩ ፡ (ዮዲ፲፪ ፡ ፲፯ ። ኢዮ፴፭ ፡ ፱ ። ኢሳ፳፯ ፡ ፲፯ ። ሔኖ፹፱ ፡ ፳፱) ።

**አዐውየወ** ፤ አስጮኸ ፤ አስጨነቀ ፤ አስለቀሰ ። እንዘ ፡ ታገዕሩ ፡ ወታዐወይዉ ፡ ነዳየ ፡ (ኢሳ፶፰ ፡ ፱) ።

**ዐውያ** ፤ (ያት) ፤ ጩኸት ፤ ቡታ ፡ እሪታ ፤ ልቅሶ ፡ ዋይታ ። ጊዜ ፡ ዐውያከ ። ዐውያተ ፡ ነዳያን ። ዐውየወት ፡ ዐውያተ ፡ ዐቢይተ ፡ (ኢሳ፶፰ ፡ ፱ ። ኢዮ፴፱ ፡ ፳፰ ። ሔኖ፹፭ ፡ ፮) ።

**ዐዌት** ፤ (ትግሬ) ፤ ድል ፤ አሸናፊነት ፤ አስጨኺነት ።

**ዐውከከ** ፤—አስጨነቀ ፤—ወከከ ፤ አውከከ ።

**ዐውሎ** ፤ (ታት ። ሱር ፡ ዑላታአ ፤ ዐላታአ ። ዕብ ፡ ዐልዖል) ፤ በቁሙ ፤ ጥቅል ፡ ነፋስ ፤ ጠሮ ፤ ሾርፌት ፤ የትቢያ ፡ ማዕበል ፡ የሚያስነሣ ፤ ቤት ፡ የሚያናውጥ ፡ የሚገለብጥ ፤ ተግባ ፡ ከዝናብ ፡ በፊት ፡ የሚነፍስ ። ነፋስ ፡ የሚያስነሣው ፡ ማዕበል ፡ ሞገድ ፡ የባሕር ፡ ሁከት ። ከመ ፡ ጸበል ፡ ዘይነሥኦ ፡ ዐውሎ ። ዐውሎ ፡ ኀያል ፡ ያነቅዓ ። ዐውሎ ፡ ማይ ። ተንሥኡ ፡ ላዕሌየ ፡ ዐውሎታት ፤ ወመዋግድ ፡ ተሰዐሉ ፡ ላዕሌየ ፡ (ኢዮ፳፩ ፡ ፲፰ ። ሕዝ፲፫ ፡ ፲፩ ። መዝ ፡ ፷፰ ። ፊልክ ፡ ፳፰) ።

**ዕዋል** ፤ (ላት ። ዕብ ፡ ዑል ፤ ዐይር) ፤ ዕጓል ፤ ታናሽ ፡ ልጅ ፤ ሕፃን ፤ ግልገል ፤ ውርንጫ ። ዕዋል ፡ ዕጓለ ፡ እድግት ። ትረክቡ ፡ እድግተ ፡ ወዕዋለ ፡ (ዘካ፱ ፡ ፱ ። ማቴ፳፩ ፡ ፪) ።

ዕዋል ፡

**ዐዊም** ፤ ሞት ፤ (ዖመ ፡ የዐውም ፡ ይዑም ። ዐረ ፡ ዐመ ፤ ቀመ ። ዕብ ፡ ዑብ) ፤ መሸፈን ፤ ማልበስ ፤ ማጨለም ፤ የዛፍ ፡ የቅጠል ፤ የጉም ። ከጥሬው ፡ በቀር ፡ አንቀጹ ፡ አይገኝም ።

**ዖም** ፤ ለምለም ፤ ሣር ፡ ቅጠል ፡ ግጫ ፡ ሽንበቆ ፤ የመሰለው ፡ ኹሉ ፤ ምድር ፡ የሚያለብስ ፡ የሚሸፍን ። ጽፍቅ ፡ ዱር ፤ ደን ፡ ወማ ፡ ማካ ፤ ታላላቅ ፡ ዛፍ ፡ ክንፋም ፡ ቅጠላም ። ሡሉ ፡ ዖመ ፡ ብርዕ ፡ ወኅሰት ። ይበቍል ፡ ዖም ፡ ውስተ ፡ በድው ፡ (ኢሳ፲፱ ፡ ፮ ። ፴፭ ፡ ፯) ። ሡሉ ፡ ዖም ፡ ጽፉቅ ። ታሕተ ፡ ሡሉ ፡ ዖም ፡ ዘቦ ፡ ጽላሎት ። ዖመ ፡ ባሳን ፡ (፬ነገ ፡ ፲፯ ፡ ፬ ። ኤር፪ ፡ ፳ ። ዘካ፲፩ ፡ ፪) ።

**ዖማት** ፤ ለምለሞች ፤ ዱሮች ፤ ዛፎች ። ዕፀው ፡ እለ ፡ ይፈርዩ ፡ ወዖማት ፡ (ኩፋ ፡ ፪) ።

**አዕዋም** ፤ ዝኒ ፡ ከማሁ ። ነዋኀት ፡ አዕዋም ። ውስተ ፡ አዕዋሚሃ ፡ (ኢሳ፴፯ ፡ ፳፬ ። ኤር፳፩ ፡ ፲፬) ።

**ዐዊፍ** ፤ ፎት ፤ (ዖፈ ፡ የዐውፍ ፡ ይዑፍ ። ዕብ ፡ ዐፍ ፡ ያዑፍ) ፤ አፈፍ ፡ ወፈፍ ፡ በርደግ ፡ ማለት ፤ ክንፍን ፡ መዘርጋት ፤ ብር ፡ ቱር ፡ ማለት ፤ መብረር ፡ መስረር ፤ እንደ ፡ ደመና ፡ በአየር ፡ መኼድ ፤ መክነፍ ። ወፈፍተኛ ፡ ማለት ፡ ከዚህ ፡ የወጣ ፡ ነው ።

**ዖፍ** ፤ (ዕብ ፡ ዖፍ ። ሱር ፡ ዓውፋ) ፤ በቁሙ ፤ ወፍ ፡ ባለክንፍ ፤ የሚበር ፡ የሚሰር ፤ ታናሹም ፡ ታላቁም ፤ ያንድነት ፡ ስም ፡ ነው ። ዖፍ ፡ ዘይሰርር ። ከመ ፡ ዖፍ ፡ አፍርኅቲሃ ፡ ዘትሴውር ፡ በክንፉ ፡ (ኢሳ፴፩ ፡ ፭ ። ደራሲ) ።

**ዖፍ** ፤ (ትግሬ) ፤ አንበሳ ፤ ዕጓለ ፡ አንበሳ ።

**አዕዋፍ** ፤ (ፋት) ፤ ወፎች ፤ በራሮች ። ነጽሩ ፡ አዕዋፈ ፡ ሰማይ ። እምሡሉ ፡ አዕዋፍ ፡ ትንእስ ፡ ንህብ ። ዘወገሮን ፡ ለአዕዋፍ ፡ (ማቴ፮ ፡ ፳፮ ። ሢራ፲፩ ፡ ፫ ። ፳፪ ፡ ፳) ።

አዕዋፍ ፡

**ዐዊቅ** ፤ ቆት ፤ (ዖቀ ፡ የዐውቅ ፡ ይዑቅ ። ዕብ ፡ ዑቅ ፤ ሣቀየ ፤ አሳመመ) ፤ ማወቅ ፤ ማስተዋል ፤ ምስጢሩ ፡ ጥበቃ ፡ ጥንቀቃ ፡ ነው ። ዑቅ ፡ ትእዛዘ ፡ ወግበር ። ዑቅዎሙ ፡ ልከለባት ። ዑቅ ፡ ዘንተ ፡ ከመ ፡ ኢታግብእ ፡ ለወልድየ ። ዑቅኬ ፡ ኢያስሕቱ ክሙ ። ዑቁ ፡ ርእሰክሙ ፡ (ኩፋ ፡ ፳፩ ። ፊልጵ፫ ፡ ፪ ። ማቴ፳፬ ፡ ፬ ። ማር፲፫ ፡ ፱) ።

**አዖቀ** ፤ አሳወቀ ፤ አስታወቀ ፤ ገለጠ ፤ አስረዳ ። ነገርከ ፡ ያዐውቀከ ። ናሁ ፡ አዖቅክሙ ፡ ከመ ፡ ኢይፌ

ቅድ ፡ ንሥቶት ፡ ወአያቅ ፡ ዐልወቶሙ ። ኢያያቅ ፡ ፍ ድፋዴ ፡ ክብሮሙ ፡ (ማር፲፱ ፡ ፰ ። ዮሴፍ ። አፈ ፡ ድ፩) ።

**ተዐውቀ ፤** ታወቀ ፤ ተረዳ ፤ ጐላ ፡ ተገለጠ ። ይትዐወቅ ፡ እምርሑቅ ፡ ዘይክል ፡ ነቢበ ። ሕልመ ፡ ሌሊት ፡ ዘኢይትዐወቅ ። ከመ ፡ ይትዐወቅ ፡ ጽድቅ ። ተዐውቀ ፡ እግዚ ፡ በይሁዳ ። ዘተዐውቀ ፡ አበሳሁ ፡ በ ውስተ ፡ ፍትሕ ፡ (ሚራ፰፩ ፡ ፯ ። ኢዮ፰ ፡ ፰ ። ሚክ፮ ፡ ፩ ። መዝ ፡ ፸፭ ። ዲድ ፡ ፲) ።

**ዕዉቅ ፤ (ቃን ፡ ቃት ፡ ውቅት) ፤** የታወቀ ፤ የተረዳ ፤ ዕውቅ ፤ ግልጥ ። አኮ ፡ ዴበ ፡ ሚመታት ፡ ዕዉ ቃት ፡ (ስንክ ፡ መጋ፲፱) ።

**ዑቀት ፤** ማወቅ ፤ መታወቅ ፤ አስተዋወቅ ፤ ዕ ውቅነት ፤ ዕውቀት ፡ ዕውቂያ ፡ (ፍ ፡ ን ፡ ፴፫) ።

**ዐውቅ ፤ (ቃን) ፤** ዐውቂያ ፤ የሚያውቁት ፤ ም ስጢር ፡ የሚነግሩት ፤ ወዳጅ ፤ ባልንጀራ ። ዐውቅየ ። ወከመ ፡ ዐውቃንየ ፡ ከንኩ ፡ በማእከሎሙ ፡ (መዝ ፡ ፺፱ ። አረጋ ፡ ድ፳፩) ።

**ተዓወቀ ፤** ተዋወቀ ፤ ተላመደ ፤ ተወዳጀ ፡ ተዛ መደ ።

**አስተዓወቀ ፤** አስተዋወቀ ፤ አላመደ ፤ አለማ መደ ።

**ዐዊር ፤ ሮት ፤ (ያረ ፡ የዐውር ፡ ይዑር ። ዕብ ፡ ዐዌር ። ሱር ፡ ዓዋር ። ዐረ ፡ ዐዊረ ፤ ዐ ወረ ፤ ነቈረ) ፤** መታወር ፤ ዕውር ፡ መኾን ፤ ከማየት ፡ መከልከል ፤ መደናበር ፤ ዐይን ፡ ፈሶ ፡ ፈርጦ ፡ ገበጣ ፡ መ በሎ ፤ ተደፍኖ ፡ ተጨፍኖ ፤ ወይም ፡ ፈጦ ፡ ጕርጦ ፤ ፈዞ ፡ በልዞ ። እቀሥፍ ፡ ሹሎ ፡ አፍራሰ ፡ አሕዛብ ፡ በዐዊር ። ያኑ ፡ አግብርተ ፡ እግዚ ። ያራኒ ፡ አዕይንትየ ፡ እምአን ብዕ ። ትዐውር ፡ ወኢትሬኢ ፡ ፀሓየ ። አዕይንት ፡ ነዳር ያት ፡ የዐውራ ፡ (ዘካ፲፪ ፡ ፬ ። ኢሳ፵፪ ፡ ፲፱ ። ኢዮ፲፯ ፡ ፯ ። ግብ፲፫ ፡ ፲፩ ። ግንዘ) ።

**ዐዋር ፤ (ዐረብ) ፤** ዕውር ፤ ጠንባሳ ፤ ዐይኑ ፡ የ ጠፋ ፤ የፈሰሰ ፤ የዐዊር ፡ ምስጢር ፡ ከብርሃኑ ፡ ይልቅ ፡ ዐይኑ ፡ ብሌኑ ፡ ከወጣ ፡ በኋላ ፤ ባደውን ፡ ያለ ፡ ጕድጓ ድና ፡ ቈርበት ፡ ያሳያል ።

**ዐዋውርት ፤** ዕውሮች ፤ ዕውራኖች ። መርሐ ፡ ዐዋውርት ፡ (ገድ ፡ ዘሚ) ።

**ዕዉር ፤ (ራን ፡ ራት ፡ ውርት) ፤** በቁሙ ፤ የታወረ ፤ ዝኒ ፡ ከማሁ ፡ ለዐዋር ። ዝ ፡ ቀትል ፡ በመጥባ ሕት ፡ ተሰምየ ፡ ሞት ፡ ዕዉር ። ዕዉራን ፡ ይሬእዩ ። ብእሲ ፡ ዘዕውርት ፡ አሐቲ ፡ ዐይኑ ፡ (ዮሴፍ ። ማቴ ፲፩ ፡ ፭ ። ስንክ ፡ ሐም፲፩) ።

(ላ) **ዕወር ፤** መታወር ፤ ዕውርነት ። ይቀሥፈከ ፡ በ ድቀት ፡ ወበዕወር ፡ (ዘዳ፳፰ ፡ ፳፰) ።

**ዑረት ፤** ዝኒ ፡ ከማሁ ፤ ዕውርነት ። በእኪት ፡ ዑረት ፡ ልቡ ። ዑረት ፡ ልብ ፡ የአኪ ፡ እምዑረት ፡ ዐ ይን ፡ (ዲድ ፡ ፱ ። ሲኖ ዶ ። ማር፫ ፡ ፭ ። ሮሜ ፡ ፲፩ ፡ ፳፭) ።

**አዕወረ ፤ አዖረ ፡ (ያዐውር ፡ ያዑር) ፤** ዐወረ ፤ አሳወረ ፤ ዐይን ፡ አወጣ ፤ አሶጣ ፡ ዕውር ፡ አደረገ ፤ አስደረገ ። ወአዕይንቲሁ ፡ ለሴዴቅያስ ፡ አዖረ ። አዑ ሮሙ ፡ አዕይንቲሆሙ ፡ ወአዖሮሙ ። ሕልያን ፡ ያዐ ውር ፡ ዐዕይንተ ፡ (ኤር፵፮ ፡ ፯ ። ፬ነገ ፡ ፮ ፡ ፲፰ ። ዘፀ ፳፫ ፡ ፰) ።

ዕዉር ፡

**ተዐወረ ፤ (ይትዔወር) ፤** ዐይኑን ፡ ጨፈነ ፤ ቸል ፡ አለ ፤ ናቀ ፤ ዕውር ፡ መሰለ ፤ አያየ ፡ እንዳላየ ፡ ኾነ ፤ ደፈረ ። ይትዔወር ፡ ነፍሶ ። ይትዔወር ፡ ቢጾ ። ኅፍ ረት ፡ ተዐውሮቱ ፡ ለቢጽከ ። ኢይባእ ፡ ውስተ ፡ ምሥ ዋዕ ፤ ወእመሰ ፡ ተዐወረ ፡ ከመ ፡ ይባእ ፡ (ሚራ፲፱ ፡ ፰ ። ፳፱ ፡ ፲፱ ። ፵፩ ፡ ፳፩ ። ቀሌ) ።

**ተዐዋሪ ፤** ቸል ፡ ባይ ፤ ቸልተኛ ። አይቴ ፡ ለተ ናስሎ ፡ ተዐዋርያን ፡ (ግንዘ) ።

**ትዕውርት ፤** ቸልታ ፤ ቸልተኛነት ፤ ንቀት ፤ ድ ፍረት ።

**ዐውስት ፤—እሞራ ፤—አውስት ።**

**ዐዊት ፤—ስመ ፡ ሀገር ፤—አዊት ።**

**ዐዘበ ፤—ፈሰሰ ፤—ዐዚብ ፡ ዐዘበ ።**

**ዐዘበ ፤ (ዕብ ፡ [ዐዘብ]) ፤** አዳነ ፤ ዐገዘ ፡ ረዳ ፤ አናጣ ፤ የሸከም ። ነጸርኩ ፡ እመ ፡ ቦ ፡ ዘይዔዝበኒ ፡ ሰ ብእ ፡ ወአልቦ ፡ (ሚራ፺፭ ፡ ፯ ። ዘፀ፳፫ ፡ ፭) ።

—፤ ተወ ፡ ጣለ ፡ ወረወረ ። ሰበቀን ፡ ተመልከት ፤ ከዚህ ፡ ጋራ ፡ አንድ ፡ ነው ።

**ዐዛብ ፤** በቁሙ ፤ የቦክ ፡ እበት ፡ ፍግ ፡ ፋንድያ ፤ ወደርሽ ፡ የሚጣል ።

**ዐዘዘ ፤—በቁሙ ፤—አዝዘ ፡ አዘዘ ።**

**ዐገዘ ፤ ዘት ፤ (ዐዘዘ ፡ ይዔዝዝ ፡ የዐ ዝዝ ። ዐረ ፡ ዐዘ ። ዕብ ፡ ዐዛዝ) ፤** መጽናት ፤ መበ ርታት ፤ መጠንከር ፤ መሠልጠን ። ማጽናት ፤ ማበርታት ፤ ልብን ፡ ሰውነትን ። ከመ ፡ የዐዝዝ ፡ ወየኀይል ፡ ዲበ ፡ ምድር ። ወዐዘዘ ፡ ላዕለ ፡ ትዕይንት ፡ ግብጽ ። ዐዝዝ ፡ ለነ ። ዘይዔዝዝ ፡ ትፍሥሕት ፡ (ሔኖ፺፪ ፡ ፱ ። ዘፀ፲፬ ፡ ፳፬ ። ቅዳ ። መዝ ፡ ፵፯) ። አዘዘን ፡ ተመልከት ።

**ዐዚዝ ፤ (ዛን ፡ ዛት ፡ ዛዝ) ፤** ጥኑ ፡ ብርቱ ፡ ጠ ንካራ ፤ ልባም ። መንፈስ ፡ ዐዚዝ ። ነገሥት ፡ ዐዚዛን ። ብእሲት ፡ ዐዛዝ ፡ (መዝ ፡ ፺ ። ሔኖ፹፰ ፡ ፭ ። ምሳ፲፪ ፡ ፬) ። ዐዞ ፡ ዐዛውንት ፡ ማለት ፡ ከዚህ ፡ ወጥቷል ።

**ዕዙዝ ፤ (ዝዝት)** ፤ የጠና ፡ የበረታ ፤ ብርቱ ፡ ጠንካራ ፤ የማይፈርስ ። **ዕዙዝ ፡ መንግሥት ። ጐዩ ፡ ውስተ ፡ ዕዙዝ ፡ ደብር ። ወበረድስ ፡ ብዙኅ ፡ ጥቀ ፡ ወዕዙዝ ፡** (ቅዳ ። መቃ ። ዘፀ፱ ፡ ፳፬) ።

**ዕዘዝ** ፤ ጥናት ፡ ብርታት ፡ ጥንካሬ ፡ ኀይል ፤ ሥልጣን ፡ ክብር ፡ ልዕልና ። **ዕዘዘ ፡ መዝራዕትከ ። ቶማስ ፡ ዘአርአየ ፡ ዕዘዘ ። ሞት ፡ በዕዘዝ ፡ ይኄይስ ፡ እምሐዩው ፡ በንሳር ። ዕዘዝክሙ ፡ ወሰርጕ ፡ ክብርክሙ ። ንስሩ ፡ እምድኅረ ፡ ዕዘዝ ። እመ ፡ አውዐይኩ ፡ ለመቅደስ ፡ ይትአተት ፡ ዕዘዘሙ ፡** (ጥበ፲፩ ፡ ፳፪ ። ስንክ ፡ የካ፪ ። ዮሴፍ) ።

**አስዐዘዘ ፤ አስያዘዘ** ፤ አፈዘዘ ፤ አደነዘዘ ። **አስከሮ ፡ ወአስያዘዘ ። ወአስያዘዘ ፡ ጺኮ ፡** (ስንክ ፡ የካ፪ ። ንሐ፳፰ ። ዘፍ፴፪ ፡ ፴፩ና ፡ ፴፪) ።

—፤ አስቈጣ ፤ አስፈዘዘ ፤ አሳዘነ ፤ አሳፈረ ፤ አስቀጠጠ ። **ልሳን ፡ ኅቡእ ፡ ያስያዝዝ ፡ ገጸ ፡** (ምሳ፳፭ ፡ ፳፫) ።

—፤ ተከተለ ፤ ሻ ፡ ፈለገ ፤ አፈንፈነ ። **ዘያስያዝዝ ፡ ነገረ ፡ ኢይድኅን ፡** (ምሳ፲፱ ፡ ፯) ።

**መስያዝዝ** ፤ የሚያፈዝ ፤ የሚያደነዝዝ ፤ አፍዝ ፤ አደንግዝ ። **ወይን ፡ መስያዝዝ ፡** (አርጋ ፡ ፬) ። አፍዝ ፡ አደንግዝ ፡ የዓሣ ፡ ስም ፡ ነው ፤ መጠኗና ፡ መልኳ ፡ ታናሽ ፡ ኹና ፡ ግርማዋ ፡ የሚያስደነግጥ ፤ ሲይዟት ፡ እጅ ፡ የምታፈዝ ፡ ሲበሏት ፡ የምታደነግዝ ፡ ዓሣ ፡ ወጋሮች ፡ ለይተው ፡ የሚያውቋት ፡ ከወንዝ ፡ ዓሣ ፡ ኹሉ ፡ የተለየች ፡ መርዛም ፡ ዓሣ ፡ አለች ፡ ይባላል ።

**ሰያዛዝ** ፤ መፍዘዝ ፤ መስለል ፤ ድንዛዜ ፤ የኹ ማት ፡ ደዌ ፤ የበሽታ ፡ ጠንከ ። ቍጣ ፡ ሐዘን ፡ ኀፍረት ፤ ስቅጥጥታ ። **ሕማም ፡ ወሰያዝዝ ፡** (ኩፋ ፡ ፳፫) ።

**ዐዛል ፤— ብርቱ ፤—አዛል ።**

**ዕዝል ፤ (ሕዝል ፤ ሐዘለ)** ፤ የዜማ ፡ ስም ፤ ፪ኛ ፡ ዜማ ። **ሠለስቱ ፡ ዜማ ፤ ዘውእቱ ፡ ግእዝ ፡ ወዕዝል ፡ ወአራራይ ፡** (ስንክ ፡ ግን፲፩) ።

**ዕዝል ፤ (ላት)** ፤ መዝሙር ፤ የመዝሙር ፡ ስም ፤ ዜማው ፡ ዕዝል ፡ የኾነ ፤ በዕዝል ፡ ዜማ ፡ የሚያዜሙት ። **ዕዝል ፡ ዘነግህ ፤ ዕዝል ፡ ዘማርያም ፤ ህየንተ ፡ ዕዝል ፡ ዘነግህ ፡ ግእዝ ። ዕዝል ፡ ዘሙታን ፡** (ድጓ ። ግንዘ) ።

**ዐዥም ፤ (ዐረ ፡ ዐጀም)** ፤ ስመ ፡ ነገድ ፤ ፋርስ ፤ የፋርስ ፡ ሕዝብ ፡ (አቡሻ) ። ሀገሪትን ፡ ተመልከት ።

**ዕዝን ፤—ዠሮ ፤—አዚን ፡ አዘነ ።**

**ዐዚቅ ፤ ቆት ፤ (ዐዘቀ ፡ የዐዝቅ ፡ ይዕዝቅ ። ዐረ ፡ ዐዘቀ ። ዕብ ፡ ዓዜቅ)** ፤ መፋር ፤ መቈፈር ፤ መብሳት ፡ መስርሰር ፤ ማጕድጐድ ፡ ማጥለቅ ፤ ማዘቅ ፤ ዝቅ ፡ ማድረግ ፤ የሖሬ ፡ የጕድጓድ ።

**ዐዘቅት ፤ (ታት)** ፤ በቁሙ ፤ ጕድጓድ ፡ ሖሬ ። **ከመ ፡ ዐዘቅት ፡ ዘኢይነፀፍ ፡ ማዩ ። ዐዘቅት ፡ ንፀፍት ። ወውስተ ፡ ዐዘቅታት ፡** (ኢሳ፶፰ ፡ ፲፩ ። ፪ጴጥ ፡ ፪ ፡ ፲፯ ። ፩ነገ ፡ ፲፫ ፡ ፯) ።

**ዐዘቃት** ፤ ዐዘቅቶች ፤ ጕድጓዶች ። **ኵሉ ፡ ዐዘቃት ፡ ዘከረዩ ፡ ደቀ ፡ አብርሃም ፡** (ዘፍ፳፮ ፡ ፲፭) ።

**ዐዚር ፤ ሮት ፤ (ዐዘረ ፡ የዐዝር ፡ ይዕዝር ። ዕብ ፡ ዐዛር ፤ ረዳ ፡ ዐገዘ)** ፤ መበተን ፤ መዘርዘር ፤ መርጨት ፤ መፈንጠቅ ።

**ተዐዝረ** ፤ ተበተነ ፤ ተዘራ ፡ ተረጨ ፤ ተሠራጨ ፤ ተናኘ ፡ ተወራኘ ፤ የጮራ ፡ የጭፍራ ። **ወተዐዝሩ ፡ ላዕሌሁ ፡** (መሳ፲፭ ፡ ፱) ።

**ምዕዛር ፤ (ራት)** ፤ የብርሃን ፡ ወንፊት ፤ ብርሃን ፡ የሚነዛበት ፤ ብሱ ፡ ንዳላው ። **ወክነፊሁ ፡ ዘምዕዛረ ፡ ፀሓይ ፡** (መጽ ፡ ምስ) ። ያቡሻህር ፡ የመርሐ ፡ ዕውር ፡ የሒሳብና ፡ የቍጥር ፡ መምራን ፡ ለፀሓይ ፡ ፳፻፲፭ ፤ ለጨረቃ ፡ ፻፩ ፡ ምዕዛር ፡ አላቸው ፡ ይላሉ ። «የትርጓሜያቸውም ፡ ምክንያት ፤ ንባቡ ፡ ምስጢሩ ፤ ሥሩ ፡ አነጋገሩ ፡ ይህ ፡ ነው ፡ (ዘፍ፩ ፡ ፲፮) ። ሙሴ ፤ **ወገብረ ፡ እግዚአብሔር ፡ ክልኤተ ፡ ብርሃናተ ፡ ዐቢይተ ፤ ዘየዐቢ ፡ ብርሃን ፡ ከመ ፡ ይምልክ ፡ መዓልተ ፤ ወዘይንእስ ፡ ብርሃን ፡ ከመ ፡ ይምልክ ፡ ሌሊተ ፤ ምስለ ፡ ከዋክብት ፡** ያለውን ። ቅዱስ ፡ ጳውሎስ ፤ **ካልእ ፡ ክብሩ ፡ ለፀሓይ ፤ ወካልእ ፡ ክብሩ ፡ ለወርኅ ፤ ወካልእ ፡ ክብሮሙ ፡ ለከዋክብት ፡** ብሎ ፡ ነገረን ፡ (፩ቆሮ ፡ ፲፭ ፡ ፵፩) ። ሊቃውንትም ፡ በቅዳሴያቸው ፤ **ወአመ ፡ ፈጠረ ፡ ፀሓየ ፡ ወወርኀ ፡ አኮ ፡ ከመ ፡ ያብርሁ ፡ ሎቱ ፡ ከመ ፡ ዘጸልም ፤ አላ ፡ ጸገ ዎሙ ፡ ንስቲተ ፡ እምዘዚአሁ ፡ ብርሃን ፤ መጠነ ፡ ኅጠተ ፡ ሥርናይ ፤ ወበእንተ ፡ ዝ ፡ አብርሁ ፡ ዲበ ፡ ሰብእ ፡** ብለው ፡ አስተማሩን ፡ (ቅዳ ፡ ግሩ) ። ይህንንም ፡ መጠነ ፡ ኅጠተ ፡ ሥርናይ ፡ የተባለውን ፡ ብርሃን ፤ ከሺሕ ፡ መጠን ፡ ይከፍሉታል ። ከዚህም ፡ ከሺሑ ፡ ፳፻፲፭ቱ ፡ ለፀሓይ ፡ ይደርሳታል ፡ በምዕዛሯ ፡ ልክ ፤ ፬፻፩ ፡ ይተርፋል ። ከዚህ ፡ ደግሞ ፡ ፻፩ቱ ፡ ለጨረቃ ፤ ፻ው ፡ ለከዋክብት ፤ ፻ው ፡ ለደመናት ፤ ፻ው ፡ ለቀላያት ፡ ይደርሳቸዋል ። ይህም ፡ ለፀሓይ ፡ የሚደርሳት ፡ ፳፻፲፭ቱ ፡ በ፯፰ ፡ ቢቀምሩት ፡ ፺ ፡ ክፍል ፡ ኹኖ ፡ ፭ ፡ ይተርፋል ፤ ይህም ፡ ፺ቱ ፡ ክፍል ፡ ከነግህ ፡ እስከ ፡ ቀትር ፡ በየሰዓቱ ፡ ይሰጣታል ። እንዲህ ፡ ማለት ፡ የምዕዛሯን ፡ መከፈት ፡ መዘጋት ፡ መናገር ፡ ነው ፤ ፺ቱ ፡ ምዕዛሮች ፡ ግን ፡ መቼም ፡ መች ፡ አይዘጉም ። ከ፯ ፡ ሰዓት ፡ በኋላ ፡ ፺፰ቱ ፡ ይዘጋል ፤ እስከ ፡ ፯ ፡ ሰዓት ፡ ኹሉም ፡ ፈጽሞ ፡ ይዘጋል ። ባንድ ፡ ዕለት ፡ ስድስት ፡ ተውሳክ ፤ ስድስት ፡ ሕጸጽ ፡ አላት ። ለጨረቃ ፡ ይደርሳታል ፡ ያል ነው ፡ ፻፩ቱ ፡ ደግሞ ፡ ፲፭ ፡ ሱባዔ ፡ ይኾናል ፤ ይህም ፡ ከዕለተ ፡ ሠርቅ ፡ እስከ ፡ ዕለተ ፡ ገሀሀ ፡ በየዕለቱ ፡ ይሰጣታል ። ከ፲፭ ፡ ቀን ፡ በኋላ ፡ በየዕለቱ ፡ ፯ ፡ ፯ ፡ እጅ ፡ ይነሣታል ፤ እስከ፲፭ ፡ ቀን ። እንዲህ ፡ ማለት ፡ የምዕዛሯን ፡ መከፈት ፡ መዘጋት ፡ መናገር ፡ ነው ፡ እንጂ ፤ ከአፍኣ ፡ የሚሰጣት ፡ ሌላ ፡ ብርሃን ፡ አለ ፡ ማለት ፡ አይደለም ። ለፀሓይ ፡ ምዕዛር ፡ እንዳላት ፤ ለጨረቃም ፡ አላት ፡ ብለው ፡ ይተረጕማሉ» ።

**ምዕዛር ፤ (ዕብ ፡ አሐር)** ፤ ድኅር ፤ ኋላ ፡ ዠርባ ። **ትሬኢ ፡ ምዕዛርየ ፤ ወገጽየሰ ፡ ኢያስተርኢ ፡ ለከ ፡** (ዘፀ፴፫ ፡ ፳፫) ።

**ማዕዘር** ፤ ብርሃን ፤ የጮራ ፡ እግር ፤ ቀርኑ ፤ ጦሩ ፤ የሚዋጋው ። እንተ ፡ ሠረቀ ፡ ማዕዘኑ ፡ (ስንክ ፡ መጋ፳) ።



ማዕዘር ፡

**መዓዝር** ፤ ብርሃኖች ፤ የብርሃን ፡ ቀርኖች ። መዓዝረ ፡ ፀሓይ ፤ መዓዝረ ፡ ስብሐት ፡ (መጽ ፡ ምስ) ።

**ተማዕዘረ** ፤ በራ ፤ ብርሃን ፡ ኾነ ፤ ፈለቀ ፤ አን ጸበረቀ ። እስመ ፡ በሠራኄ ፡ ገጹ ፡ ለጰራቅሊጦስ ፡ ተ ማዕዘኑ ፡ (ገድ ፡ ተክ) ።

**ዐዜራህ** ፤ (ዕብ ፡ ዐዛራህ) ፤ የምሥዋዕ ፡ ዕርከን ፤ የሕንጻው ፡ ዝናር ፤ ዙሪያውን ፡ የሚከብ ፡ መ ደብ ፡ (ሕዝ፵፫ ፡ ፲፬) ።

**ዐጢን** ፤ ኖት ፤ (ዐጠነ ፡ የዐጥን ፡ ይዕ ጥን ። ዕብ ፡ ቃጣር ፤ ቀተረ) ፤ ማጠን ፤ ማጤስ ፤ ማ ብነን ፤ በጢስ ፡ ማፈን ፤ መሥዋዕት ፡ መሠዋት ፤ ማንደድ ፡ ማቃጠል ። ዐጢነ ፡ ዕጣን ። ከመ ፡ ይዕጥን ፡ ዕጣነ ። ሥዑ ፡ ወዐጠኑ ፡ ለአጋንንት ። ሶበ ፡ ኀደግዎ ፡ ዐጢነ ፡ ለንግሥተ ፡ ሰማይ ፡ (ኩፋ ፡ ፶ ። ፪ዜና ፡ ፪ ፡ ፬ ። ኢሳ፷፭ ፡ ፫ ። ኤር፵፭ ፡ ፲፰) ።

**ዐጣኒ** ፤ (ኒት ፡ ንያን ፡ ያት) ፤ የሚያጥን ፤ የሚያጤስ ፤ ዐጣኝ ።

**ዐጠንት** ፤ ዐጣኞች ። ካህናት ፡ ሰማይ ፡ ቅዉ ማን ፡ በዕበይ ፤ ዐጠንተ ፡ መንበሩ ፡ ለአዶናይ ፡ (ሳታ) ።

**ምዕጣን** ፤ ማጠኛ ፤ ማጤሻ ፤ ቦታ ። ምሥዋዕ ፡ ዘምዕጣን ፡ (ዘሌ፬ ፡ ፯) ።

**ማዕጠንት** ፡ (ታት) ፤ ማጠኛ ፤ ማጤሻ ፤ ጥና ። ማዕጠንተ ፡ ወርቅ ። ወማዕጠንታቲሃ ፡ (ራእ ፰ ፡ ፫ ። ዘኍ፬ ፡ ፲፬) ።



ማዕጠንት ፡

**ተዐጥነ** ፤ ታጠነ ፤ ተጤሰ ። ዐጠኑት ፡ ዐጤሱ ለት ።

**ዕጥነት** ፤ ማጠን ፤ መታጠን ፤ አስተጣጠን ። ይዕጥን ፡ ውስቴቱ ፡ ዕጥነተ ፡ ዘዘልፍ ፡ (ዘፀ፴ ፡ ፰) ።

**ዕጥነት** ፤ ሽታ ፤ መዐዛ ። ዕጥነታ ፡ ከርቤ ፡ ወ ስኂን ፡ እምኵሉ ፡ ጸበለ ፡ አፈው ፡ (ማሕ፫ ፡ ፯) ።

**ዕጣን** ፤ (ናት) ፤ በቁሙ ፤ ሽቱ ፤ የሽቱ ፡ ቅ መም ፤ ለቤተ ፡ መቅደስ ፡ የተበጀ ፡ የተዘጋጀ ፤ መሥዋዕት ፡ ቍርባን ፡ የሚኾን ፡ የሚጤስ ፡ የሚታጠን ። ገበርተ ፡ ዕ ጣን ፡ ወአፈው ። ጸሎተ ፡ ዕጣን ። ሰዓተ ፡ ዕጣን ። ምሥ ዋዕ ፡ ዘዕጣን ። ዕጣን ፡ ቅድው ፡ (፩ዜና ፡ ፱ ፡ ፴ ። ቅዳ ። ሉቃ፩ ፡ ፲ ። ዘሌ፴ ፡ ፩ ። ፴፭—፴፯) ።

**ዕጣነ ፡ ሞገር** ፤ ቅኔ ፤ የቅኔ ፡ ስም ፤ ከዕጣንና ፡ ከቍርባን ፡ በኋላ ፡ የሚቀኙት ፡ (መጽ ፡ ቅኔ) ።

**ዐጢፍ** ፤ ፎት ፤ (ዐጠፈ ፡ የዐጥፍ ፡ ይ ዕጥፍ ። ዐረ ፡ ዐጠፈ ። ዕብ ፡ ወሱር ፡ ዐጣፍ) ፤ መሥራት ፤ ማጠፍ ፤ መጠቅለል ፤ ማልበስ ፡ መሸፈን ፡ ማጕናጠፍ ፤ መጠቅለያውን ፤ የሸማኔ ። ዐጸፈን ፡ ተመል ከት ፤ የዚህ ፡ ጎረ ፡ ቤት ፡ ነው ።

**ተዐጥፈ** ፤ ተሠራ ፤ ታጠፈ ፤ ተጠቀለለ ፤ ዝ ሓው ፡ ልብሱ ።

**ዕጡፍ** ፤ የተሠራ ፤ የታጠፈ ፤ የተጠቀለለ ፤ መ ዘራዝር ፡ የገባ ። ከመ ፡ ዕጡፈ ፡ ፀምር ፡ ዘአልጸቀ ፡ ይ ግምድዎ ፡ (ኢሳ፴፰ ፡ ፲፪) ።

**ዐጥፍ** ፤ በቁሙ ፤ የተሠራ ፡ ልብስ ። ሠርዌ ፡ ዐጥፍ ፡ ዘመዐስቃን ፡ (፪ነገ ፡ ፳፩ ፡ ፲፱) ።

**ዐጢቅ** ፤ ቆት ፤ (ዐጠቀ ፡ የዐጥቅ ፡ ይዕ ጥቅ) ፤ መታጠቅ ፤ መቀነት ፤ ወገብን ፡ ማሰር ፡ ማጥበቅ ፤ ማሸረጥ ፡ ማሸንፈጥ ፤ ማገልደም ። ዕጥቆ ፡ ውስተ ፡ ሐ ቌክ ። እለ ፡ የዐጥቁ ፡ ቅናተ ፡ መንግሥት ። ገብሩ ፡ ሎሙ ፡ ሞራአ ፡ ዘየዐጥቁ ፡ (ኤር፲፫ ፡ ፩—፪ ። አፈ ፡ ተ፳ ። ቀሌ) ።

**ዐጣቂ** ፤ (ቂት ፡ ቅያን ፡ ያት) ፤ የታጠቀ ፡ የሚታጠቅ ፤ ታጣቂ ። ለሐቌክ ፡ ሰላም ፡ ቅናተ ፡ ል ቡና ፡ ዐጣቂ ፡ (ደራሲ) ።

**ዕጠቅ** ፤ መታጠቅ ፤ አስተጣጠቅ ፤ ትጥቅ ፤ ማ ጠቆ ። ወዕጠቆሙ ፡ ይፈትሑ ፡ ሐራ ፡ (ደራሲ) ።

**ዐጥቅ** ፤ በቁሙ ፤ ያገዳና ፡ የቀልጥም ፡ ወሰን ፡ መገናኛው ፤ እንደ ፡ ትጥቅ ፡ ያለው ። ዐጥቅ ፡ የለሽ ፡ እን ዲሉ ፤ ወሰን ፡ የለሽ ፡ ሲሉ ።



ዐጥቅ ፡

**አዕጠቀ** ፤ አስታጠቀ ። አዕጥቀኒ ፡ ኀይላቲ ከሙ ፡ ወአቅንቶኒ ፡ ለጸብእ ፡ (ስንክ ፡ ታኅ፲፬) ።

**ዐጣርድ** ፤ (ዐረ ፡ ዐጣሪድ) ፤ ኮከብ ፤ የኮ ከብ ፡ ስም ፡ ወይም ፡ ሥዕሉ ፡ ምስሉ ፤ ስብአ ፡ ልስጥራን ፡ የሚያመልኩት ። ሄርሜንን ፡ ተመልከት ፤ ከዚህ ፡ ጋራ ፡

አንድ፡ነው። ወሰመይዎ፡ ለአሐዱ፡ እምኔሆሙ፡ መሸተሪ፡ ወለካልኡ፡ ዐጣርድ፡ (አፈ፡ ተ፳፮። ግብ፲፱፡ ፲፱)።

**ዐጢስ፤ ሰት፤ (ዐጠሰ፡ የዐጥስ፡ ይዕጥስ። ዐረብ። ዕብ፡ ዐጣሽ)፤** ማንጠስ፤ ድንገት፡ ባፍና፡ ባፍንጫ፡ መጮኽ፤ መተንፈስ፤ ከጕንፋን፡ ወይም፡ ከከፉ፡ ሽታ፡ የተነሣ። ማፋሸግ፡ ማላቀቅ፡ ማዛጋት፤ አፍን፡ መክፈት፤ ዋሻ፡ ማስመሰል።

**ዕጠስ፤** ዕንጥስታ፤ ንጥሻ፤ ፍሽጊያ፤ ክፍት፡ አፍንት። ባለብሉዮች፡ ግን፡ ቅንድብ፡ ይሉታል። በዕጠሱ፡ ይበርቅ፡ ብርሃን። ዕጠስ፡ ወሀኬት፡ (ኢዮ፵፩፡ ፱። አፈ፡ ተ፳፯)።

**ዐይ፤—ምን፤—አይ።**

**ዐይግ፤ (ጋት)፤** ኵሬ፤ የውሃ፡ መቋሚያ፤ መጠራቀሚያ፤ ጕድጓዳ፡ በታ፤ ዐውደ፡ ማይ፤ ጉባኤ፡ ማይ፤ ታናሽ፡ ባሕር። በአሐቲ፡ ዐይግ፡ ማይ፤ ወውእቱ፡ ዐይግ፡ ማይ፡ ተሠጠ፡ (ሔኖ፹፱፡ ፳፫፡ ፳፱—፳፮)።

**አዕያግ፤ (ጋት)፤** ኵሬዎች፤ የውሃ፡ መቋሞች። አዕያጊሆሙ። አዕያጋተ፡ ማይ። ዝናም፡ መልአ፡ ኵሎ፡ አዕያጋተ፡ ዘሀሎ፡ ኀቤሆሙ፡ (ዘፀ፯፡ ፲፱። ዘሌ፲፩፡ ፴፮። ዮሴፍ)።

**ዐይግን፤ (ዕብ፡ አጋን። ሱር፡ አጋና። ዐረ፡ ኢጋንት)፤** ጣሳ፤ ፍንጃል፤ ኵባያ፤ ዳካ፤ ለገን። ቈጆ፤ ማለቢያ፤ የስሬት፡ ዕቃ፤ ደም፡ ተቀብቶ፡ እንደ፡ ሸክላና፡ እንደ፡ ፍንጃል፡ ያለ፤ ውሃ፡ የሚይዝ፡ የሚቋጥር። ዐይግን፡ ፀፂይ። ወመልአ፡ ዐይግነ፡ (መሳ፮፡ ፴፰። ፮፡ ፴፰)።

**ዐይጋን፤** ኵባዮች፤ ፍንጃሎች፤ የሸክላ፡ ጥዎች፤ እጀታ፡ ጕሮ፡ ያላቸው። አርባዕቱ፡ ምእት፡ ዐይጋነ፡ ወይን፡ (ገድ፡ አዳ)። ጋን፡ ማለት፡ ከዚህ፡ ይስማማል፤ ገንዕን፡ ተመልከት።

**ዐይጥ፤ (ዕብራ፡ ዐይጥማ፡ አሞራ)፤** በቁሙ፤ የሌት፡ ወፍ፤ ነገደ፡ እንጄዋ።

**ዐየየ፤—መሰለ፤—አይይ፡ አየየ።**

**ዐይይ፤ ዮት፤ (ዐየየ፡ የዐይይ፡ ይዕየይ፡ ይዕይይ። ዐረ፡ ዐዪየ)፤** መሳት፤ መሳሳት፤ ከመንገድ፡ መውጣት፤ መዞር፡ መባከን፤ ፈልጎ፡ ማጣት። ወየዐይይ፡ እንተ፡ በዙለሄ። በአይ፡ ፍና፡ እስመ፡ ዐየይኩ፡ (ቅዳ፡ ሕር። ቄር፡ ጸላ)።

**ዕዩይ፤ (ያን፡ ያት፡ ይይት)፤** ራሱ፡ የዞረ፤ እንቡዝ፤ ባካና። አ፡ ዘእንበለ፡ ልብ፡ ዕዩይ፡ ኢለቦከ፡ ምስጢረ። ዘእምባሕር፡ ወእሞት፡ ዕዩይ። ዕዩያነ፡ ኀሊና፡ (ተረ፡ ቄር። አፈ፡ ተ፱)።

**ዐዪል፤ ሎት፤ (ዔለ፡ የዐይል፡ ይዒል። ዕብ፡ ዐላህ)፤** ላይ፡ ላዩን፡ መዞር፤ መባከን፡ መብረር፤ ማውተት፡ መንከርተት፤ ያሞራ፡ የወፍ። ርቆ፡ መኼድ፤ ጋራ፡ ዙሮ፡ ወንዝ፡ ተሻግሮ፡ መሸሽ፡ መሰደድ። ወደ፡ ዱር፡ ወደ፡ በረሓ፡ ወደ፡ ጋራ፡ ወደ፡ ተራራ፡ መውጣት፡ መሰምረት፤ መናወዝ፡ መቃበዝ፡ ጕባውን፡ ተሬውን፡ ዋሻውን፡ ጕሬውን፡ መዕለል፡ መጕብኘት፤ የዐዳኝ፡ የመናኝ። አዐይል፡ ውስተ፡ አድባር፡ ከመ፡ ዖፍ። እንዘ፡ የዐይል፡ አድባረ፡ ወአውግረ። በውስተ፡ በድው፡ ኀበ፡ ዒልክሙ፡ በበ፡ መራዕይክሙ። ንዒል፡ ውስተ፡ አድባር፡ ወበአታት፡ ወግበበ፡ ምድር፡ (መዝ፡ ፲። ስንክ፡ ታኅ፲። ሆሴ፲፫፡ ፩—፮። ድጓ)። በዔለ፡ ፈንታ፡ ተዐየለ፡ ይላል፤ ኢያስኝም። አሐተ፡ ዕለተ፡ እንዘ፡ ይትዐየል፡ ውስተ፡ በድው፡ (ስንክ፡ ጥር፳፱)።

**ዐያል፤ (ሊ፡ ሊት)፤** የሚዞር፤ ዘዋሪ፤ ቅብዝብዝ። እንዘ፡ ዐያለ፡ የሐውሩ። ከመ፡ ንህብ፡ ዐያሊት፡ ከማሁ፡ አባ፡ ዮሐኒ፡ ዘዔለ፡ (ሄርማ። ገድ፡ አዳ። ድጓ)።

**ዒለት፤** መዞር፤ ዙረት፡ አዟዟር።

**አዔለ፤** አዞረ፤አባከነ፤አንከረተተ። አዔሎሙ፡ ውስተ፡ ገዳም። አዒልዎ፡ ውስተ፡ ይእቲ፡ ሀገር፡ (ዘኍ፴፪፡ ፲፫። ኢዮ፲፪፡ ፳፬። ስንክ፡ መጋ፲፭)።

**ዔላ፤ (ላት)፤** ዐዘቅተ፡ ማይ፤ የውሃ፡ ጕድጓድ፤ መከማቻ፡ መጠራቀሚያ። ዒላ፡ ዘውእቱ፡ ምእላደ፡ ማይ፤.....ያመጽኡ፡ ሎሙ፡ ማየ፡ ወይመልእዎ፡ በዒላት፡ (ታምረ፡ ማር)።

**ዐያም፤ (ዕብራ)፤** ብርቱ፡ ጠንካራ፤ ዐያሌ፡ ብዙ፤ የሕዝብ፡ የመንጋ።

**ምዕያም፤ (ማት)፤** በረት፤ ጎል፤ ምስሓግ፤ ብዙ፡ መንጋ፡ የሚያድርበት፤ የሚመሰግበት። አይቴ፡ ኀለፈት፡ እምዕያማ፡ ማርያም፡ ጣዕዋ፡ (ደራሲ። ሔኖ፹፮፡ ፱)።

**ዔመ፤** አፈገ፤ መሰገ፤ አገባ፤ አጕረ።

**ዐየነ፤—ተከባከበ፤—አይኖ፡ አየነ።**

**ዐይን፤ (ዕብ፡ ዐዪን። ዐረ፡ ዐይን። ሱር፡ ዐይና)፤** በቁሙ፤ የማየት፡ ሕዋስ፤ ማያ፡ መመልከቻ። ማኅቶቱ፡ ለሥጋ፤ ውእቱ፡ ዐይንከ። ይትረአዩ፡ ዐይነ፡ በዐይን፡ (ማቴ፮፡ ፳፪። ኤር፴፱፡ ፬)።



ዐይን፡

**አዕይንት፤** ዐይኖች፤ የሥጋ፡ መብራቶች። ይኔጽራ፡ አዕይንቲሁ። ጠፍአ፡ አዕይንቲነ፡ (ኢሳ፲፯፡ ፯። ሰቈ፬፡ ፲፯)።

**ዐይን፤ ሰብአ፡ ዐይን፤** ሰላይ፤ ጕበኛ፤ መልከተኛ። ወፈነወ፡ ዳዊት፡ አዕይንተ። አኮኑ፡ አዕይንት፡ እሙንቱ። ፈኑ፡ ዕደወ፡ ሰብአ፡ ዐይን፡ (፩ነገ፡ ፳፮፡ ፬። ፪ነገ፡ ፲፡ ፫። ፍ፡ ነ፡ ፭)።

**ዐይን** ፤ ዐይነት ፤ መልክ ፤ ሕብር ፤ ፊት ፡ ለፊት ፡ ያለ ፡ ትይዩ ፡ አንጻር ፤ ዐይን ፡ የሚያየው ፡ የሚያርፍበት ።

**ዐይን** ፤ ዐይነታ ፤ ዋና ፤ ጭንሬታ ። እመ ፡ ኢተ ረከበ ፡ ዐይኑ ፡ ያገብእ ፡ አምሳሊሁ ፡ (ፍ ፡ ነ ፡ ፵፩) ።

—፤ የሚዘን ፡ ምላስ ፤ ውልብልቢት ፤ ላንሴታ ። እንተ ፡ ታገብእ ፡ ዐይነ ፡ መዳልው ፡ (ኢሳ፵ ፡ ፲፭) ።

—፤ ብስ ፤ ነዳላ ፤ ሽንቍር ፤ ፍልፍል ፤ የገበጣ ፡ የስፌፍ ፡ ዐይነት ፤ ሽከራ ፤ ጠቃጠቆ ። የመርፌ ፡ ዐይን ፤ ገበጣ ፡ ዐ ይን ፤ ዐይናማ ፡ ደንጊያ ፡ እንዲሉ ።

**ዐይነ ፤ ማኅተም** ፤ የማኅተም ፡ ዐይነት ፤ በ ማኅተም ፡ ላይ ፡ የተሣለ ፡ የተቀረጸ ፡ መልክ ፤ ወይም ፡ የታተመ ፡ የማኅተም ፡ ቅድ ፡ (ዘፀ፳፰ ፡ ፲፩ና ፡ ፳፩) ።

**ዐይነ ፤ ወርቅ** ፤ የወፍ ፡ በሽታ ፤ ዐይንን ፡ ጥ ፍርን ፡ ሽንትን ፡ ሰውነትን ፡ ብጫ ፡ የሚያደርግ ፤ ወርቅ ፡ የሚያስመስል ። የክፉ ፡ ዐይን ፡ ደዌ ፤ አስተያየቱ ፡ እንደ ፡ ጦር ፡ ኹኖ ፡ የሚወጋ ። ተዘከር ፡ ከመ ፡ እኩይ ፡ ዐይነ ፡ ሰብእ ። ነጸሩ ፡ በመዐት ፡ ወመጽለወት ፡ (ሢራ፴፩ ፡ ፲፫ ። አስቴ፩ ፡ ፩—፪) ።

**ዐይን** ፤ ምንጭ ፤ ውሃው ፡ እንደ ፡ እንባ ፡ ኹኖ ፡ ሲወጣ ፡ ሲፈልቅ ፡ የሚታይበት ። ይትከሀልኑ ፡ ይፃእ ፡ እምአሐዱ ፡ ዐይን ፡ ማይ ፡ መፃር ፡ ወማይ ፡ ጥዑም ። ወሀለዉ ፡ ህየ ፡ ዐሠርቱ ፡ ወክልኤቱ ፡ ዐ ይን ። አቀመ ፡ አዕይንቲሁ ፡ ለተከዚ ፡ (ያዕ፫ ፡ ፲፩ ። ዘፀ፲፭ ፡ ፳፯ ። ሱቱ ፡ ዕዝ፲፫ ፡ ፵፱ ። ድጓ) ።

**ዐይነ ፡ ምድር** ፤ ጕድጓድ ፤ ዐዘቅተ ፡ ኰስሕ ፤ የጕድጓድ ፡ ምንጭ ፤ ውሃው ፡ ከውስጥ ፡ ከመሬት ፡ የሚ ፈልቅ ፤ እንዳዲስ ፡ አበባ ፡ ያለ ።

(ጥ) **ዐየነ ፤ (ዕብ ፡ ዐዬን)** ፤ ዐይናማ ፡ ኾነ ፤ ዐይን ፡ አወጣ ። ምንጭ ፡ ፈለገ ፤ በታ ፡ ሰለለ ፤ ጐበኘ ፤ ለሰፈር ። ዐይኑን ፡ ጣለ ፤ ትክ ፡ ብሎ ፡ አየ ፤ አስተዋለ ። አጥልቆ ፡ ዐሰበ ፤ መረመረ ፤ ፈተሸ ፤ ቀመለ ፤ የነገር ። ገ መተ ፤ ገመገመ ፤ ይህን ፡ ያኽል ፡ አለ ፤ የዋጋ ፡ የከሳ ። በዕጹብ ፡ እመ ፡ ዐየነ ፤ ንረክብ ፡ ምግባረ ፡ ዘውስተ ፡ ምድር ። የዐይኑ ፡ ሎሙ ፡ ዘይሁብዎሙ ፡ (ጥበ፱ ፡ ፲፱ ። ዘሌ፲፱ ፡ ፳ ። ዘፀ፳፩ ፡ ፴፩ ። ፪ቆሮ ፡ ፲ ፡ ፲፪) ። በዐ የነ ፡ ፈንታ ፡ ተዐየነ ፡ ይላል ፤ አያሰኝም ። እንዘ ፡ ይት ዔየዮ ፡ ዘልፌ ፡ እመ ፡ ይፈርህ ፡ ወይጸንዕ ፤ በጽኑዕ ፡ ይትዔየነኒ ፡ (ገድ ፡ ኪሮ) ። ርእየን ፡ ተመልከት ።

**ዐየነ ፤ (ትግሬ)** ፤ አበደ ፤ እብድ ፡ ኾነ ፤ ልቡ ፡ ጠፋ ።

**ተዐየነ** ፤ ተጐበኘ ፤ ተሰለለ ፤ ተመረመረ ፤ ም ንጩ ፡ በታው ። ተገመገመ ፤ ዋጋው ።

**ተዐየነ** ፤ ከተመ ፤ ምንጭ ፡ ይዞ ፡ ሰፈረ ፤ ጐዠ ፡ ሠራ ፤ ድንኳን ፡ ተከለ ፤ ሕዝቡ ። እለ ፡ ይቀድሙ ፡ ተዐይኖ ። ወተዐየኑ ፡ ውስተ ፡ አቤኔዜር ፡ (ዘኍ፪ ፡ ፫ ። ፩ነገ ፡ ፬ ፡ ፩) ።

—፤ ከበበ ፤ ዐጠረ ፤ ዙሪያውን ፡ ያዘ ፤ በዙሪያ ፡ ሰፈረ ። ሶበ ፡ ዮን ፡ ተዐይኖ ፡ ላዕለ ፡ ሀገር ። ወተዐየና ፡ ለሀገር ፡ ወዐገታ ። ወይትዐየኑኪ ፡ (ዮሴፍ ። ሉቃ፲፱ ፡ ፵፫) ።

**ዕዩን ፤ (ናን ፡ ናት ፡ ይንት)** ፤ የተጐበኘ ፤ የተመረመረ ፤ የተገመገመ ፤ የተመረጠ ፡ የተለቀመ ፤ ም ርጥ ። ዕጣን ፡ ዕዩን ፡ ዘድቁቅ ፡ (ዘሌ፲፮ ፡ ፲፪) ።

**ትዕይንት ፤ (ታት)** ፤ ሰፈር ፤ ከተማ ፤ መን ደር ፤ ብዙ ፡ ድንኳን ፤ ጐዠ ፡ ቤት ፤ ዳስ ፡ በረት ። ቀርበ ፡ ሙሴ ፡ ኀበ ፡ ትዕይንት ፤ ወቀመ ፡ ውስተ ፡ አንቀጸ ፡ ትዕ ይንት ፡ (ዘፀ፴፪ ፡ ፲፱ና ፡ ፳፮) ።

—፤ ሰራዊት ፡ ጭፍራ ፤ ጓዝ ፡ ወገን ፤ ሕዝብ ፡ ቤተ ፡ ሰብ ። ጉባኤ ፡ ማኅበር ፡ ሸንጎ ፤ የሰው ፡ መንጋ ፤ ባንድነት ፡ የሚ ሰፍር ፡ የሚንጋጋ ። መንግሥትን ፡ ተመልከት ። ወሰበለ ፡ መልአከ ፡ እግዚ ፡ ዘየሐውር ፡ ቅድመ ፡ ትዕይንቶሙ ፡ ለደቂቀ ፡ እስራኤል ። ወትዕይንቶሙሰ ፡ ለኢሎፍሊ ፡ ተዐየኑ ፡ ፈለገ ። ትዕይንቶሙ ፡ ለእለ ፡ ቀሬ ፡ (ዘፀ፲፱ ፡ ፲፱—፳ ። ፩ዜና ፡ ፲፩ ፡ ፲፭ ። ሚራ፵፭ ፡ ፲፰) ።

**ተዓይን** ፤ ሰፈሮች ፤ ድንኳኖች ፤ ከተሞች ። ሰራዊቶች ፤ ጭፍሮች ፤ ማኅበሮች ። ተዓይኒሆሙ ፡ ለኤ ዶምያስ ። እምዝሉ ፡ ተዓይኒሁ ፡ ለያዕቆብ ። ወር እየ ፡ ያዕቆብ ፡ ተዓይነ ፡ እግዚ ። እመኒ ፡ ጸብአኒ ፡ ተዓ ይን ። ተዓይነ ፡ ክርስቶስ ፡ (መዝ ፡ ፹፪ና ፡ ፹፯ ። ዘፍ ፴፪ ፡ ፩—፪ ። መዝ ፡ ፳፯ ። ስንክ ፡ ሐም፲፪) ።

**ተዓየነ** ፤ ተሳፈረ ፤ ተሰፋፈረ ፤ ጐን ፡ ለጐን ፡ ወይም ፡ ፊት ፡ ለፊት ።

(ጥ) **ዐይሮ ፤ ሮት ፤ (ዐየረ ፡ ይዔይር ፡ የዐ ይር ። ዐረ ፡ ዐየረ ። ዕብ ፡ ሔሬፍ)** ፤ ማየር ፡ መቀላቀል ፤ የማዕደናት ። መስደብ ፡ ማዋረድ ፤ መገደር ፡ መላገድ ፤ መናቅ ፡ ማቅለል ፤ አሳልፎ ፡ መስጠት ፤ ራስን ፡ ወይም ፡ ሌላውን ። ሕዝብ ፡ ዘዐየረ ፡ ነፍሶ ፡ ለሞት ፡ (መሳ፭ ፡ ፲፰) ። መጽሐፍ ፡ ግን ፡ በዐየረ ፡ ፈንታ ፡ ተዐ የረ ፡ ይላል ፤ አድራጊውን ፡ በተደራጊ ፤ የተሳሳተ ፡ ነው ። ኢይትዐየር ፡ እንዘ ፡ ይብል ፤ አ ፡ ዕዉር ፡ አ ፡ ጽሙም ፡ አ ፡ ሐጺጽ ፡ አ ፡ ገብር ፡ አ ፡ ፀጋማዊ ፡ አ ፡ ሀካይ ፤ ወዘ ተርፉ ፡ ትዕይርታተ ። ጸሐፈ ፡ እንዘ ፡ ይትዔየሮ ፡ ለእ ግዚ ። ወእመሰ ፡ ቦ ፡ ዘተዐየሩክሙ ፡ በእንተ ፡ ስሙ ። ዘይትዔየር ፡ በክብረ ፡ ርእሱ ፡ (ፍ ፡ ነ ፡ ፱ ። ፪ዜና ፡ ፴፪ ፡ ፲፯ ። ፩ጴጥ ፡ ፬ ፡ ፲፬ ። አርጋ ፡ ፫) ።

**ተዐየረ ፤ (ተደራጊ)** ፤ ተሰደበ ፤ ተዋረደ ፤ ተናቀ ፤ ተጠቃ ፤ ተግዳሮት ፡ ሰማ ።

**ዕዩር ፤ (ራን ፡ ራት ፡ ይርት)** ፤ የተሰደበ ፤ ስዱብ ፤ ወራዳ ፤ ጥቁ ። ንከውን ፡ ዕዩራነ ፡ (ዮዲ፰ ፡ ፳፪) ።

**ትዕይርት ፤ (ታት)** ፤ ስድብ ፤ ውርደት ፤ ስ ግድ ፤ ተግዳሮት ፤ ጡር ፡ መስቃ ። ትዕይርተ ፡ ይከ ውዎ ። ከመ ፡ ኢይስማዕ ፡ ትዕይርተ ። ትዕይርቱ ፡ ለ ክርስቶስ ። እንዘ ፡ ንጸውር ፡ ትዕይርቶ ፡ (ጦቢ፫ ፡ ፱ና ፡ ፲፫ ። ዕብ፲፩ ፡ ፳፯ ። ፲፫ ፡ ፲፫) ።

**ዕይር** ፤ በቁሙ ፤ ቅልቅል ፡ ድብልቅ ፤ የታየረ ።

**ዔር ፤ (ዕብ ፡ ዒር)** ፤ ጠባቂ ፡ መልአክ ። ምስ ጢሩ ፡ ግን ፤ ነሣቲ ፡ ደያኒ ፡ ማለት ፡ ነው ። ወናሁ ፡ ዔር ፡ ቅዱስ ፡ (ዳን፬ ፡ ፲) ።

**ዔረግ፤(ዕብ፡ ሄሬግ፤ የሰይፍ፡ ሞት። ዐረ፡ ሐርግ)፤** ወጥመድ፤ አሽክላ፤ ያውሬ፡ መያዣ። እስመ፡ ፍቅረ፡ ወይን፡ ተብህለ፡ ለሰይጣን፡ ዔረጉ፡ (ደራሲ)።

**ዔረግ፤(ዕብ፡ ክሉብ)፤** ቀፎ፤ ቅርጫት፤ የአዕዋፍ፡ ቤት፤ ከቀጫጭን፡ ሐረግ፡ ወይም፡ ከሽቦ፡ የተሠራ፤ ሐረግን፡ ተመልከት። ከመ፡ ዔረግ፡ ዘምሉእ፡ አዕዋፈ፡(ኤር፭፡ ፳፯)። በፍሬ፡ ፈንታ፡ ዔረግ፤ በዔረግ፡ ፈንታ፡ ሙዳይ፡ ይላል፤ የተሳሳተ፡ ነው። ሙዳየ፡ ዔረግ፡(ዓሞ፰፡ ፩—፪)። ዕብራይስጡ፡ ግን፤ ክሉብ፡ ቃይጽ፡ ይላል፤ የበጋ፡ ቅርጫት፡ ማለት፡ ነው፤ ፍሬ፡ የተመላ፡ ማለትን፡ ያሳያል። ባለብሉዮች፡ ግን፡ በለው፡ ሰይፍ፤ ጸብታ፡ ፃግታ፡ ይሉታል፤ የበጻ፡ ጸብት፡ ንዋየ፡ ሐቅል፡ ማለት፡ ነው። ዳግመኛም፡ ሙዳየ፡ ዔረግ፡ በማለት፡ ፈንታ፡ ቈረጽ፡ ይቈርጽ፡ ይላል፤ ይህን፡ ደግሞ፡ መቀስ፡ ይሉታል፤ ንባቡም፡ ፍችውም፡ አልተ ሳከም።

**ዐኪው፤ ዎት፤(ዐከወ፡ የዐኵ፡ ይዕኵ)፤** መከልከል፤ ማስቀረት፤ እንዳይገባ፡ ማድረግ።

**ታዕካ፤(ካት)፤** የንጉሥ፡ ቤት፤ ቤተ፡ መንግሥት፤ አዳራሽ፡ ታላቅ፡ ከፍተኛ፤ ከፍ፡ ባለ፡ ቦታ፡ የተሠራ፤ ግቢ፤ ሰፈር፤ ክልካይ፡ አስከልካይ፡ ዘበኛ፡ አጋፋሪ፡ ያለበት። ታዕካ፡ ንጉሥ። ጸግዎ፡ ሰላመ፡ ለንጉሥ፤ ለታዕካሁ፡ ወለሰራዊቱ። ቈስጠንጢኖስ፡ ታዕካ፡ ንበ፡ ዘሐነጸ፡ ሎቱ። ማርያም፡ ታዕካ፡ በምድር፡ ወታዕካ፡ በሰማይ፤ ታዕካ፡ መንግሥተ፡ ሰማያት፡(አቡሻ፡ ፶። ቅዳ። ስንክ፡ ጥር፳፯። ድጓ። መቃ)።

**ዐኵት፤(ዕብ፡ ዐሮብ)፤** ክልካይ፡ አጋፋሪ፤ የበር፡ መቅሠፍት። ተባይ፤ ተናካሽ፡ ፍጥረት፤ በየስሙና፡ በየመልኩ፤ የሚነድፍ፡ የሚቈነጥጥ፤ የሚያቈስል፡ የሚያሳብጥ፤ የሚያሳክክ፡ የሚያንገበግብ፤ ተርብ፡ የውሻ፡ ንብ፤ የበሬ፡ የበረሓ፡ ዝንብ፤ ትንኝ፡ ቅማል፤ ቍንጫ፡ ትኋን፤ ዘመሚት፡ ጕንዳን፤ የመሰለው፡ ኹሉ። ፈነወ፡ ዐኰተ፡ ወበልዖሙ፡(መዝ፡ ፸፯ና፡ ፶፬። ጥበ፲፱፡ ፲)።

**ዐኮ፤—አይዶለም፤—አኪው፡ አከወ፤ አኮ።**

**ዐከየ፤—ከፉ፤—አክይ፡ አከየ።**

**ዐኪክ፤ ከት፤(ዐከከ፡ የዐክክ፡ ይዕክክ)፤** መጥገብ፤ መጠገብ፤ መሰልቸት፤ ዕክክ፡ ማለት። ብዙ፡ ውሃ፡ መያዝ፤ እስከፍ፡ እስከ፡ ክንፈር፡ መንተርፈፍ፡ መምላት፤ የጋን፡ የማድጋ፡ (ዮሐ፪፡ ፯)።

**ማዕክክ፤(ዕብ፡ ኪዮር)፤** ድስት፤ ማሰሮ፡ ምንቸት፤ የሚጣድ። ገንቦ፡ ማድጋ፤ እንስራ፡ ጋን፡ ዝንግሪር፤ ዋዲያት፡ ለገን፤ ማጠቢያ፡ መታጠቢያ፤ የውሃ፡ ዕቃ፡ ኹሉ፤ ክብንት፡ ያለው። ጣሳ፡ ኰባያ፡ ዋንጫ፡ ጽዋዕ፡ ሳይቀር፡ መቅጃውን፡ ኹሉ፡ ያሳያል። ኬጥሮጋ ውሎስን፤ ንብቲራን፡ መቅለድን፡ ተመልከት፤ ከዚህ፡ ጋራ፡ አንድ፡ ነው። ዘገብረ፡ ማዕክክ፡ ብርት፤ ወገብሮ፡ ለውእቱ፡ ማዕከክ፡ ከመ፡ ይትኀፀቡ፡ ውስቴቱ። ሕንብርትኪ፡ ከመ፡ ማዕከክ፤ ጽዋ፡ (ዘፀ፴፰፡ ፳፯—፳፰። ማሕ፯፡ ፫)።

**መዓክክት፤** ታላላቅ፡ ድስቶች፤ ጋኖች፤ መታጠቢያዎች። ወመዓክክቲ፡(፪ነገ፡ ፰፡ ፰)።

**ዐከለ፤—በላ፤በቃ፤—አኪል፡ አከለ።**

**ዐልጎ፤ ጎት፤(ዐለገ፡ ይዔልግ፡ የዐልግ። ዐረ፡ ዐለጀ)፤** ማሸነፍ፤ መጣል፤ ድል፡ መንሣት፤ በላይ፡ መኾን፤ የትግል፡ የውጊያ። መሻጠጥ፤ መጋጠጥ፤ ከሥሩ፡ መቍረጥ፤ የኀፍረት። ትግሬ፡ ግን፡ ዐለገ፡ ብሎ፡ ሰወረ፡ ደበቀ፡ ይላል፤ ምስጢሩ፡ ኀፍረት፡ ነው።

**ዕልገት፤** ማሸነፍ፤ መጣል፤ መግደል፤ መስለብ፤ መግፈፍ። የድል፡ ምልክት፤ ምርኮ፡ ሰለባ፡ የደም፡ ሽማ፤ ትምክሕት፤ ድንፋታ፤ ልዕልና፡ ከፍታ፤ ቅርርት፡ ፍክራ፤ የኀርግንነት፡ ሥራ። ዕልገተ፡ ቈላፉን። ዘብዙኀ፡ ዕልገቱ። ወሎቱሰ፡ አግብኡ፡ ሎቱ፡ ዕልገቶ፡ በእልፍ። በመጥባሕትከ፡ ዕልገትከ። ያነብሮሙ፡ በዕልገቶሙ፡ መልዕልተ፡(፩ነገ፡ ፲፰፡ ፳፭። ፪ነገ፡ ፳፫። ሚራ፵፯፡ ፮። ዘዳ፴፫፡ ፳፱። ኢዮ፴፮፡ ፯)።

**ዐልጋ፤** በቁሙ፤ መተኛ፤ ትእምርተ፡ ክብር።

**ዐልጌን፤** ተራዳ፤ ረዥም፡ ዕንጨት፤ የሰው፡ መስቀያ። አዘዘ፡ አርያኖስ፡ ከመ፡ ይስቅልዎ፡ በዐልጌን፡ ወይንድፍዎ፡ በአሕጻ፤ ወአልቦ፡ ዘለከፎ፡(ስንክ፡ የካ፳)።

**ዐለደ፤—አከማቸ፤—አልዶ፡ አለደ።**

**ዐሊው፤ ዎት፤(ዐለወ፡ የዐሉ፡ ይዕሉ፤ ዐለየ። ዕብ፡ ዐዌል። ሱር፡ ዑል። ዐረ፡ ዓል)፤** መቀበል፤ ማስተጋባት፤ የሰሙትን፡ ዜማ፡ መልሶ፡ መጮኽ፤ መናገር። የገደል፡ የተራራ፤ የተመሬ፡ የደብተራ። ድምፀ፡ ቃል፡ ዘአድባር፡ መፍርሃን፡ እስ፡ ያወሥኡ፡ ወየዐልዉ፡ ድምፀ፡ በበይናቲሆሙ። ወእኮ፡ ይባቤ፡ አድባር፡(ጥበ፲፯፡ ፲፰። ሕዝ፯፡ ፯)።

—፤ መወንጀል፡ መበደል፤ ልብን፡ ሐሳብን፡ ወደ፡ ክፉ፡ መመለስ፤ ውልን፡ መሐላን፡ ቃል፡ ኪዳንን፡ ማፍረስ፤ መሸፈት፡ መሸፈጥ፡ መክዳት፡ መካድ፤ ዐሎ፡ ማለት። ይህ፡ ኹሉ፡ የወንጀል፡ ስልት፡ ነው። ዘዐለወ፡ በወግዝ። ዐለዉ፡ ልቦሙ፡ ከመ፡ ኢየኀልዩ። ዐለዉ፡ ሕገከ። ዐለዉ፡ ኪዳንየ። ዐለወ፡ ሕዝበ፡ እስራኤል፡ እምቤተ፡ ዳዊት። ዐለወቶ፡ ለምታ። ዐለዎ፡ ሴዴቅያስ፡ ለንጉሠ፡ ባቢሎን። ኵልክሙ፡ ተዐልዉኒ፡(፩ዜና፡ ፪፡ ፯። ኢሳ፶፱፡ ፲፭። ዳን፯፡ ፲፩። ሆሴ፰፡ ፩። ፪ዜና፡ ፲፡ ፲፱። ሚራ፳፫፡ ፳፫። ኤር፶፪፡ ፫። ማቴ፳፯፡ ፴፩)።

—፤ ምክርን፡ ትምርትን፤ መልክን፡ ጠባይን፡ መለወጥ፤ መገልበጥ። ዐልዋ፡ እግዚአ፡ ለምክሩ። ይፈቅዱ፡ ይዕልዉ፡ ትምህርቶ። እከዩሃ፡ የዐልዎ፡ ለራእያ፡(፪ነገ፡ ፲፭፡ ፴፩። ገላ፩፡ ፯። ሚራ፳፩፡ ፲፯)።

**ዐሊው ፤** መፈጸም ፣ መምላት ፤ መተው ፤ የ ሥራ ፣ የሹመት ። መቅዳት ፣ መገልበጥ ፤ መተርጐም ፣ መመለስ ፤ ከመጽሐፍ ፣ ወደ ፣ መጽሐፍ ፤ ከቋንቋ ፣ ወደ ፣ ቋንቋ ። መጽሐፍ ፣ ግን ፣ በዐለወ ፣ ፈንታ ፣ ኹሉንም ፣ አዕለወ ፣ ይላል ፤ አድራጊውን ፣ ባስደራጊ ፣ አንቀጽ ፣ **እለ ፡ አዕለዉ ፡ ምግቦሙ ፡ በንጽሕ ። አዕሉ ፡ እንከሰ ፡ ወን ትኅሉብ ፡ ምግበከ ፡** (ቅዳ ፣ ዮሐ ። ሉቃ፲፯ ፣ ፱) ። **አን በበ ፡ ዘውስቴታ ፡ ወአዕለዋ ። ፈነውነ ፡ ለከ ፡ አዕሊወነ ። ሀብኒ ፡ መጽሐፈ ፡ ከመ ፡ ኣዕልዎ ፤** ቀዳ ። **አስተሐ መመ ፡ አዕልወቶ ። አዕለዋ ፡ እምልሳነ ፡ ጽርእ ፡ ኀበ ፡ ልሳነ ፡ ዐረቢ ። ወዘአዕለዋ ፡ ሕጹጽ ፡ ወኀጥእ ፡** (ኩፋ ፣ ፰ ። ተረ ፣ ቄር ። ሄርማ ። ፊልክ ። አፈ ፣ ወር ። ፍ ፣ ነ) ።

**ዐላዊ ፤ (ዊት ፡ ውያን ፡ ያት) ፤** ወንጀለኛ ፤ እንቢተኛ ፤ ሽፍታ ፤ ለዋጭ ፤ ገልባጭ ፤ መላሽ ። **ዐላዌ ፡ ነጋሢ ። ወአእመሮ ፡ ከመ ፡ ዐላዊ ። ዐላውያነ ፡ ጽድቅ ፡** (ዮሐ፲፱ ፣ ፲፪ ። ቲቶ፫ ፣ ፲፩ ። ሮሜ፪ ፣ ፰) ። በዐላዊ ፣ ፈ ንታ ፣ አዕላዊ ፣ ይላል ፤ የተሳሳተ ፣ ነው ። **ወአዕላዊሁኒ ፡** (ፍ ፣ ነ) ።

**አዕለወ ፤ (አስደራጊ) ፤** አስወንጀለ ፤ አስከዳ ፤ አስካደ ፣ ዐሎ ፣ አስኘ ፣ አስለወጠ ። **ዘአዕለዎሙ ፡ ለሕ ዝብ ፡ በምክሩ ። ያዐልዎሙ ፡ ለሕዝብነ ። ሶበ ፡ አዕለ ውዎ ፡ ለሃይማኖት ፡** (ሚራ፵፯ ፣ ፳፫ ። ሉቃ፳፫ ፣ ፪ ። ክብ ፣ ነገ) ።

—፤ አስፈጸመ ፤ አስተወ ። አስቀዳ ፤ አስመለሰ ። ምስክሩን ፣ በዐሊው ፣ ተራ ፣ ተመልከት ።

**አዕላዊ ፤** የሚያስክድ ፤ የሚያስከዳ ። የሚያስተ ረጕም ፣ የሚያስቀዳ ።

**ተዐልወ ፤** ተከዳ ፤ ተካደ ፤ ተጣለ ። **አመ ፡ ይ ትዐለዉ ፡ ሰብእ ፡ ኅያላን ፡** (መክ፲፪ ፣ ፫) ።

—፤ ተለወጠ ፤ ሌላ ፣ ኾነ ። **እምነግሀ ፡ እስከ ፡ ሠርክ ፡ ትትዐለው ፡ መንበርት ፡** (ሚራ፲፰ ፣ ፳፮) ።

—፤ ተቀበለ ፤ የሀብት ፣ የትምርት ። **ወተዐልዉ ፡ ነቢያት ፡ እምኔሁ ። ትምህርት ፡ ዘመሀርኩክሙ ፤ ዘከመ ፡ ተ ዐሎክሙ ፡** (ሚራ፵፰ ፣ ፰ ። ፩ቆሮ ፣ ፲፭ ፣ ፩) ።

—፤ ተቀዳ ፤ ተመለሰ ፤ ተተረጐመ ። **እምነ ፡ ዐረቢ ፡ ለ ግእዝ ፡ መጻሕፍት ፡ ተዐልዋ ። ወመክብበ ፡ መጻሕ ፍትሰ ፡ ዘብሉይ ፡ ተዐልዋ ፡ እምዕብራይስጢ ፡ ኀበ ፡ ግእዝ ፡** (ስንክ ፣ ነሐ፳ ። መጽ ፣ ምስ) ። የግእዝ ፣ ብሉ ያት ፣ በዘመነ ፣ ብሉይ ፣ ከዕብራይስጥ ፣ ተቀድተዋል ፣ ማ ለት ፤ ሳይከከና ፣ ሳይበከ ፤ ሳይጋገር ፣ ምጣድ ፣ ሳይነካ ፤ እምኀበ ፣ አልበ ፣ የተገኘ ፣ የሕልም ፣ እንጀራ ፣ ነው ፤ ት ምርት ፣ ቀስቅሶት ፣ ከንዋመ ፣ ሀኬት ፣ ለነቃው ፣ ለዛሬ ፣ ዘመን ፣ ልጅ ፣ አያጠግብም ።

**ዕልው ፤ (ዋን ፡ ዋት ፡ ሉት) ፤** የወንጀለ ፤ ዐመፀኛ ፤ ክፉ ፤ ጠማማ ፤ ልውጥ ፤ ከሓዲ ። **ንጉሥ ፡ ዕ ልው ። ትውልድ ፡ ዕሉት ። ለዕልዋን ፡ ዕልወ ፡ ፍኖት ፡ ይፌኑ ፡ ሎሙ ። ዕልዋነ ፡ ሃይማኖት ። ዕልዋን ፡ ወመ ናፍቃን ፡** (ስንክ ፣ መጋ፰ ። መዝ ፣ ፸፯ ። ምሳ፳፩ ፣ ፰ ። ዲድ ፣ ፴፫ ። ቀሌ) ።

**ዕልወት ፤ (ታት) ፤** መወንጀል ፤ መለወጥ ፤ ወንጀል ፤ ዐመፅ ፤ ክዳት ፤ እንቢታ ፤ እደጋ ፣ ጥፋት ። **እ ስመ ፡ ዕልወተ ፡ ሕግ ፡ ውእቱ ፡ ዝ ፡ ግብር ። አዝማነ ፡ ዕልወታት ። ንትሉ ፡ በዕልወትነ ። ትበጽሖሙ ፡ ዕልወ ቶሙ ። እምኀበ ፡ እግዚ ፡ ኮነት ፡ ዕልወት ፡ አኪዝያስ ፡** (ዲድ ፣ ፲፭ ። ስንክ ፣ ነሐ፳ ። ኤር፲፰ ፣ ፲፪ ። ኢዮ፳፩ ፣ ፲፯ ። ፪ዜና ፣ ፳፪ ፣ ፯) ።

—፤ መቅጃ ፤ መዝገብ ፤ ረቂቅ ፤ መዠመሪያ ፣ የወጣ ፣ መጽሐፍ ። ወይም ፣ ቅጅ ፤ ግልባጭ ፤ ከዚያው ፣ ከም ንጭ ፣ የተቀዳ ፤ የቅጅ ፣ ቅጅ ፣ ያይደለ ። **ሀሎ ፡ ኀቤነ ፡ ዕልወቱ ፡ ለውእቱ ፡ መጽሐፍ ፡** (ተረ ፣ ቄር፲፭) ።

**ዐልው ፤ ዓልዋ ፤ (ጽር ፤ አልዎይ ። ሱር ፡ ዐልዋይ ። ዕብ ፡ አሃል ። ዐረ ፡ ዑድ) ፤** ሽቱ ፤ የሽቱ ፣ ስም ፤ ዋግራ ፤ ሬት ። **ከርቤ ፡ ወዐልው ። ዕፀው ፡ ዘዓልዋ ፡** (ማሕ፬ ፣ ፲፬ ። ሔኖ፴፩ ፣ ፪ ። ዮሐ ፲፱ ፣ ፴፱) ።

**ዐለየ ፤ (ዐለወ) ፤** ወንጀለ ፤ ሸፈተ ፤ ዐሌ ፣ አለ ፤ እንቢ ፣ አለ ፤ ጠመመ ፤ ለገመ ። ወና ፣ የ ፣ ተወራራሾች ፣ ስለ ፣ ኾኑ ፣ በዐለወ ፣ ፈንታ ፣ ዐለየ ፣ ይላል ። **ዐለዩ ፡ ወ ሚጡ ፡ ልቦሙ ፡** (ግብ፯ ፣ ፴፱) ።

**ዕሉይ ፤** ወንጀለኛ ፤ ክፉ ፣ ወስላታ ። **አ ፡ አ ብድ ፡ ወዕሉየ ፡ ኅሊና ፡** (መቃ) ።

**ማዕሌት ፤** ወንጀል ፤ ግፍ ፣ በደል ፤ አሉታ ፤ እ ንቢታ ፤ ኀጢአት ፤ ክፋት ። **ማዕሌተ ፡ ሀገር ። በማዕሌ ቶሙ ፡ ዘዐለዉከ ። መልአከ ፡ ማዕሌት ። ከመ ፡ ይኅ በር ፡ ማዕሌቶሙ ። ማዕሌተ ፡ ይገብር ፡ ላዕሌከ ፡ ዓ ሞጽ ፡** (ሚራ፳፯ ፣ ፭ ። ዳን፱ ፣ ፯ ። ፫ነገ ፣ ፲፩ ፣ ፲፱ ። ሆ ሴ፯ ፣ ፱ ። ዓሞ፯ ፣ ፲፩) ።

**ተማዕለየ ፤ (ዲ ፡ ቃ ፡ ግ) ፤** ዐለየ ፤ ዐለወ ፤ ወ ንጀለ ። **ተማዕለዩ ፡ ሎቱ ፤ ሖሩ ፡ ይትማዕለይዎሙ ፡** (መቃ) ።

**መምዕላይ ፤** ወንጀለኛ ፤ ሽፍታ ፤ ወያኔ ፣ አረ መኔ ፣ ክፉ ፣ ጨካኝ ። **ንጉሥ ፡ ዘእንበለ ፡ ሕግ ፡ ኢን ጉሥ ፡ ውእቱ ፤ አላ ፡ መምዕላይ ። ሰበርከ ፡ ስነኒሁ ፡ ለመምዕላይ ፡ ንጉሠ ፡ ገሃነም ፡** (መጽ ፣ አዳር ፣ ፶ ። ግ ንዘ) ። መዐለን ፣ ተመልከት ፤ የዚህ ፣ ወንድም ፣ ነው ።

**ዐልሎ ፤ ሎት ፤ (ዐለለ ፡ ይዔልል ፡ የዐ ልል ። ዕብ ፡ ዐላል ፤ ጽኑ ፡ ሥራ ፡ ሠራ) ፤** ማለል ፤ ዐለላ ፣ ቀለም ፣ ማግባት ፤ መንከር ። **አዘዘ ፡ ከመ ፡ ኢይልበሱ ፡ ክርስቲያን ፡ ወአይሁዳውያን ፡ ልብሰ ፡ ጸዐዳ ፡ ግሙራ ፤ አላ ፡ የዐልሉ ፡ ልብሶሙ ፡ በኒል ፡** (ስንክ ፣ ኅዳ፳፩) ።

—፤ መውገዝ ፤ መለየት ፤ ሕርም ፣ ማለት ፤ ለገዳም ፣ ለ ቤተ ፣ ክሲያን ፣ ጕልት ፣ መጕለት ። **እምዘዐለልዎ ። አ ዐልሎ ፡ ሎቱ ፡ ወለአህጉሪሁ ፡** (ዘሌ፲፱ ፣ ፵፯ ። ዘኍ ፳፩ ፣ ፪—፫) ።

**ተዐለለ ፤ (ተዐለ) ፤** ታለለ ፤ ተለየ ፤ ተጕለተ ። **እጼሊ ፡ ከመ ፡ አነ ፡ እትዐለል ፡ እምክርስቶስ ፡** (ሮ ሜ፱ ፣ ፫) ።

**ዕሉል፤(ላን፡ላት፡ልልት)፤** የተለየ፤ልዩ፤ ውጉዝ፤ ብቸኛ ። ይኩን፡ዕሉለ ። ይሰመዩ፡ፈሪሳው ያን፡ ወትርጓሜሁ፡ ለዝ፡ስም፡ ዕሉላን፡(ዮሴፍ)።

—፤ የታለለ፤ ቀለም፡ የገባ ። አልባስ፡ ምሥዋዕ፡ ይኩኑ፡ጽዕድዋነ፤ወአኮ፡ዕሉላነ፡በዘዘ፡ዚኣሁ፡ሕብራት፡(ፈ፡መ፡፴፩፡፩)።

**ማዕለል፤** ዐለላ፤ ማለያ፤ ቀለም፤ ብዙ፡ ዐይነት፡ ያለው ። ኢትሠአን፡አማኢነ፡ዕሉለ፡በማዕለል፤ ወኢሕልቀተ፡ ወርቅ፡ ውስተ፡ አዲብዲክ፡(ፍ፡ነ፡፲፭)።

**ማዕለልት፤** ጕልት፤ገንዘብ፤ምሎ፡ተፈጥሞ፡ ሕርም፡ ይኹንብኝ፡ብሎ፡የሰጡት ። ወሰመዩ፡ስሞ፡ ለውእቱ፡መካን፡ማዕለልት፡(ዘኍ፳፩፡፫)።

**ዐልሞ፤ ሞት፤(ዐለመ፡ ይዔልም፡ የዐልም፤ ዐረብ)፤** ማለም፤ ማመልከት፤ ስምን፡ መጣፍ፡ ማተም፤ መፈረም ። በቅድመ፡እለ፡ቀሙ፡ወዐለሙ፡ውስተ፡ይእቲ፡ መጽሐፍ፡(ኤር፴፱፡፲፱)።

—፤ ማስተማር፤ መስበክ፤ መንገር ። አበው፡ ናሁ፡ ዐለሙ፤ወሰመዩ፡ትሕትና፡በአስማት፡ ሠናያት፡ወትእምርት፡ትርፍት፡(ፊልክ፡፪፶፱)።

**መዐልም፤(ዐረ፡ሙዐሊም)፤** መምህር፤ ሰባኪ፤ አስተማሪ፤ ሊቅ፡(አዋል)።

**ተዐለመ፤** ተመለከተ፤ ባለምልክት፡ ኾነ ። ተጣፈ፡ ተነገረ፤ ትምርቱ ። ተማረ፤ ትምርት፡ ገባው፤ መዐልም፡ ኾነ፤ ሰውየው ።

**ዐላማ፤(ትግሬ፡ዐለመት)፤** በቁሙ፤ ምልክት፤ ባንዲራ ። ሰንደቅን፡ ተመልከት፡(ዐማርኛ)።

**ተዐልመ፤(ዕብ፡ሄዓሌም)፤** ዕልም፡ አለ፤ ታባ፡ ተሰወረ፤ ከመታየትና፡ ከመታወቅ ።

**ዕሉም፤** ዕልም፡ ያለ፤ ኅቡእ፡ ረቂቅ፤ ስዉር፡ ድብቅ ። መጽሐፍ፡ ግን፡ በዕሉም፡ ፈንታ፡ ዓለም፡ ይላል ። ወዓለምነሂ፡ ውስተ፡ ብርሃነ፡ ገጽከ፡(መዝ፡፹፱)።

**ዓለም፤(ዕብ፡ ቴቤል ። ዐረ፡ መስኩነት)፤** በቁሙ፤ ዓለመ፡ ሰብእ፤ ሰው፡የሚኖርበት፡ ምድር፡ መሬት፤ የአዳም፡ ክፍል፤ የልጆቹ፡ በታ ። ለእግዚ፡ ምድር፡በምልኣ፤ዓለምኒ፡ወዙሉሙ፡እለ፡



ዓለም፡

ይነብሩ፡ውስቴታ፡(መዝ፡፳፫ ። ኢሳ፲፱፡፲፯ ። ፴፱፡፩ ። ኩፋ፡፩)።

**ዓለም፤(ማት)፤ ዐረብ ። ዕብ፡ ዖላም ። ሱር፡ ዓላም)፤** ጊዜ፤ ዘመን፤ ትውልድ፤ ያለፈ፤ ቅድም፤ ጥንት፤ ትካት፤ ወይም፡ ወደ፡ ፊት፡ የሚመጣ፡ ወራት፤ ወትር፤ ዘልፍ፤ ድንት፤ መቼም፡ መች፤ የሰው፡ ዕድሜ፤ መዋዕለ፡ሕይወት ። በከመ፡ መዋዕለ፡ዓለም ። ወለዓለምኒ፡ ቀደምት ። ከነ፡ አርኣያ፡ ለዓለም፡ ከመ፡ይነስሑ ። ነቢያት፡እለ፡እምዓለም፡(ሚክ፯፡፲፬ ። ፪ጴጥ፡፪፡፭ ። ሚሬ፵፱፡፲፯ ። ግብ፫፡፳፩)።

—፤ ፍጥረት፤ ዘመደ፡ ፍጥረት፤ እግዜር፡ ከእሑድ፡ እስከ፡ ዐርብ፡ የፈጠረው፤ ሰማይ፡ ከነዜጋው፤ ምድር፡ ከነመንጋው ። ወይም፡ ሰማይ፡ ከነግሡ፡ ከነደመናው፤ ምድር፡ ከነልብሱ፡ ከነጕተናው ። እምፍጥረተ፡ ዓለም ። እምቅድመ፡ዓለም ። ሰማያት፡ወምድር፤ምስለ፡ዙሉ፡ዓለሞሙ፡(ኢዮ፫፡፲፰ ። ቅዳ፡ዲዮ ። ግሩ)።

—፤ ሰው፤ የሰው፡ ነገድ፤ ነፍስ፡ ያለቸው፡ ሥጋ ። ወፀአ፡ ትእዛዝ፡ ከመ፡ ይጸሐፍ፡ዙሉ፡ዓለም ። ዓለምኒ፡ቦቱ፡ኮነ፤ ወዓለምሰ፡ ኢያእመሮ ። ዝንቱ፡ዓለም፡(ሉቃ፪፡፩ ። ዮሐ፩፡፲ ። ሮሜ፭፡፩)።

—፤ ከተማ፡ መዲና፤ ሹመት፡ ብዕል፤ ሥጋዊ፡ አኗዋር ። ነበረ፡ውስተ፡ዓለም፡ እምቅድመ፡ ይመንኵስ፤ዕሥራ፡ዓመተ ። ፈለሱ፡ ገዳመ፡ወመነኑ፡ ዓለመ፡(ስንክ፡ ሐምሌ ። ቀሌ)።

**ዓለማዊ፤** የዓለም፤ ዓለመኛ፤ ዘመናይ፤ ሥጋዊ፤ ሕዝባዊ፤ ካህን፡ መነኰሴ፡ ያይደለ ። ብዕል፡ ዓለማዊት ። ደብተራ፡ዓለማዊ ። ግብራት፡ ዓለማውያት ። እመሂ፡ ካህን፡ወእመሂ፡ዓለማዊ፡(ፈ፡መ፡፲፰፡፩ ። አፈ፡ ድ፲፩ ። ፊልክ፡፫ ። ቀሌ)።

**ገዘ፡ዓለም፤** በታ፤ዘመን፤ ዓለመ፡ ሥጋ፤ ሰው፡ እስከ፡ ሞትና፡ እስከ፡ ምጽአት፡ የሚኖርበት ።

**ዓለም፡ ዘይመጽእ፤** ዓለመ፡ነፍስ፤ ከሞትና፡ ከኅልፈት፡ በኋላ፡ የሚመጣው ። ኢበዝ፡ ዓለም፤ ወኢበዘይመጽእ፡(ማቴ፲፪፡፴፪)።

**ለዓለም፤(ዕብ፡ ልዖላም)፤** ለወትሮ፤ ለዘላለም ። ለዝሉፉ፤ ዘልፈ፤ ወትረ፤ በኵሉ፡ ጊዜ፤ በኵሉ፡ ዘመን ። ፍጻሜ፡ ላለውም፡ ለሌለውም፡ ኹሉ፡ ይነገራል፤ እንደ፡ እስከ፡ ነው ። ፍጻሜ፡ ላለው፡ ሲነገር፤ ምድርሰ፡ ለዓለም፡ትቀውም ። ኢይትሀወክ፡ ለዓለም፤ እነብር፡ቤተከ፡ለዓለም፡ ይላል፡(መክ፩፡፬ ። መዝ፡ ፷፬)። ፍጻሜ፡ ለሌለው፡ ሲነገር፤ቦኑ፡ለዓለም፡አሐዩ ። ቦኑ፡ለዓለም፡ ይነብር፡መዐቱ ። አኮ፡ለዓለም፡ዘእትመዐዕ ። ወይነግሥ፡ለቤተ፡ ያዕቆብ፡ለዓለም፡(ኢዮ፯፡፲፮ ። ኤር፫፡፭ ። ኢሳ፶፯፡፲፮ ። ሉቃ፩፡፴፫)።

—፤ አካቶ፤ ፈጽሞ፤ በውነት፤ መቼም፡ መች ። አንስ፡ ኢየዐልወከ፡ ግሙራ፡ ባለው፤ ለዓለም፤ እንዲል፡(ማቴ፳፮፡፴፫)። ኢይትሀወክ፡ ለዓለም፡ ያለውም፡ እንደዚህ፡ ሊፈታ፡ ይቻላል ።

**ለዓለመ፡ ዓለም፤** ዝኒ፡ ከማሁ፤ ለዘላለም ። ይህ፡ ግን፡ ዕጥፍ፡ ድርብ፡ ቃል፡ ስለ፡ ኾነ፤ ተለ

ይቶ ፡ ፍጻሜ ፡ ለሌለው ፤ ለማይጨረስ ፡ ይነገራል ። ኢይጠፍእ ፡ ለዝሉፉ ፡ ወለዓለመ ፡ ዓለም ። ወደምሰስከ ፡ ስሞሙ ፡ ለዓለመ ፡ ዓለም ። መንበርከ ፡ እግዚኦ ፡ ለዓለመ ፡ ዓለም ፡ (ሚራ፹፱ ፡ ፱ ። መዝ ፡ ፱ና ፡ ፵) ።

**ዘለዓለም** ፤ ዝኒ ፡ ዓዲ ፡ ከማሁ ፤ በቁሙ ፡ ዘላለም ፤ ለወትሮ ፡ የሚኖር ፤ ኅልፈት ፡ ፍጻሜ ፡ የሌለው ። እግዚአብሔር ፡ ዘለዓለም ። መንግሥቱ ፡ ዘለዓለም ። ሠናኔ ፡ ዘለዓለም ፤ ሕይወት ፡ ዘለዓለም ፡ (ቅዳ ። ዳንኤ ፡ ፩፫ ። ፲፱ ፡ ፱ ። ማቴ፳፱ ፡ ፵፮) ።

**ዘለዓለማዊ** ፤ የዘላለም ፤ ቀዋሚ ፡ ነዋሪ ፤ ኀላፊ ፡ ያይደለ ። ምጽላላቲሆሙ ፡ ዘለዓለማዊት ፡ (ፊልክ ፡ ፫) ።

**እስከ ፡ ለዓለም** ፤ ዝኒ ፡ ዓዲ ፡ ከማሁ ፤ እስከና ፡ ለ ፡ አንድ ፡ ወገን ፡ ናቸው ፤ የሚመጣን ፡ ጊዜ ፡ ያሳያሉ ። እስከ ፡ ዘላለም ፤ እስከ ፡ ወትሮው ፤ እስከ ፡ መቼም ፡ መች ። እምቅድመ ፡ ዓለም ፡ ወእስከ ፡ ለዓለም ፡ አንተ ፡ ክመ ፡ (መዝ ፡ ፹፱ ። ቅዳ ፡ ዲዮ) ።

**ዐላሞት** ፤ (ዕብራ) ፤ ንዋየ ፡ ማሕሌት ፤ የበገና ፡ ስም ፤ አንድ ፡ ዐይነት ፡ በገና ፤ ባለስድስት ፡ አውታር ። ላዕለ ፡ ዐላሞት ፡ (፩ዜና ፡ ፲፭ ፡ ፳) ።

**ዐለቅት** ፤ (ዕብ ፡ ዐሉቃህ ። ሱር ፡ ዓላቅታእ ። ዐረ ፡ ዐለቀት) ፤ ዐልቅት ፤ የትል ፡ ዐይነት ፤ ከውሃ ፡ ከረግረግ ፡ የሚገኝ ፤ የሚነክስ ፡ የሚጣበቅ ፤ ከያዘ ፡ የማይለቅ ፤ ደም ፡ የሚመጥ ፡ የሚመጠምጥ ፤ ውጋት ፡ ቍርጥማት ፡ ያለበት ፡ ሰው ፡ እንዳጋሚና ፡ እንደ ፡ ዋጋምት ፡ የሚሻው ፡ የሚያስፈልገው ። ለዐለቅት ፡ ባቲ ፡ ሠላስ ፡ አዋልድ ፡ (ምሳ፴ ፡ ፲፭) ።



ዐለቅት ፡

**ዐለስ** ፤ (ዐረብ) ፤ ዐኝ ፤ የስንዴ ፡ ዐይነት ፤ ፍሬው ፡ ቀጫጭን ፤ ቅንጣቱ ፡ ቀጠጠ ፡ እንደሚባል ፡ ማሽላ ፡ በያንዳንዱ ፡ ቂንድ ፡ መንታነት ፡ ያለው ። ጣዕሙና ፡ መልኩ ፡ የስንዴ ፡ ወገን ፡ ስለ ፡ ኾነ ፤ መጽሐፍ ፡ በሥርናይ ፡ ፈንታ ፡ ዐለስ ፡ ይላል ፤ የመላሽ ፡ ስሕተት ፡ ነው ፡ (ሉቃ፳፱ ፡ ፴፩ ። ዲድ ፡ ፴፩) ። ሕንፈጽን ፡ ተመልከት ።

**ዓም** ፤ (ዐረብ) ፤ ዓመት ፤ ዘመን ፤ ብዙ ፡ ቀን ፡ የዕለታት ፡ ድምር ፤ ዐውዳቸውና ፡ ቀመራቸው ፤ ፫፻፷፭ ፡ ዕለት ፡ ከዕለት ፡ ርቦ ፤ በውስጡ ፡ አራት ፡ ክፍሎች ፤ ዐሥራ ፡ ኹለት ፡ ወሮች ፡ ያሉት ። ሥሩና ፡ ምንጩ ፡ ዐመመ ፡ ነው ፤ በአልፍ ፡ ሲጣፍ ፡ ግን ፡ እመምና ፡ ገዝም ፡ ያሳያል ። በውእቱ ፡ ሳብዕ ፡ ዓም ። በሣልስ ፡ ዓም ፡ እምዘነግሠ ። በዙሉ ፡ ዓም ፡ ወዓመት ። ዓም ፡ እምዓም ። ዓመ ፡ ከመ ፡ ዮም ። እመ ፡ ትፈሪ ፡ ለዓሙ ፡ (ዘሌ፳፭ ፡ ፳ ። አስቴ፩ ፡ ፫ ። ኩፋ ፡ ፺ና ፡ ፴፱ ። ዘፍ፲፰ ፡ ፲ ። ሉቃ ፲፫ ፡ ፬) ።

**ዓመት** ፤ (ታት) ፤ በቁሙ ፤ ዝኒ ፡ ከማሁ ። በቀዳሚ ፡ ዓመተ ፡ መንግሥቱ ። ትመውት ፡ በዝንቱ ፡ ዓመት ። ምእት ፡ ወኀምሳ ፡ ዓመት ፡ ሎቱ ። ዓመታተ ፡ ብዙኀ ፡ ሐይወ ። ኍልቈ ፡ ዓመታቲከ ፡ (ዳን፺ ፡ ፩ ። ኤር፴፩ ፡ ፲፮ ። ጦቢ፲፱ ፡ ፲፩ ። ኢዮ፴፰ ፡ ፳፩) ።

**ዓመተ ፡ ዓለም** ፤ ከጥንት ፡ ከፍጥረት ፡ ከአዳም ፡ ዠምሮ ፡ ያለው ፡ ዘመን ።

**ዓመተ ፡ ሥጋዌ** ፤ ቃል ፡ ሥጋ ፡ ኹኖ ፡ ከተወለደበት ፤ ዓለም ፡ በሐዲስ ፡ ተፈጥሮ ፡ ከተፈጠረበት ፤ ከዳግማይ ፡ አዳም ፡ ከክርስቶስ ፡ ወዲህ ፡ ያለው ፡ ዘመን ።

**ዓመተ ፡ ምሕረት** ፤ ዝኒ ፡ ከማሁ ፤ የይቅርታ ፡ ዘመን ፤ ዘመነ ፡ ሥጋዌ ።

**ዐምበር** ፤—ሽቱ ፤—ዐንበር ።

(ጥ) **ዐምዶ** ፤ ዶት ፤ (ዐመደ ፡ ይዔምድ ፡ የዐምድ ። ዕብ ፡ ዐማድ ፤ ቆመ ፡ ቀጥ ፡ አለ) ፤ መደገፍ ፤ ማስደገፍ ፤ ማቆም ፡ ማጽናት ፤ ማሸራሸት ፤ እንዳይወድቅ ፡ እንዳይነቃነቅ ፡ ማድረግ ። ረበቦ ፡ ከመ ፡ ሠቅ ፡ ወበነፋስ ፡ ዐመዶ ፤ በኪኑ ፡ ዐመዶ ፡ ለሰማይ ፡ በነፋስ ። ይዌስን ፡ ቦኖዳ ፡ ወይዔምድ ፡ በነፋስ ። ዘዐመድካ ፡ ለምድር ፡ በሥላሴከ ፡ (መቃ ። ቅዳ ፡ ግሩ ። ድጓ) ። ባለቅኔዎች ፡ ግን ፡ ፈጠረ ፡ ብለው ፡ ይጨምሩበታል ።

**ዐማዲ** ፤ የሚደግፍ ፤ ደጋፊ ፤ የሚያቆም ፡ የሚያጸና ። ዐማዴ ፡ ሰማይ ፡ ወምድር ፡ (ሊጦን) ።

**ዐምድ** ፤ (ዕብ ፡ ዐሙድ ። ሱር ፡ ዓሙዳእ ። ዐረ ፡ ዐሙድ ፤ ዒማድ) ፤ በቁሙ ፤ ዋና ፤ ቀዋሚ ፤ ተሸካሚ ፤ ድጋፍ ፤ ባላ ፤ ምሰሶ ፡ ወጋግራ ፤ ተራዳ ፤ ቅልጥም ፡ አገዳ ፤ ጣያት ፤ ሐውልት ፤ የመጽሐፍ ፡ ገጽ ። ዐምደ ፡ ኀጺን ። ዐምደ ፡ ሰኖባር ። ዐምደ ፡ ሐመር ። ዐምደ ፡ ጾም ፤ ዘውእቱ ፡ አርብዓ ፡ ዕለት ። ዐምዳ ፡ ወአብራዊሃ ። ዐምደ ፡ ሀገረ ፡ ፀሓይ ፡ (ኤር፩ ፡ ፲፰ ። ስንክ ፡ ሐም ፡ ፩ና ፡ ፳፱ ። አቡሻ ፡ ፳፺ ። ዘፀ፳፭ ፡ ፴፩ ። ኤር፵ ፡ ፲፫) ። ሉሕ ፡ ጠርብ ፡ ሳንቃ ፡ ሰሌዳ ፡ በማለት ፡ ፈንታ ፡ ዐምድ ፡ ይላል ፤ ቀዋሚነቱን ፡ ሲያይ ፡ (ዘፀ፳፮ ፡ ፳፫—፳፱) ።

**አዕማድ** ፤ ዐምዶች ፤ ድጋፎች ፤ ቋሞች ፡ ተሸካሞች ፤ የእግር ፡ አገዶች ። አዕማደ ፡ ዘንድቅ ፡ ወአዕማደ ፡ ዘእብን ። አዕማደ ፡ ወርቅ ፡ እለ ፡ ይቀውሙ ። ጸጸሳት ፡ ኄራን ፡ ዘይብልዎሙ ፡ አዕማድ ። አዕማደ ፡ እግር ፡ (ሥር ፡ አኵ ። ሚራ፳፯ ፡ ፲፰ ። ስንክ ፡ ጥር፯ ። ፩ነገ ፡ ፲፯ ፡ ፯) ።

—፤ የግስ ፡ ነገዶች ፤ ወይም ፡ ጸዋትወ ፡ ግስ ። እሊሁም ፡ አድራጊ ፡ አስደራጊ ፡ ተደራጊ ፡ ተደራራጊ ፡ አደራራጊ ፡ ናቸው ፤ ቀተለን ፡ ተመልከት ።

**ዐምዳዊ፤ዘዐምድ፤** የዐምድ፡ሰው፤እንደ፡ ዐምድ፡ ቋሞ፤ በዐምድ፡ ራስ፡ ላይ፡ ማማ፡ ሠርቶ፤ ወይም፡ ከምዱ፡ ጋር፡ ታስሮ፡ ተቈራኝቶ፡ የሚኖር። ስምዖን፡ዐምዳዊ። አጋቶን፡ዘዐምድ፡(ፊልክ፡፵፮። ስንክ፡መስ፲፱)።

**ምዕማድ፤(ዳት፤መዓምድ)፤** ማቆሚያ፤ የዐምድ፡ እግር፤ ስክተት፤ መሠረት። ሰመንቱ፡ አዕማድ፤ወምዕማዶሙኒ፡ዘብሩር፡ዐሥርቱ፡ወስድስቱ፤ወሰለ፡አሐዱ፡ዐምድ፡በበ፡ ክልኤ፡ ምዕማዲሁ። ወበእንተ፡ዝ፡ ፈቀደ፡ ያስተዳንዕ፡ ምዕማዲሁ፡(ዘፀ፴፯፡፳፭። አፈ፡ድ፫)።

**ዐምሐራ፤—ዐማራ፤—ዐመመ።**

**ዐመ፤ዐመመ፤(ዐረ፡ዓመ። ዕብ፡ዐሜም)፤** ጠቈረ፡ ጨለመ፤አደፈ፡ ጐደፈ፤ ደፈረሰ። በዛ፡ ጸና፡ በረታ፤ ጌመን፡ እይ።

**ዐም፤(ዕብ)፤** ሕዝብ፡ ነገድ፤ ብዙ፡ ሰው። ቋንቋውና፡ ሕጉ፡ ግዛቱ፡ መንግሥቱ፡ አንድ፡ የኾነ፤ ጉባኤ፡ ሰብእ፡ ማኅበረ፡ ሰብእ።

**ዐምሐራ፤(ዐም፡ ሐራ)፤** ዐማራ፤ ጨዋ፡ ሕዝብ፤ ነጻነት፡ ያለው፡ ባለነጻ፤ ግዑዝ፡ አግዓዚ። ሐረረን፡ ተመልከት። ወኮነ፡በምድረ፡ዐምሐራ፡(ገድ፡ ተክ)።

**ዐምሐራይ፡ ዊ፤** ያማራ፡ ወገን፤ ልሳን፡ ቋንቋ፤ ዐማርኛ፤ ከዐረብና፡ ከዕብራይስጥ፡ ከግእዝ፡ ከአራም፡ የወጣ።

**ዐምዓም፤(ዐረ፡ ዐም፤ ጅም፤ ቀምቃም፤ ድፍርስ፡ ግም፡ እድፍ፡ ውሃ)፤** ውሃማ፡ ቦታ፤ ማጥ፤ ረግረግ፤ ጭቃው፡ የሚውጥ፤ የሚያሰምጥ። ጽቡረ፡ዐምዓም። አውፅአኒ፡እምውስተ፡ዐዘቅት፡ዐምዓም። ዐምዓሙሰ፡ወዐዘቅቱ። ዐምዓመ፡ ኀጢአት፡(ኢሳ፲፱፡፳፫። መዝ፡፴፱። ባሮክ። ሕዝ፵፯፡፲፩። ግንዘ)።

**ዐማኑኤል፤(ጽር፡ ሄማኑኢል። ዕብ፡ ዒማኑኤል)፤** የሥግው፡ ቃል፡ ስም፤ በኩነት፡ በተዋሕዶ፡ የተሰጠው። ዒማኑ፡ ምስሌነ፤ ኤል፡ አምላክ፤ በተገናኝ፡ አምላክ፡ ምስሌነ፤ ወይም፡ ምስሌነ፡ አምላክ። አምላክ፡ ከኛ፡ ጋራ፡(ማቴ፩፡፳፫። ኢሳ፯፡፲፬)። ሊቃውንት፡ ግን፡ አምላክ፡ ወሰብእ፡ ብለው፡ የምስጢር፡ አፈታት፡ ይፈቱታል። ዐማኑኤል፡ ዘበትርጓሜሁ፡አምላክ፡ወሰብእ፤እስመ፡ውእቱ፡አምላክ፡ በመለኮቱ፤ ወሰብእ፡ በትስብእቱ፡ ዘነሥአ። ወዝ፡ ስም፡ዘውእቱ፡ ዐማኑኤል፡ ዐቢይ፡ጥቀ፡ ወኢይደሉ፡ ፈሊጦቱ፤ወውእቱ፡ ዘበአማን፡ ምስጢር፡ ለጽንዐ፡ሃይማኖት፡(ሃይ፡ አበ፡ ጎርጎ፡ ዘኑ። ሳዊ፡ ዘአን)። ኢየሱስን፡ ተመልከት።

**ዐምዓም፤—ረግረግ፤—ዐመመ።**

**ዐምፆ፤ ፆት፤(ዐመፀ፡ ይዔምዕ፡ የዐምፅ። ዕብ፡ ሐማስ፤ ሐሜጽ)፤** ማመፅ፤ መሸፈት፤ መበደል፤ ክፉ፡ መኾን፤ ግፍ፡ መሥራት፤ መሰረቅ፡ መቀማት። ኢዐመፅነ፡ኪዳነከ። ይዔምፁ፡እግዚ። ወዐመፅክሙ፡ዐስቦሙ፡(መዝ፡፵፫። ሮሜ፫፡፳፭። ያዕ፭፡፬)።

**ዐማፂ፤(ፂት፡ ፅያን፡ ያት)፤** ዐመጠኛ፤ በደለኛ፤ ክፉ፤ ዋሾ። ዐማፂ፡ ወጽልሕው። ዐማፅያነ፡ጸላእኩ፡(መዝ፡፻፲፫። ፻፲፰)።

**መዐምፅ፤(ፅት፡ ፃን፡ ፃት)፤** ዝኒ፡ ከማሁ። ኢትኩን፡መዐምፀ፡(ዘፀ፳፫፡፩። ምሳ፲፱፡፳፰)።

**ዐመፃ፤** ዐመጥ፤በደል፤ግፍ፤ኀጢአት፡ ክፋት፤ ውሸት። ዐመፃ፡ወፅአት፡እመዛግብቲሃ። ልህቀት፡ዐመፃ፡ዲበ፡ምድር። ገበርት፡ዐመፃ፡(ሔኖ። ኩፋ። መዝ፭፻፡፭)።

**ተዐመፀ፤** ተገፋ፤ተበደለ፤ግፍ፡ ተቀበለ። ይትዔመፀ፡ከመ፡ሐሳዊ፡(ተረ፡ ቄር)።

**ዕሙፅ፤(ፃን፡ ፃት፡ ምፅት)፤** የተገፋ፤የተበደለ። ዘከዐወ፡ ደመ፡ዐማፂ፡ላዕለ፡ ደመ፡ዕሙፅ። ዕሙፃን፡(ዮሴፍ። ፊልክ፡፫)።

**ተዓመፀ፤** ተጋፋ፤ተገፋፋ፤ተጣላ፤ግፍ፡ተሣራ፤ ተበዳደለ። ለምንት፡ ትትዓመፁ፡ በበይናቲክሙ። ኅፍረት፡ ተዓምፆ፡ ምስለ፡ ዐርክከ፡(ግብ፯፡፳፮። ሢራ፵፩፡፲፰)።

**አስተዐመፀ፤(አዐመፀ)፤** አሳመጠ፤ አሸፈተ፤ ግፍ፡ አሠራ።

**አስተዓመፀ፤** አባደለ፤አበዳደለ፤አጋፋ፤ግፍ፡ አሣራ።

**ዐሚቅ፤ ቆት፤(ዐመቀ፡ የዐምቅ፡ ይዕምቅ። ዕብ፡ ዐማቅ። ዐረ፡ ዐሙቀ)፤** መታመቅ፤ ዕሙቅ፡ መኾን፤ መጐድጐድ፤ መጥለቅ፤ መሰወር፡ መራቅ፤ ከመታየትና፡ ከመታወቅ። እስከ፡ የዐምቅ፡ ምድሩ፡ከመ፡ግብ። የዐምቅ፡እምነ፡ቀላይ፡ ምክሩ። እምቅድመ፡ ይዕምቁ፡ ቀላያት። እምቅድመ፡ ይዕምቅ፡ ባሕር፡(ገድ፡ ተክ። ሢራ፳፬፡፳፱። ቅዳ፡ አፈ። መጽ፡ ምስ)።

**ዕሙቅ፤(ቃን፡ ቃት፡ ምቅት)፤** በቊሙ፤ የጠለቀ፤ ጥልቅ፤ ወደ፡ ቻች፡ የራቀ፡ ሩቅ፤ኅቡእ፡ ረቂቅ፤ የማይታይ፡ የማይታወቅ፤ ጨለማ፡ ውድቅት። በማይ፡ ልዑል፡ ወምድር፡ ዕሙቅ። ቈላ፡ዕሙቅ። ግብ፡ዕሙቅ። ቀላይ፡ዕሙቅ። ይከሥት፡ ዕሙቃተ፡እምጽልመት። ይመክሩ፡ ዕሙቀ፡ ምክረ። ዘዕሙቅ፡ ከናፍሪሁ። ሌሊተ፡ዕሙቀ፡(ምሳ፳፭፡፫። ሔኖ፳፯፡፫። መዝ፡ ፷፰። ኢዮ፲፪፡፳፪። ኢሳ፳፱፡፲፭። ሕዝቅ፡ ፳። ኪዳ)።

**ዕመቅ፤(ቃት)፤** ጥልቀት፤ ጥልቅነት፤ አጠላለቅ፤ ጥልቅ። ዕመቀ፡ቀላይ። ዕመቃቲሆሙ፡ ለአብሕርት። ዕመቀ፡ ምስጢር። አ፡ ዕመቂሁ፡ ለብዕለ፡ ጥበቢሁ፡(ኢዮ፲፮፡፰። ቅዳ፡ ሕር። ቄር። ሮሜ፲፩፡፴፫)።

**ማዕምቅ ፤ ት ፤ (ቃት) ፤** ጥልቅ ፡ በታ ፤ ጕድጓድ ፤ ዐዘቅት ፤ የምድር ፡ ቤት ፤ ገደል ፤ ዋሻ ፡ ቈላ ፤ መቀራቅርት ፤ ዘብጥ ፡ ዘቅዛቃ ፡ ወዳቃ ። ማዕምቀ ፡ ባሕር ። ማዕምቅቲሃ ፡ ለምድር ። ወአውደቆ ፡ ውስተ ፡ ማዕምቅ ። ዡሉ ፡ ማዕምቅ ፡ ይምላእ ፡ (መዝ ፡ ፷፰ ። ኵፋ ፡ ፩ ። ራእ፷ ፡ ፫ ። ኢሳ፵ ፡ ፬ ። ባሮ፩ ፡ ፯) ።

**መዓምቅ ፤ ት ፤** ጥልቆች ፤ ጕድጓዶች ፤ መዓምቅተ ፡ ሲኦል ፡ (ምሳ፲፬ ፡ ፲፪) ።

**አዕመቀ ፤** አጠለቀ ፤ አስጠለቀ ፤ ጥልቅ ፡ አደረገ ፤ አስደረገ ። አዕምቁ ፡ ለክሙ ፡ ኅበ ፡ ትነብሩ ። ጥቀ ፡ አዕመቀ ፡ ከርየ ፡ ግብ ። ኢይክል ፡ አዕሚቆ ፡ ኀልዮ ፡ (ኤር ፵፱ ፡ ፱ ። ፴ ፡ ፰ ። ሉቃ፮ ፡ ፵፰ ። ቅዳ ፡ አፈ ። ዮሐ ። ግሩ) ። አዕምቅ ፡ (አሙቅ) ፡ ላሕዎቶ ፡ (ሚራ፴፰ ፡ ፲፯) ።

**ተዓመቀ ፤ ተዐማመቀ ፤** ተማመቀ ፤ ተናነቀ ፤ ተጣቈነ ፤ ተጋፋ ፡ ታገለ ፤ ለመጣል ፡ ለማውደቅ ፤ በታች ፡ ለማድረግ ። ኢትትዐማመቅ ፡ ምስለ ፡ ሰይጣናት ፤ ደረት ፡ ለደረት ፡ አትጋፋ ፡ (ፊልክ ፡ ፳) ።

**ዓመት ፤—በቁሙ ፤—ዓም ።**

**ዐንበዘ ፤—ተነበዘ ፤—ነበዘ ፤ አንበዘ ።**

**ዐንበሪ ፤ ር ፤ (ዕብ ፡ ዳግ ፤ ታኒን ፤ ሊዉያታን) ፤** ታላቅ ፡ ዓሣ ፤ እንደ ፡ ዘንዶ ፡ ያለ ። ዐንበሪ ፡ ዐቢይ ። ዐንበሬ ፡ ባሕር ። ዐንበሪ ፡ አንስቲያዊት ፡ ዘስማ ፡ ሌዋታን ። ይባርክዎ ፡ ዐንበር ፡ ወዡሉ ፡ ዘይትሐወስ ፡ ውስተ ፡ ማይ ፡ (ዮና፪ ፡ ፩ ። መዝ ፡ ፻፬ ። ሔኖ፷ ፡ ፯ ። ጸሎ ፡ ፫ ፡ ደቂ) ። ስምንቱ ፡ ከዐበረና ፡ ከነበረ ፡ ከኹለቱ ፡ የተዳቀለ ፡ ነው ፤ ምስጢሩም ፡ ታላቅነትና ፡ ነባርነት ፡ ነው ፤ አንባ ፡ እንደ ፡ ማለት ።

ዐንበሪ ፡ አንስቲያዊት ፡

**ዐናብርት ፤** ዐንበሪዎች ፤ ታላላቅ ፤ ዓሦች ፤ ብሄሞትና ፡ ሌዋታን ፡ (ዘፍ፩ ፡ ፳፩ ። ኵፋ ፡ ፪ ። ኢዮ፱ ፡ ፲፫) ። ብሄሞትን ፡ ተመልከት ።

**ዐንበር ፤ (ዐረ ። ዕብ ፡ ዐንባር) ፤** የሽቱ ፡ ጭቃ ፤ ሲፈጭ ፡ ሲደቈስ ፡ ወይም ፡ በእሳት ፡ ሲጤስ ፡ ሽታው ፡ የሚገን ፡ የሚጣፍጥ ። በዐንበር ፡ ፈንታ ፡ ዐምበር ፡ ይላል ፤ የተሳሳተ ፡ ነው ፡ (ዮሴፍ) ።

**ዐንበሳ ፤—በቁሙ ፤—አንበሳ ፤ በስበሰ ።**

**ዐኒግ ፤ ጎት ፤ (ዐነገ ፡ የዐንግ ፡ ይዕንግ ። ዐረ ፡ ሐነጀ) ፤** መሥራት ፤ መጠምዘዝ ፤ ማጕበጥ ፤ የቀለበት ። ማንገት ፤ ማሰር ፡ ማንጠልጠል ፤ የጌጥ ፡ የክታብ ።

**ዐንግ ፤ (ዕብ ፡ ኔዜም ። ጽር ፡ ሄኖቲያ) ፤** ጕትቻ ፤ ቀለበት ፤ ንጽ ፡ መንደልት ፤ ያፍንጫ ፡ ወይም ፡ የጆሮ ፡ ጌጥ ፤ ንጽ ፡ ያፍንጫ ፤ መንደልት ፡ የጆሮ ።

**አዕኑግ ፤** ጕትቾች ፤ ቀለበቶች ፤ ንጾች ፤ መንደልቶች ፡ (ዘፍ፳፬ ፡ ፳፪ ። ኢሳ፫ ፡ ፳ ። ሕዝ፲፮ ፡ ፲፪) ።

ዐንግ ፡

**ዐንገት ፤ (ዐረ ፡ ዑንጉግ) ፤** በቁሙ ፡ ክሳድ ፤ ማንገቻ ፤ የጌጥ ፡ የሽልማት ፡ ማሰሪያ ።

**ዐንጉግ ፤** ዐንገታም ፤ ዐንገተ ፡ ወፍራም ። የባሕር ፡ አውሬ ፤ አርጃኖ ፡ (ዘሌ፲፩ ፡ ፴) ።

**ዐናጉግ ፤** የባሕር ፡ አራዊት ፤ አርጃኖች ፡ (መቃ ፡ ገ፲፪) ።

**ዐንጐጕ ፤ (ጓት ፤** ዝኒ ፡ ከማሁ ። ዐንጐጓት ፡ ወብሔ ፡ (መጽ ፡ ምስ) ።

ዐንጉግ ፡

**ዕንጐት ፤ (ታት ። ዕብ ፡ ዱዳኢም ። ዐረ ፡ ሉፋሕ ። ጽር ፡ ማንድራጎሬ) ፤** ዕንጐችት ፤ የሽቱ ፡ ቅጠል ፡ ሽቱነት ፡ ያለው ። ዕንጐችት ፡ ፪ ፡ ዐይነት ፡ ነው ፤ ታላቅና ፡ ታናሽ ። ኮልን ፡ ተመልከት ፤ ከዚህ ፡ ጋራ ፡ አንድ ፡ ነው ፤ ባለብሉዮች ፡ ግን ፡ ትርንጎ ፡ ይሉታል ። በገነቶሙ ፡ ዕንጐታት ፡ ተረክቡ ፡ (ስንክ ፡ ጥቅ ፳፰ ። ማሕ፯ ፡ ፲፬ ። ዘፍ፴ ፡ ፲፬) ።

**ዕንዚራ ፤—የዘፈን ፡ ዕቃ ፤—ነዘረ ፡ እንዚራ ።**

**ዐንዘረ ፤—አስጮኸ ፤—ነዘረ ፡ አንዘረ ።**

**ዐኒን ፤ (ዐረብ) ፤** አባለ ፡ ዘርዕ ፤ ደካማ ፡ ኰሳሳ ፤ የታሸ ፡ የተኰላሸ ፤ ፍሬው ፡ የወጣ ፤ ወይም ፡ ያበጠ ፡ የተነፋ ፤ ደዌ ፡ ያደረበት ። ዘይትበሀል ፡ እልዐኒን ፤ ዘውእቱ ፡ ኅፍረት ፡ ሥጋ ፡ ንኡስ ፡ (ፈ ፡ መ ፡ ፲፪ ፡ ፩) ።

**ዕንፎራ ። (ጽር ፡ አናፎራ) ፤** አኰቴት ፤ ኅብስተ ፡ መሥዋዕት ። ጸሎተ ፡ ዕንፎራ ፡ (ቅዳ) ።

**ዐንፀወ ፤—ደረቀ ፤—ነፀወ ፡ አንፀወ ።**

**ዐንጼዋ ፤—ዐይጥ ፤—ነጽይ ፡ ነጸየ ፤ አንጼዋ ።**

**ዐኒቅ ፤ ቆት ፤ (ዐነቀ ፡ የዐንቅ ፡ ይዕንቅ ። ዕብ ፡ ዐናቅ ። ዐረ ፡ ዐነቀ) ፤** መክበብ ፤ ማጠር ፤ ዐንገትን ፡ በጌጥ ፤ ማሰር ፡ ማንገት ፤ ባንገት ፡ መሸከም ፤ ማንጠልጠል ። መርዘም ፤ መብለጥ ። ዕንቈ ፡ ውስተ ፡ ክ

ማድከ። ብፁዕ ፡ ዘጸሮ ፡ ወዘዐነቀ ፡ በከማዱ ፡ ለዝ ንቱ፡ጸሎት። ሰላም፡ለከማድኪ፡ ቃማ፡ንጽሕ፡ዘ ዐነቀ፡(ምሳ፫ ፡ ፫ ። ግንዘ ። ደራሲ) ። በዐንቀ ፡ ፈንታ ፡ ተ ዐንቀ ፡ ይላል ፤ ስሕተት ፡ ነው ። ወይትዐነቅ፡ቀጸላ፡ወ ርቅ፡(አዋል) ።

**አዕነቀ** ፤ አሸከመ ፤ ጫነ ፤ አስነገተ ፤ አሳሰረ ። አቡየ፡አዕነቀክሙ፡ጋጋ፡ክቡደ። ኣዐንቀ፡ባዝግና፡ ወርቅ፡ውስተ፡ክማዱ ። አዕነቅዋ፡ባዝግና፡ወርቅ፡ (፫ነገ ፡ ፲፪ ፡ ፲፩ ። ዳንኤ ፡ ፮ ። ገድ ፡ ተክ) ።

**ዕንቍ** ፤ ክቡር ፡ ደንጊያ ፤ ብዙ ፡ ዐይነት ፡ ያ ለው ፤ ያንገት ፡ ጌጥ ፡ ሽልማት ፤ ተሰክቶ ፡ ባንገት ፡ የሚ ታሰር ፤ የሚሰደር ፡ የሚደረደር ። ህየ፡ሀሎ፡ዕንቍ፡ዘ የኀቱ፡ወዕንቍ፡ሐመልሚል ። እማንቱ፡ዕንቊ፡ባ ሕርያት፡ክቡራት ። ዕንቍ፡ዘተሰክዐ፡በፈትለ፡ሜ ላት ። ዕንቊ፡ኢያሰጺ ድ፡(ዘፍ፪ ፡ ፲፪ ። ስንክ ፡ ሚያ፳ ። አርጋ ። ራእ፬ ፡ ፫) ።

**አዕናቍ** ፤ ዕንቆች ፤ የከበሩ ፡ ደንጎች ። ሰሐባ፡ ለጥበብ፡እምአዕናቍ፡(ኢዮ፳፰ ፡ ፲፰) ።

**ማዕነቅ** ፤ ቀኖስ ፤ ቡላል ፤ የርግብ ፡ ዐይነት ፡ ወፍ ፤ ዐንገቷ ፡ ሐር ፡ የታሰረበት ፡ የሚመስል ፡ (ዘፍ፲፭ ፡ ፱ ። ማሕ፩ ፡ ፲) ።

**መዓንቅ** ፤ ቀኖቮች ፤ ቡላሎች ። ያመጽእ፡ ክልኤተ፡መዓንቀ፡(ዘሌ፭ ፡ ፯) ።

**ዓናቅ** ፤ **ዔናቅ** ፤ ረዐይታዊ ፤ ኀያል ፡ ሐርበኛ ፤ እጅግ ፡ ብርቱ ፤ መለሎ ፡ ረዥም ፡ ወርዳም ፡ ቁመታም ፤ መጠኑ ፡ ከሰው ፡ ልክ ፡ ያለፈ ። ርኢነ፡ትውልዶ፡ለዔ ናቅ ። ወኮነ፡ ቅድሜሆሙ፡ ከመ፡ አናብጥ፡ (ዘኍ ፲፫ ፡ ፳፰ ፡ ፴፫) ። ናፊልን ፡ እይ ፤ ከዚህ ፡ ጋራ ፡ ፩ ፡ ነው ።

**ዕንቈራ** ፤—**የማር ፡ ሰፈፍ** ፤—**ነቀ ር ፡ ነቈረ** ፤ **እንቈራ** ።

**ዐንሰበ** ፤ **(ዐሰበ** ፤ **ሐሰበ)** ፤ ነሲብ ፡ ጣለ ፤ ገመተ ፤ አሻረተ ። ስሯጽ ፡ ግስ ፡ ነው ፤ ዐሰበን ፡ ተመል ከት ።

**መዐንስብ** ፤ **(ብት ፡ ባን ፡ ባት)** ፤ ሻር ተኛ ፤ መለኛ ፤ በነሲብ ፡ በግምት ፡ የሚናገር ። መዐንስበ፡ አራዊት፡ ወእመ፡ አኮ፡ ዐቃቢሆሙ ። ማርያን፡ ወ መዐንስባን፡(ኪዳ ። ዲድ ፡ ፲፫) ።

**ዕንሰራ** ፤ **(ዕብ ፡ ዐጺራ)** ፤ የሕዝብ ፡ ስብ ሰባ ፤ ጉባኤ ፤ ዐቢይ ፡ በዓል ፤ በዓለ ፡ ሠዊት ፤ በዓለ ፡ ኀ ምሳ ፤ ጰራቅሊጦስ ። በዓለ፡ዕንበራ፡(ዮሴፍ) ። ሥሩና ፡ ምንጩ ፡ ዐጸረ ፡ ነው ፤ ከንሰረም ፡ ጋራ ፡ ይስማማል ።

**ዐንሰር** ፤ **(ዐረ ፡ ዑንጹር)** ፤ የፍጥረት ፡ ጠ ባይ ፡ ባሕርይ ።

**ዐናስር** ፤ **(ዐረ ፡ ዐናጺሩ)** ፤ ህላውያት ፤ አ ሥራወ ፡ ፍጥረት ፤ አራቱ ፡ ባሕርያት ። ደንገፀ፡ ኵሉ፡ ዐናስረ፡ፍጥረት ፤ ወአንከሩ፡ ኵሎሙ፡ ፍጡራን፡ (ሃይ ፡ አበ ። ገድ ፡ አዳ) ። መተርጕማን ፡ ግን ፡ አለቆች ፡ ይሉታል ።

**ዐናት** ፤ **(ትግ ፡ ወዐም)** ፤ በቁሙ ፤ ማኽል ፡ ራስ ፤ የናላ ፡ ርግብግቢት ።

**ዐናቶት** ፤ **(ዕብራ)** ፤ ስመ ፡ ሀገር ፤ ስጣዊ ፡ (ኤር፩ ፡ ፩) ።

**ዓሣ** ፤ **ት** ፤ **(ዕብ ፡ ዓሽ ። ዐረ ፡ ዑሸት** ፤ **ዕዊ)** ፤ በቁሙ ፤ የባሕር ፡ እንስሳ ፡ መልኩና ፡ ነገዱ ፡ የተ ለየ ። የስሙ ፡ ምስጢር ፡ እንደ ፡ ትልና ፡ እንደ ፡ ከይሲ ፡ አለእግር ፡ መኼድ ፡ በልብ ፡ መሳብ ፡ ነው ፤ ዋነተኛነትም ፡ አለፀት ። እገሌ ፡ ዓሣ ፡ ነው ፡ እንዲሉ ። በከመ፡ዓሣ፡ ሶበ፡ወፅአ፡እማይ፡ይመውት፡ፍጡነ ። ዓሣተ፡ባ ሕር፡ወአዕዋፈ፡ሰማይ፡(ፊልክ ፡ ፳፩ ። ዘፍ፩ ፡ ፳፮) ።



ዓሣ ፡

**ዐሠየ** ፤—**ዋጋ ፡ ሰጠ** ፤—**ዐስይ ፡ ዐሰየ** ።

**ዐሠቀ** ፤—**ሠራ** ፤—**ዐስቆ ፡ ዐሰቀ** ።

**ዐሠር** ፤—**ፍለጋ** ፤—**አሠረ** ።

**ዐሥሮ** ፤ **ሮት** ፤ **(ዐሠረ ፡ ይዔሥር ፡ የ ዐሥር ። ዕብ ፡ ወሱር ፡ ዐሣር ። ዐረ ፡ ዐሸረ)** ፤ ዐሥር ፡ ማድረግ ፤ ዐሥራት ፡ ማውጣት ፤ ካሥር ፡ አንድ ፡ መስጠት ፤ ወይም ፡ መቀበል ፤ መውሰድ ። ዐሠረ፡እም ኵሉ ፤ ከመ፡የዐሥር ፤ ለዐሥሮ ። ፈጸምከ፡ዐሥሮተ፡ ኵሉ፡ዐሥራት ። ዐሥራተ፡ይዔሥር፡(ኩፋ ፡ ፴፫ ። ዘዳ ፳፮ ፡ ፲፪ ። መቃ) ።

—፤ መዋራት ፤ ኑልኝ ፡ ማለት ፤ ማደም ፤ መቅጠር ፤ ዐ ዋጅ ፡ መንገር ፤ ሕዝብን ፡ ሰራዊትን ፡ መሰብሰብ ፤ ማከብ ። በልዎሙ፡ለእለ፡ዐሠርናሆሙ ። ገብረ፡ምሳሐ፡ዐ ቢየ፡ወዐሠሮሙ ፡ ለብዙኃን ። ዐሥሩ፡ጾብአ፡(ማ ቴ፳፪ ፡ ፬ና ፡ ፰ ። ሉቃ፲፬ ፡ ፲፮—፲፯ ። ዮኤ፫ ፡ ፱) ።

**አዐሠረ** ፤ ዐሥር ፡ አስደረገ ፤ ዐሥራት ፡ አሶጣ ፤ ግብር ፡ ቀረጥ ፡ አስከፈለ ። ወአዕዲደ፡ወፍርክሙ፡ያ ዔሥረክሙ፡(፩ነገ ፡ ፰ ፡ ፲፯) ።

**ተዐ(ሥ)ሠረ** ፤ ተጠራ ፤ ታደመ ፤ ተቀጠረ ። እለ፡ተዐሥሩ፡ለመርዓ ። እለ፡ ተዐሠሩ፡ ውስተ፡ ከብካብ፡(ስንክ ፡ ጥቅ፲፬ ። ማቴ፳፪ ፡ ፫) ።

**ዕሡር** ፤ የተጠራ ፤ ዕድመኛ ፡ (ስንክ ፡ የካ፳) ።

**ዐሡር** ፤ ቀጠሮ ፤ የቀጠሮ ፡ ቀን ፤ ጊዜ ፡ ሰዓት ። ሶበ፡በጽሐ፡ዐሡር፡(ሉቃ፲፬ ፡ ፲፯) ።

**ተዐሠረ** ፤ ዐሥር ፡ ኾነ ፤ ዐሥር ፡ ተባለ ፤ ከ ሥር ፡ ተከፈለ ፤ ዐሥራት ፡ ወጣለት ፤ ታሸረ ።

**ዐሥሩ** ፤ (የቤት) ፡ ዐሥር ፡ (የ ፡ ፲) ፤ የቍጥር ፡ ስም ፤ መዠመሪያ ፡ ቀመር ፤ ያንድ ፡ ቤት ፡ ፍጻሜ ፤ የዘ ጠኝ ፡ ተከታይ ፤ በዘጠኝና ፡ በካያ ፡ መካከል ፡ ያለ ፡ ቍ ጥር ፤ ካንድ ፡ እስከ ፡ ዘጠኝ ፡ ያሉትን ፡ አኃዞች ፡ በመጫ

ውም ፡ የፍቅርና ፡ የርኅራኄ ፡ ሥራ ፡ ምክርን ፡ ርዳታን ፡ የመሰለው ፡ ኹሉ ፡ የግዜር ፡ ትእዛዝ ፡ ስለ ፡ ኾነ ፡ ምጽዋት ፡ ይባላል ። ስኢለ ፡ ምጽዋት ። ውሂበ ፡ ምጽዋት ። ብዙኀ ፡ ምጽዋት ፡ ገበርኩ ፡ ለአኀውየ ። ሚጡ ፡ ንዋየ ክሙ ፡ ወሀቡ ፡ ምጽዋተ ፡ ለነዳያን ፤ ደዮ ፡ ውስተ ፡ ሙዳየ ፡ ምጽዋት ። ምጽዋታት ፡ (ሚል፲፩ ፡ ፳፩ ። ፲፪ ፡ ፲፩ ። ጦቢ፩ ፡ ፫ ። ፍ ፡ ነ ፡ ፲፮ ። ስንክ ፡ ኅዳ፲፱) ።

**መጽወተ ፤ (መጠወ) ፤** ሰጠ ፡ መጠ(ጸ)ወተ ፤ ትእዛዝ ፡ ፈጸመ ። ይምሕሩ ፡ ወይመጽውቱ ። ኢትበል ፡ እምፈተውኩ ፡ ይኩን ፡ ሊተ ፡ ብዙኅ ፡ ንዋይ ፡ ከመ ፡ እመጽውት ፡ ላዕለ ፡ ነዳያን ። ይኩን ፡ መሓሪ ፡ ወመጽዋቴ ፡ (ምሳ፲፫ ፡ ፱ ። አፈ ፡ ተ፫ ። ዲድ ፡ ፱) ።

**ተመጽወተ ፤** ተመጠወተ ፤ ምጽዋት ፡ ተቀበለ ፤ ድኻው ። ይትመጸወት ፡ በአንቀጸ ፡ ሀገር ፡ (ስንክ ፡ ጥቅ፱ ። ታኅ ፡ ፲) ። ተሰጠ ፡ ዐለፈ ፤ ተናኘ ፡ ታደለ ፤ ገንዘቡ ።

**ጽሒብ ፤ ቦት ፤ (ጸሐበ ፡ ይጽሕብ ፡ ይጽሐብ ። ዐረ ፡ ጸዐበ ፤ ዐጸበ) ፤** መድከም ፤ መታከት ፤ መሰልቸት ፤ መሰቀቅ ፤ መቸገር ፡ መጨነቅ ፤ ከዝብዘባ ፡ ብዛት ፡ የተነሣ ፤ ነጠየን ፡ ተመልከት ።

**አጽሐበ ፤** አደከመ ፤ አሰለቸ ፤ ዘበዘበ ፤ ነዘነዘ ፤ በጠኝ ፡ አድርገልኝ ፡ ብሎ ። አጽሐበ ፡ ነፍሶ ፡ በጾም ፡ ወበጸሎት ። ምንተ ፡ አጽሐብኩከ ። ከመ ፡ ኢያጽሕብዎ ፡ ለንጉሥ ። ኢታጽሕቦ ፡ ወኢትስአሎ ፡ (ስንክ ፡ ግን፲ ። ሚክ፯ ፡ ፫ ። ዳን፯ ፡ ፱ ። ሚል፴፱ ፡ ፴፩) ።

**ጻሕብ ፤** ዝብዘባ ፤ ንዝንዛ ፤ ጭቅጭቅ ፤ ሙገት ፤ ድካም ፤ መከራ ። ተዐቀብ ፡ ከመ ፡ ኢያብእከ ፡ ውስተ ፡ ጻሕብ ። በኢፈቂደ ፡ ጻሕብ ። ዕቀብ ፡ ዙሉነ ፡ ዘእንበለ ፡ ጻሕብ ። አዕረፈ ፡ ዮም ፡ እምጻሕቡ ፡ (ሚል፳፱ ፡ ፲፫ ። ፳፱ ፡ ፯ ። ቅዳ ። ስንክ ፡ ታኅ፱) ።

**ጻሕብ ፤ (ብት ፤ አጽሕብት) ፤** ሸክላ ፤ የሸክላ ፡ ዕቃ ፤ ከጣባ ፡ እስከ ፡ ዋዲያት ፤ ከጋን ፡ እስከ ፡ ምንቸት ፤ ከጐልላት ፡ እስከ ፡ መግላሊት ፤ በየስሙና ፡ በያይነቱ ። ፍችው ፡ ደካማ ፤ ድኩም ፡ ማለት ፡ ነው ። የማበ ፡ ፊቀን ፤ ርኩት ፤ ራዎት ፤ የመሰለው ፡ ኹሉ ። ዝቅንና ፡ ኔባልን ፡ ተመልከት ። ጻሕብ ፡ ስቁር ። ጻሕበ ፡ ማይ ። ወድቀ ፡ ጻሕብ ። ጻሕብ ፡ ዘልሕዙት ። ነሥአት ፡ ክልኤተ ፡ አጽሕብተ ፡ ወይን ፡ (ሚል፳፩ ፡ ፲፱ ። ማር፲፱ ፡ ፲፫ ። ኢሳ፴ ፡ ፲፱ ። ሕዝ፱ ፡ ፱ ። ፩ነገ ፡ ፳፩ ፡ ፲፰) ።

**ጽሒድ ፤ ዶት ፤ (ጽሕደ ፡ ይጽሕድ ፡ ይጽሐድ) ፤** መጥዳት ፤ መለዘብ ፤ መለስለስ ፤ ልሙጽ ፡ መኾን ። ወጽሕደ ፡ እምቅብዕ ፡ ነገሩ ፡ (መዝ ፡ ፶፱) ።

**ጽሑድ ፤ (ዳን ፡ ዳት ፡ ሑድ) ፤** የጠዳ ፡ ጥዱ ፤ ልዝብ ፡ ልሙጽ ፤ ለስላሳ ፤ ልም ፤ ንጹሕ ። እስመ ፡ ጽሑድ ፡ ክርስቶስ ፤ ወመንክር ፡ ጽሕደቱ ፡ ሥጋሁ ፡ (መጽ ፡ ምስ) ።

(ጥድ) **ጽሕድ ፤** በርሚል ፤ የንጨት ፡ ጋን ፤ ከለሀበ ፡ ጠርብ ፡ የሚሠራ ፤ የሸክላ ፡ ጋን ፤ ማድጋ ፡ ፊቀን ። ዕብራይስጡ ፡ ግን ፡ ጥልቅ ፡ ልሙጽ ፡ ጕድጓድ ፡ ይላል ።

ጽሕድ ፡ ስቍርት ፡ ዘማዊት ። በጽሕድ ፡ ፈንታ ፡ ጽዕድ ፡ ይላል ፤ የጣፊ ፡ ስሕተት ፡ ነው ፡ (ምሳ፳፫ ፡ ፳፯) ።



(ጥድ) ጽሕድ ፡

**ጽሕደት ፤** መለዘብ ፤ አለዛዘብ ፤ ልዝብነት ፤ ልስላሴ ፤ ጥዳት ፤ ንጽሕና ። ከመ ፡ ሜላት ፡ ንጹሕ ፡ ጽሕደተ ፡ ሥጋሃ ፡ ለማርያም ፤ እስመ ፡ ኢበቊለ ፡ ውስቴታ ፡ ሦክ ፡ ንጣውእ ። ጽሕደተ ፡ ሜላት ፡ (መጽ ፡ ምስ ። አርጋ ፡ ፱) ።

**አጽሐደ ፤** አጠዳ ፤ አለዘበ ፤ አለሰለሰ ፤ ቀባ ፤ ሾመ ። ርጢናት ፡ እለ ፡ ይፈትሓ ፡ ሕብጠተ ፡ ወያጽሕዳ ፡ ቍስላተ ። ያጽሕደኒ ፡ እምስሕክትየ ። ወአጽሐድከ ፡ በቅብዕ ፡ ርእስየ ። አጽሕዶሙ ፡ እደዊሆሙ ፡ (ፈ ፡ መ ፡ ፫ ፡ ፫ ። ስንክ ፡ ሚያ፲፮ ። መዝ ፡ ፳፱ ። ዘፀ፳፰ ፡ ፵፩) ።

**ጽሕድ ፤ (ዳት ፤ አጽሓድ) ፤** አርዝ ፤ ጥድ ፡ ዘግባ ፤ የጥድ ፡ የዘግባ ፡ ዐይነት ፤ የሊባኖስ ፡ ዛፍ ፤ መዐዛው ፡ የጠዳ ፤ ሲጠርቡትና ፡ ሲያለዝቡት ፡ ስለት ፡ የሚቀበል ፤ ጽሕደት ፡ የሚስማማው ፤ የማይፍረከረክ ። አርዝን ፡ ተመልከት ፤ ከዚህ ፡ ጋራ ፡ ፩ ፡ ነው ። ንግዘም ፡ ሰግላ ፡ ወጽሕደ ። ዕፀ ፡ ጽሕድ ። ፍሬ ፡ ጽሕድ ፡ (ኢሳ፱ ፡ ፲ ። ዘሌ፲፬ ፡ ፬ና ፡ ፮ ። መ ፡ ፈ) ።



ጽሕድ ፡

**ጻሕው ፤—ትእዛዝ ፤—ጻው ።**

**ጽሒው ፤ ዎት ፤ (ጽሕወ ፤ ጸሐወ ፡ ይጽሑ ፡ ይጽሐው ። ሱር ፡ ጻሕዎ ። ዐረ ፡ ጸሒየ ፤ ጸሓ) ፤** መብራት ፤ መጥራት ፤ ብሩ ፡ መኾን ፤ የሰማይ ፡ የዝናም ። አንዘ ፡ ያንጠብጥብ ፡ ዝናም ፡ ወእምዝ ፡ ጽሕወ ፡ (ስንክ ፡ ሚያ፳፱) ።

—፤ መንቃት ፤ መመለስ ፤ መትጋት ፤ ከንቅልፍ ፡ ከስካር ፡ ከሀኬት ። ሶበ ፡ እጽሑ ፡ እምንዋምየ ። ሶበ ፡ ጽሕወ ፡ እምወይኑ ። ንጽሐው ፡ እምንዋመ ፡ ስካር ። ጸሐዉ ፡ እምስካረ ፡ ወይን ። ወጸሐዉ ፡ ለጸሎት ፡ (አርጋ ፡ ፱ ። ዘፍ፱ ፡ ፳፱ ። መጽ ፡ ምስ ። ቄር ፡ ጸላ ። ፩ጴጥ ፡ ፱ ፡ ፯) ።

**ጽሕው፤(ዋን፡ ዋት፡ ሒት)፤** የጠራ፤ የፀራ፤ ቍልጭ፡ ያለ። ጽሕው፡ ብሔር። አየር፡ ጽሕወ፡ ኮነ፡(ማቴ፲፮፡ ፪። አፈ፡ ድ፹፪)።

**ጸሐየ፤(ዕብ፡ ጻሐሕ)፤** ጸሐወ፤ በራ፤ ጠራ፤ ጽሩይ፡ ኾነ፤ ጽርየቱ፡ መልክ፡ የሚያሳይ፡ እስኪ ኾን፡ ድረስ፤ የውሃ፡ የሸክላ፡ የማዕደን። ጽሕወና፡ ጸሐየ፡ አንድ፡ ዘር፡ ናቸው።

**ጸሓይ፤** በቁሙ፡ ፀሓይ። ኹለተኛውን፡ ፀ፡ ተመልከት፤ ሊጣፍ፡ የሚገባው፡ በዚህ፡ ጸ፡ ነበረ፤ ስለ፡ ልማድ፡ ወደ፡ ፀጸ፡ ኼዷል።

**መጽሒት፤(ታት፤ መጻሕይ)፤** መስታዮት፡ ንጹሕ፡ ብሩህ፡ ጽሩይ፤ መልክ፡ የሚያሳይ፤ ማይ፡ ስማይ፡ የሚመስል። መጽሒት፡ ዝሕልት። መጽሒት፡ ብርህት። ከመ፡ ዘይሬኢ፡ ፍጥረተ፡ ገጹ፡ በመጽሒት፡(ሢራ፲፪፡ ፲፩። ቀሌ። ያዕ፩፡ ፳፫)።



መጽሒት፡

**ጻሕየየ፤(ተቀ፡ ግ)፤** አየ፤ ተመለከተ፤ በመስታዮት፤ በመነጽር። ወንሕነሰ፡ ክሡተ፡ ገጸ፡ ንጻሕይይ፡(ድጓ)። በጻሕየየ፡ ፈንታ፡ ተጻሕየየ፡ ይላል፤ በሕተት፡ ነው። ዘኢተጻሕየይከ፡ በመጽሒተ፡ ገጹ፡ ስኢየቡስ፡(መጽ፡ ምስ)።

—፤ ዐረመ፤ አጠራ፤ የፊቱን፡ ጕድፍ፡ የኆርሱን፡ እድፍ፤ የመጽሐፍን፡ ጸያፍ። ለየ፤ ነቀሰ፤ ቈረጠ፤ ቈጠቈጠ። ጻሕይይ፡ ክርዳደ። ወንጻሕይይ፡ እምኔሃ፡ ለሥዋከ፡ ረቢዓን። እንዘ፡ ትጻሕይዩ፡ እምኔሆሙ፡ ዘሎ፡ ምግባራተ፡ እኩይ፡(ኪዳ። ቀሌ)።

**ተጻሕየየ፤** ታረመ፤ ተነቀሰ፤ ተለየ፤ ዐረሙ። ታረመለት፤ ፀረም፡ ጠፋለት፤ እኽሉ፡ ተክሉ፡ መጽሐፉ፤ ባለመስታዮቱ።

**ጽሕዩይ፤(ያን፡ ያት፡ ይይት)፤** የታረመ፤ ዐርም፤ እድፍ፡ ጕድፍ፡ ጸያፍ፡ የሌለበት።

**ጽሕያይ፤** ዐረም፤ ዐረሞች፤ እድፍ፤ ጕድፍ።

**ጸሐለ፤(ጸሊሕ፡ ጸልሐ፤ ጸልሐወ)፤** ጣፈ፤ ቀረጸ፤ በደንጊያ፡ ላይ፤ እንዳሠርቱ፡ ቃላት።

**ምጽሓል፤(ዕብ፡ ዔጥ)፤** ብርዕ፤ አፈ፡ ምሣር፤ መጣፊያ፤ መቅረጫ። ባለብሎዮች፡ ግን፡ ስሌዳ፡ ይሉታል። በምጽሓለ፡ ኀጺን፡ ወዐረር፡ እመ፡ ጸሐፎ፡ ውስተ፡ ኰዅሕ፡(ኢዮ፲፱፡ ፳፬)። ብረቱን፡ ብርዕ፤ ርሳሱን፡ ቀለም፡ አድርጎ፡ ማለት፡ ነው።

**ጸሕል፤(ዕብ፡ ጻላሐት። ሱር፡ ጽሊሓ)፤** በቁሙ፤ ወጭት፤ ሳሕን፤ ዝርግ፤ ጠፍጣፋ፤ ክብ፡ ወይም፡ ሞላላ። ለጕድጓዳውም፡ ይነገራል። ሀበኒ፡ በጻሕል፡ ርእሶ፡ ለዮሐንስ። እስ፡ ትንፅቡ፡ ጽዋዐ፡ ወጻሕለ። ጻሕለ፡ ፀቢየ፡ ዘወርቅ፡ ንጡፍ፡(ማቴ፲፬፡ ፰። ፳፫፡ ፳፭ና፡ ፳፮። ዮሴፍ)።

**ጻሕላት፤(አጽሓል፤ አጽሕል፤ ልት)፤** ጸሕሎች። ጻሕላት፡ ዘብሩር። አጽሕለ፡ ወመዳምሐ። ወአጽሕልት፡ ዕሥራ፡ ወተስዐቱ፡(ስንክ፡ ሠኔ፲፫። ዘፀ፴፰፡ ፲፱። ዕዝ፩፡ ፱)።

**ጽሒም፤ ሞት፤(ጸሐመ፡ ይጽሕም፡ ይጽሐም። ዕብ፡ ጻማሕ)፤** መብቀል፤ መውጣት፤ ማደግ፡ መርዘም፤ የሣር፡ የጠጕር፡ የጥርስ፡ የቀንድ፤ የመሰለው፡ ኹሉ። ጸምሐን፡ ተመልከት፤ የዚህ፡ መንቲያ፡ ነው፤ ምስጢራቸው፡ ፩፡ ወገን፡ ቢኾን፡ ንባባቸው፡ በፊደል፡ መዛወር፡ ተለያይቷል፤ መዛወሩም፡ ቀሐመን፡ ቀምሐ፡ ብለው፡ እንደሚገሉት፡ ነው።

**ጸሓም፤(ማን፤ ጸሐምት)፤** ጢማም፤ ሪዛም፤ ባለጢም፤ ጢመ፡ ረዥም። ጸሓም፡ ወጸጓር፡(ገድ፡ ፊቅ)።

**ጽሕም፤(ማት፤ አጽሓም)፤** በቁሙ፤ ጢም፤ ሪዝ፤ ሸንጕበት፤ ሽፋሽፍት፤ ባገጭ፤ በጕንጭና፡ በጕንጭ፤ በከናፍር፡ ላይ፡ የሚበቅል፡ ጠጕር። ሥዕርተ፡ ጽሕምየ። ወከነ፡ ጽሕሙ፡ ነዊኀ፤ ወይበጽሕ፡ እስከ፡ ኅባኔሁ። ልጺያን፡ አጽሓሚሆሙ፡(ዕዝ፱፡ ፫። ስንክ፡ ግንቦ። ኤር፵፰፡ ፴)። ምስጢሩ፤ ከደጉ፡ በኋላ፡ የሚሠርጽ፡ የኋላ፡ ቡቃያ፡ ማለት፡ ነው።

**ጽሒፍ፤ ፎት፤(ጸሐፈ፡ ይጽሕፍ፡ ይጽሐፍ። ዐረ፡ ጸሐፈ)፤** መጣፍ፤ ፊደልን፡ ከብራና፡ ከወረቀት፡ ላይ፡ በቀለም፡ መሣል፡ መንደፍ። ስሌዳው፡ የዕፅ፡ የእብን፡ የማዕደን፡ ቢኾን፤ ቀለም፡ የወደቀበትን፡ መቈፈር፡ መፈልፈል፡ ለማስመጥ፤ ወይም፡ ዙሪያውን፡ መንቀስ፡ መቅረጥ፡ ለማሳበጥ፤ እንደ፡ ማኅተም። ማስብ፡ መቍጠር፤ በፊደል፡ በአኃዝ። የተጣፈውን፡ የተቈጠረውን፡ ጠንቅቆ፡ ማወቅ፤ በልቡና፡ ማኖር። ጠቢባን፡ እሙንቱ፡ ውስተ፡ ጽሒፍ። ጸሐፍኩ፡ በእዴየ። ጸሐፎ፡ በጽሌ፡ ልብከ። ወይጽሕፎሙ፡ ሕዛን። ጸሐፊዮ፡ ለዝ፡ ብእሲ፡ ከመ፡ ዘሞተ፡(ሱቱ፡ ዕዝ፲፬፡ ፳፯። ፊልሞ፡ ፲፱። ምሳ፫፡ ፫። ኢሳ፲፡ ፲፱)። ከተበን፡ ተመልከት።

**ጸሓፊ፤(ፊት፡ ፍያን፡ ያት፤ ሐፍት)፤** የሚጥፍ፤ ጣፊ፤ ቈጣሪ፤ ሹም፤ ዐዋቂ፡ ብልኅ፡ ጠቢብ። ቀለመ፡ ጸሓፊ። ጸሓፊ፡ በራዊት። ጸሐፍተ፡ መባእ። ዕዝራ፡ ጸሓፊ፡ ሕጉ፡ ለእግዚ። ጸሓፊ፡ ሀገር። ጸሐፍተ፡ ሀገር፡(መዝ፡ ፵፬። ኢሳ፴፯፡ ፳፪። ዘዳ፲፯፡ ፲፰። ዕዝ፯፡ ፲፩። ማቴ፳፪፡ ፴፭። ሉቃ፲፩፡ ፵፭)።

**አጽሐፈ፤** አስጣፈ፤ አስቈጠረ። ለዘጸሐፎ፡ ወለዘአጽሐፎ፡ ለዝንቱ፡ መጽሐፍ። አጽሐፈ፡ ዘሎ፡ ብሔሮ፡ ከመ፡ የሀቡ፡ ጸባሕተ። ዘአጽሐፉ፡ ሎቱ፡ ትእዛዘ፡(ቀሌ። ፬ነገ፡ ፳፫፡ ፴፭። ፍ፡ ነ፡ ፴፫፡ ፱)።

**ተጽሕፈ፤** ተጣፈ፤ ተቈጠረ፤ ተጣፈበት። ተ

ጽሕፈ፤ዐርከ፤እግዚ፤ውስተ፤ጽላተ፤ሰማይ። ለተጽሕፎ፤ሀገረ፤ዳዊት፤ዐርገ። ጽላት፤እለ፤ተጽሕፋ፤በአጻብዒሁ፤ለእግዚ፤(ኩፋ፤ ፲፱ ። ስንክ፤ ታኅሣሥ ። ዘዳ፱፤ ፲)።

**ጽሑፍ፤(ፋን፤ፋት፤ሕፍት)፤** የተጣፈ፤ የተቈጠረ። ሖሎ፤ ዘጽሑፍ፤ ውስተ፤ ዝንቱ፤መጽሐፍ። እለ፤ ጽሑፋን፤ በበ፤ አስማቲሆሙ። ጽሑፋት፤ በዕብራይስጥ። መጽሐፍ፤ ጽሕፍት፤(ኤር ፴፩፤ ፲፫ ። ፩ዜና፤ ፱፤ ፵፩ ። ኩፋ፤ ፲፪ ። ራእ፩፤ ፩)። አገባብ፤ ሲወድቅበት፤ባይወድቅበትም፤ ቀዳማይ፤ ቦዝ፤ አንቀጽ፤ ይኾናል ። እስመ፤ ጽሑፍ፤ በከመ፤ ጽሑፍ፤ ቢል፤ እንደ፤ ተጣፈ፤ ተጥፎ፤ እንዳለ ። ጽሑፍ፤ ለእግዚ፤ ትሰግድ፤ ተጥፏል፤ ያሰኛል ።

**ጽሕፈት፤(ታት)፤** መጣፍ፤(ጥጣ)መጣፍ፤ አጣጣፍ፤ ጥፈት፤ ቍጥር ። ጽሕፈተ፤ሠናየ፤የአምር። መሃሬ፤ጽሕፈት። ጽሕፈታተ፤እደዊሆሙ፤(ስንክ፤ ኅዳ፱ ። ፈ፤ መ፤ ፪፤ ፲፩ ። ያዕ፤ ዘእል)።

**ጻሕፍ፤(ፋት)፤** ጥፈት፤ቍጥር ። ወዝንቱ፤ ጻሕፍ፤ቀዳሚ፤(ሉቃ፪፤ ፪)።

**መጽሐፍ፤(ብ፤ መጻሕፍት፤ ታት)፤** በቁሙ፤ መጣፍ፤ በላዩ፤ ቃል፤ ነገር፤ የተጣፈበት፤ ብራና፤ ወረቀት፤ ነደው፤ ባንድነት፤ የታሰረና፤ የተያዘ፤ የተሰፋ፤ የተጠረዘ፤የታፈፈ፤ የተደጐሰ፤ ቅዱስ፤ ክታብ፤ አምላካዊ፤ ንባብ፤ ብሉይ፤ ሐዲስ፤ ሌላውም፤ ኹሉ፤ ደብዳቤ፤ ሳይቀር ። በከመ፤ ይቤ፤ መጽሐፍ። ቅዱሳት፤መጻሕፍት። መጻሕፍታቲሁ፤ወመጻሕፍተ፤አበዊሁ። ይምሀርዎሙ፤መጽሐፈ፤ወነገረ፤ፋርስ። መጽሐፈ፤ መልእክት፤(ዮሐ፳፤ ፴፫ ። ሮሜ፩፤ ፪ ። ኩፋ፤ ፵፩ ። ዳን፩፤ ፬ ። ግብ፱፤ ፪)።

—፤ ወግ፤ ታሪክ፤ ትምርት፤ ዕውቀት፤ ስፍር፤ ቍጥር፤ ተርትሮ፤ ደምሮ፤ የሚጥፉት ። ስማ፤ለዳቤር፤ሀገረ፤መጽሐፍ። አብዝኆ፤መጻሕፍት፤ያዘነግዐ፤ልበ። መጽሐፈ፤ ልደቱ፤ ለኢየሱስ፤(ኢያ፲፭፤ ፲፭ ። ግብ ፴፯፤ ፴፱ ። ማቴ፩፤ ፩)። መጽሐፍ፤ በስምና፤ በግብር፤ እየተናበበ፤ እንዳወራረዱ፤ ይፈታል፤ ምስጢሩ፤ ግን፤ ከመጽሐፍነት፤ አይወጣም ።

**ምጽሓፍ፤(ፋት)፤** መጣፊያ፤ መቍጠሪያ፤ መማሪያ፤ የጥፈት፤ የትምርት፤ ቤት ።

**ጻሕጻሕ ፤—ፍሳሽ፤ ጠፈጠፍ፤—ወጺሕ፤ ወጽሐ ።**

**ጽሒቅ፤ ቆት፤(ጽሕቀ፤ ይጽሕቅ፤ ይጽሐቅ ። ዕብ፤ ጻሔቅ፤ ሣቀ ። ሹቅ፤ ፈተወ)፤** መውደድ፤ መመኘት፤ መፈለግ፤ መሻት፤ ማሰብ፤ መትጋት ። ፈተወን፤ ተመልከት፤ የዚህ፤ ከተማ፤ ነው ። ኅሊናሁ፤ ይጽሕቅ፤ ኀበ፤ ምንዙስና። የኀሥሡ፤ ወይጽሕቁ፤ ገጸ፤ ለሰሎሞን። እጽሕቅ፤ለክሙ፤ዘልፈ። ኢንጽሐቅ፤ለግብረ፤ዓለም፤(ስንክ፤ መስ፲፱ ። ፪ዜና፤ ፱፤ ፳፫ ። ፪ጴጥ፤ ፩፤ ፲፪ ። አፈ፤ ተ፳፮)።

**ጸሓቂ፤(ቂት፤ ቅያን፤ ያት)፤** የሚወድ፤ የሚተጋ፤ ዐሳቢ ። ጸሓቂ፤በመንፈሱ፤ ወዳማዊ፤በገድሉ። ለባዊ፤ ወጸሓቂ። ፊልጶስ፤ ጸሓቂ፤ውስተ፤ትምህርት። ጸሓቅያን፤ለሠናይ፤(ገድ፤ ተክ ። ኪዳ ። ቄር ። ፍ፤ ነ፤ ፲)።

**ጽሑቅ፤(ቃን፤ ቃት፤ ሕቅት)፤** የተጋ፤ ትጉህ፤ ንቁህ ። ጽሑቅ፤ለፍቅር። ጽሕቅተ፤ኩኒ፤ለውሂበ፤መፍቅድየ። ጽሕቅት፤ ለተማህሎ፤(አርጋ፤ ደራሲ)።

**ጻሕቅ፤(ቃት)፤** ፈቃድ፤ ሐሳብ፤ ትጋት ። ጻሕቅክሙ፤ላዕለ፤ሰሚዐ። ኢይትሀከይ፤ጻሕቆሙ፤ለእለ፤የኀሥሡ፤ ንስሓ። ይሚጥ፤ ጻሕቃተ፤በአስተዳልዎ፤ዘይትፈቀድ። ጻሕቀ፤ጽድቅ፤(አፈ፤ ድ፱ ። ዲድ፤ ፮ ። ፍ፤ ነ፤ ፴፱፤ ፪ ። ቄር፤ ጸላ)።

**አጽሐቀ፤** አስመኘ፤ አስፈለገ፤ አተጋ፤ አሳሰበ፤ አሳዘነ ። ለዝንቱ፤ ብእሲ፤ ኢያጽሐቀ፤ ምርዐውና፤ ዲበ፤ ምድር። ወከመ፤ ዝ፤ አጽሐቀ፤ ኅሊናሁ፤ ለሐዋርያ፤ ወአገበሮ፤ከመ፤ ይጽሐፍ። ላሕምኑ፤ አጽሐቀ፤ ለእግዚ። ወአጽሐቀቶ፤ ለጳውሎስ፤(መዋሥ ። አፈ፤ ወር፤ መቅ ። ፩ቆሮ፤ ፱፤ ፱ ። ግብ፲፮፤ ፲፮)።

**ጽሕርት፤—ድስት፤—ጽሀርት ።**

**ጻሕስ፤—ሽብሽብ፤—ፅሒስ፤ ፀሐሰ ።**

**ጽኅድ ፤—ጥድ፤ ዛፍ፤—ጽሒድ፤ ጽሕደ ።**

**ጸጥ፤(ዐረ፤ ጸሀ ። ዕብ፤ ሀስ)፤** በቁሙ፤ ዝም፤ ፀክም፤ ጫ፤ ማለት፤ ጸጥታ፤ ዝምታ፤ ጫታ፤ ርጋታ፤ አለድምፅና፤ አለሁከት፤ መኾን ። ወጸጥ፤ ይብል፤እስመ፤አልቦ፤ድምፅ፤ወቃል፤(ሱቱ፤ ዕዝ፮፤ ፴፱)።

—፤ ትእዛዝ፤ አንቀጽ፤ ዝም፤ በል፤ ዕሽ፤ ዕሻ፤ አርምም፤ ተፈፀም፤ ወህዳእ፤ ብሂል ።

**ጸዩአ፤አት፤(ጼአ፤ ይጸይእ፤ ይጺእ ። ዕብ፤ ጼእ፤ ጼአህ፤ ኵስ)፤** መግማት፤ መሽተት፤ መቈነስ፤ መበስበስ፤ እስኪተላ፤ ድረስ ። ወፅአን፤ ተመልከት፤ የዚህ፤ መንቲያ፤ ነው ። ይጸይእ፤ተከዚ። ጼአት፤ምድር። ወድአ፤ ጼአ። ዘይጸይእ፤ አፉሁ። ጼአ፤ቍስሊሁ። ሰብእ፤እምከመ፤ሞተ፤ ይጸይእ። እንዘ፤ሕያው፤ትጸይእ፤ነፍስቱ፤(ዘፀ፯፤ ፲፰ ። ፰፤ ፲ ። ዮሐ፲፩፤ ፴፱ ። መ፤ ፈ ። ዮሴፍ ። ኢዮ፲፱፤ ፲ ። ሚራ ፲፤ ፱)።

**ጽዩእ፤(አን፤ አት፤ ይአት)፤** የገማ፤ ግም፤ ግማታም፤ የቈነሰ፤ የበሰበሰ ። ጼና፤ጽዩእ። ደመና፤ ጽዩእ፤ ወጸሊም፤ በረድ። አይሁዳዊ፤ ዕልው፤ ወጽልሕው፤ ወጽዩአ፤ አፍ፤ ወርኩስ፤ ከናፍር። ኀልቃ፤ መዋዕልየ፤ እንዘ፤ ጽዩኣት። ሖሉ፤ ሰብእ፤ ያንሶስዉ፤ ላዕለ፤ አብድንት፤ ወላዕለ፤ ጽዩእ፤ እስከ፤ በልዑ፤ ጽዩአ፤(ግንዘ ። ስንክ፤ መስ፲፰ ። ሲኖዶ ። ኢዮ ፲፯፤ ፲፩ ። ዮሴፍ)።

**ጺአት፤** መግማት፤አገማም፤ግምንት፤ግማት፤ ዐይን፡ ምድር፤ እድፍ፡ ርስሐት፡ ዝገት። የዐርግ፡ ጺ አቱ። ይጼኑ፡ ጺአተሙ። መሬት፡ ወሐመድ፡ ወዕፄ፡ ወጺአት። ጼና፡ ጺአቱ። ወርቅ፡ ዘይጸዕ፡ እምጺ አቱ፡ (ዮኤ፪፡ ፳። ኢሳ፴፬፡ ፫። መቃ። መዋሥ። ገድ፡ አዳ። ሄርማ)።

**ጺእ፤** ግማት፤ ክፉ፡ ሽታ። ምሉኣ፡ ጺእ፡ ወርሖስ፡ ወትዕገልት፡ (መቃ)።

**ጺአት፤—መስከ፤ ጨፈ፤—ጊያት።**

**ጼደነት፤ (ታት። ዕብ፡ ጼዳኒ፤ ተንኰለኛ፤ አጥማጅ፤ ዐዳኝ)፤** የዱር፡ የበረሓ፡ ዛር፤ ጋኔን። ይትራከቡ፡ ህየ፡ አጋንንት፡ ወጼደነታት፤ ወ ይጸርሑ፡ ሥሉሙ፡ (ኢሳ፴፬፡ ፲፭ና፡ ፲፬)። ሰገሮ፡ በማ ለት፡ ፈንታ፡ ጼደንት፡ ይላል፤ የተሳሳተ፡ ነው፤ ባለብሉ ዮች፡ ግን፡ ኹሉንም፡ ሐሰይ፤ ወይም፡ ጌሊ፡ ደንጊያ፡ ልብሱ፡ ይሉታል። አዋልደ፡ ጼደነታት። ይበክዩ፡ ከመ፡ ጼደነታት፡ (ኤር፭፩፡ ፴፱። ሔኖ፲፭፡ ፪)። መጽ አሞንና፡ ጽግንትን፡ ተመልከት።

**ጼው፤ (ዐረ፡ ጸዋ። ዕብ፡ ጺያ፤ ደረቅ፡ በረሓ፤ ምድረ፡ በዳ)፤** ጨው፤ ዐሸቦ፡ አሞሌ፤ በቈላ፡ በረሓ፡ ከውሀማ፡ መሬት፡ የሚገኝ፤ በውሃ፡ የሚ ቀልጥ፡ የሚሸሽ፤ መጣጣ፡ ሖምጣጣ፤ መባልዕትን፡ ኹሉ፡ የሚያጣፍጥ፤ ከኹል፡ ገብ፤ በብዙ፡ ወገን፡ የሚ ፈለግ። አንትሙ፡ ጼዉ፡ ለምድር፤ ወእመሰ፡ ጼው፡ ለስሐ፡ በምንት፡ እንከ፡ ይቄስምዎ። ወዘርዐ፡ ውስቴታ፡ ጼወ። ሐውልተ፡ ጼው። ወረሰያ፡ ለም ድር፡ ጼወ። ባሕረ፡ ጼው። ገዳመ፡ ጼው፡ (ማቴ፭፡ ፲፫። ማር፱፡ ፶። መሳ፱፡ ፵፭። ዘፍ፲፱፡ ፳፮። መዝ፡ ፻፯። ኩፉ፡ ፲፫። ስንክ፡ ግንቦ፳፩)።

**ጼዋት፤ ጽያው፤ አጽያው፤** ጨዎች፤ ዐ ሸቦዎች፤ አሞሌዎች። ዐሸቦ፡ እንኳሩ፡ ብትን፤ አሞሌ፡ ጥርቡ፡ ምእዙን። (ተረት)፤ ምላጭ፡ ዐበጠ፡ በምን፡ ይ በጡ፤ ጨው፡ ዐለጠ፡ በምን፡ ያጣፍጡ። የመንዙሴ፡ ሎሌ፤ የከረምት፡ አሞሌ። ሐሬ፡ ብሎ፡ ጨዋ፡ ማለት፡ ዐ ማርኛው፡ ከዚህ፡ ወጥቷል፤ ምስጢሩም፡ የጨው፡ ነው።

**ጸዪሕ፤ ሖት፤ (ጼሐ፡ ይጸይሕ፡ ይ ጺሕ። ዕብ፡ ጻሕ፤ ጠራ፤ በራ፤ ነጣ)፤** መጥ ረግ፤ ማስወገድ፤ መደልደል፤ ማስተካከል፤ ማበጀት፡ ማዘጋጀት፤ የመንገድ። ጺሑ፡ ፍኖተ፡ ቅድመ፡ ገጹ። ጺሑ፡ ፍኖተ፡ ለሕዝብ። ኢጼሐ፡ መንገደ። ዘይ ጸይሕ፡ ፍኖተከ፡ (ኢሳ፶፯፡ ፲፬። ፷፪፡ ፲። ኤር፲፡ ፳፫። ማር፩፡ ፪)።

**ጸያሒ፤ (ሒት፡ ሕያን፡ ያት)፤** የሚጠ ርግ፤ ጠራጊ። ዮሐንስ፡ ጸያሔ፡ መብእስ፡ (ድጓ)።

**ተጼሐ፤** ተጠረገ፤ተደለደለ፤ተበጀ፡ ተዘጋጀ፤ ተከናወነ። ትጸያሕ፡ ፍኖተ፡ ራትዓን። ይጸያሕ፡ ዐ ውዱ፡ ለማኅፈድ። ይጸያሕ፡ ሎቱ፡ ሥሉ፡ ግብር፡ (ኤር፳፯፡ ፯። ሄርማ። አፈ፡ ተ፳፯)።

**ጽዩሕ፤ (ሓን፡ ሓት፡ ይሕት)፤** የተጠረገ፤ የተደለደለ፤ የቀና፡ ቅን፤ ትክክል። ፍኖት፡ ጽዩሕ፡ ወርሒብ። ሥሉ፡ ግብር፡ ይከውን፡ ጽዩሐ፡ በኀቤነ። እስመ፡ ትሩፎሙ፡ ጽይሕት፡ ግብር፡ (አፈ፡ ተ፲፱ና፡ ፳፯። ፊልክ፡ ፫)።

**ጽያሕ፤ (ሓት)፤** ጥርጊያ፤ አውራ፡ መን ገድ፤ ታላቅ፡ ጐዳና፤ እሾኽ፡ ዕንቅፋት፡ የሌለበት። ጽ ያሐ፡ ንጉሥ፡ (ቁር፡ ጸላ)።

**መጽያሕት፤** ዝኒ፡ ከማሁ። ፍኖተ፡ ጽኑ ዓን፡ መጽያሕት። ይኩን፡ ሥሉ፡ መብእስ፡ መጽያ ሕተ፡ ርቱዐ። ስእኑ፡ ሐዊረ፡ መጽያሕት፡ (ምሳ፲፭፡ ፲፱። ኢሳ፵፡ ፬። ፶፱፡ ፲፬)። ፍኖትን፡ ተመልከት።

**ጺም፤ (ዕብ፡ ጺይይ፤ ጼይም)፤** የዱር፤ የበረሓ፡ አራዊት፤ በምድረ፡ በዳ፡ የሚኖሩ። ጺም፡ ምስለ፡ ኢም፡ (ኤር፶፡ ፴፱)። ጺያ፡ ጭው፡ ያለ፡ በ ረሓ፤ ጺይም፡ በረኸኞች። የኢምን፡ ፍች፡ በቦታው፡ ተመልከት። ባለብሉዮች፡ ግን፡ ኢምን፡ ቀኝ፤ ጺምን፡ ግራ፤ የብስ፡ ይሉታል።

**ጽዮን፤ (ዕብ፡ ጺዮን)፤** ስመ፡ ሀገር፤ የኢያ ውሴዎን፡ አንባ፤ ዳዊት፡ የያዛት፤ ሀገረ፡ ዳዊት። ፍችው፡ ጸወን፤ ምልክት፡ ማለት፡ ነው፡ (መዝ፡ ፪)።

**ጼንዎ፤ ዎት፤ (ጼነወ፡ ይጼኑ፤ ምዕዝ)፤** መሽተት፤ ሽታ፡ መዐዛ፡ መስጠት፤ የክፉ፡ የበጎ። ጺእ፡ ለክፉ፡ ብቻ፤ ጼነወ፡ ለኹሉ፡ ይኾናል። ይጼኑ፡ ጺአ ተሙ። ሶበ፡ ጼነዎ፡ ይጐይይ። ወሶበ፡ ጼነዎ፡ ጼ ናሁ፡ ለዝክቱ፡ ጋኔን፡ ጐየ፤ የክፉ፡ (ጦቢ፰፡ ፲፰። ፰፡ ፫)። ዘሠናየ፡ ይጼኑ። ዘትጼኑ፡ ቀፀ። ወጼነወ፡ ጼና፡ ምዑዝ፡ ፈድፋደ። ጼነዎ፡ ጼና፡ ዕፍረት፡ (አርጋ፡ ፩። ስንክ፡ ጥቅምና፡ ፳። የካ፩)።

**ጼናዊ፤ (ዊት፡ ውያን፡ ያት፤ ጼነውት)፤** የሚሸት፤ የሚገማ፤ ግም፡ ግማታም፤ በሽታጣ። ጨናዊ፡ እንዲል፡ (ትግሬ)።

**ጺንው፤ (ዋን፡ ዋት፡ ኑት፤ ንውት)፤** የሸተተ፤ ሽታው፡ የተለወጠ፤ የገማ፡ የበሸቀጠ።

**ጼና፤ (ናት)፤** ሽታ፤ መዐዛ፤ ጠረን። ጼና፡ ሕ ሡም፡ ወጽዩእ፡ ወፍጉግ፡ ጥቀ። ንኩን፡ ንጹሓነ፡ እምሥሉ፡ ጼና፡ ኀጢአት። ወአልቦ፡ ባዕሌሆሙ፡ ጼና፡ ዘእሳት። ጼና፡ ተይ። ጼና፡ ዕፍረት። ጥዑም፡ ጼና፡ መዐዛሁ፡ (ግንዘ። ቅዳ። ዳንኤ፡ ፫፳። ሔኖ። ስ ንክ፡ የካ፩። መዋሥ)።

**አጼነወ፤ (ዐረ፡ ሸመ)፤** አሸተተ፤ አነፈነፈ። ወአጼነወ፡ እግዚ፡ መዐዛ፡ ሡናየ። ኢአንፎሙ፡ ለአ ጼንዎ፡ ነፋስ። እምርሑቅ፡ ያጼንዎ፡ ለቀትል። ፈ ትል፡ ሶበ፡ ያጼኑ፡ እሳተ፡ (ዘፍ፰፡ ፳፩። ጥበ፲፩፡ ፲፩። ኢዮ፴፱፡ ፳፭። መሳ፲፮፡ ፱)።

**አጼንዎ፤** ማሽተት፤ ያፍንጫ፡ ሥራ። ሕዋ ስን፡ ተመልከት።

**መጼንው፤** የሚያሸት፤ የሚያነፈንፍ፤ አሽ ታች።

**ጼናታም** ፤ ጤናዳም ፤ የሚሸት ፤ ሽታማ ፤ ባለ ሽታ ። አዛብ ፡ ወጼናታም ፡ (ሉቃ ፲፩ ፡ ፵፪) ።



ጼናታም ፡

**ጸይፎ ፤ ፎት ፤ (ጸየፈ ፡ ይጼይፍ ፡ ይጸይፍ)** ፤ (ጥየ) መጸየፍ ፤ ጸያፍ ፡ መኾን ፤ መባል ፤ መንቀፍ ፤ መኰሳተፍ ። የቅኔ ፡ የንገር ፤ የጥፈት ፤ ያንደበት ። ማጸየፍ ፤ መንቀፍ ፤ ጸያፍ ፡ መያዝ ። (ጥጸ) መጸየፍ ፤ መጥላት ።

**ጸያፍ ፤ (ፍት ፡ ፉን ፡ ፉት)** ፤ በቁሙ ፤ አለስልቱ ፡ አላገባቡ ፡ የተጣፈ ፡ የተነገረ ፡ ቃል ፤ ኵልታፋ ፤ ረ ፡ ሲሉት ፡ ለ ፡ የሚል ። ጸያፍ ፡ ወላዕላዐ ፡ ልሳን ፡ አነ ። ልሳን ፡ ጸያፍ ። ወአፉየ ፡ ሙሴ ፡ ለእመ ፡ ከነ ፡ ጸያፈ ፤ ጰራቅሊጦስ ፡ አሮን ፡ ይኩነኒ ፡ አፈ ። በሃማን ፡ ወጸያፋን ፡ (ዘፀ ፬ ፡ ፲ ። ፯ ፡ ፩ ። ኢሳ ፴፪ ፡ ፴፬ ። ፴፪ ፡ ፬ ። ደራሲ ። ቀሌ) ።

**አጸየፈ ፤ (አስደራጊ)** ፤ አስጠየፈ ፤ አስነቀፈ ፤ ጸያፍ ፡ አሰኘ ።

**ጺጽ ፤ (ብ ፡ ጻይጽ ፡ ዕብራ)** ፤ አበባ ፤ ን ፡ ድብድብ ፡ በጣም ፡ ያልፈካ ፡ ያልፈነዳ ፤ ወይም ፡ የእሸት ፡ ወለባ ፡ ገለባ ፡ ጥርጣሪ ። አፒልያኖስ ፡ ወሀቦ ፡ ውስተ ፡ እዴሁ ፡ ጺጸ ፤ ወይቤሎ ፡ ገር ፡ ውስተ ፡ ገጹ ፡ ለዝንቱ ፡ ነዳይ ፡ (ስንክ ፡ ሐም ፳) ።

**ጸይቆ ፤ ቆት ፤ (ጸየቀ ፡ ይጼይቅ ፡ ይጸይቅ ። ዕብ ፡ ጻቅ ፤ ያጻቅ ፤ ወደየ ፡ ከዐወ)** ፤ መጤቅ ፤ መበከል ፤ ጢቅ ፡ ማለት ፤ የመርዝ ፡ የምራቅ ፤ የስድብ ፡ የስብቅ ፤ ከባብ ፡ ከሰይጣን ፡ ከክፉ ፡ ሰው ፡ አፍ ፡ የሚወጣ ፡ (ራእ ፲፪ ፡ ፲፭ ። ኢዮ ፭ ፡ ፲፭ ። ፪ ፡ ፭ ። መዝ ፡ ፵፫ ፡ ፲፮) ።

**ጸያቂ** ፤ የሚጤቅ ፤ ጤቀኛ ፡ መርዘኛ ፤ መስተዋድይ ፤ ሰብቀኛ ፤ አጥፊ ፤ ቀጣፊ ፤ ተንኰለኛ ። እስመ ፡ ጸያቂ ፡ ውእቱ ፡ ከመ ፡ አቡሁ ፡ ዲያብሎስ ፡ (መቃ ፡ ገ፲፯ ። ሲኖዶ ። ዮሐ ፰ ፡ ፵፬ ። ዘፍጥ ፡ ፭ ። ፎንገ ፡ ፳፪ ፡ ፲፱—፳፪) ።

**ጽያቄ** ፤ መጤቅ ፤ ጢቅታ ፤ ምራቅ ፤ መርዝ ፤ ስብቅ ፤ ተንኰል ።

**ጸከ ፤ ጸኰ ፤ (ብ ፡ ጸኳት)** ፤ ጭን ፤ ሹልዳ ፤ ታፋ ። ነደፍዎ ፡ በሐጽ ፡ ጸከ ። እግዚአብሔር ፡ ተጋደሎ ፡ ወአስያዘዘ ፡ ጸከ ፡ ወሰመየ ፡ እስራኤል ፤ ወበእንተ ፡ ዝ ፡ ኢይበልዑ ፡ አይሁድ ፡ ሥርዋተ ፡ ጸኰ ፡ (፩ነገ ፡ ፴፭ ፡ ፫ ። ዮሴፍ ። ስንክ ፡ ነሐ፳፰) ። ባለብሉዮች ፡ ግን ፡ ትከሻ ፡ ይሉታል ። ጋላም ፡ ጨኩ ፡ ነቡኤ ፡ ይላል ፡ ትከሻ ፡ ወረደኝ ፡ ሲል ፤ ጨኩና ፡ ማንቃ ፡ ይመሳሰላሉ ፤ አንድ ፡ ወገን ፡ ናቸው ። ቍጽን ፡ ተመልከት ።

**ጽሌ ፤—የመጣፍ ፡ ገበታ ፤—ጸልዮ ፡ ጸለየ ።**

**ጸሊእ ፤ አት ፤ (ጸልአ ፡ ይጸልእ ፡ ይጽላእ ። ዕብ ፡ ሳኔእ ። ሱር ፡ ስናእ ። ዐረ ፡ ሸነአ)** ፤ መጥላት ፤ መጠየፍ ፤ መቈጣት ፡ መንቀፍ ፤ መቀየም ፡ መናቅ ፤ ልብን ፡ ማራቅ ። ጊዜ ፡ ለጸሊእ ። አፈድፈዱ ፡ ጸሊኦቶ ። ዘትጸልእ ፡ ለርእስከ ፡ ኢትግበር ፡ ዲበ ፡ ቢጽከ ። አፍቀሩ ፡ ዘጸላእክሙ ፡ አነ ። ጣዖተ ፡ ጸልአት ፡ ነፍስየ ፡ (መክ ፫ ፡ ፰ ። ዘፍ፴፯ ፡ ፰ ። ዲድ ፡ ፩ ። ኢሳ ፳፯ ፡ ፱ ። ኩፋ ፡ ፳፩) ። ምዝርና ፡ ጸልአ ፡ ባማርኛ ፡ ይተባበራሉ ። (ግጥም) ፤ ጮማውና ፡ ጠጁ ፡ መልቶ ፡ በቤታቸው ፤ እግዚያሔር ፡ ጠላና ፡ እንጀራ ፡ ነማቸው ።

**ጸላኢ ፤ (ኢት ፡ እያን ፡ ያት)** ፤ የሚጠላ ፡ ጠላት ፤ ምቀኛ ፤ ባለጋራ ፤ ደመኛ ። በእንተ ፡ ጸላኢ ፤ ከመ ፡ ትንሥቶ ፡ ለጸላኢ ። ጸላእያንየ ፡ ወቀናእያንየ ። ጸላእያነ ፡ እግዚ ። አፍቅሩ ፡ ጸላእተክሙ ፡ (መዝ ፡ ፰ ። ዮሴፍ ። ሮሜ ፭ ፡ ፲ ። ማቴ ፭ ፡ ፵፬) ።

**ጽልእ ፤ (አት)** ፤ ጥል ፡ ጠብ ፤ ቂም ። ፍጹመ ፡ ጽልአ ፡ ጸላእክዎሙ ። በልቦሙ ፡ ይሠይሙ ፡ ጽልአ ። ኅድጋ ፡ ለጽልእ ፡ (መዝ ፡ ፻፴፰ ። ኤር ፱ ፡ ፰ ። ሚራ፳፰ ፡ ፯) ።

**አጽልአ** ፤ አስጠላ ፤ አስነቀፈ ፤ አስቀየመ ። አጽላእክሙኒ ፡ በኀበ ፡ ሕሎሙ ። ቦ ፡ ዘያጸልእ ፡ ርእሶ ፡ በብዝኀ ፡ ነቢቡ ። ከመ ፡ ኢታጽልአ ፡ ለቢጽከ ፡ (ዘፍ ፴፬ ፡ ፴ ። ሚራ፳ ፡ ፭ ። ፴፬ ፡ ፲፯) ።

**መጽልእ** ፤ የሚጠላ ፤ የሚያስጠላ ፤ ተጠይ ፡ አስጠይ ፤ አስቀያሚ ። መጽልእ ፡ ዘከመ ፡ ዝ ፡ ብእሲ (ሚራ፳ ፡ ፲፭) ።

**ተጸልአ** ፤ ተጠላ ፤ ተነቀፈ ። ርእየ ፡ ከመ ፡ ትጸላእ ፡ ልያ ። ዘተጸልኡ ፡ በኀበ ፡ እግዚ ። እስመ ፡ ዕሩየ ፡ ተጸልኡ ፡ (ኩፋ ፡ ፳፰ ። ዘፍ፳፱ ፡ ፴፩ ። ምሳ፳፱ ፡ ፴፭ ። ጥበ፲፱ ፡ ፱) ።

**ጽሉእ ፤ (አን ፡ አት ፡ ልእት)** ፤ የተጠላ ፤ የተነቀፈ ፡ ንቁፍ ። ለእመ ፡ ከነ ፡ ውእቱ ፡ ግብር ፡ ጽሉአ ፡ እምኢገብርዎ ። ጽሉእ ፡ በኀበ ፡ እግዚ ፡ ትዕቢት ። ትከውኑ ፡ ጽሉኣነ ፡ በእንተ ፡ ስምየ ፡ (ዮሴፍ ። ሚራ፲ ፡ ፯ ። ማቴ፲ ፡ ፳፪) ።

**ጽልአት** ፤ መጥላት ፤ መጠላት ፤ አጠላል ፤ ጠላትነት ።

**ተጻልአ** ፤ ተጣላ ፤ ተጠላላ ፤ ተነቃቀፈ ። ኢትፍቅድ ፡ ተጻልኦ ፡ ምስለ ፡ ሰብእ ፡ (ምሳ፫ ፡ ፴) ።

**አስተጻልአ** ፤ አጣላ ፤ አጠላላ ። ዘያስተጻልእ ፡ ብእሴ ፡ ምስለ ፡ ብእሲቱ ፡ (ቄድር) ።

**ጸልእ ፤—ቍስል ፤—ጸሊዕ ፡ ጸልዐ ።**

**ጸላእ ፤—ቋጥኝ ፤—ጸውልዐ ፤ ጸላዕ ።**

**ጸሊብ ፤ ቦት ፤ (ጸለበ ፡ ይጸልብ ፡ ይጽልብ ፤ ዐረብ ። ሱር ፡ ጻላብ ። ዕብ ፡ ታላህ) ፤** መስቀል ፤ ማንጠልጠል ፤ በችንካር ፡ በሐብል ፡ የፈያት ፡ የንዋያት ። ኔስታሊንና ፡ ስቀለን ፡ ተመልከት ።

**ተጸልበ ፤** ተሰቀለ ፤ ተንጠለጠለ ፤ ከምድር ፡ ከፍ ፡ አለ ። ተጸልበ ፡ ምስለ ፡ ዙሉ ፡ ቤቱ ። ኀበ ፡ ተጸልበ ፡ እግዚእሙ ፡ (አስቴ፰ ፡ ፲፫ ። ራእ፲፩ ፡ ፰) ።

**ጽሉብ ፤ (ባን ፡ ባት ፡ ልብት) ፤** የተሰቀለ ፡ ስቁል ፤ ቅንው ፡ ቅቱል ።

**ጸልበ ፤ (ዐረ ፡ ጸሊብ) ፤** መስቀል ፤ መስቀያ ፤ መሰቀያ ። ሰላም ፡ ለስቅለትከ ፡ መልዕልተ ፡ ቅዱስ ፡ ጸልበ ። ሶበ ፡ ተረክበ ፡ ጸልቦሁ ፡ ለወልድ ። ሥሉጠ ፡ ልደት ፡ ክርስትስ ፡ ወመሥዋዕተ ፡ እብ ፡ ዘደበ ፡ ጸልበ ፡ (ስንክ ፡ ኅዳ፰ ። መጋ፳፯ ። ድጓ ። ቅኔ) ።

**መጽለብት ፤ (ታት) ፤** ዝኒ ፡ ከማሁ ። ከመ ፡ ትጠቀም ፡ በመጽለብትከ ፡ እማእከለ ፡ መንበርት ፡ (ቅዳ ፡ ዮሐ) ።

**ጸልሀወ ፤—ሸነገለ ፤—ጸልሐ ።**

**ጸሊው ፤ ዎት ፤ (ጸለወ ፡ ይጸሉ ፡ ይጽሉ ። ጸለየ) ፤** መቀቀር ፤ ማቀርቀር ፤ ማዘንበል ፤ የዥሮ ። መስማት ፡ ማድመጥ ፤ መታዘዝ ። ወጽልዉ ፡ እዝነክሙ ፡ ኀበ ፡ ቃለ ፡ አፉየ ። ጸመመት ፡ እዝን ፡ እምጸሊዎቱ ። ሶበ ፡ ኢጸለወ ፡ ትእዛዘ ፡ ንጉሥ ፡ (መዝ ፡ ፸፯ ። አዋል ። ስንክ ፡ ሠኔ፳፩) ።

**ጽልው ፤ (ዋን ፡ ዋት ፡ ሉት) ፤** የቀቀረ ፤ ያዘነበለ ፤ የንቃ ፡ የተጋ ። ሰላም ፡ ለእእዛኒከ ፡ ጽልዋተ ፡ እለ ፡ ኮና ፤ አምኃ ፡ ነገር ፡ ያብኣ ፡ ለመኩንን ፡ ውስጥ ፡ ኅሊና ። ኢትኩን ፡ ነሣኤ ፡ ገጽ ፡ ወኢጽልወ ፡ ልብ ። እንው ፡ መስተጋድላን ፤ ጽልዋን ፡ ለጸሎት ፡ ዘወትር ፡ (ደራሲ ። ዲድ ፡ ፴፩ ። ቄድር) ።

**ጸሎት ፤** በቁሙ ፤ ጸለየ ። ጸልዮና ፡ ጸሊው ፡ አንድ ፡ ዘር ፡ ናቸው ፤ ወና ፡ የ ፡ ተወራራሾች ፡ ስለ ፡ ኾኑ ፤ በጸሌት ፡ ፈንታ ፡ ጸሎት ፡ ይላል ፤ ጸለየን ፡ ተመልከት ።

**ጸለወ ፤ (ዐረ ፡ ጸላ ። ዕብ ፡ ጻላህ) ፤** ጠበሰ ፤ አበሰለ ፤ በፍም ፡ በነዲድ ። አዘዘ ፡ ይጽልውዎ ፡ ገጸ ፡ ውስተ ፡ እቶነ ፡ ብሊኔ ፡ (ስንክ ፡ ሠኔ፲፱) ።

**ጸላዊ ፤ መጽልው ፤** የሚጠብስ ፤ ጠባሽ ፤ አብሳይ ።

**መጽለወ ፤ (ዲቃ ፡ ግ ። ዐረ ፡ መዘለ) ፤** ጠወለገ ፤ ደከመ ፡ ዛለ ፤ ዝልፍልፍ ፡ አለ ። ዐፀ ፡ ሕይወት ፡ እንተ ፡ ኢትመጸሉ ። ፈርሀት ፡ ንግሥት ፡ ወመጽለወት ፡ ወተንተነት ። ወኢይፈቅድ ፡ እፈንዎሙ ፡ ጽዉማነ ፤ ከመ ፡ ኢይመጽልዉ ፡ በፍኖት ፡ (አርጋ ። አስቴ ፡ ፩ ። ማቴ፲፩ ። ፴፪) ፡ በመጽለወ ፡ ፈንታ ፡ ተመጽለወ ፡ ይላል ፤ ስሕተት ፡ ነው ። ይትመጸለዉ ፡ ወይቈጽሩ ፡ ገጾሙ ። ተመጽለዉ ፡ በድንጋጼ ፡ እንዘ ፡ ይደመሙ ፡ ጥቀ ፡ (ማቴ፮ ፡ ፲፮ ። ጥበ፲፯ ፡ ፫) ።

**ምጽልው ፤ (ዋን ፡ ዋት ፡ ሉት) ፤** የጠወለገ ፤ ጠውላጋ ፤ ደካማ ፤ ዝልፍልፍ ። ማዕር ፡ ልምሉም ፡ ወአኮ ፡ ምጽልው ። ወነበርነ ፡ ውዱቃኒነ ፡ ውስተ ፡ ምድር ፡ ከመ ፡ እንተ ፡ ሰብእ ፡ ምጽልዋን ፡ (ስንክ ፡ የካ፲፯ ። ኪዳ ፡ ፩) ።

**መጽ(ጥ)ለውዝ ፤** መጥረቢያ ፡ መዘለፊያ ፤ ወይም ፡ ወቅለምት ።

**አመጽለወ ፤** አጠወለገ ፤ አሳፈረ ፤ አነወረ ፤ ነቀፈ ፤ አጸየፈ ፤ ሰደበ ። አመጽሉ ፡ ገጸ ፡ ለነሣኢ ፡ ገጽ ፡ (አፈ ፡ ተ፩) ። ይኸውም ፡ ስለ ፡ ሃይማኖት ፡ ነው ፤ ስለ ፡ ሌላ ፡ አይደለም ፡ (ሉቃ፳፱ ፡ ፳፩ ። ግብ፯ ፡ ፶፩—፶፱ ። ፳፫ ፡ ፫) ።

**ጸልሐ ፤ (ዕብ ፡ ጻላሕ) ፤** ጣሰ ፤ ሡንጥቆ ፡ ዐለፈ ። አማረ ፤ ተዋበ ፤ ተከናወነ ፤ በመልክ ፡ በግብር ፡ ባነጋገር ።

**ጸልሐወ ፤ (ተቀ ፡ ግ) ፤** ሸነገለ ፤ አሞኘ ፤ አታለለ ። ጸልሐዉ ፡ በልሳኖሙ ፡ (መዝ ፡ ፭ ። ቄር) ።

**ጸልሓዊ ፤ (ዊት ፡ ውያን ፡ ያት) ፤** የሚሸነግል ፤ ሸንጋይ ፤ አታላይ ፤ ከዳተኛ ። መጽሐፍ ፡ ግን ፡ በጸልሓዊ ፡ ፈንታ ፡ ጽልሕው ፡ ይላል ፤ የጣፊና ፡ የመላሽ ፡ ስሕተት ፡ ነው ። ብእሲ ፡ ዐማዊ ፡ ወጽልሕው ። ኃጥኣን ፡ ወጽልሕዋን ፡ (ዮሴፍ ። ቀሌ) ።

**ተጸልሐወ ፤** ተታለለ ፤ ተሸነገለ ፤ ተሞኘ ፤ ተበለጠ ።

**ጽልሕው ፤ (ዋን ፡ ዋት ፡ ሑት) ፤** የተሸነገለ ፤ ሸንግል ፤ ሞኝ ፤ ተላላ ፤ ዘላላ ።

**ጽልሑት ፤** ሽንገላ ፤ ክዳት ፤ ተንኰል ፤ የፑሊቲክ ፡ ቃል ። ዐመፃ ፡ ወጽልሑት ። ይገብሩ ፡ ላዕሌሁ ፡ ጽልሑተ ። ዘእንበለ ፡ ጽልሑት ፡ ወኢሀኬት ፡ (ዘካ፩ ፡ ፱ ። ዳን፲፩ ፡ ፳፫ ። ፍ ፡ ነ ፡ ፴) ።

(ሀ) **ጸለጠ ፤ (ዐረ ፡ ጸለተ) ፤** ጨለጠ ፤ መጠጠ ፤ ባዶ ፡ አደረገ ። ወይጸልጥ ፡ (አዋል) ።

(ሠ) **ጸልዮ ፤ ዮት ፤ (ጸለየ ፡ ይጼሊ ፡ ይጸሊ ። ጸለወ) ፤** መጸለይ ፤ መለመን ፤ መሳል ፤ ማመስገን ፤ ከአምላክ ፡ ጋራ ፡ መነጋገር ። አውተረ ፡ ጸልዮ ። አንትሙሰ ፡ ሶበ ፡ ትጼልዩ ፡ ከመ ፡ ዝ ፡ በሉ ። ጸሎተ ፡ ጸለየ ፡ ለእግዚ ፡ እንዘ ፡ ይብል ፡ (ሉቃ፳፱ ፡ ፵፱ ። ማቴ፮ ፡ ፱ ። ኩፋ ፡ ፳፯) ።

**ጸላዪ ፤ (ዪት ፡ ይያን ፡ ያት) ፤** የሚጸልይ ፤ ጸላይ ፤ ጸሎተኛ ። ፈሪሳዊ ፡ ጸላዪ ፡ ወመጸብሓዊ ፡ ጸላዪ ፡ (ፊልክ ፡ ፴፩) ።

**መጸልይ ፤** ዝኒ ፡ ከማሁ ። ረከቦ ፡ ጽዉመ ፡ ወጽምወ ፡ ወመጸልየ ፡ (ፊልክ ፡ ፻፴፯) ።

**ምጽላይ ፤ (ያት) ፤** መጸለያ ፤ የጸሎት ፡ ቦታ ፤ ቤተ ፡ ክሲያን ፤ ምኵራብ ፤ መስጊድ ። ምጽላየ ፡ መሀይምናን ። ዘይጼሊ ፡ ኀበ ፡ ምጽላየ ፡ አይሁድ ፡ ወአረሚ ፡ (ቅዳ ፡ ጎር ። ቀሌ) ።

**ጸሎት ፤ (ታት ። ሱር ፡ ጽሎታ ። ዐረ ፡ ጸላዋት) ፤** በቁሙ ፤ ልመና ፤ ምስጋና ። ጸሎትሰ ፡ ተናግሮተ ፡ ሰብእ ፡ ኀበ ፡ እግዚ ፡ ልዑል ፤ እንዘ ፡ የአዙቶ ፡ ወይሴብሖ ፡ ወይትአመን ፡ በእግዚእናሁ ፤ ወበተአምኖ ፡ በአበሳሁ ፡ ወኀሚሥ ፡ እምኔሁ ፡ በዘያሠምሮ ፡ ቦቱ ። ወጸሎትሰ ፡ ዘተአዘዘ ፡ ላዕለ ፡ ኵሎሙ ፡ ምእመናን ፡ በኵሉ ፡ ዕለት ፡ ሰብዐቱ ፡ ጊዜያት ። ቤትየሰ ፡ ቤተ ፡ ጸሎት ። ሠናይ ፡ ውእቱ ፡ ጸሎት ፡ (ፍ ፡ ነ ፡ ፲፬ ። ኢሳ፶፮ ፡ ፯ ። ጦቢ፲፪ ፡ ፰) ።

**ጸሎት ፤ (ዕብ ፡ ኔዴር) ፤** ስለት ፤ ብፅዐት ። በፅዐን ፡ ተመልከት ። ጸለይኩ ፡ ጸሎተ ፡ አመ ፡ ጕየይኩ ፡ እምገጸ ፡ ጌሳው ፡ እኁየ ። ጸሎታ ፡ ዘከመ ፡ ነበበት ፡ በከናፍሪሃ ። ወሀቦ ፡ ለልዑል ፡ ጸሎተከ ፡ (ኵፋ ፡ ፴፩ ። ዘኍ፴ ፡ ፯ ። መዝ ፡ ፵፱) ።

**ተጸለየ ፤** በቁሙ ፤ ተጸለየለት ፤ ተጸለየበት ፤ ተለመነ ፡ ተመሰገነ ፤ ጸሎት ፡ ምስጋና ፡ ቀረበለት ። ዘአሐደ ፡ ይሰገድ ፡ ወአሐደ ፡ ይሴባሕ ፡ ወአሐደ ፡ ይጼለይ ፡ (መጽ ፡ ምስ) ።

**ጽሉይ ፤** የተጸለየበት ፤ ጸሎት ፡ የደረሰበት ። ዘይት ፡ ጽሉይ ፤ ማየ ፡ ምንዛህ ፡ ጽሉይ ፡ (መጽ ፡ ምስ) ።

**ጽሌ ፤ (ላት) ፤** የጸሎት ፡ መጣፍ ፤ እንደ ፡ ሳታትና ፡ እንደ ፡ ዳዊት ፤ እንደ ፡ ቅዳሴ ፡ ያለ ።

**ጽሌ ፤ (ለውሒ ፤ ሰሌዳ) ፤** የመጣፍ ፡ ገበታ ፤ ከመጣፉ ፡ ጋራ ፡ በቶታን ፡ በጥራዝ ፡ በድጕስ ፡ ቈርበት ፡ የሚያያዝ ፤ ከቈርበቱ ፡ ላይ ፡ ብዙ ፡ ዐይነት ፡ ሐረግ ፤ ሥዕል ፡ መስቀል ፡ የሚሣልበት ፡ የሚታተምበት ፤ ጌጣም ፡ ሽልምልም ።

—፤ ታቦት ፤ የመጽሐፍ ፡ ዐይነት ፤ ሐረጉና ፡ ጌጡ ፡ በመጽሐፍ ፡ ድጕስ ፡ አምሳል ፡ የሚሠራ ፤ በላዩ ፡ ስመ ፡ አምላክና ፡ ዐሠርቱ ፡ ቃላት ፡ ባጭር ፡ ቃል ፡ የሚጣፉበት ፤ መሥዋዕት ፡ የሚሠዋበት ፤ ከዕፅ ፡ ከእብን ፡ በረድ ፡ የሚቀረጽ ። ታቦትን ፡ ተመልከት ። ወአኮ ፡ በጽሌ ፡ ዘእብን ፡ ዘእንበለ ፡ ጽሌ ፡ ልብ ፡ ዘሥጋ ። ወወሀቦ ፡ ለሙሴ ፡ በደብረ ፡ ሲና ፡ ክልኤ ፡ ጽላተ ፡ ሕግ ፡ ጽላተ ፡ ዘእብን ፡ (፪ቆሮ ፡ ፫ ፡ ፫ ። ዘፀ፴፩ ፡ ፲፰) ። ጽሌ ፡ ጽላት ፡ ለዕፅና ፡ ለእብን ፡ ለማዕደን ፡ ብቻ ፡ እንጂ ፡ ለከርታስና ፡ ለብራና ፡ አይኾንም ። ጽላተ ፡ ሰማይ ። ጽላተ ፡ ብርት ፤ ጽላተ ፡ ብሩር ። ጽላተ ፡ ሐመር ፡ (ኵፋ ፡ ፫ ። ዮሴፍ ። ስንክ ፡ ግንቦ፩) ። ጽሌ ፡ ላንድ ፤ ጽላት ፡ ለኹለት ፤ ለብዙም ፡ ይኾናል ። ባማርኛ ፡ ግን ፡ አንዱ ፡ ብቻ ፡ ጽላት ፡ ይባላል ፤ ይኸውም ፡ ሥራው ፡ በመጽሐፍ ፡ አምሳል ፡ መኾኑን ፡ ያሳያል ፤ አንድ ፡ ቅጠል ፡ ከርታስ ፡ ወይም ፡ ብራና ፡ በኹለት ፡ ወገን ፡ ስለ ፡ ተጣፈበት ፡ ኹለት ፡ ገጽ ፡ እንዲባል ፤ ጽላት ፡ ማለትም ፡ እንደዚህ ፡ ነው ።

**ጸለተ ፤ (ዲ ፡ ቃ ፡ ግ) ፤** ጋገረ ፤ ጠፈጠፈ ፤ ኰበት ፡ አስመሰለ ፤ አሣሣ ፤ ሸለመ ፡ ጠቀጠቀ ፤ የቂጣ ፡ የመጠቃ ፡ የጥረሾ ። ሐማሴኖች ፡ ኅኅ ፡ ይሉታል ።

**መጸለት ፤ (ዕብ ፡ ማጸት) ፤** ፍጹም ፡ ናእት ፤ ቂጣ ፤ ወዲያው ፡ ተለውሶ ፡ የሚጋገር ፤ የፋሲካ ፡ ምግብ ፤ አይሁድ ፡ እስከ ፡ ሰባት ፡ ቀን ፡ የሚበሉት ። ናእትንና ፡ ፍሥሕን ፡ ተመልከት ። ወቀርበ ፡ በዓለ ፡ መጸለት ፡ ዘስሙ ፡ ፋሲካ ። ወበጽሐት ፡ ዕለተ ፡ መጸለት ፡ አመ ፡ ይጠብሑ ፡ ፍሥሐ ። አስትዓ ፡ ዘመጸለት ፡ (ሉቃ፳፪ ፡ ፩ና ፡ ፯ ። ማር፲፬ ፡ ፩ና ፡ ፲፪ ። ሲኖዶ) ።

(፩) **ጸሊል ፤ ሎት ፤ (ጸለለ ፡ ይጸልል ፡ ይጽልል ። ዕብ ፡ ጻላል ። ዐረ ፡ ጸለ ። ሱር ፡ ጻሊል) ፤** መጥለል ፤ መጥራት ፤ ጥሩ ፡ መኾን ፤ መፍሰስ ፤ መቅለጥ ፤ መንጠር ፤ ለመጥራት ። አድራጊም ፡ ይኾናል ።

—፤ መስፈፍ ፤ መንከፈፍ ፤ መንሳለል ፤ መዋኘት ። ጸለለ ፡ ዝክቱ ፡ ኀጺን ። ጸለለት ፡ ታቦት ፡ ላዕለ ፡ ማይ ። ኢተሠርሙ ፡ ውስተ ፡ ባሕር ፤ አላ ፡ ጸለሉ ፡ መልዕልተ ፡ ማይ ፡ (፬ነገ ፡ ፮ ፡ ፮ ። ዘፍ፯ ፡ ፲፰ ። መቃ ፡ ገ፪) ። ሩፋኤል ፡ መልአከ ፡ ራማ ፡ ባሕረ ፡ ሥጋዌ ፡ አመ ፡ ጸበተ ፡ እንዘ ፡ እምነ ፡ ቈጽል ፡ ይነሥእ ፡ አርኣያ ፡ ወእምነ ፡ ሐመር ፡ አምሳለ ፤ ለባሕረ ፡ ሥጋዌ ፡ ላዕሌሁ ፡ ጸለለ ። ዕመቀ ፡ ባሕርዩሰ ፡ ይርአይ ፡ ፈጣሬ ፡ አመ ፡ በእንቲኣነ ፡ ክህለ ፤ ወረደ ፡ ታሕተ ፡ ወተቈልቈለ ፤ ከመ ፡ እማእከል ፡ ኢተርፈ ፡ ወኢተለዐለ ፤ አርአየነ ፡ ኖጻሁ ፡ መስቀለ ፡ (ሥላሴ ፡ ቅኔ) ።

—፤ በአየር ፡ በኀዋ ፡ መርበብ ፤ መሰቀል ፤ ረቦ ፡ ተዘርግቶ ፡ መኼድ ፤ ያሞራ ፡ የደመና ፡ የመሰለው ፡ ኹሉ ። ጸለለ ፡ መንፈስ ፡ ቅዱስ ፡ ላዕለ ፡ ማያት ። ወመንፈስ ፡ እግዚ ፡ ይጸልል ፡ መልዕልተ ፡ ማይ ፡ (ቀሌ ። ዘፍ፩ ፡ ፪) ።

—፤ (ጥጠ) መጠለል ፤ ጥላ ፡ መያዝ ፤ ከጥላ ፡ ማረፍ ፡ መጠጋት ። መጽሐፍ ፡ ግን ፡ በጸለለ ፡ ፈንታ ፡ አጽለለ ፡ ይላል ፤ ስሕተት ፡ ነው ። ያጸልል ፡ ታሕተ ፡ ኵሉ ፡ ዕፀው ። ረከበ ፡ ዕፀ ፡ ጽፍቅተ ፡ ወአጽለለ ። ያጸልሉ ፡ ታሕቴሁ ፡ አራዊተ ፡ ገዳም ፡ (ሚራ፳፮ ፡ ፲፪ ። ተረ ፡ ባሮ ። ዳን፬ ፡ ፱) ።

**ጸላሊ ፤ (ሊት ፡ ልያን ፡ ያት) ፤** የሚጠል ፤ የሚሰፍ ፤ የሚረብ ፡ የሚከንፍ ፤ የሚጠለል ፤ ከጥላ ፡ የሚያርፍ ።

**ጽላል ፤ (ላት) ፤** ጥላ ፤ ድባብ ፤ አጕበር ፤ የሚወጠር ፡ የሚገተር ፤ ፀሓይ ፡ የሚከለክል ።

ጽላል ፤

**ጽላሎት ፤ (ታት ። ዕብ ፡ ጼል) ፤** በቁሙ ፤ ጥላ ፤ ታች ፤ ከፊፍ ፡ ጨለማ ፤ አርኣያ ፡ አምሳል ፤ የዛፍ ፡ የገደል ፡ የሌላውም ፡ ኹሉ ፤ በፀሓይ ፡ ጊዜ ፡ የሚታይ ፡

የሚለይ፤ ብርሃን ፡ ፀሓይ ፡ የሌለበት ። ጽላሎተ ፡ ዕፀ ። ጽላሎት ፡ አድባር ። ጽላሎቱ ፡ ለአምላክ ፡ በማይ ። እስመ ፡ ጽላሎታ ፡ ይእቲ ፡ አፅት ፡ ለእንተ ፡ ትመጽእ ፡ ሠናይት ፡ (ሕዝ፮ ፡ ፲፫ ። መሳ፱ ፡ ፴፮ ። መዝ ፡ ፺ ። ዕብ፲ ፡ ፩) ።

—፤ ቤት፤ ድንኳን፤ ማረፊያ ፡ ማደሪያ ። ሕብእ ፡ ኒዳየ ፡ ወአኅድሮ ፡ ውስተ ፡ ጽላሎትከ ። ጽላሎተ ፡ ቤትየ ፡ (ኢሳ፶፰ ፡ ፯ ። መዝ ፡ ፲፱፻ ፡ ፻፴፩) ።

**ጽላሎተ ፡ ሞት፤ (ዕብ ፡ ጸልማዌት)፤** የሞት ፡ ጥላ፤ ውድቅት፤ ጽኑዕ ፡ ድቅድቅ ፡ ጨለማ፤ ገሃነም ፡ (ኢዮ፫ ፡ ፭ ። መዝ ፡ ፹፮ ። ማቴ፬ ፡ ፲፮) ።

**ጸለሎ፤** ጥላት፤ የጥቀርሻ ፡ ዐይነት ። ከመ ፡ ጸለሎ ፡ መቅፀፊት ፡ ያደምዮ ፡ ለገጽ ፡ (አርጋ ፡ ፪ ። ዮኤ፪ ፡ ፮ ። ናሖ፪ ፡ ፲) ።

**አጽለለ፤** አጠራ፤ አጠለለ፤ አሰፈፈ ፡ አንጓለለ ። ለኀጺን ፡ ማሕጼ ፡ አጽብሎ ፡ ዲበ ፡ ማይ ፡ (አርጋ ፡ ፬) ።

—፤ አስጠጋ፤ አስጠለለ፤ ከጥላ ፡ አሳረፈ፤ ራሱን ፡ ወይም ፡ ሌላውን ። ታጽልሉ ፡ ታሕተ ፡ ዕፀ ። መኑ ፡ ያጸልል ። ወአጽለለ ፡ ህየ ፡ (ዘፍ፲፰ ፡ ፬ ። መዝ ፡ ፲፬ ። ማቴ፳፭ ፡ ፲፮) ።

**ምጽላል፤ (ላት)፤** ማጥለያ፤ ማጥሪያ ። መጠጊያ ፡ ማስጠጊያ፤ ጥላማ ፡ ቦታ፤ የዛፍ ፡ ሥር፤ ዳስ፤ ድንኳን፤ ጐጆ፤ ቤት፤ ማኅደርነት ፡ ያለው ፡ ኹሉ ። ወሕነጸ ፡ ምጽላላተ ፡ ሎቱ ፡ ወለእንስሳቲሁ ። ወይትከሉ ፡ ምጽላሎሙ ። ከመ ፡ ምጽላላተ ፡ ቄዳር ። ለአዕዋፍኒ ፡ ምጽላል ፡ ቦሙ ። ምጽላላቲሆሙ ፡ ዘለዓለማዊት ፡ (ኩፉ ፡ ፲፯ ። ኤር፯ ፡ ፫ ። ማሕ፩ ፡ ፭ ። ማቴ፰ ፡ ፳ ። ፊልክ ፡ ፫) ።

**ምጽላል፤ (ዕብ ፡ ሱኮት)፤** ዳስ፤ ጥላ፤ ከለላ፤ ለበዓል ፡ ለድግስ ፡ የሚሠራ ። የአይሁድ ፡ በዓል፤ በጥቅምት ፡ እኩሌታ ፡ የሚውል ። በምጽላል ፡ ፈንታ ፡ መጸለት ፡ ይባላል፤ የመኣሸና ፡ የጣፋ ፡ በሕታት ፡ ነው ። ከመ ፡ ይንበሩ ፡ ደቂቀ ፡ እስራኤል ፡ በመጸለት ። ወውእቱ ፡ መቅድመ ፡ ገብረ ፡ በዓለ ፡ መጸለት ። ወቀርበ ፡ በዓለ ፡ መጸለቶሙ ፡ ለአይሁድ ፡ (ዕዝ ፡ ነሐ፰ ፡ ፲፬ ። ኩፉ ፡ ፲፯ ። ዮሐ፯ ፡ ፪) ።

**መጸለት፤—ቂጣ፤—ጸለየ ፡ ጽሌ ፡ ጽላት ፡ ጸለተ ።**

(ጥ) **ጸልሎ፤ ሎት፤ (ጸለለ ፡ ይጼልል ፡ ይጸልል)፤** መጸለል፤ በላይ ፡ ኹኖ ፡ ማጥላት፤ ጥላ ፡ መኾን፤ ማልበስ ፡ መክደን፤ መሸፈን፤ መከለል ፡ መጋረድ፤ ማጨለም ። ይጼልላ ፡ ደመና ፡ ለደብተራ ። ወአዘዘ ፡ እግዚ ፡ ሐምሐመ ፡ ወበቈለ ፡ ወጸለሎ ፡ መልዕልተ ፡ ርእሱ ፡ ለዮናስ ። ጸለለ ፡ ከመ ፡ ወይን ፡ ማኅደሮ ። አልከወኒ ፡ ወጸለለኒ ፡ አዕይንትየ ። ይጼልሉ ፡ ወይቀትሉ ፡ (ዘኍ፱ ፡ ፲፰ ። ዮና፬ ፡ ፮ ። ሰቈ፪ ፡ ፮ ። ኢዮ፲፮ ፡ ፲ ። ኩፉ ፡ ፱) ።

—፤ እጅን ፡ ክንፍን ፡ ወደ ፡ ላይ ፡ በስተላይ ፡ መዘርጋት፤ በውስጥ ፡ ማደር፤ መምላት ። ንስፍሕ ፡ ለከ ፡ አእዳወ ፡ መዝራዕት ፡ ወንጼልል ፡ ዲበ ፡ ዝንቱ ፡ መሥዋዕት ። እስመ ፡ ኪሩብ ፡ ጸለሉ ፡ ክነፊሆሙ ፡ መልዕልተ ፡ መካና ፡ ወጸለልዋ ፡ ለታቦት ። ወሰእነ ፡ ሙሴ ፡ በዊእ ፡ ውስተ ፡ ደብተራ፤ እስመ ፡ ጸለለ ፡ ደመና ። ኀይለ ፡ ልዑል ፡ ይጼልለኪ ። ወይጼልል ፡ ዲቤሆሙ ፡ (ቅዳ ፡ ጎር ። ፫ነገ ፡ ፰ ፡ ፯ ። ዘፀ፵ ፡ ፴፬ ። ሉቃ፩ ፡ ፴፭ ። ራእ፯ ፡ ፲፭) ።

**ተጸለለ፤** ተጋረደ፤ ተሸፈነ፤ ታወረ ። ተጸለለ ፡ አዕይንትየ ። ወተጸለለ ፡ ልቦሙ ፡ ከመ ፡ ኢያእምርዎ ፡ (ግብ፲፫ ፡ ፲፩ ። ሮ፪ ፡ ፲፩ ። ቅዳ ፡ ግሩ) ።

**ጽሉል፤ (ላን ፡ ላት ፡ ልልት)፤** የተጋረደ፤ የተሸፈነ፤ ሽፍን፤ ድፍን ። ጽሉል ፡ አዕይንቲሆሙ ። ናሁ ፡ ጽሉል ፡ ልቦሙ ፡ ወእዘኒሆሙ ። አብዳን ፡ ወጽሉላነ ፡ ልብ ፡ (ሔኖ ፡ ፹፱ ። ፴፫ ። ኤር፯ ፡ ፲ ። ዲድ ፡ ፱) ።

**ጽላሌ፤** መጋረድ፤ (ጥጋ) መጋረጃ፤ አገራረድ፤ ግርደሽ፤ ጨለማ፤ ዕውርነት ። ጽላሌ ፡ ኀይል ፡ ዘመንፈስ ፡ ቅዱስ ። ወጽላሌ ፡ ኀበፈ ፡ እምአዕይንተ ፡ ይሥሐቅ ፡ ወርእየ ። ግዝረትስ ፡ ጽላሌ ፡ ልብ ፡ በመንፈስ ። በእበዶሙ ፡ ወበጽላሌ ፡ ልቦሙ ። ጽላሌ ፡ ዐይን ፡ (ቅዳ ፡ ሕር ። ኩፉ ፡ ፴፩ ። ሮሜ፪ ፡ ፳፱ ። ኤፌ፬ ፡ ፲፰ ። አርጋ ፡ ፩) ።

**ጸሊም፤ ሞት፤ (ጸልመ ፡ ይጸልም ፡ ይጽልም ። ዕብ ፡ ጼሌም ። ሱር ፡ ጻልማ፤ ጨለማ፤ ሥዕል፤ ምስል)፤** መጨለም፤ መምሸት፤ ውድቅት ፡ ጨለማ ፡ መኾን፤ ጨለማ ፡ መልበስ፤ መጥቈር፤ ጥላት ፡ መምሰል፤ መፍዘዝ፤ ከማየት ፡ መከልከል ። ወድአ ፡ ጸልመ ። እስመ ፡ ጽልመትኒ ፡ ኢይጸልም ፡ በኀቤከ ። ጸልመ ፡ ዙሉ ፡ ዓለም ። ጸልመ ፡ ፀሓይ ። ጸልመ ፡ ገጹ ። ጸልመ ፡ ዐይኑ ። ተጸለለ ፡ ወጸልመ ፡ (ዮሐ፮ ፡ ፲፯ ። መዝ ፡ ፻፴፰ ። ማቴ፳፯ ፡ ፵፭ ። ራእ፮ ፡ ፲፪ ። አስቴ፯ ፡ ፰ ። ሰቈ፭ ፡ ፲፯ ። ግብ፲፫ ፡ ፲፩) ።

—፤ መከዳት ፡ መካድ፤ ከዳተኛ ፡ መኾን ። ጠለመን ፡ እይ፤ የዚህ ፡ ጎር ፡ ነው ።

(ጥ) **ጸሊም፤ (ማን ፡ ማት ፡ ላም፤ ለምት)፤** ጥቍር፤ ጠቋራ፤ ከሰልማ፤ ቅጽልና ፡ በቂ ፡ ይኾናል ። ዘጽሑፍ ፡ በጸሊም ። አባ ፡ ሙሴ ፡ ጸሊም ። አፍራስ ፡ ጸሊማን ። ጸላም ፡ አነ ። ይመጽእ ፡ ለቢሶ ፡ ጸሊመ ። ለምንትኑ ፡ ለበስከ ፡ ጸሊማተ ፡ (አቡሻ ፡ ፴፫ ። ስንክ ፡ ሠኔ፳፱ ። ዘካ፩ ፡ ፰ ። ማሕ፩ ፡ ፭ ። ዮሴፍ ። ፊላስ) ።

**ጽሉም፤** የጨለመ፤ የጠቈረ፤ ጭልም ፡ ያለ፤ የጨለማ ፡ ቦታ ። ጽሉም ፡ ኅሊናሆሙ ። ጽሉመ ፡ ልብስ ። ጽሉማነ ፡ ምድር ፡ (ኤፌ፬ ፡ ፲፰ ። ቀሌ ። መዝ ፡ ፹፫) ።

**ጽልመት፤ (ዐረ ፡ ዙልመት ። ዕብ ፡ ሐሼኽ)፤** መጨለም፤ መጥቈር፤ አጨላለም ። ጨለማ፤ ሌሊት፤ የጨረቃ ፡ ጠፍ፤ ወይም ፡ ሠርቅ ። ጥቍረት ፡ ጥቍርነት ። በምስጢር፤ ኀጢአት ፡ ክሕደት፤ ድንቍርና፤ ሐዘን ፡ መከራ ፡ ይኾናል ። ጸልመት ፡ ፀሓይ ፡

ዐበ፡ ርእየት፡ ፈጣሪን፡ ስቁለ፤ ወኮነ፡ መጠነ፡ ጽል መታ፡ እምጊዜ፡ ስድስቱ፡ ሰዓት፡ እስከ፡ ጊዜ፡ ተስ ዐቱ፡ ሰዓት። ወጽልመት፡ መልዕልተ፡ ቀላይ፤ ወፈ ለጠ፡ እግዚ፡ ማእከለ፡ ብርሃን፡ ወጽልመት፤ ወሰ መዮ፡ ለብርሃን፡ መዓልተ፡ ወለጽልመት፡ ሌሊተ። በካልእ፡ ወርኀ፡ አመ፡ ዐሡሩ፡ ወሰኑዩ፡ ለጽል መት። ቍስል፡ ይእቲ፡ ለልብ፡ ወጽልመት፡ ለገጽ፡ ወሐዘን፡ ለነፍስ፡ ብእሲት፡ እኪት። ወገጹ፡ ዘፍ ፁም፡ በጽልመት፡ (ስንክ፡ መጋቢት ፳፱። ዘፍ፩፡ ፪ና፡ ፬፡ ፭። ፯፡ ፲፭። ፰፡ ፬። ሢራ፳፭፡ ፳፫። ኪዳ)።

**አጽለመ፤** አጨለመ፤ ጨለማ፡ አደረገ፤ አጠ ቈረ፤ ከሰል፡ አስመሰለ፤ አጠፋ፡ ለወጠ። ያጸልም፡ መዓ ልተ፡ ከመ፡ ሌሊት። ኣጻልም፡ ደመና፡ ላዕለ፡ ም ድር። እከዩሃ፡ ያጸልሞ፡ ከመ፡ ርእየተ፡ ድብ፡ ለገጻ። ቅንአተ፡ እከይ፡ ያጸልም፡ ሠናያተ። ስካር፡ ያጸልም፡ ልበ። ገልዓት፡ ዘአጽለምዎሙ፡ በፍ ሕም፡ (ዓሞ፭፡ ፰። ዘፍ፬፡ ፲፬። ሢራ፳፭፡ ፲፯። ጥበ፬፡ ፲፪። ቀሌ። ስንክ፡ መጋቢት)።

**መጽልም፤ (ምት፡ ማን፡ ማት)፤** የሚ ያጨልም፤ የሚያጠቍር፤ አጥቋሪ።

—፤ የጨለመ፤ የጠቈረ፤ ጽሉም፤ ጸሊም። በውስተ፡ መጽልም፡ መካን። ኢትኅሥሥ፡ ርእየተ፡ ገጽየ፡ እስመ፡ ገጽየ፡ መጽልም፡ ከመ፡ ኀጣውእየ። አንበ፡ መጽልመ፡ ገጽ፡ ወብዙኀ፡ አበሳት፡ (ኩፋ፡ ፭። ስንክ፡ ሐም፲። ታኅ፲፬)።

**ጸልመተ፤ (ጽልመት፤ ጸልመ)፤** ጨ ለመ፤ ጠቈረ፤ ደነቈረ። በጸልመ፡ ፈንታ፡ ጸልመተ፡ እ ያለ፡ ይገኛል። ይጸለምቱ፡ በእንተ፡ መንሱት። ትጸ ለምት፡ ነፍሳቲሆሙ። ይጸለምት፡ ልቡ፡ ወይረ ስያ፡ ለእግዚ፡ (ፊልክ፡ ፲፬። ፴፭። ፻፶፯)።

**ጽልሙት፤ (ጽሉም)፤** የጨለመ፤ የጠቈረ፤ ጥቍር፤ ጨለማ፡ ጥቍረት፡ የጸናበት። እንዘ፡ ብሩ ሃን፡ ንሕነ፡ ዘኢጽልሙታን። ከዋክብት፡ ጽልሙ ታን። ጽልሙታን፡ ራእይ፡ ሕዝብ። አባ፡ ሙሴ፡ ጽ ልሙት፡ (አፈ፡ ድ፭። ይሁ፡ ፲፫። ራደሲ። ፊልክ፡ ፴፯)።

**አጸልመተ፤ (አጽለመ)፤** አጨለመ፤ አጠ ቈረ፤ ጨለማ፡ አለበሰ።

**ጸሊዕ፤ ዖት፤ (ጸልዐ፡ ይጸልዕ፡ ይጽ ላዕ። ጸልእ)፤** ማቄም፡ መለገም፤ ማድፈን፤ ማቅ በር፤ ማበጥ፡ መቍሰል፤ መፍረጥ፡ መምገል። ጸምእና፡ ጸምዐ፡ አንድ፡ እንደ፡ ኾኑ፡ ጸልአና፡ ጸልፀም፡ አንድ፡ ዘር፡ ናቸው፤ ዐ፡ በአ፡ መለወጡ፡ የቍስሉን፡ ዐይን፡ አፉንና፡ ፍንጩን፡ ያሳያል።

**ጸልዕ፤ (ዐሪ፡ ሰልዐት)፤** ቍስል፤ ዕባጭ፤ የበትር፡ የደዌ፡ የመቅሠፍት። ቾፌ፡ ጭንቍር፤ ዋጣ፡ ቂጥኝ፤ ኩብሽ፤ ንቀርሳ፤ የመሰለው፡ ኹሉ። ጸልዕ፡ ዘ ይመግል። ወበኵሉ፡ ዲበ፡ ጸልዕየ፡ ቍስለ። ወመ ጽአ፡ ላዕሌሆሙ፡ ጸልዕ፡ እኩይ፡ (ኢሳ፩፡ ፮። መዝ፡ ፴፰። ራእ፲፮፡ ፪)። ምስጢሩ፡ ጽልእን፡ አይለቅም፤ የሚጠላና፡ የሚያስጠላ፤ የሚያስቀይም፤ የሚያስጠይፍ፤ ማለት፡ ነው።

**አጽልዕት፤** ቍስሎች፤ መቅሠፍቶች። ኢየ ሱስ፡ ክርስቶስ፡ ዘአጽልዕቲሁ፡ ምስሌሁ፤ ወመስ ቀለ፡ ሞቱ፡ ቅድሜሁ። አጽልዕት፡ ዘይፈልሕ፡ ዲበ፡ ሰብእ፡ ወእንስሳ። ሐማመ፡ አጽልዕቲሆሙ፡ (ደ ራሲ። ዘፀ፱፡ ፱—፲፭። ራእ፲፮፡ ፲፩)።

**ጸሎት፤—በቁሙ፤—ጸለወ፤ ጸለየ።**

**ጸለተ፤—ጋገረ፤—ጸለየ፡ ጽላት።**

**ጽመ፤—ዝም፡ ብሎ፤—ጸመመ።**

**ጸመ፤—ጦመ፤—ጸዊም፡ ጸመ።**

**ጸሚእ፤ አት፤ (ጸምአ፡ ይጸምእ፡ ይ ጽማእ። ዕብ፡ ጻሜእ)፤** መጥማት፤ መጠማት፤ ውሃ፡ መጠጥ፡ መፈለግ፤ መናፈቅ። ጸምዐን፡ ተመል ከት፤ የዚህ፡ መንቲያ፡ ነው። እለ፡ ጸምኡ፡ ይሑሩ፡ ኀበ፡ ማይ። ዘጸምአ፡ ይምጻእ፡ ኀቤየ፡ ወይስ ተይ። ጸምአት፡ ነፍስየ፡ ኀበ፡ አምላኪየ፡ ሕያው። ነፍስየኒ፡ ከመ፡ ምድረ፡ በድው፡ ጸምአተከ፡ (ኢሳ ፶፭፡ ፩። ዮሐ፯፡ ፴፯። መዝ፡ ፵፩ና፡ ፻፵፪)።

**ጽሙእ፤ (አን፡ ኣት፡ ምእት)፤** የተጠማ፤ የናፈቀ። ወበከመ፡ ጽሙእ፡ ዘየሐልም፡ እንዘ፡ ይ ሰቲ፡ ማየ፡ ወነቂሆ፡ ዓዲሃ፡ ጽምእት፡ ነፍሱ። ዘእ ሙንቱ፡ ጽሙኣን፡ እምቃለ፡ እግዚ። ከመ፡ ይትመ ርሐ፡ በቃላቲከ፡ እለ፡ ጽሙኣን፡ ለነጽሮትከ፡ (ኢሳ ፳፱፡ ፰። መጽ፡ ምስ። አረጋ፡ ድ፪)።

**ጽምእ፤ (ኣት)፤** ጥም፤ ጥማት፤ የውሃ፡ ዕ ጦት፤ የመጠጥ፡ ችጋር። ጽምአ፡ ማይ። ብሔረ፡ ጽ ምእ። እመውት፡ በጽምእ፡ (ዓሞ፰፡ ፲፩። ዘዳ፴፪፡ ፲። መሳ፲፭፡ ፲፰)።

**አጽምአ፤** አስጠማ፤ ውሃ፡ ነሣ፤ ከለከለ፤ ውሃ፡ ውሃ፡ አሰኘ፤ የደዌ፡ የምግብ። አጽማእኳሁ፡ እምስታየ፡ ገነት። አርኀብዎ፡ ወአጽምእዎ፡ (መቃ። ፫ነገ፡ ፳፪፡ ፳፯)።

**ምጽማእ፤** መጠሚያ፤ ማስጠሚያ፤ ደረቅ፡ በረሓ። ወረሰየ፡ ምጽማአ፡ ሙሓዘ፡ ማይ፡ (መዝ፡ ፻፮)።

**ጸምአ፤—ቀረበ፤ አደመጠ፤—ጸምዐ።**

**ጸመደ፤—ጠመደ፤—ፀሚድ፡ ፀመደ።**

**ጸምሀየ፤—ጠወለገ፤—ጸምሐ።**

**ጻምዎ፤ ዎት፤ (ጻመወ፡ ይጻሙ። ጻመ)፤** መጣመን፤ መድከም፤ መሥራት፤ መጣር፤ መ ትጋት፤ ለሥራ። ጸመንና፡ ደከመን፡ ተመልከት። በከ፡ ጻመውኩ። አኮ፡ ለባሕቲትየ፡ ዘጻመውኩ። ሐም ሐም፡ ዘኢጻመውከ። ጻሙ፡ ለምህሮ፡ (ኢሳ፵፱፡ ፬። ሢራ፳፬፡ ፴፬። ዮና፬፡ ፲። ፪ጢሞ፡ ፭፡ ፰)።

**ጺማዊ፤ (ዊት፡ ውያን፡ ያት)፤** የሚደ ክም፤ ተግቶ፣ የሚጥር፤ የሚሠራ። ጺማዊ፡ በገድሉ፡ (ገድ፣ ተክ። ስንክ፣ ኅዳ፲፱። መጋ፲፯)።

**ጺማዊ፤ (ጺማ፡ ዊ)፤** የድካም፤ ባለድካም፤ ደካማ።

**ጺማ፤ (ማት)፤** ጣመን፤ ድካም፤ ሥራ፤ ሥ ቃይ፣ መከራ። ጺማሆሙ፡ ዘእንበለ፡ በቍዕ። ይሴ ሰዩ፡ እምጺማ፡ እደዊሆሙ። የዐርሩ፡ ጺድቃን፡ እ ምጺማ፡ ኃጥኣን። ምግባራቲሁ፡ ወጺማቲሁ፡ (ጥበ ፫፣ ፲፩። ስንክ፣ ጥር፲፯። ሔኖ፶፯፣ ፫። ፊልክ፣ ፹)።

**አጺመወ፤** አደከመ፤ አታከተ፤ ሣቀየ፤ መ ከራ፣ አሳየ። ኢታጺምዎ፡ ለሊቅ። አጺመወት፡ ሥጋሃ፡ በተፀምዶ፡ ጾም፡ ወጸሎት። ነበረ፡ በጾም፡ ወበጸ ሎት፡ ወአጺመወ፡ ሥጋሁ፡ ፈድፋደ፡ (ማር፳፡ ፴፭። ስንክ፣ ጥቅ፩። ግን፲፩)።

(ጥ) **ጸምዎ፤ (ጺመወ። ዐረ፡ ጺመተ)፤** መጨ መት፤ ዝም፣ ዕክም፣ ጸጥ፣ ማለት፤ ሕዋሳተ፣ አፍኣን፣ መጠበቅ፤ አለመታወክ፤ ዳተኛ፣ ዝምተኛ፣ መኾን፤ ከማ ስተዋል፣ ጋራ፤ የመንዥሴ። ሀድአን፣ ተመልከት፤ የዚሀ፣ ከተማ፣ ነው።

**ጽምው፤ (ውት፡ ዋን፡ ዋት)፤** የረጋ፣ የጨ መተ፤ ጭምት፤ ዝም፣ ዕክም፣ ጸጥ፣ ያለ፤ ዝምተኛ፤ ሀዱእ። ጽምው፡ በቃሉ፡ ወራትዕ፡ በልሳኑ። የዋህ፡ ወጽምው። ውስተ፡ መካን፡ ግሑሥ፡ ወጽምው፤ ጭር፣ ጭ፣ ያለ፣ (ሲኖዶ። ሄርማ። ግንዘ)።

**ጽማዌ፤** መጨመት፤ ጭምትነት፤ ዝምታ፤ ጭታ፤ ርጋታ፤ ጸጥታ። ሶበ፡ ይከውን፡ ጽማዌ። ብ እሲ፡ ጠቢብ፡ ያመጽእ፡ ጽማዌ። ሰላም፡ ወጽ ማዌ። ጽማዌ፡ ነፍስ። ወሰደደቶ፡ ውስተ፡ መካነ፡ ጽማዌ፡ (ምሳ፯፣ ፱። ፲፩፣ ፲፱። ፩ዜና፣ ፱፣ ፵። ስንክ፣ ታኅ፳። አፈ፣ ተ፲፱)።

**ጽሙና፤** ጭምትነት፤ ድካም፤ ጸጥታ፤ የገዳም፣ ሥርዐት፤ ጾም፣ ትሕርምት፤ ምናኔ፤ ብቸኝነት። ትሜህ ረነ፡ ጽሙና፡ ወትዕግሥተ፡ ወጸሎተ። መፍቀሬ፡ ጽሙና፡ ወጸሎት። ኅሩያን፡ መነኮሳት፡ ዘንብረቶሙ፡ ጽሙና። ፈለሰ፡ ገዳመ፡ ውስተ፡ ጽሙና፡ (ዲድ፣ ፳፱። ስንክ፣ ሚያ፲። ሐም፳፩። ፊልክ፣ ፵)። ጸመ፣ ጸ መወ፤ ጸመወ፤ እሊሀ፣ ፫ቱ፣ ፩፣ ዘር፣ ናቸው።

**ጸሚሕ፤ ሖት፤ (ጸምሐ፡ ይጸምሕ፡ ይ ጽማሕ። ዕብ፡ ጸማሕ)፤** መብቀል፤ መውጣት፤ ማደግ፤ የቡቃያ።

**ጸምሐየ፤ (ተቀ፡ ግ)፤** መጽለው፤ ጠወለገ፤ ፈራ፣ ዛለ፤ ተሽመለመለ፤ ተለወጠ፤ መድረቅ፣ ገመረ። የ፣ ጸሐየ፣ ካለው፣ የመጣ፣ ነው። ጸምሐየ፡ ከመ፡ ሐ ምለ፡ መሎኬ፡ በውስተ፡ ሐሩር። ርኢ፡ ከመ፡ ኢጸ ምሐየ፡ በለስ። ደቂቅኪ፡ እለ፡ ጸምሐዩ። ወዘኢ ይጸመሐ። ዘእንበለ፡ ይጸምሐ፡ (ኢዮ፳፱፣ ፳፱። ተረ፣ ባሮ። ኢሳ፶፩፣ ፳። ፩ጴጥ፣ ፩፣ ፱። ጥበ፪፣ ፰)።

በጸምሐየ፣ ፈንታ፣ ተጸምሐየ፣ ይላል፤ ስሕተት፣ ነው። በእንተ፡ ትሕርምቶሙ፡ ወድካሞሙ፡ ደግደገ፡ ሥጋሆሙ፡ ወተጸምሐየ። ተጸምሐያ፡ በረኃብ፡ አ ንስት። ወሶበሂ፡ ትጸውሙ፡ ኢትጸምሕዩ፡ (ፊልክ፣ ፲፯። ሰቈ፭፣ ፲። ማቴ፮፣ ፲፮)። ኹለተኛም፣ ጸምሐየየ፣ ተጸምሐየየ፣ እያለ፣ ኹለተኛ፣ የ፣ ይጨምራል፤ የጣፊ፣ ስሕተት፣ ነው፣ (ማር፣ ይሥ፲፫፣ ፩)።

**ጽምሑይ፤ (ያን፡ ያት፡ ሒት)፤** ምጽ ልው፤ የጠወለገ። ሣዕር፡ ጽምሑይ። ኮነ፡ ገጹ፡ ድ ሙነ፡ ወሕብሩ፡ ጽምሑየ፡ (ሄርማ። ፊልክ፣ ፻፳፱)።

**አጸምሐየ፤** አጠወለገ፤ አሳረረ፤ አቃጠለ፤ አ ጠፋ፤ ለወጠ። ላህበ፡ ነድኂ፡ ኢያጸምሐየ፡ ሥጋ፡ እ ንስሳ። ፍርሀተ፡ እግዚ፡ እምከመ፡ ኀደረት፡ ው ስተ፡ ብእሲ፡ ታየብስ፡ ሥጋሁ፡ ወታጸመሒ፡ አዕፀ ምቲሁ። ሐሜቶሙ፡ ታጸምሕያ፡ ለሃይማኖቶሙ። ኢያውሥአት፡ ለአሐቲ፡ እምኔሆን፡ ወኢያጸምሐ የት፡ ገጻ፡ ወኢተሀውከ፡ ልባ፡ (ጥበ፲፱፣ ፳። ፊልክ፣ ፲፮። ሄርማ። ዮሴፍ)።

ጸምላጥ፤—ጨምጫማ፤—መለጠ።

**ጸሚም፤ ሞት፤ (ጸመ፡ ይጸምም፡ ይጽ ምም። ዐረ፡ ጸሚመ)፤** መዘጋት፤ መደፈን፤ መደን ቈር፤ የጆሮ፣ የአፍ። ጸሙ፡ እዘኒሆሙ፡ ከመ፡ ኢይ ስምዑ። ይትመሰው፡ አባሉ፡ ወይጸምም፡ እዝኑ፡ (መቃ፣ ፲፭። ግንዘ)።

—፤ መጥመም፤ መለገም፤ ዝም፣ ቸል፣ ችላ፣ ማለት፤ እያዩ፣ እየሰሙ፣ እንዳለየና፣ እንዳልሰማ፣ መኾን። መ ጽሐፍ፣ ግን፣ ጸመ፣ ጸመመ፣ በማለት፣ ፈንታ፣ ተጽመመ፣ ተጸመመ፣ ይላል፤ አያስኼም። መኑ፡ ጸውዖ፡ ወተጸ መሞ። ኀፍረት፡ ተጸምሞቱ፡ ለዘይጼውዕከ። እግ ዚኦ፡ ኢትጸመመኒ፡ ስእለትየ። ይጸመም፡ ከመ፡ ዘ ኢይሰምዕ። እመ፡ ተጸመምኪ፡ ዮም፡ (ሢራ፯፣ ፲። ፵፭፣ ፰። መዝ፣ ፺፰። ቅዳ፣ ግሩ። አስቴ፬፣ ፲፬)።

**ጸማም፤ (ምት፡ ማን፡ ማት)፤** ጠማማ፤ ልግመኛ፤ ቸልተኛ፤ ደንቈሮ፣ (ትግሬ)።

**ጽሙም፤ (ማን፡ ማት፡ ምምት)፤** ደን ቈሮ፤ ጆሮው፣ የተዘጋ፣ የተደፈነ፤ ዝም፣ ቸል፣ ያለ። ኢትንብብ፡ ሕሡመ፡ ላዕለ፡ ጽሙም። በሃም፡ ወ ጽሙም። ከመ፡ ጽሙም፡ ዘኢይሰምዕ። ለጽሙ ማን፡ መፈውስ፡ (ዘሌ፲፱፣ ፲፱። ሉቃ፲፩፣ ፲፬። መዝ፣ ፴፯፣ ፶፯። ኪዳ)።

—፤ ደረቅ፤ ጥብቅ። ኵሡሕ፡ ጽሙም፡ (ማር፣ ይሥ ፳፰፣ ፱)።

**አጽመመ፤** ዘጋ፤ ደፈነ፤ አደንቈረ። አጽመሙ፡ እዘኒሆሙ፡ ከመ፡ ኢይስምዑ። ዘያጸምም፡ እዘ ኒሁ፡ ከመ፡ ኢይስማዕ፡ ዐውያተ፡ ነዳይ። ላኪሆሙ፡ ለአብዳን፡ ያጸምም፡ እዝነ። ድምፀ፡ በፌልያ፡ ያ ጸምም፡ እዘኒሁ፡ (ኢሳ፯፣ ፲። ዲድ፣ ፲፱። ሢራ፳፯፣ ፲፱። ፴፯፣ ፳፰)።

**መጽመሚ** ፤ ገሮ ፡ የሚደፍን ፤ የሚያስደፍን ፤ ከመስማት ፡ የሚከለክል ። አፍ ፡ የሚያሲዝ ፤ ዝም ፡ የሚ ያሰኝ ። መስም ፡ ቅጽል ፡ ከኹለት ፡ አዕማድ ፡ እንዲወጣ ፡ አስተውል ።

(ጥ) **ጽም** ፤ ድንቍርና ፤ ዝምታ ፤ ጸጥታ ፤ ከንቱ ፤ ብላሽ ፤ ኆስሕ ፤ ዐዘቅተ ፡ ኆስሕ ።

**ጽመ** ፤ ዝም ፡ ብሎ ፤ በዝምታ ፤ በጸጥታ ። ባሕቲቱ ፡ ይነብር ፡ ጽመ ፡ ውስተ ፡ ምግሓሡ ፡ ጽ ርሑ ። ወጽመ ፡ ይትገደፍ ፡ (መሳ፫ ፡ ፳፱ ። ማቴ፲፩ ፡ ፲፯ ። ማር፯ ፡ ፲፱) ።

**ጽሚት ፤ ጽምሚት** ፤ ጥመት ፤ ጠማም ነት ፤ ልግም ፤ ቸልታ ። ዝምታ ፤ ቀስታ ፤ ድብቃ ፡ ስወራ ፤ ምስጢራዊ ፡ ሥራ ። ከመ ፡ ይቅትሎ ፡ ለንጹሕ ፡ በጽ ሚት ። ሀብት ፡ ዘበጽሚት ። ዘአስሐቶ ፡ ለልብየ ፡ በጽምሚት ፡ (መዝ ፡ ፱ ። ምሳ፳፩ ፡ ፲፬ ። ኢዮ፴፩ ፡ ፳፯) ።

**ጽሚተ ፤ ጽምሚተ** ፤ ዝም ፡ ብሎ ፤ ቀስ ፡ መስስ ፡ ብሎ ፤ በቀስታ ፤ ስውሮ ፤ ተሰውሮ ፤ በስውር ፤ በ ምስጢር ፤ በስርቆሽ ፤ በድብቅ ፤ በሹልክታ ፤ በሹክሹክታ ። ማይ ፡ ዘየሐውር ፡ ጽምሚተ ። መከረ ፡ ጽሚተ ፡ ይኅድጋ ። ዐርገ ፡ ጽሚተ ፡ ወአከ ፡ ገሃደ ። አልቦ ፡ ዘተናገርኩ ፡ ጽምሚተ ፡ ወኢምንተኒ ፡ (ኢሳ፰ ፡ ፮ ። ማቴ፩ ፡ ፲፱ ። ዮሐ፯ ፡ ፲ ። ፲፰ ፡ ፳) ።

**ጸመተ** ፤ ጨመተ ፡ ዝም ፡ አለ ፡ ረጋ ፤ ጭምት ፡ ኾነ ።

**ጸመመ** ፤—አሰረ ፡ ጠቀለለ ፡ ፈወሰ ፤—ፀ መመ ።

**ጸምዐ** ፤ (ጸሚአ ፡ ሰሚዕ) ፤ መስማት ፡ ፈለገ ፤ ለሰሚዕ ፡ ቸኰለ ፤ ልሽማ ፡ ልስማ ፡ አለ ። ዘሩ ፡ ጸሚአ ፡ ነው ፤ ዐ ፡ ከሰሚዕ ፡ መጥቶ ፡ በአ ፡ ፈንታ ፡ ገብ ቷል ፤ ምስጢሩ ፡ ጽምእን ፡ አይለቅም ፡ (ዓሞ፰ ፡ ፲፩) ።

**አጽምዐ** ፤ ቀቀረ ፡ ቀፈረ ፤ አዘንበለ ፤ ገሮውን ፡ ሰጠ ፤ አቀረበ ፤ ለመስማት ። ሰማ ፤ አደመጠ ። አሰማ ፡ አስደመጠ ፤ አስደራጊ ። ጸለወንና ፡ አዘነን ፡ ተመልከት ። አጽምዕ ፡ እዝነከ ፡ ወስምዐኒ ። አጽምዑኒ ፡ ፍትሐ ፡ ከናፍርየ ። አጽማዐኩ ፡ ሕቀ ፡ በእዝንየ ። እዝን ፡ ያጸ ምዕ ፡ ዙሎ ፡ ምሳሌ ፡ (፬ነገ ፡ ፲፱ ፡ ፲፯ ። ኢዮ፲፫ ፡ ፮ ። ሚራ፶፩ ፡ ፲፯ ። ምሳ፲፱ ፡ ፱) ።

**አጽማዒ ፤ መጽምዕ ፤ ዒ** ፤ የሚያደምጥ ፤ አድማጭ ፤ ሰሚ ፤ አስማታም ፤ ባላሾክሺኪ ። የተማረ ፡ ሊቅ ፤ መጽሐፍ ፡ የሚያሰማ ፤ ተርጓሚ ፡ ሰባኪ ። መጽ ምዒ ፡ ነገር ፡ (ኢሳ፫ ፡ ፫) ።

**ጸማዕት** ፤—ዋሻ ፡ በአት ፤—ጸወማ ዕት ።

**ጸሚቅ ፤ ቆት** ፤ (ጸመቀ ፡ ይጸምቅ ፡ ይጽምቅ ። ዕብ ፡ ጻማቅ ፤ ደረቀ) ፤ መጭመቅ ፤ መጥመቅ ፤ ውሃውን ፡ ለማውጣት ፡ ለማድረቅ ። ጠመቀን ፡ እይ ፤ የዚህ ፡ መንቲያ ፡ ነው ።

**ጽሙቂም** ፤ (ዕብራ) ፤ ዘቢብ ፤ ደረቅ ፡ የወ ይን ፡ ዘለላ ፤ የበለሰ ፡ ቋንጣ ፡ (፩ነገ ፡ ፳፭ ፡ ፲፰) ። ሙዳየ ፡ ዘቢብ ፡ ባለው ፡ ጽሙቂም ፡ እያለ ፡ ይገኛል ፤ ጺሚቅ ፡ አንድ ፤ ጽሙቂም ፡ ብዙ ።

**ጸምር** ፤—የበግ ፡ የፍየል ፡ ጠጕር ፤—ፀ ምር ።

**ጸመተ** ፤—ጨመተ ፤—ጸሚም ።

**ጸምቶ ፤ ቶት** ፤ (ጸመተ ፡ ይጸምት ። ዕብ ፡ ጻማት ፤ አጠፋ) ፤ ማለቅ ፤ መጣመት ፤ ተጨ ርሶ ፡ መጥፋት ።

**አጸመተ** ፤ አጣመተ ፤ ፈጀ ፡ ጨረሰ ፤ አጠፋ ፡ ደመሰሰ ። ያጸምቶሙ ፡ መጥባሕት ፡ (ዘዳ፴፪ ፡ ፳፭) ።

**ጸንአ** ፤—ጠና ፡ በረታ ፤—ጸኒዕ ፡ ጸንዐ ።

**ጽንጕን** ፤ (ጸንቀቀ) ፤ ጭቃ ። ከመ ፡ ጽን ጕን ፡ ዘይከይዱ ። ጽንጕነ ፡ ፍኖት ። ጽንጕነ ፡ መር ሕብ ፡ (ሚክ፯ ፡ ፲ ። ዘካ፱ ፡ ፫ ። ፲ ፡ ፭ ። መዝ ፡ ፲፯) ።

**ጽንጉፍ** ፤ (ነገፈ) ፤ ጥኑ ፤ ከባድ ፤ ጣሎኝ ፡ ጣለኝ ፡ የሚል ፤ ጥንብ ፤ ዐይን ፡ ምድር ፤ ሬሳ ፤ ጭን ጋፍ ፡ ሙቶ ፡ የሚወርድ ፡ የሚወለድ ። ነገፈን ፡ ተመል ከት ፤ አባቱ ፡ ርሱ ፡ ነው ። ክቡድ ፡ እብን ፡ ወጽንጉፍ ፡ ጾረ ፡ ኆጻ ፡ (ምሳ፳፯ ፡ ፫) ።

**ጸንገፈ** ፤ ጨነገፈ ፤ ጣለ ፤ አሶረደ ።

**ጸኒሕ ፤ ሖት** ፤ (ጸንሐ ፡ ይጸንሕ ፡ ይጽ ናሕ ። ዕብ ፡ ጻናሕ ፤ ጸነ ፡ ወድቀ ። ቃዌሀ ፤ ቈየ) ፤ ደጅ ፡ መጥናት ፤ መቈየት ፤ መጠበቅ ፤ መታገሥ ፤ ተስፋ ፡ ማድረግ ፤ ማድባት ፡ ማሸመቅ ፤ ማድፈጥ ፤ መዘ ጋጀት ፤ የከፉ ። ጸኒሐ ፡ ጸናሕክዎ ፡ ለእግዚ ። መንግሥ ትከ ፡ ይጸንሐከ ። ዐይነ ፡ ዘማዊ ፡ ይጸንሕ ፡ ጽልመተ ። እስከ ፡ እትመየጥ ፡ መንገሌከ ፡ ጽንሐኒ ፡ ጸኒሐ ፤ እ ስመ ፡ ድኅረ ፡ ሞቱ ፡ ለሰብእ ፡ አልቦቱ ፡ ንስሓ ። ጽን ሕዋ ፡ ለምሕረቱ ። ጽናሕ ፡ ፍሬሃ ፡ ቡሩክ ። ይጸ ንሕ ፡ ወይትኄባእ ፡ ከመ ፡ አንበሳ ። ይጸንሕ ፡ መቅ ሠፍት ፡ ለእኩያን ፡ (መዝ ፡ ፴፱ ። ዳን፱ ፡ ፳፫ ። ኢዮ ፳፱ ፡ ፲፭ ። ደራሲ ። ሚራ፲ ፡ ፯ ። ፰ ፡ ፲፱ ። መዝ ፡ ፱) ።

**ጸናሒ** ፤ (ሒት ፡ ሕያን ፡ ያት) ፤ ደጀ ፡ ጠኝ ፤ ጠባቂ ፤ ሸማቂ ። ጸናሒ ፡ ወመስተዐግሥ ። ጸና ሕያን ፡ ተስፋ ፡ ክቡር ። ጸናሕያን ፡ ፍኖት ፡ (ጥበ ፡ ጠቢ ። ስንክ ፡ የካ፳፰ ። ዮሴፍ ። ምሳ፲፱ ፡ ፳፱) ።

**ጽኑሕ** ፤ (ሓን ፡ ሓት ፡ ንሕት) ፤ ያደባ ፤ የ ሸመቀ ፤ የተዘጋጀ ፤ ዝግጁ ። አንበሳ ፡ ዘጽኑሕ ፡ ለመ ሚጥ ። ጽኑሕ ፡ መልአከ ፡ እግዚ ፡ በሰይፍ ፡ ይሥጽ ርከ ። ጽኑሕ ፡ ሎቱ ፡ ኅሳር ፡ ዐጹብ ። ወበከመ ፡ ጽ ኑሕ ፡ ለሰብእ ፡ ምዕረ ፡ መዊት ፡ (መዝ ፡ ፲፮ ። ዳን፩ ፡ ፶፱ ። ኢዮ፲፰ ፡ ፲፪ ። ዕብ፱ ፡ ፳፯) ።

**ጽንሐት** ፤ መቈየት ፤ መታገሥ ፤ አቈያየት ። ቈይታ ፤ ደጅ ፡ ጥናት ፤ ሽመቃ ።

**ጽንሕ** ፤ ዝኒ ፡ ከማሁ ፤ ቈይታ ፤ ሽመቃ ።

**አጽንሐ፤** አቈየ፤ አስቈየ፤ ደጀ፡ አስጠና፤ አዘጋጀ። አጽናሕክሙ፡ ወነፃኅክሙ። ሰማዕተ፡ ባልሐ፡ ዐስቦሙ፡ አጽንሐ። ይቤሎሙ፡ ያጽንሑ፡ ሎቱ፡ ሐመረ፡ (መዝ፡ ፷፱። መዋሥ። ማርቆ፡ ፱)።

**አጽናሒ፤ መጽንሒ፤** የሚያቈይ፤ የሚያዘጋጅ። አጽናሒ፡ ፍዳ፡ (ጥበ፡ ጠቢ)።

**መጽንሕ፤** መጥን፤ መቈያ፤ መስተንግዶ፤ መተያያ። አውገዘ፡ ከመ፡ ኢየሀቡ፡ ግብረ፡ ወመጽንሐ፡ በኀይል፡ ዘእንበለ፡ ፈቃዶሙ፡ ሰበ፡ የአቱ፡ ንጉሥ፡ (ሥር፡ አኵ)።

**ተጽንሐ፤** ተጠባበቀ፤ ተቈያየ። ተጻንሑ፡ ቢጸክሙ፡ (፩ቆሮ፡ ፲፩፡ ፴፫)።

**ጸንሕሐ፤ (ተቀ፡ ግ)፤** ጤሰ፡ ነደደ፡ ተቃጠለ፤ ሸተተ፤ መሥዋዕት፡ ኾነ። በጸንሕሐ፡ ፈንታ፡ ተጸንሕሐ፡ ይላል፤ አያሰኝም፤ የጸንሐ፡ ቅጥይ፡ ነው፡ (አርጋ)።

**ጽንሓሕ፤ (ሓሒት)፤** የሚቃጠል፡ መሥዋዕት፤ ቍርባን፤ ሥብሕ፤ ዕጣን፤ ጢሱ፡ መዐዛው፤ ምሥዋዑ፡ ጥናው። አዕረገ፡ ጽንሓሐ፡ ዲበ፡ ምሥዋዕ። ወጽንሓሐኒ፡ ኢትሠምር። ጽንሓሐ፡ መሥዋዕት። ተዐጥነ፡ ጽንሓሐ፡ ወተዐውደ፡ ወትጸርሐ። ኣዐርግ፡ ጽንሓሐ፡ ለእግዚ፡ (ኵፋ፡ ፯። መዝ፡ ፶። መዋሥ። ግንዘ። መጽ፡ ምስ)። በጽንሓሕ፡ ፈንታ፡ ጽንሓሒ፡ ይላል፤ የተሳሳተ፡ ነው፡ (፪ዜና፡ ፯፡ ፯። ፰፡ ፲፪። ፲፫፡ ፲፭)።

**አጸንሕሐ፤** ሠዋ፤ መሥዋዕት፡ አቀረበ፤ አጤሰ፤ አቃጠለ፤ አሸተተ። አጸንሕሐ፡ ጽንሓሐ። ለአጸንሕሖ፡ ቍርባን። ወኢኀበ፡ ያጸነሕሑ፡ ዕጣነ፡ (ስንክ፡ ሚያ፳፯። መጽ፡ ምስ። ዳንኤ፡ ፲፱)።

**አጸንሓሒ፤** የሚያጤስ፡ የሚያቃጥል፤ አሻታች። ሚካኤል፡ ሣውዕ፡ አጸንሓሒ፡ ሠናይ፡ ጼና፡ መዐዛ፡ (ደራሲ)።

**አጽናሕንሐ፤ (የቅጥይ፡ ቅጥይ)፤** ወዘወዘ፤ አወዛወዘ፤ ለማጠን፤ የጥና፡ የማጠንት።

**ጸኒን፤ ኖት፤ (ጸነ፡ ይጸንን፡ ይጽንን። ደነነ። ዕብ፡ ጻናን፡ ቈረ)፤** መጽነን፤ መጕንበስ፤ መዘንበል፤ ማድላት፡ ማጋደል፤ ማርገዝ፡ ማዘብዘብ፤ የከብ፡ የግንብ። ኀይለ፡ ሃይማኖት፡ ዘኢይጸንን። ወኀሊና፡ ንጹሐ፡ ዘኢይጸንን፡ ጸግወነ። ሶበ፡ ርእየ፡ ከመ፡ ጸነ፡ ልቡ። ኢትጽንኑ፡ መንገለ፡ ፍኖተ፡ ሕገጋት፡ አፍአዊት። ለእመ፡ ጸነ፡ አረፍት፡ መንገለ፡ ፍኖት፡ (ኪዳ። ስንክ፡ መስከ። ፈ፡ መ፡ ፲፰፡ ፩። ፍ፡ ነ፡ ፴፯)። ጸንጸንን፡ ተመልከት፤ የዚህ፡ ዲቃላ፡ ነው። በጸነ፡ ፈንታ፡ አጽንን፡ ይላል፤ ስሕተት፡ ነው። አጽነነት፡ ታቦት። ታጸንን፡ ምድር፡ (፩ዜና፡ ፲፫፡ ፱። ኢሳ፳፬፡ ፳)።

**ጸናኒ፤ (ኒት፡ ንያን፡ ያት)፤** የሚጸን፤ የሚጠም፤ ጠማማ፤ አድላዊ።

**ጽኑን፤ (ናን፡ ናት፡ ንንት)፤** የጸነነ፤ የዘነበለ፤ ያረገዘ፡ ያዘበዘበ፤ ሊወድቅ፡ ሊናድ፡ የቀረበ። ከመ፡ አረፍት፡ ጽንንት፡ (መዝ፡ ፷፩)።

**ጽንት፤** መጽነን፡ መዘንበል፤ መጥመም፤ መጣመም፤ ጠማምነት። እመ፡ ከነ፡ ጽነቱ፡ መንገለ፡ ሐጼር። ንዐቀብ፡ ሃይማኖተ፡ ርትዕተ፡ ዘእንበለ፡ ጽንት፡ (ፍ፡ ነ፡ ፴፯። ሃይ፡ አበ)።

**ጽናኔ፤** ዝኒ፡ ከማሁ። በርትዕ፡ ዘእንበለ፡ ጽናኔ፡ (አፈ፡ ተ፴፱። ፍ፡ ነ፡ ፵፩፡ ፱)።

**አጽነነ፤** አጠነነ፤ አጠመመ፤ አዘነበለ፤ አስጐንበሰ፤ አዋረደ። አጽንኑ፡ ርእሶ። ሕልያን፡ ያዐውር፡ ወያጸንን፡ ነገረ፡ ርትዕ። መኑ፡ አጽነኖ፡ ለሰማይ፡ ዲበ፡ ምድር። አጽንኒ፡ ቀሡተኪ። አጽንን፡ እዝነከ፡ ለርእየ፡ ሕልመ፡ አቡከ። አጽንኑ፡ እንዘ፡ ኢይዜሮ፡ እምድማሬሁ፡ (ዮሐ፲፱፡ ፴። ዲድ፡ ፱። ኢዮ፴፰፡ ፴፱። ዘፍ፳፱፡ ፲፱። ሔኖ፹፩፡ ፪። ቅዳ፡ አፈ)።

**ጸኒዕ፤ ዖት፤ (ጸንዐ፡ ይጸንዕ፡ ይጽናዕ። ዕብ፡ ጻናዕ፤ ታገሠ)፤** መጥናት፤ መጠንከር፤ መበርታት፡ ማየል፤ መድረቅ፡ መክረር፤ ጸንቶ፡ መኖር፤ ቀዋሚ፡ መኾን። ጸንዐ፡ ልቡ። ወጸንዓ፡ እገሪሁ፡ ወሐቌሁ። ጸንዐ፡ ላዕሌሆሙ፡ ቀትል። ትጸንዕ፡ እምኵሎሙ። ሀገር፡ ትጸንዕ፡ በጥበቢሆሙ፡ ለሊቃውንት። ኢይጸንዕ፡ ቃሉ፡ (ዘፀ፯፡ ፲፫። ግብሮ፡ ፯። ኢሳ፵፱፡ ፳፩። ሕዝ፲፱፡ ፱። ፍ፡ ነ፡ ፵፩፡ ፱)።

—፤ መታወቅ፡ መታመን፤ ርግጥ፡ መኾን። ማደግ፡ መጐልመስ፤ አካለ፡ መጠን፡ ማድረስ። መብዛት፡ መፈድፈድ። መርቀቅ፡ መጥለቅ፡ መጨለም፤ የምስጢር። ናሁ፡ ጸንዐ፡ በኀበ፡ ማእምራን፡ ከመ፡ ቍርባን፡ በጸሎተ፡ ካህን፡ ይከውን፡ ሥጋሁ፡ ለኢየሱስ። ወልድየ፡ ዓዲሁ፡ ደቂቅ፡ ወኢጸንዐ። ሶበ፡ ጸንዐ፡ ላዕሌሆሙ፡ ዕግተት። ነዳየ፡ ሃይማኖት፡ ይሁዳ፤ ሜጦ፡ ሰወልድ፡ ሰርጐ፡ አቡሁ፡ ጸፀዳ፤ እስመ፡ ጸንዐ፡ ቦቱ፡ ካሕደ፡ ልብ፡ ዕዳ፡ (ፈ፡ መ፡ ፳፯፡ ፯። ፩ዜና፡ ፳፱፡ ፩። ዮሴፍ። ቅኔ)። የጸንዐ፡ ዐማርኛ፡ እንደ፡ ኾነ፡ ብዙ፡ ስልት፡ አለው፤ ምስጢሩ፡ ግን፡ ከጽንዕ፡ አይወጣም፤ መንገዱም፡ የሰብሐና፡ የገብረ፡ ነው፤ ሲላላ፡ ገብረን፤ ሲጠብቅ፡ ሰብሐን፡ ይመስላል፤ በሰብሐ፡ መንገድ፡ ሲገሰስ፡ ገቢር፡ እንጂ፡ ተገብሮ፡ አይኾንም፤ ይኸውም፡ ለብቻው፡ ተጥፏል።

**ጽኑዕ፤ (ዓን፡ ዓት፡ ንዕት)፤** የጠና፤ ጥኑ፤ ብርቱ፤ ጠንካራ፤ ጥብቅ፤ ደረቅ፡ ከራራ። እብን፡ ጽኑዕ። ኵኵሕ፡ ጽንዕት። አመ፡ ጽኑዐ፡ ይገብር፡ መሠረታተ፡ ምድር። አጽዋናት፡ ጽኑዓን። አህጉር፡ ጽኑዓት፡ (ጥበ፲፩፡ ፱። ኢሳ፶፩፡ ፩። ምሳ፰፡ ፳፱። ፪ቆሮ፡ ፲፡ ፬። ኵፋ፡ ፲፩)።

—፤ ጨካኝ፤ ዐርበኛ፤ ታላቅ፤ ብዙ። ጽኑዕ፡ ልብ። ጽኑዕ፡ በውስተ፡ ቀትል። ሕዝብ፡ ጽኑዕ፡ (ምሳ፲፯፡ ፳። ሚራ፵፯፡ ፩። ኢሳ፳፡ ፳፱)።

**ጽንዐት፤ (ታት)፤** መጥናት፤ መጠንከር፤ ጥናት፤ ጥንካሬ፤ ጭካኔ፤ ብዛት፤ ብርታት፤ ብርቱነት።

ጽንዐተ፡ ልብ። ትክለተ፡ ወጽንዐተ። ሶበ፡ ርእየ፡ ጽንዐተሙ። ጽንዐተ፡ ዝኩ፡ ሥቃይ። ጽንዐተ፡ ቍር፡ (አፈ፡ ድጓ። ቅዳ። ስንክ፡ ኅዳ፳፯። አፈ፡ ድጓ። ግብ ፳፰፡ ፪)።

**ጽንዕ፤ (ዓት)፤** ጥናት፤ ብርታት፤ ኀይል፤ ጥንካሬ፤ ጠፈር። ጽንዐ፡ ልብ። በብዝኀ፡ ጽንዑ። ጽንዐ፡ ሰማይ፡ (ማር፲፯፡ ፲፱። መዝ፡ ፻፶። ዘፀ፳፬፡ ፲)።

**አጽንዐ፤** አጠና፤ አበረታ፤ አጠነከረ፤ መሠረተ፤ አጠበቀ፡ ጠረነቀ፤ ሳበ፡ ገተረ፤ ዘረጋ፡ አከረረ፤ ያዘ፡ ጨበጠ። አጽንዑ፡ ገጸሙ፡ እምኵሉሙ። አሙ፡ ያጸንዕ፡ መንበሮ፡ ባዕለ፡ ንፋሳት። ወአጽንዐ፡ እገሪሆሙ፡ ውስተ፡ ጕንድ። አጽንዐ፡ አውታረ፡ አርጋኖን። እመታ፡ ታጸንዕ፡ ሰፈቲል። ዘያጸንዕ፡ ሰብዐተ፡ ኮከበ፡ በየማኑ። ወያጸንዑ፡ ውስተ፡ እደዊሆሙ፡ ፀበርተ፡ (ኤር፭፡ ፫። ምሳ፳፡ ፳፯። ግብ፲፯፡ ፳፱። ዘርዐ፡ ያዕ። ምሳ፳፱፡ ፴፯። ራእ፪፡ ፩። ፯፡ ፱)። ያዘ፡ ጨበጠ፡ ማለት፡ ጣሬና፡ መላሽ፡ በእንዝና፡ በእንዝ፡ ፈንታ፡ ያጸንዕ፡ እያሉ፡ ስለ፡ ጣፉት፡ እንጂ፡ ዘይቤው፡ አይደለም።

—፤ ጠበቀ፤ አጠና፤ ያዘ፤ የሕግ፡ የትምርት። አጽንዐ፡ ዘብከ። አጽንዖ፡ ሃይማኖት። ሶበ፡ ያነብቦ፡ ለመጽሐፍ፡ አሐደ፡ ጊዜ፡ ያጸንዖ፡ (ራእ፫፡ ፲፩። ቅዳ። ስንክ፡ ሐም፫)።

**አጽናዒ፤** የሚያጠና፤ አጥኚ፡ (ፈላስ)።

**መጽንዕ፤ ዒ፤** መጥኛ፤ ማጥኛ። የሚያጠና፤ መጥኔ፤ አጥኚ፤ ደጋፊ። መጥኔ፡ ይስጥኽ፡ እንዲሉ። ረዳኤ፡ ወዐቃቤ፡ ወመጽንዒ። ኃረይ፡ መዝሙረ፡ መጽንዒ፡ ወመድኅኔ፡ (ግንዘ። ፊልክ፡ ፲፷፫)።

**ተጻንዐ፤ (ጸንዐ)፤** ተጣና፤ ተበራታ፡ ተጠናከረ፤ በገዛ፡ እጁ፡ ወይም፡ ርስ፡ በርሱ። ተደራጊና፡ ተደራራጊ፡ ነው፤ እንደ፡ ተባረከ፡ ኹለት፡ ያሳያል። ተደራጊ፡ ሲኾን፡ የጸንዐ፡ ድርብ፡ ነው። ተደራጊም፡ ቢኾን፡ ተደራራጊነት፡ አይቀርም፤ የሕዋሳትን፡ ርስ፡ በርስ፡ ይሻል። ጊዜ፡ ተጻንዖተ፡ ተቃትሎተ፡ በይጣናት፡ ምስሌሆሙ፡ (ፊልክ፡ ፹፩)።

**አስተጻንዐ፤ (አጽንዐ)፤** አጣና፤ አበራታ፤ አጠናና፡ አበረታታ፤ አይዞኽ፡ አይዞኽ፡ አለ። አድራጊና፡ አደራራጊ፡ ነው፤ ባድራጊነቱ፡ የአጽንዐ፡ ድርብ። በምስጢር፡ ግን፡ አደራራጊነት፡ አይቀርም። አስተጻንዐ፡ መዝራዕተ፡ ወአቍልቍለ፡ ኵናተ። ፈቀደ፡ ያስተጻንዕ፡ ምዕማዲሁ። ዘንተ፡ ይቤ፡ ከመ፡ ያስተጻንዖሙ። ያስተጻንዑ፡ ፍኖረተ፡ በቅድመ፡ ክልኤቱ፡ ካህናት፡ በአንብሮተ፡ እድ፡ ወበመስቀል፡ ወበሕልቀት፡ (ገድ፡ ተክ። አፈ፡ ድ፫። ፍ፡ ን፡ ፳፱፡ ፫)።

(ጥ) **ጸንዖ፤ ዖት፤ (ጸንዐ፡ ይጼንዕ፡ ይጸንዕ)፤** አጽንዖ፤ ማጥናት፤ ማበርታት፤ ማጠንከር፤ ማደስ፡ መጠገን። ጸንዖሙ፡ ለአኀዊከ። ወአስተርአዮ፡ መልአክ፡ ዘይጼንዖ። ዘይጼንዖ፡ መፍቅደ፡ ብሔር። በዘይጼንዖ፡ ቤደቀ፡ (ሉቃ፳፪፡ ፴፪ና፡ ፵፫። ሚራ፴፰፡ ፴፱። ፱፻፡ ፳፪፡ ፭)።

**ጸናዒ፤ (ዒት፡ ዕያን፡ ያት፤ ዕት)፤** አጽናዒ፤ የሚያጠና፤ የሚያበረታ፤ አይዞኽ፡ ባይ፤ ኀያል፤ ዐርበኛ፤ የጦር፡ አለቃ። ምስለ፡ ሠለስቱ፡ ጸናዕት። ዕደው፡ ጸናዕት፡ (፩ዜና፡ ፲፩፡ ፲፱። ፳፭፡ ፩)። ጽኑዓን፡ ኀያላን፡ በማለት፡ ፈንታ፡ ጸናዕት፡ ይላል፤ አያስኼም። አህጉር፡ ጸናዕት። ዙሉ፡ ሰራዊተ፡ ጸናዕት፡ (፪ዜና፡ ፰፡ ፱። ፩ዜና፡ ፲፱፡ ፰)።

**ተጸንዐ፤** ተጠና፤ ተያዘ፤ ከልብ፡ ገባ፤ ተረዳ፤ ትምርቱ፡ ቃለሙ።

**ጽኑዕ፤** የተጠና፤ የተለመደ፤ በቃል፡ የተያዘ።

**ጽናዔ፤** ማጥናት፤ መጠናት፤ አጠናን፤ ጥናት፤ ጥኑነት። ከመ፡ ያስተርኢ፡ ጽናዔሃ፡ ወአፍቅሮታ፡ (ፊልክ፡ ፻፵)።

**ምጽናዕ፤ (ዓት)፤** መጥኛ፤ መጠንከሪያ፤ ማጥኛ፡ ማበርቻ። ሰማይ፤ ጠፈረ፡ ሰማይ፤ ከሀሮስ፡ ጋራ፡ ርስ፡ በርሱ፡ የተጠናና። ሀኖስን፡ ተመልከት። ወበዕለተ፡ ሳኒት፡ ገብረ፡ ምጽናዓተ፡ ማእከለ፡ ማይ። እፎኬ፡ ዘኢንኀሉ፡ ምጽናዓተ፡ ሰማይ። ለዘመጽአ፡ ወልድ፡ በአፈ፡ ነቢያት፡ ተሰቢኮ፤ ከመ፡ ያስተፋኑ፡ ሐራ፡ መልአኮ፡ እስከ፡ ምጽንዓት፡ ኀምስ፡ ሚካኤል፡ ተሰውኮ፡ (ኩፋ፡ ፪። መጽ፡ ምስ። ስንክ፡ ታኅ፲፪)።

**ጸኒፍ፤ ፎት፤ (ጸንፈ፡ ይጸንፍ፡ ይጽንፍ። ዕብ፡ ጻናፍ)፤** ማልበስ፤ ማጐናጠፍ፤ ማጠፍ፤ ማፍና፡ ማፉን፡ መግጠም፤ ወይም፡ መጠምጠም፤ መጠቅለል፤ የልብስ፡ የፈትል። ዳርቻ፡ ማፍ፡ መኾን፤ ወደ፡ ዳር፡ መውጣት፤ ዳር፡ ዳር፡ ማለት።

**ጸናፊ፤ (ፊት፡ ፍያን፡ ያት)፤** የሚጸንፍ፤ ዳርቻ፡ የሚኾን፤ ጽንፋይ፤ አፍኣዊ፤ ዘአፍኣ። ዐጸድ፡ ጸናፊ። ጸናፊ፡ ጽልመት። ጸናፊት፡ ደብተራ፡ (ራእ፲፩፡ ፪። ማቴ፰፡ ፲፪። ዕብ፱፡ ፯)።

**ጽንፈት፤** ዳርቻ፡ መኾን፤ ዳርቻነት። አፍኣ፡ ዕዳሪ፤ ከውስጥ፡ ከቤት፡ ከቅጥር፡ ውጭ። አዘዘ፡ ያውፅእዎ፡ ኀበ፡ ጽንፈተ፡ ጽልመት፡ (ቀኖ፡ ኒቅ፡ ፰፱)።

**ጽናፌ፤** ዝኒ፡ ከማሁ። ውስተ፡ ብካይ፡ ወሐቅየ፡ ስነን፡ ወጽናፈ፡ ጽልመት፡ (ቀሌ)።

**ጽንፍ፤ (ዐረ፡ ጺንፍ)፤** ማፍ፤ ዘርፍ፤ ዳርቻ፡ ጠረፍ፤ ወደብ፡ ገደብ፤ ወሰን፡ ደንበር። ጽንፈ፡ ልብስ። ጽንፈ፡ ውሒዝ። ጽንፈ፡ ባሕር። ጽንፈ፡ ምድር፡ (ሩት፫፡ ፱። ሚራ፵፡ ፲፮። ፪ዜና፡ ፰፡ ፲፯። ሕኖ፲፰፡ ፭)።

**ጽንፍ፤ አጽናፍ፤** ማፎች። ጽንፊሁ፡ ለልብስ። ጽንፈ፡ አልባስ። አጽናፈ፡ ዓለም፤ አጽናፈ፡ ሰማይ። አጽናፈ፡ ምድር። ውስተ፡ ኵሉ፡ አጽናፍ። መላኬ፡ ኵሉ፡ አጽናፍ፡ (ዘፀ፳፰፡ ፴፱። ዘኍ፲፭፡ ፴፰። መዝ፲፰ና፡ ፱። ቅዳ። ስንክ፡ መስ፱)።

**መጽንፍት፤ (ዕብ፡ ሚጽኔፌት)፤** የራስ፡ ልብስ፤ ጌጥ፡ መሸፈኛ፤ ሰበን፤ ጥምጥም፡ ከንቶቡ፤ ክህናት፡ አራት፡ የሚለብሱት፡ (ሕዝ፳፩፡ ፳፮)።

**ጸንፈርት፤—ወፈንጠር፤—ፀንፈርት።**

**ጸንጽሎ፤ ሎት፤(ጸንጸለ፡ ይጸነጽል፡ ይጸንጽል። ዕብ፡ ጺልጼል)፤** መጸንጸል፡ መም ታት፤ ማንሿሿት፤ መደወል፡ ማቃጨል፤ ማቅጨልጨል፤ የማዕደን። ዘሩ፡ ነጸለ፡ ነው።

**ጸንጻሊ፤** የሚያቃጭል፡ የሚያንሿሿ፤ ደዋይ፡ አቃማይ፡ (አርጋ፡ ፩)።

**ጸንጸል፤(ብ፡ ጸናጽል፤ ላት)፤** ሻሹራ፤ ቃ ጭል፤ በቁሙ፡ ጸናጽል። ወገብሩ፡ ጸናጽለ፡ ዘወርቅ። አርባዕተ፡ ምእተ፡ ጸናጽለ። ጸናጽላተ፡ ብሩር። እ ሰኒ፡ በጸናጽል፡ ወእሰኒ፡ በከበሮ። ጸናጽል፡ ዘሠናይ፡ ቃሉ፡(ዘፀ፴፮፡ ፴፭። ፪ዜና፡ ፱፡ ፲፫። መጽ፡ ምስ። ፩ ዜና፡ ፲፫፡ ፰። መዝ፡ ፻፶)።



ጸንጸል፡

**ተጸንጸለ፤** ተመታ፤ ተቃጨለ። አንቲ፡ ተጸን ጻሊ፡(አርጋ፡ ፩)።

**ጽንጹል፤** የተመታ፡ የተቃጨለ፤ ቅጭል፡ ቅ ጭል፡ ሿ፡ ሿ፡ የሚል።

**ጽንጻሌ፤** መቅጨልጨል፤ መንሿሿት፤ ጸና ጽል፡ አያያዝ፤ አመታት።

**ጸንጸነ፤ (ጸኒን፡ ጸኖ)፤** ጠነጠነ፤ ነቀዘ፤ አ ረጀ፡ ተበላሸ፤ ከንቱ፡ ኾነ።

**ጽንጹን፤(ናን፡ ናት፡ ጽንት)፤** የጠነጠነ፤ የነቀዘ፤ ያረጀ፡ ያፈጀ፤ የዣገዠ፡ ዥዥ፤ የተበላሸ፡ ብ ልሹ፤ ጥንጣናም፡ ነቀዛም፡ ከንቱ። ብሂልሰ፡ ኢህሎ፡ ቃለ፡ እግዚ፤ ሕስው፡ ወዘጽንጹን፡ ኅሊና፡ ነገር፡ ው እቱ። ያርኢ፡ ጳውሎስ፡ በሡሉ፡ ከመ፡ ክህነት፡ ዘ ኦሪት፡ እንተ፡ በደም፡ ወጢስ፡ ከመ፡ ጽንጽንት፡ ይእቲ፡ ወኢትበቍዕ፤ ወአልባቲ፡ ኀይል፡ ግሙራ፡ (ቄር፡ እስት። ተረ)። ሐሳብ፡ በእንተ፡ ጽንዐት፡ ወጽ ንጽንት፤ ጨፈቃ፡ ፅንጨት፡ የሚቈረጥበት፡ ወራት። በ መስከረም፡ እስከ፡ ዐሥርቱ፡ ወኀምስቱ፡ ጽንዐት፤ ወእምዝ፡ ጽንጽት፤ በጥቅምት፡ እስከ፡ ዐሥራ፡ ወሠለስቱ፡ ጽንዐት፤ ወእምዝ፡ ጽንጽንት፡(መ፡ ፈ)። ከኅዳር፡ እስከ፡ ነሐሴ፡ ላሉትም፡ ወሮች፡ እንደዚሁ፡ ጽንዐትና፡ ጽንጽንት፡ አላቸው።

**ጽንጽንያ፤(ያት)፤** ጥንጣን፤ ነቀዝ፤ ዝንብ፡ ትንኝ። ጽንጽንያ፡ ምጢት። በዓለ፡ ጽንጽንያ። ጽ ንጽንያት፡ ንሕሳን፡(መክ፲፡ ፲፭። ፪ነገ፡ ፩፡ ፪። ፍ፡ ነ፡ ፲፪)።

**ጸናጺት፤** ዝኒ፡ ከማሁ፤ ዝንብ፤ የዝንብ፡ ( ገን፤ ትንኝ፡ ዐኾት፤ ተቈናጣጭ፡ ፍጥረት። ጻጹትንና ዐኾትን፡ ተመልከት። ይስሕቦ፡ እግዚ፡ ለጸናጺት፡ ( ለንህብኒ፡(ኢሳ፯፡ ፲፰። ዘፀ፰፡ ፲፯—፳፯)። በጸናጺት ፈንታ፡ ጻጹት፡ ይላል፤ ፍችው፡ ፩፡ ነው፤ ብቻ፡ ታ ናሽነትን፡ ያሳያል።

**ጸንቀቀ፤(ጠንቀቀ)፤** ነከረ፤ ዘፈቀ፤ አጨ ቀየ፡ አጨማለቀ፤ ለወሰ፡ በከለ፤ ፈጽሞ፡ አሳደፈ፤ አዝ ለፈለፈ። ዘብሑ፡ ዳቤላ፡ ጠሊ፡ ወጸንቀቁ፡ ልብሶ ለዮሴፍ፡ በደም፡(ኩፋ፡ ፴፬። ዘፍ፴፯፡ ፴፩)። ዘሩ፡ ጠንቀቀ፡ ነው፤ ጠ፡ ለጸ፡ ተለውጧል፤ ምስጢሩም፡ ፈጽሞ፡ ጠንቅቆ፡ ያሰኛል። ጽንጕን፡ ማለት፡ ከዚህ፡ ወጥቷል፤ ቀና፡ ገ፡ በብዙ፡ ቦታ፡ ይወራረሳሉ፤ ጸና፡ ጠ፡ እንዲወራረሱ።

**ተጸንቀቀ፤** ተነከረ፤ ተጨማለቀ፤ ፈጽሞ፡ አ ደፈ።

**ጽንቁቅ፤(ቃን፡ ቃት፡ ቅቅት)፤** የተነ ከረ፤ በርስሐት፡ በደም፡ የተበከለ፤ እድፋም፡ ጨምላቃ፤ ዥልፍልፍ። አመ፡ ከንኪ፡ ዕራቀኪ፡ ወሀሎኪ፡ ጽንቅ ቅት፡ በደምኪ፡(ሕዝ፲፮፡ ፳፪)።

**ጽንቃቄ፤** መነከር፡ መዘፈቅ፤ መጨማለቅ። እድፍ፤ ርስሐት፤ ጭቅቅት።

**ጸንሰ፤—ፀነሰ፥አረገዘ፤—ፀኒስ፡ ፀንሰ።**

(ጥን) **ጸንሰ፤ ሶት፤(ጸነሰ፡ ይጼንስ፡ ይጸንስ)፤** መቸገር፤ ማጣት፤ መደኽየት፤ አይቶ፡ ፀጣ፡ ችጋረኛ፡ መ ኾን፤ መዋረድ፡ መመስከን። ዘሩና፡ ምስጢሩ፡ የፀንሰ፡ ነው፤ ፅንስ፡ እያደገና፡ እየጠና፡ እንዲኼድ፡ የችግሩን፡ ጽ ናት፡ ያሳያል። መጽሐፍ፡ ግን፡ በጸነሰ፡ ፈንታ፡ ተጸነሰ፡ ይላል፤ ተ፡ ያማርኛ፡ ነው፤ የጸነሰ፡ ፍች፡ ተቸገረ፡ ማለት፡ ስለ፡ ኾነ፡ ጸሐፊና፡ መላሽ፡ አላገባቡ፡ ጥፈውታል። እምከመ፡ ተጸነሰ፡ ካልእከ። ይጼነሱ፡ አክለ፡ ወ ማየ። እምይእዜሰ፡ ኢይጼነስ፡ እንከ፡(ዘሌ፳፭፡ ፴፱። ሕዝ፬፡ ፲፯። ሚራ፲፭፡ ፳፱)።

**ጽኑስ፤(ሳን፡ ሳት፡ ንስት)፤** የተቸገረ፤ ችጉር፤ አይቶ፡ ፀጣ፤ ችጋረኛ፤ ድኻ፡ ወራዳ፤ ለማኝ፡ ቢጋች፤ ጦም፡ ፀዳፊ፤ ምስኪን። ወኢትትህከይ፡ ገቢረ፡ ሠናይ፡ ለጽኑስ። ጽኑሳን፡ እምዙሉ፡ ሠናያት። ወ አልቦ፡ እምውስቴቶሙ፡ ጽኑስ፡(ምሳ፫፡ ፳፯። ኢ ዮ፴፡ ፬። ግብ፬፡ ፴፬)። ዘታጼንስ፡ ዘታስተጼንስ፡ በማ ለት፡ ፈንታ፡ ዘጽንሰት፡ ይላል፤ አያሰኝም። ዘጽንሰት፡ ጥቀ፡ አውፅአታ፡(ሬልክ፡ መጨ)።

**ጽናሴ፤** መቸገር፡ ማጣት፤ ችግር፡ ዕጦት፤ ድኽነት፡ (ሬልክ)።

**ተጽናስ፤** ዝኒ፡ ከማሁ፤ ችግር፤ ችጋር፡ ቀ ጠና፤ ረኃብ፡ ዕርዝና፤ ፍጹም፡ ድኽነት። ተጽናስከ፡ ይሰድዶሙ፡ ለአፀርከቲከ። ዘይፈቅዱ፡ ለተጽና ሶሙ። ብዕልሰ፡ እመ፡ በጽድቅ፡ ወበኀጢአት፡ ተጽ ናስ፤ አክአብ፡ እንዘ፡ ሀሎ፡ እምኢተጸነሰ፡ ኤልያስ፡ (ሚራ፲፪፡ ፱። ያዕ፪፡ ፲፯። ቅኔ)።

**አጼነሰ ፤ አስተጼነሰ ፤** አስቸገረ ፤ ችጋር ፡ አመጣ ፤ ነማ ፡ አሳጣ ። ኢያስተጼንስ ፡ እግዚ ፡ ነፍሰ ፡ ጻድቅተ ። ኢያስተጼንሰሙ ፡ እምበረከቱ ፡ (ምሳ፲ ፡ ፫ ። መቃ ። መዝ ፡ ፹፫) ።

**ጼናታም ፤—ጤናዳም ፤—ጼነወ ።**

**ጸንጺወ ፤ (ጸነፈ ፤ ጸንፈወ) ፤** ጨቈነ ፡ ደፈጠጠ ፤ መታ ፡ ቀጠቀጠ ፤ አጠዘ ፡ ጠመዘዘ ። ከልብስ ፡ ዕጥበትና ፡ ዘፈረ ፡ ልብስን ፡ ከማከረር ፡ ከመፍተል ፡ ከመቋጨት ፡ የመጣ ፡ ቃል ፡ ነው ፤ ጸነፈን ፡ ተመልከት ። እምንእሱ ፡ አጸንጽዎ ፡ አዕፅምተ ፡ ገበዋቲሁ ። ወያጸነጽዉኒ ፡ አዕፅምትየ ፡ (ሚራ፴ ፡ ፲፪ ። መዝ ፡ ፴፩) ።

- **ተጸንጺወ ፤** ተጨቈነ ፤ ተቀጠቀጠ ፤ ተጠመዘዘ ።

**ጽንጽው ፤ (ዋን ፡ ዋት ፡ ጹት) ፤** የተጨቈነ ፤ የተቀጠቀጠ ፤ ቅጥቅጥ ፤ ጠማማ ፡ ቈልማማ ። ዘጽንጽው ፡ ወዘጽቱም ። መንኰብያቲሁ ፡ ጽንጽዋት ፡ (ዘሌ፳፪ ፡ ፳፬ ። ኪዳ) ።

**ጸንጸላዕት ፤** የእሳት ፡ እራት ። ወከመ ፡ ጸንጸላዕት ፡ ትወድቁ ፡ ማእከለ ፡ እሳት ፡ (ድር ፡ ሰን) ።

**ጽዕብ ፤ ብት ፤ (ዕብ ፡ ጻቡዕ ። ዐረ ፡ ፀቡዕ) ፤** ነጣቂ ፡ አውሬ ፤ የዥብ ፡ የውሻ ፡ ወገን ፤ ማሽ ፡ ፋሪ ፤ መቃብር ፡ ቈፋሪ ፤ ሬሳ ፡ እያወጣ ፡ የሚበላ ። ባለብሉዮች ፡ ግን ፡ ተቈናጣጭ ፡ ዝንብ ፡ ይሉታል ።



ጽዕብ ፡

**አጽዓብ ፤ አጽዕብት ፤** ነጣቆች ፡ አራዊት ፤ ማሾች ፡ ሬሳ ፡ አውጭዎች ፤ ከብዙ ፡ በቀር ፡ ባንድ ፡ አይገኝም ። አዝእብተ ፡ ወአክልብተ ፡ ወአጽዕብተ ፡ (ሔኖ ፡ ክ፹) ።

**ጽዒድ ፤ ዶት ፤ (ጸዐደ ፡ ይጽዕድ ፡ ይጽዐድ ። ዕብ ፡ ጻዐድ) ፤** አጥብቆ ፡ መኼድ ፡ መራመድ ፤ በኀይል ፡ መርገጥ ፡ እግርን ፡ ማንሣት ፤ መር ፡ መር ፡ አፈፍ ፡ አፈፍ ፡ ማለት ፤ የጕበዝና ፡ የወታደር ፡ የሰልፈኛ ፡ አካኼድ ፡ አረጋገጥ ። ርምጃ ፡ ርግጫ ፡ እንዲል ፡ (ሰልፍ ፡ አስተማሪ) ።

—፤ መጣድ ፡ ማስረር ፤ በሦስት ፡ ጕልቻ ፡ ላይ ፡ ማኖር ። በውስጡ ፡ ያካኼድ ፡ ምስጢር ፡ አለበት ፤ ከጕልቻ ፡ እስከ ፡ ጕልቻ ፡ ያለው ፡ መጠነ ፡ ምሥጋርን ፤ ቢያንስም ፡ መጠነ ፡ ስኵናን ፤ የድስቱና ፡ የምጣዱ ፡ ምጥቀት ፡ በእግር ፡ እንግሥ ፡ ልክ ፡ መኾኑን ፡ ከዚያ ፡ አለመብለጡን ፡ ያሳያል ፤ ቢበልጥም ፡ በመዝለልና ፡ በመፈንጨት ፡ ሎቤ ፡ በመምታት ፡ ይመስላል ።

**ጸዓዲ ፤ (ዲት ፡ ድያን ፡ ያት) ፤** የሚኼድ ፤ የሚጥድ ፡ ጣጅ ። (ተረት) ፤ የቤት ፡ ጣጅ ፤ የዱር ፡ ጠማጅ ።

**ተጽዕደ ፤** ተጣደ ፤ ምድር ፡ ለቀቀ ፤ ከጕልቻ ፡ ላቀ ፤ በላይ ፡ ኾነ ፤ ጕልቾች ፡ የሳንሳ ፡ ያዙት ፤ ተሸከሙት ።

**ጽዑድ ፤ (ዳን ፡ ዳት ፡ ዕድ) ፤** የተጣደ ፡ ተጥዶ ፡ ያለ ፤ የተደላደለ ።

**ጽዕደት ፤** መጣድ ፤ (ጥጣ) መጣድ ፤ አጣጣድ ፤ ጥደሽ ፤ በቁሙ ፡ ጥደት ፤ ምጣድ ፤ ዝርግ ፡ ክብ ፤ የሸክላ ፡ የብረት ። ዲያቆናት ፡ ግን ፡ በጽዕደት ፡ ፈንታ ፡ ጽዕዱት ፡ ይሉታል ፤ ስሕተት ፡ ነው ።

**ምጽዓድ ፤** መጣጃ ፤ ምድጃ ፤ ጕልቻ ፤ የምጣድ ፡ ቤት ፤ በቁሙ ፡ ምጣድ ፤ ምንን ፡ (ዐማርኛ) ።

**ጻዕደወ ፤ (ትግ ፡ ጸዕደ) ፤** ነጣ ፤ ነጭ ፡ ኾነ ፤ ጠራ ፡ በራ ፤ ንጣቱ ፡ ጥራቱ ፡ ከልክ ፡ ዐለፈ ። ወአልባሲሁኒ ፡ በረቁ ፡ ወጻዕደዉ ፡ ጥቀ ፡ ከመ ፡ በረድ ፡ ዘኢይክል ፡ መሀፒል ፡ አጻዕድዎ ፡ ከማሁ ። ጻዕደዉ ፡ እምበረድ ። ተኀፀበኒ ፡ ወእጻዐዱ ፡ እምበረድ ። ይጻዐዱ ፡ አርእስተ ፡ ደቂቅ ፡ በሚበት ። ወለእመ ፡ ጻዕደወ ፡ ቋዕ ፡ ከመ ፡ ራዛ ፡ (ማር፱ ፡ ፫ ። ሰቈ፬ ፡ ፯ ። መዝ ፡ ፶ ። ኩፋ ፡ ፳፫ና ፡ ፴፯) ።

**ጻዕዳዊ ፤ (ዊት ፡ ውያን ፡ ያት) ፤** የሚነጣ ፤ የሚጠራ ፤ ንጣት ፡ ጥራት ፡ የሚስማማው ። ቢያጥቡ ፡ አይጠራ ፡ እንዲሉ ።

**ጽዕድው ፤ (ዋን ፡ ዋት ፡ ዱት) ፤** የነጣ ፤ የጠራ ፤ ኖራ ፡ የመሰለ ። ጽዕድዋን ፡ አርጋብ ። አእዱግ ፡ ጽዕድዋን ። ጽዕዱት ፡ ወብርሀት ። ወጽዕዱት ፡ ይእቲ ፡ ከመ ፡ ባሕርይ ፡ (ስንክ ፡ ጥር፲፩ ። መሳ፭ ፡ ፲ ። ማሕ፰ ፡ ፭ ። ራእ፳፩ ፡ ፲፩) ።

**ጽዕዳዌ ፤ (ውያት) ፤** መንጣት ፤ መጥራት ፤ ንጣት ፡ ጥራት ፤ አንጣጥ ፤ ነጭነት ። እግዚአብሔር ፡ አክበረከ ፡ በጽዕዳዌ ፡ ጸጕር ። ጽዕዳዌ ፡ ፀምር ። ጽዕዳዌ ፡ ወልታ ፡ (አፈ ፡ ተጒና ፡ ፲፪ ። ስንክ ፡ መስ፳፱) ። በጽዕዳዌ ፡ ፈንታ ፡ ጻዕዳ ፡ ጽዕዱት ፡ ይላል ፤ ስሕተት ፡ ነው ። አስተርአየ ፡ ጻዕዳሆን ፡ ለእማንቱ ፡ አብትር ። ዕጹብ ፡ ለዐይን ፡ ሥነ ፡ ጽዕዱቱ ፡ (ዘፍ፴ ፡ ፴፯ ። ሢራ፵፫ ፡ ፲፰) ።

**ጸዐዳ ፤ (ዓድው) ፤** ነጭ ፤ ጥሩ ። እኍየሰ ፡ ጸዐዳ ፡ ወቀይሕ ። ልብሱ ፡ ጸዐዳ ፡ ከመ ፡ በረድ ። ዘጸዐዳ ፡ ጸጕሩ ። አፍራስ ፡ ጸዓድው ። አልባስ ፡ ጸዓድው ። አክሊላት ፡ ጸዓድው ፡ (ማሕ፭ ፡ ፲ ። ዳን፯ ፡ ፱ ። ዘፍ፴ ፡ ፴፱ ። ዘካ፩ ፡ ፰ ። ራእ፬ ፡ ፬ ። አርጋ) ።

**ጸዐድዒድ ፤ (ድት ፡ ዳን ፡ ዳት) ፤** ፍጹም ፡ ነጭ ፤ ነጫነጭ ፤ ጸዐዳዊ ፤ ወደ ፡ ነጭነት ፡ የሚያደላ ። ናርዶስ ፡ ዘጸገየ ፡ በጸዐድዒድ ። አ ፡ ጽጌያት ፡ ሥነክሙ ፡ ጸዐድዒደ ፤ እግዚ ፡ ይርአይ ፡ እምሰማይ ፡ ወረደ ። ሕብራት ፡ ጸዐድዒዳን ፡ (አርጋ ፡ ፪ ። ስንክ ፡ መስ፳፰ ። ፊላስ) ።

**አጻዕደወ ፤** አነጣ ፡ አጠራ ፤ ነጭ ፡ አደረገ ። አጻዕድዎ ፡ ከመ ፡ በረድ ። በዘአጻዕደወት ፡ አዕጹቂሃ ። ኢትክል ፡ አጻዕድዎ ፡ አሐተ ፡ ሥዕርተ ፡ ርእስከ ፡ (ኢሳ፩ ፡ ፲፰ ። ዮኤ፩ ፡ ፯ ። ቢኖ ይ) ።

**ጽዒጥ ፤ ጠት ፤ (ጽዕጠ ፤ ጸዐጠ ፡ ይጽዕጥ ፡ ይጽዐጥ ። ዐረ ፡ ሰ ፤ ጸዐጠ) ፤** መቀመም ፡

ማጠፈጥ፤ ማንጠር፣ ማቅለጥ፤ መቅባት፣ መርጨት፣ መረብረብ፤ የሽቱ፣ የመድኀኒት። ዕቍብተ፡ ሥራይ፡ ይጽዕጡ፡ ፈውሰ፡ ለቍሱላን፡ በዘይት፡ ሃይማኖት። ዕፍረት፡ ዘእደ፡ ዮሴፍ፡ ጸዐጠ። እእዳወ፡ ፍቅርኪ፡ በላዕሌየ፡ ይጽዕጣ፤ ዕፍረተ፡ መዐዛ፡ ወቅብዐ፡ ዘብዙኅ፡ ሤጣ። ጸዐጡ፡ ሥጋየ፡ በከርቤ፡ ወበሰሊክ፤ (መጽ፡ ምስ። ስንክ፡ መጋቢት። ኀሐ፲፯። አቡሻ፡ ፴፯)።

ጸዓጢ፤ የሚቀምም፤ የሚያጣፍጥ፣ አጣፋጭ፤ ሽቱ፣ ሽያጭ።

መጽዕጥ፤ (ጣን፣ ጣት። መጻዕጥ፣ ጣት) ፤ ዝኒ፡ ከማሁ፤ የሴት፣ ሲኾን፣ ጥ፡ ይጠብቃል። ይነሥእ፡ አዋልዲከሙ፡ ለመጽዕጣት፤ (፩ነገ፡ ፰፡ ፲፫)።

ተጽዕጠ፤ ተቀመመ፤ ተጣፈጠ፤ ተነጠረ፤ ተዘጋጀ። ተቀባ፣ ተረጨ፣ ተረበረበ፤ ሽቱው፣ ሰዉ፣ ልብሱ።

ጽዑጥ፤ (ጣን፣ ጣት፣ ዕጥ) ፤ የተጣፈጠ፤ የተነጠረ፤ ጥሩ፣ ዝግጁ። የተቀባ፣ ቅቡዕ። ዕፍረተ፡ መዐዛ፡ ጽዑጥ። አፈዋተ፡ ርሔ፡ ጽዑጣን፡ ዘይትዐቀብ፡ በቀርን፡ ቅብዐ፡ ዘጽዮን፤ (ስንክ፡ የካ፲። መጽ፡ ምስ)።

(ሉ) ጽዕጥ፤ ጽዒጥ፤ ጥሩ፣ ሽቱ። ጽዒጥ፡ ዘጸዓጢ። ጽዒጥ፡ ወዕጣን፤ (ዘፀ፴፡ ፳፭ና፡ ፴፱። መቃ)።

አጽዐጠ፤ አስቀመመ፤ አስጣፈጠ፤ አስነጠረ፤ ቀምሙ፣ አጣፍጡ፤ አንጥሩ፣ አቅልጡ፣ አለ።

አጽዓጢ፤ መጽዐጢ፤ ዕጥ፤ የሚያስቀምም፤ የሚያስነጥር፤ ሽቱ፣ የሚያስበጅ።

ጽዒል፤ ሎት፤ (ጸዐለ፣ ይጼዕል፣ ይጽዐል። ዕብ፣ ጼኤል፤ እሾኽም፣ የሽቱ፣ ዕንጨት) ፤ መጣል፣ ማጣጣል፤ መስደብ፣ ማርከስ፤ ማዋረድ፣ ማሳነስ፤ ማቃለል፣ ማኰሰስ፤ መንቀፍ፤ ማጸየፍ፤ ቝል፣ አፍ፣ እሾኽ፣ አፍ፣ መኾን፤ መባል። በእንተ፡ ፀሪፍ፡ ወጽዒል። ለእመ፡ አዕበይከ፡ አፉከ፡ ወጸዐልካሁ። እንዘ፡ ይጼዕልዎ፡ ኢጸዐለ። ወይጼዕሉኒ፡ ኵሎሙ፡ ጸላእትየ፤ (ፈ፡ መ፡ ፰። ሢራ፳፪፡ ፳፱። ፩ጴጥ፡ ፪፡ ፳፫። መዝ፡ ፵፩)። ጸልእን፡ ተመልከት፤ የዚህ፡ መንትያ፡ ነው።

ጸዓሊ፤ (ሊት፣ ልያን፣ ያት) ፤ የሚጥል፣ ጣይ፤ የሚሰድብ፤ ሰዳቢ፤ ተሳዳቢ፤ ስድብ፣ ዐዋቂ። ዐቡይ፡ ወጸዓሊ። ብእሲት፡ ጸዓሊት። አብያተ፡ ጸዓልያን፡ ያንኀል፡ እግዚ፤ (ሢራ፳፫፡ ፰። ምሳ፲፭፡ ፳፭። ፳፭፡ ፳፱)። ጸዓሊና፡ ፀሐይ፡ በማርኛ፡ ይተባበራሉ። (ግጥም) ፤ መሽ፣ መሰለኝ፣ ሲጨልም፤ እንደ፣ ቀን፣ ጣይ፣ የለም።

አጽዐለ፤ አሰደበ፤ አስነቀፈ፤ አስናቀ፤ ወልድ፡ አብድ፡ ያጼዕል፡ አባሁ። ወዘኢያጽዐለ፡ እዝማዲሁ። ከመ፡ ኢያጽዕላ፡ ርእሶን። እስመ፡ ተዋርዶ፡ ኢያጼዕል፤ (ምሳ፳፰፡ ፯። መዝ፡ ፲፬። ፩ጢሞ፡ ፭፡ ፲፬። ተረ፡ ቄርሎ)።

መጽዕል፤ (ልት፣ ላን፣ ላት) ፤ የሚሰድብ፤ የሚያሰድብ፤ አሰዳቢ፣ አስነቃፊ። መሰደቢያ፣ ማሰደቢያ።

ተጽዕለ፤ ተጣለ፤ ተሰደበ፤ ተዋረደ። ተጽዕልኩ፡ በኀበ፡ ኵሎሙ፡ ጸላእትየ። ንበርሕ፡ ወንጼዐል። ወተጽዐልክሙ፤ (መዝ፡ ፴። ፩ጢሞ፡ ፬፡ ፲። ዕብ፲፡ ፴፫)።

ጽዑል፤ (ላን፣ ላት፣ ዕልት) ፤ የተጣለ፤ የተሰደበ፤ ስዱብ፤ ነውረኛ፤ ንቁፍ። ዘማ፡ ወጽዕልት፡ ኢያውስቡ፤ (ዘሌ፳፩፡ ፯ና፡ ፲፬። ኢሳ፰፡ ፲፭። ምሳ፳፱፡ ፶፰)።

ጽዕለት፤ (ታት) ፤ መስደብ፤ መሰደብ፤ አሰዳደብ። ስድብ፤ የቃል፣ በትር፤ ቍስሉ፣ የማይሽር። (ቀረት)፤ የባለጌ፣ ንደለ፣ ቃል፤ እንደ፣ ሽመል፣ ይወቃል። እምአፈ፡ አብዳን፡ ትወፅእ፡ በትረ፡ ጽዕለት። ጽዕለተ፡ ብዑላን። ከመ፡ ኢይደቅ፡ ውስተ፡ ጽዕለት። ክብሩ፡ ለብእሲ፡ ተከልአ፡ እምጽዕለት፤ (ሢራ። መዝ፡ ፻፳፪። ፩ጢሞ፡ ፫፡ ፯። ምሳ፳፡ ፪)። ጥለት፣ ማለት፣ ከዚህ፣ የወጣ፣ ነው።

ተጻዐለ፤ ተሳደበ፤ ተሰዳደበ። ይጻዐሉ፡ ወይትዋገሩ፤ (ግብ፲፱፡ ፩)።

ጸዐመ፤—ፈጮኸ፤—ጽኢም፣ ጸአመ።

ጽዒን፤ ኖት፤ (ጸዐነ፣ ይጽዕን፣ ይጽዐን። ዕብ፣ ጻዐን፤ ተጽዕነ) ፤ መጫን፤ ማሸከም፤ ማሳዘል፤ መጥመድ፤ ማስንገት፣ ሸክምን፣ በተሸካሚ፣ ላይ፣ ማስቀመጥ፣ ማኖር፤ ወይም፣ ከርሱ፣ ጋራ፣ ማቈራኘት፣ ማሰር። እዘዘሙ፡ ይጸዐኑ፡ በውእቱ፡ ንዋይ፡ እክለ፡ ወይጽዐንዎ፡ በሐመር። ለአድግስ፡ ጸዐኖ። ጸዕነ፡ አንስቲያሁ። ጸዐና፡ ለእምከ። ጸዕኑ፡ አእዱጊሆሙ። ጸዕነት፡ አብቅሊያ። ወእጼዕን፡ ሠረገላ፡ ዲበ፡ መሠንየ፡ ከማዴ፤ (ዮሴፍ። ሢራ፴፡ ፳፫። ኩፋ፡ ፳፱፡ ፴፭፡ ፵፫። ሆሴ፲፡ ፲፭)። በጸዐነ፡ ፈንታ፡ አጽዐነ፡ ይላል፤ ስሕተት፣ ነው። አጽዐኖ፡ ዲበ፡ ፈረስ። ወአጽዐንከ፡ ሰብአ፡ ዲበ፡ አርእስቲነ። ወዲበ፡ ልዑላት፡ ያጼዕኒ፤ (አስቴ፮፡ ፱ና፡ ፲፩። መዝ፡ ፷፭። ዕንባ፡ ፲፱)።

ጸዓኒ፤ (ኒት፣ ንያን፣ ያት፤ ዐንት) ፤ የሚጭን፤ የሚያሸክም፤ ጫኝ፤ አሸካሚ።

መጽዕን፤ (ንት፣ ናን፣ ናት፤ ዐኒ) ፤ የሚጭን፤ ጫኝ። መጫኛ፤ ቅራና፤ ማሸከሚያ።

መጻዕን፤ (ናት) ፤ መጫኛች፤ ቅራኖች፤ የጭነት፣ መጣፊያዎች።

አጽዐነ፤ አስጫነ፤ ጫኑ፤ አሸክሙ፣ አለ። በአጽዐነ፣ ፈንታ፣ አስተጽዐነ፣ ይላል፤ ፍችው፣ ፩፣ ነው።

ተጽዕነ፤ ተጫነ፤ ተቀመጠ፤ ሸክም፣ ኾነ፤ በላይ። ተጫነበት፤ ተሸከመ፤ ተደበለለ፤ ጸዋሪ፣ ኾነ። ተጽዕነ፡ ላዕለ፡ ኪሩቤል። እስመ፡ ተጽዕንከ፡ ዲበ፡ አፍራሲከ። ናሁ፡ ፈረስ፡ ጸዐዳ፡ ወዘይጼዐኖ፡ ቀስተ፡ ያጸንዕ። ተጽዕነ፡ ላዕሌሁ፡ ሰይጣን፤ (መዝ፡ ፲፯። ዕንባ፡ ፫። ራእ፮፡ ፪። ስንክ፡ መስ፲፱)።

**ጽዑን ፤ (ናን ፡ ናት ፡ ዕንት) ፤** የተማነ ፤ የተማነበት ፤ ሸክም ፤ ተሸካሚ ። ዘጽዑን ፡ ዲበ ፡ አድግ ። እንዘ ፡ ጽዑን ፡ ምስሌሁ ፡ ዲበ ፡ ፈረስ ። ገመል ፡ ጽዑን ። ጽዑናን ፡ አግማሊሆሙ ፡ አፈዋተ ፡ (ስንክ ፡ የካ፲፩ ። ኅዳ፳፩ ። ሐም፳፭ ። ዘፍ፴፯ ፡ ፳፭) ።

**መስተጽዕን ፤ ተጸዓኒ ፤** የሚማን ፤ ተማኝ ፤ ተቀማጭ ። መስተጽዕነ ፡ ኪሩቤል ። መስተጽዕናነ ፡ አፍራስ ። ኅኑያነ ፡ ወመስተጽዕናነ ፡ በመሥልስት ፡ (አርጋ ፡ ፩ ። ኢዮ፩ ፡ ፲፯ ። ዘፀ፲፭ ፡ ፬) ።

**ተጻዐነ ፤** ተጫጫነ ፡ ተሸካከመ ፤ ተነባበረ ፤ አንዱ ፡ ባንዱ ፡ ላይ ።

**አስተጻዐነ ፤** አጫጫነ ፡ አሸካከመ ፤ አነባበረ ፤ አደራረበ ።

**መስተጻዕን ፤** የሚያጫጭን ፤ የሚያሸካክም ፤ አጫጫኝ ።

**ጸዓዕ ፤—ብልጭታ ፤—ፀዓዕ ።**

**ጻዕፍ ፤ (ዐረ ፡ ጸዕፍ) ፤** ጕሽ ፤ እንቡሽቡሽ ፤ ድፍርስ ፡ ብጥብጥ ፤ ገና ፡ ያልፈላ ፡ ያልበሰለ ፡ መጠጥ ፤ ዐዲስ ፡ ጠጅ ፤ የማር ፡ የወይን ። ጻዕፈ ፡ ጸግቡ ፡ ወሰክሩ ። አልቦ ፡ ዘይሰቲ ፡ ከራሚ ፡ ወይፈቅድ ፡ ጻዕፈ ። ወይሰትዩ ፡ ደሞሙ ፡ ከመ ፡ ጻዕፍ ፡ (ግብ፪ ፡ ፲፫ ። ሉቃ፭ ፡ ፴፱ ። ኢሳ፵፱ ፡ ፳፮) ።

**ጽዒቅ ፤ ቆት ፤ (ጸዐቀ ፡ ይጽዕቅ ፡ ይጽዐቅ ። ዕብ ፡ ጻዐቅ ፤ ጮኸ ፡ ከጭንቅ ፡ የተነሣ) ፤** መጭንቅ ፡ መጥበብ ፤ ጭንቅ ፡ ጥብ ፡ መኾን ፤ የቦታ ፡ የጊዜ ፤ ጸበበንና ፡ ዐጸበን ፡ ተመልከት ። ለትጽዐቆ ፡ ምድር ፡ (አርጋ ፡ ፫) ።

**አጽዐቀ ፤ (ጠዊቅ ፡ ጦቀ) ፤** አስጨነቀ ፤ አስጠበበ ፤ አጣበቀ ፡ አጣብቆ ፡ ያዘ ፤ መከራ ፡ አጸና ፡ ማቀየ ፤ አስገደደ ። ኢያገምራ ፡ ርሒበ ፡ ዓለም ፡ ወኢያጽዕቃ ፡ መጽብብ ፡ ዘመቅዐን ። ዘከርሥ ፡ ኢያጽዐቆ ። ሶበ ፡ አጽዐቆ ፡ ምንዳቤ ። እለ ፡ ያጽዕቁ ፡ ላዕለ ፡ ዕቤራት ፡ (አርጋ ፡ ፩ ። ድጓ ። ፈ ፡ መ ፡ ፲፯ ፡ ፩ ። ፍ ፡ ነ ፡ ፲፪) ።

**መጽዕቅ ፤ (ቅት ፡ ቃን ፡ ቃት) ፤** የሚያስጨንቅ ፡ አስጨናቂ ። ሕማም ፡ ወጽንዐ ፡ ንዴት ፡ መጽዕቅ ፡ (ጥበ ፡ ጠቢ) ።

**ተጽዕቀ ፤** ተጨነቀ ፤ ተጠበበ ፤ በቦታ ፡ በመከራ ። እንዘ ፡ ይጸዐቁ ፡ አሕዱ ፡ ምስለ ፡ ካልኡ ። ባልሖሙ ፡ እምነ ፡ ገዐር ፡ ወተጽዕቆተ ፡ ግብር ፡ ዘነበሩ ፡ ባቲ ፡ (መቃ ። አፈ ፡ ድ፳፯) ።

**ጽዑቅ ፤** የጠበበ ፤ ጠባብ ፤ ጭንቅ ። ጽዕቅት ፡ ፍኖት ፡ (ማቴ፯ ፡ ፲፬ ። አፈ ፡ ተ፳፱) ።

**—፤** የተጨነቀ ፤ የተጠበበ ፤ መከረኛ ።

**ጻዕቅ ፤ (ቃት) ፤** ጭንቅ ፡ ጥብ ፤ ግፊ ፤ ሥቃይ ፡ መከራ ። ብዙኅ ፡ ሰብእ ፡ ውስተ ፡ ሀገር ፡ ወኢመካን ፡ ዕሩቅ ፡ ዘእንበለ ፡ ጻዕቀ ፡ ሰብእ ፡ ጽፉቅ ። በዕለተ ፡ ጻዕቆሙ ፡ ወጻሕቦሙ ። ምንዳቤ ፡ ወጻዕቅ ። ሐዘናት ፡ ወጻዕቃተ ፡ (ዮሴፍ ። ሔኖ፵፫ ፡ ፰ ። ስንክ ፡ ጥቅ፲፪ ፡ ማር ፡ ይሥ፲፫) ።

**ተጻዐቀ ፤** ተጫነቀ ፤ ተጣበበ ፤ ተጋፋ ፤ ተነባበረ ፤ ጽፍቅ ፡ ኾነ ። አኮኑ ፡ ይጣወቅ ፡ ሰብእ ፡ ወይጻዐቀከ ፡ (ሉቃ፰ ፡ ፵፭) ።

**ተጻዓቂ ፤** የሚጫነቅ ፤ የሚጣበብ ፤ የሚጋፋ ፡ የሚፋተግ ፤ ተጨናናቂ ። መዛሕም ፤ ዘበትርጓሜሁ ፡ ተጻ(ጸ)ዓቂ ፡ (ስንክ ፡ ሠኔ፲፱) ። መዛሕምን ፡ ተመልከት ።

**ጽዒር ፤ ሮት ፡ (ጽዕረ ፤ ጸዐረ ፡ ይጽዕር ፡ ይጽዐር ። ሱር ፡ ጻዐር ። ዕብ ፡ ያጻር) ፤** መጣር ፤ መጋር ፤ መፍገርገር ፤ መፍጨርጨር ፤ በፍጹም ፡ ኀይል ፡ በፍጹም ፡ ትጋት ፡ መሥራት ፤ መድከም ፡ መቃተት ፡ ማቃሰት ።

**—፤** ማዘን ፡ መተከዝ ፤ በጻዕር ፡ መያዝ ፤ መጨነቅ ፡ መዋለል ፤ ሥቃይ ፡ መቀበል ። እስመ ፡ ጽዕረ ፡ ፈድፋደ ። ወትጼዕረኒ ፡ ልብየ ፡ (ስንክ ፡ ሐም፰ ። መገ ፡ ፲፱) ። በጽዕረ ፡ ፈንታ ፡ ተጽዕረ ፡ ይላል ፤ አያስኼም ፤ ተ ፡ ያማርኛ ፡ ነው ። የጽዕረና ፡ የጸዐረ ፡ ፍች ፡ ተሣቀየ ፡ ተጨነቀ ፡ ማለት ፡ ስለ ፡ ኾነ ፤ ግእዙን ፡ እንዳማርኛው ፡ አስኪዶታል ፤ ጭፍራነቱ ፡ የጥሕረና ፡ የጸዐለ ፡ ነው ። መኑ ፡ ውእቱ ፡ ዘተጽዕረ ፡ ከማየ ። ተጽዕረ ፡ በምንዳቤ ። እስመ ፡ አብ ፡ ይጼዐር ፡ ወይላሕ ። እለ ፡ ይጼዐሩ ፡ በሀየ ፡ (ኢዮ፲፫ ፡ ፲፱ ። ስንክ ፡ ጥር፲፩ ። ጥበ፲፱ ፡ ፲፩ ። አፈ ፡ ተ፩) ።

**ጽዑር ፤ (ራን ፡ ራት ፡ ዕርት) ፤** የተጨነቀ ፤ የተሣቀየ ፤ የሚያጥር ፤ የሚጣጣር ፤ ጣር ፡ የያዘው ፤ ለሞት ፡ የቀረበ ፤ ያዘነ ፡ የተከዘ ። ጥቀ ፡ ጽዑር ። ሕሙም ፡ ወጽዑር ። ፊልጶስ ፡ ጽዑረ ፡ ሥጋ ፡ በመቅሠፍት ። ጽዑራነ ፡ ነፍስ ። ይከውኑ ፡ ጽዑራነ ። ኑዛዜ ፡ ወትፍሥሕት ፡ ለጽዑራን ፡ (ማቴ፰ ፡ ፮ ። አፈ ፡ ተ፱ ። ስንክ ፡ ኅዳ፲፰ ። ኢዮ፫ ፡ ፳ ። ጥበ፪ ፡ ፲፱ ። ማር ፡ ይስ፲፫) ።

**ጻዕር ፤ (ራት) ፤** ጣር ፤ ጭንቅ ፤ ሥቃይ ፤ መከራ ፤ ደዌ ፤ ሕማም ፤ የሕማም ፡ ስሜት ፤ የሞት ፡ ዋዜማ ። ጻዕረ ፡ ሞት ። ጻዕረ ፡ ሕማም ። ጻዕረ ፡ ደይን ። ዘቲ ፡ ዐባይ ፡ ጻዕር ። ወርእየ ፡ ኤፍሬም ፡ ለደዌሁ ፡ ወለጻዕሩ ፡ (መገ ፡ ፲፯ ። ዮሴፍ ። ፪ጢሞ ፡ ፪ ፡ ፬ ። ሔኖ፳፪ ፡ ፲፩ ። ሆሴ፭ ፡ ፲፫) ።

**አጽዐረ ፤** አጣረ ፤ አደከመ ፤ አስጣረ ፤ አስጨነቀ ፤ ሣቀየ ፤ መከራ ፡ አሳየ ፤ አስመረረ ፤ አሳዘነ ። አጽዐርዋ ፡ ለነፍሶሙ ። ያጼዕረኒ ፡ ዘያወፅእ ፡ ለነፍስየ ። እስከ ፡ ምንትኑ ፡ ታጼዕርዋ ፡ ለነፍስየ ። እስመ ፡ ጥቀ ፡ ያጽዕሮን ። ወፈቀደ ፡ ያጽዕራ ፡ (ግብ፲፱ ፡ ፪ ። ኢዮ፲፯ ፡ ፩ ። ፲፱ ፡ ፪ ። ሄርማ ። ስንክ ፡ ኅዳ፯) ።

**መጽዕር ፤ (ርት ፡ ራን ፡ ራት) ፤** የሚያጥር ፤ የሚያስቸግር ፤ የሚሣቅይ ፤ አስጨናቂ ። መሣቀያ ፤ ማስጨነቂያ ፤ የሥቃይ ፡ መሣሪያ ።

**መጻዕር ፤ (ርት) ፤** የሚሣቅዩ ፤ ሣቃዮች ፤ ሥቃዮች ፤ የሥቃይ ፡ መሣሮች ። አዘዘ ፡ ስደተ ፡ ላዕለ ፡

ስለ፡ወለተ፡ብእሲቱ፡ቀኖናሁ፡ዐሥርቱ፡ወኀም ስቱ፡ዓመት። ዘዘመወ፡ምዕረ፡አሐተ፡ያጹርዎ፡ ቀኖና፡ቀሊለ፤ወለእመ፡ተመይጠ፡ያክብዱ፡ላዕ ሌሁ፡ቀኖና። ወሀቦ፡ቀኖናተ፡ክቡዳተ፡(ፈ፡መ፡ ፩፡፫። ፮፡፮። ስንክ፡ ንሐ፲፩)።

ቀነነ፤ ዐገገ፤ ሠራ፤ ደነባ፤ ሕግ፡ ሥራት፡ ደ ንብ፡ አቆመ፤ ቀኖና፡ ሰጠ። ቀነኑ፡ላዕለ፡ብእሲት፡ ዝግዐት። እመ፡ቦ፡ዘቀነነ፡ርእሶ፡በፈቃዱ፡(ቢኖ ደ። ቄድር)።

—፤ ቄነነ፤ መቍነን፡ ሰጠ፤ ዐደለ፤ ቈረሰ፡ ከፈለ፤ ተነ ተነ፤ ዘገነ፡ ታፈነ፤ የምግብ።

ተቀነነ፤ ቀኖና፡ ያዘ፤ ተቀበለ። ተቄነነ፤ መ ቍነን፤ አገኘ፤ ታደለ።

ቀንዐ፤—ቀና፤—ቀኒአ፡ ቀንአ።

ቅንፍዝ፤ (ዕብ፡ ቂፎድ። ሱር፡ ቂ ፉዳ። ዐረ፡ ቁንፉድ፡ ዝ)፤ ዣርት፤ እሾኻም፡ አ ውሬ፤ ጠጕሩ፡ እንደ፡ ጋሬጣ፡ እንደ፡ ምስማር፡ ያለ፤ ሽመልመሌ፡ ዐይነት፡ (ኢሳ፲፬፡ ፳፫። ፴፬፡ ፲፩)።



ቅንፍዝ፡

ቅንፍዛት፤ ቀናፍዝ፤ ዣርቶች፤ ጠጕረ፡ ክፉዎች፡ ባለሾኽ፡ ጠጕሮች።

ቀኒጽ፤ ጾት፤ (ቀነጸ፡ ይቀንጽ፡ ይቅ ንጽ)፤ መነሣት፡ መቆም፡ አፈፍ፡ በርደገ፡ ማለት፤ መ ዝለል፤ መፈንጨት፤ መቅበጥ፡ መቈጣት፡ መቀናጣት፤ መር፡ ቸር፡ ባጥ፡ ፈናጥ፡ ማለት፤ መንጠቅ፡ መሸሽ፤ መሮጥ፡ መፈርጠጥ። ቀነጸ፡እምዲበ፡ሠረገላ። ቀነጸ፡ ላዕሌሁ፡ወቀተሎ፡በሰይፍ። ቀነጹ፡ላዕለ፡በራዊተ፡ የናናውያን። ቀነጸ፡እምኔሃ፡ወወፅአ። መጽአ፡እ ንዘ፡ይቀንጽ፡(መጽ፡ ምስ። ዮሴፍ። ማሕ፪፡ ፰)።

አቅነጸ፤ አዘለለ፤አስፈነጨ፡አቀናጣ። ፍቅር፡ እንተ፡አቅነጸቶ፡እምዲበ፡ሐመር፡(መጽ፡ ምስ)።

ተቃነጸ፤ ተዛለለ፡ ተፈናጨ፡ ተፎረፈጠ።

አስተቃነጸ፤ አዛለለ፡ አፈናጨ። ፈረስከ፡ዘ ትጼዐና፡እንዘ፡ያስተቃንጽ፡እግሮ፡(ደራሲ)።

ቈንጽ፤ (ጻት)፤ ቍንጫ፤ፈርዐጽ፤የሚዘል፤ የሚፈናጠር፡ (፩ነገ፡ ፳፬፡ ፲፭)።



ቍንጽ፡

—፤ ቍንጮ፤ የቤት፡ የሰው፡ (ዐማርኛ)።

ቈንጽል፤ (ዕብ፡ ሹዓል)፤ ቀበሮ፤ ወ ይም፡ ተኵላ፤ ነጣቂ፡ የበረሓ፡ ውሻ፡ ክፉ፡ ተንኰለኛ፡ የመኳንንትና፡ የሰይጣናት፡ አምሳል። ቀበሮና፡ ተኵላ፡ እንደ፡ ነብና፡ እንደ፡ ጥቍር፡ ዝንጀር፡ ይመሳሰላሉ፤ ዘመዳሞች፡ ናቸው፤ ከጥቍሬው፡ ዝንጀር፡ ነጩው፡ እንዲከፋ፡ ከቀበሮ፡ ተኵላ፡ ይከፋል። ነገዳቸውና፡ ጠ ባያቸው፡ አንድ፡ ስለ፡ ኾነ፡ በተኵላ፡ ፈንታ፡ ቍንጽል፡ ይባል። ሖሩ፡በልዋ፡ለዛቲ፡ቈንጽል። ይበውእኑ፡ አንበሳ፡ውስተ፡ግበ፡ቈንጽል፡ አው፡ ቈንጽል፡ ኀበ፡አንበሳ። ሰይጣንሰ፡ቈንጽል፡ ኅሕባዊ፡(ሉቃ ፲፫፡ ፴፫። አዋል። ቄድር)።



ቍንጽል፡

ቈናጽል፤ ተኵሎች፤ ቀበሮዎች፡ ቀበሬርት። አሥግሩ፡ለነ፡ቈናጽለ፡ንኡሳነ። ወእንዘ፡ሠለስተ፡ ምእተ፡ቈናጽለ። ለቈናጽልኒ፡ገበብ፡ቦሙ፡(ማሕ ፪፡ ፲፭። መሳ፲፭፡ ፬። ማቴ፰፡ ፳)።

ቋንቋ፤ በቁሙ፤ ልሳን፤ የቃል፡ የነገር፡ ስልት፡ (ዐማርኛ)።

ቈንቈኔ፤ ቍንቍን፤ ጥንጣን፤ ግንደ፡ ቈር ቍር፤ ነቀዝ፤ ብል፤ ትል፤ የዕፅና፡ የእክል፡ የልብስ፡ ተባይ። ፃዔ፡ወቈንቈኔ። ከመ፡ብላዕ፡ቈንቈኔ። ልብስ፡ዘተበልዐ፡እምቈንቈኔ፡(ኢሳ፶፩፡ ፰። ማቴ ፰፡ ፲፱። መ፡ ፈ)።

—፤ ቅንቅን፤ የደሮ፡ ቅማል፤ ጤፍ፡ የሚያክል።

ቈንቈነ፤ በቁሙ፤ ነቀዘ፤ ጠነጠነ፤ ተላ፤ አረጀ፤ አፈጀ። ወአልባሲክሙኒ፡ቈንቈነ። ዘኢይበሊ፡ወዘ ኢይማስን፤ ወዘኢይቈነቍን፡(ያዕ፭፡ ፪። ቄድር)።

ቀኒት፤ ቶት፤ (ቀነተ፡ ይቀንት፡ ይቅ ንት። ዐረ፡ ነጠቀ)፤ መቀነት፤ መታጠቅ፤ ወገብን፡ ማፅር፤ ማጥበቅ፤ ማገልደም፡ ማሸረጥ፡ ማሸንፈጥ፤ ማሸንቀጥ፤ በትጥቅ፡ ማጌጥ። ቅንት፡ ሐቌከ፡ከመ፡ ብእሲ። ቅንት፡ሰይፈከ፡ኀያል፡ውስተ፡ሐቌከ። ቀነተት፡ሠቀ፡ውስተ፡ሐቌሃ። ቅንት፡ሰልብሰ፡ዐኀ፡ ወቀነትኩ። ሀየንተ፡ቅናትኪ፡ዘወርቅ፡ሐብለ፡ቅ ንቲ፡(ኢዮ፴፰፡ ፫። መዝ፡ ፵፬። ዮዲ፰፡ ፭። ሄርማ። ኢሳ፫፡ ፱)።

ቀናቲ፤ (ቲት፡ ትያን፡ ያት)፤ የሚቀንት፡ የሚያጠብቅ፤ የሚታጠቅ፤ ታጣቂ።

ቅኑት፤ (ታን፡ ታት፡ ንት)፤ የታጠቀ፤ የ ተቀነተ፤ ቅንት፤ ዝግጁ፤ ልባም። ቅኑት፡ሐቌሁ፡በወ ርቅ። ቅኑታን፡ዐለቅ። ቅኑታን፡ሰይፍት፡(ዳን፲፡ ፭። ሕዝ፳፫፡ ፲፭፡ ፲፭። ኩፋ፡ ፴፯)።

**ቅናት** ፤ (ታት ፡ ቅናውት) ፤ በቁሙ ፤ መቀነት ፡ መታጠቂያ ፤ ትጥቅ ፤ የወገብ ፡ ማሰሪያ ፤ ቀበቶ ፡ ዝናር ፡ መቀነት ። በቅናቱ ፡ ዘአዲም ። በቅናት ፡ ዘወርቅ ። አልባሰ ፡ ወቅናታተ ። ወኢይፍትሑ ፡ ቅናውቲሆሙ ፡ (ማቴ፲ ፡ ፱ ። ራእ፩ ፡ ፲፫ ። ዘፀ፳፰ ፡ ፴ ። ኢሳ፭ ፡ ፳፯) ።

**አቅነተ** ፤ አስቀነተ ፤ አስታጠቀ ፤ አሰለፈ ። ባዕድ ፡ ያቀንተከ ። አቀንተክሙ ፡ ብልባሴ ። ዘያቀንት ፡ ለሰማይ ፡ በደመና ፡ (ዮሐ፳፩ ፡ ፲፰ ። ዓሞ፰ ፡ ፲ ። መዋሥ) ።

**ቀሡት** ፤ (ዕብ ፡ ቄሣት) ፤ የቀለም ፡ ዕቃ ፤ ቢልቃጥ ፤ ሙዳየ ፡ ቀለም ፤ የገንቦና ፡ የማድጋ ፡ ዐይነት ። ገንቦ ፤ ማድጋ ፤ እንስራ ፤ የውሃ ፡ ዕቃ ፤ ፀባኣ ። ቀሡት ፡ ጸሓፊ ። ቀሡት ፡ ልሕዙት ። ስተይ ፡ ማየ ፡ እምቀሡትከ ፡ (ሕዝ፱ ፡ ፪ ። ኤር፲፱ ፡ ፩ ። ምሳ፭ ፡ ፲፭) ።



ቀሡት ፡

**ቀሡታት** ፤ **ቀሣውት** ፤ ማድጎች ። ቀሡታተ ፡ ይጽዐን ፡ በአንበሳ ። ቀሣውቲሆሙ ፡ (ደራሲ ። ኤር፲፱ ፡ ፫) ።

**ቀሢጥ** ፤ **ጦት** ፤ (ቀሠጠ ፡ ይቀሥጥ ፡ ይቅሥጥ ። ዐረ ፡ ቀሸጠ) ፤ መቅሠጥ ፤ ማንሣት ፡ ማንሣሣት ፤ ከፍሎ ፡ መስረቅ ፡ መደበቅ ፤ ማታለል ፡ መቅጠፍ ። ቀሢጠ ፡ ንዋየ ፡ ባዕድ ። ዘይቀሥጥ ፡ እምቤተ ፡ እግዚ ። ቀሠጡ ፡ መንፈቀ ፡ ሤጡ ። ከመ ፡ ትቅሥጠሙ ፡ በተሳልም ፡ ፀሮሙ ፡ (መቃ ። ቀሌ ። ግብ፭ ፡ ፪ ። ዮሴፍ) ።

**ቀሣጢ** ፤ (ጢት ፡ ጥያን ፡ ያት ፤ ሠጥ) ፤ በቁሙ ፤ ሌባ ፡ ቀጣፊ ፤ አታላይ ። በራቂ ፡ ወቀሣጢ ፡ ዘአንበሩ ፡ ብየ ፡ (አዋል) ።

**ቄሥጤ** ፤ (ዕብ ፡ ቄበህ) ፤ ቁሸት ፤ ሽንፍላ ፤ ጨጓራ ፡ (ዘዳ፲፰ ፡ ፫) ።




ቄሥጤ ፡

**ቀሢም** ፤ **ሞት** ፤ (ቀሠመ ፡ ይቀሥም ፡ ይቅሥም ። ቀጠፈ) ፤ መቅሠም ፤ መልቀም ፡ መቃረም ፤ መቍረጥ ፡ ማጨድ ፡ መጨርገድ ፤ ማርገፍ ፤ መሰብሰብ ፡ ያታክልት ። በከመ ፡ ይቀሥምዎ ፡ ለዘይት ፡ ከማሁ ፡ ይቀሥምዎሙ ። ከመ ፡ ዘየአርር ፡ ድኅረ ፡ ዘይቀሥም ። ቅሥም ፡ አስካሎ ፡ ለዐጸደ ፡ ወይን ። ቀሠምኒ ፡ ሰከ ፡ ስምዐ ፡ እመጻሕፍት ፡ (ኢሳ፳፬ ፡ ፲፫ ። ሚራ፴ ፡ ፳፭ ። ራእ፲፬ ፡ ፲፱ ። መጽ ፡ ምስ) ።

**ቀሣሚ** ፤ (ሚት ፡ ምያን ፡ ያት ፤ ሣም ፡ ሠምት) ፤ የሚቀሥም ፡ የሚለቅም ፤ ለቃሚ ፡ ቈራጭ ። አድኅነኒ ፡ እምቀሣሚ ፡ ወይን ፡ አመ ፡ ያሌዕል ፡ ማዕጸዶ ። ሶበ ፡ ቦኡ ፡ ቀሣም ፡ ኅዐሌከ ፡ (ደራሲ ። ዐብድ ፡ ፭) ።

**መቅሠም** ፤ መልቀሚያ ፤ መቍረጫ ፤ አኘዘ ፡ መቅሠሞ ፡ (ሆሴ፯ ፡ ፲) ።

**አቅሠመ** ፤ አስለቀመ ፤ አስቈረጠ ። ወያቀሥምሙ ፡ ቀሥሞ ፡ (፭ነገ ፡ ፰ ፡ ፲፱) ።

**ተቀሥመ** ፤ ተለቀመ ፤ ተቈረጠ ። እንበለ ፡ ይትቀሠም ፡ ወይን ፡ (ዘኍ፲፫ ፡ ፳) ።

**ቅሡም** ፤ (ማን ፡ ማት ፡ ሥምት) ፤ የተቀሠመ ፤ የተለቀመ ፤ ልቅም ፤ ቍርጥ ።

**ቅሥመት** ፤ መልቀም ፡ መቍረጥ ፤ መቈረጥ ፤ አቈራረጥ ፤ ቈረጣ ፡ ለቀማ ። ቅብዐ ፡ ዘይት ፡ ዘቀዳሚ ፡ ቅሥመታ ፡ (ዘፀ፳፯ ፡ ፳) ።

**ቀሥም** ፤ (ብ ፡ አቅሣም) ፤ የተክል ፡ መከር ፡ አዝመራ ፤ ፍሬው ፡ የሚለቀምበት ፤ የለቀማና ፡ የቈረጣ ፡ ወራት ። የኅብር ፡ ቀሥም ፡ ምስለ ፡ ማእረር ፡ (ዓሞ፱ ፡ ፲፫ ። ዘሌ፳፯ ፡ ፭ ። መሳ፰ ፡ ፪) ።

—፤ ፍሬ ፤ ሕንባብ ፤ አስካል ፤ ተለቅሞ ፡ ተቈርጦ ፡ ያለ ። በመዋዕለ ፡ ማእረረ ፡ ቀሥም ። አቅሣመ ፡ ዐጸድ ። ይሌፈዉ ፡ ቀሥሞ ፡ (ሚራ፳፱ ፡ ፳፯ ። ሥር ፡ ጸሎ ። ማር ፡ ይሥ፲፭ ፡ ፩) ።

**ተቅሣም** ፤ (ማት) ፤ ለቀማ ፤ ቈረጣ ፤ አዝመራ ፤ ዐጽቅ ፡ ዘለላ ። ወተቅሣመ ፡ ፍሬሃ ፡ (አርጋ ፡ ፱) ።

**ቀሠመ** ፤—አጣፈጠ ፤—ቀሰመ ።

**አስተቃሠመ** ፤—አሻረተ ፤—ቀሰመ ።

**ቀሢፍ** ፤ **ፎት** ፤ (ቀሠፈ ፡ ይቀሥፍ ፡ ይቅሥፍ ፤ ቀጠፈ ። ዐረ ፡ ቀጸፈ) ፤ መቅሠፍ ፤ መቅጠፍ ፡ መዘንጠፍ ፤ መቍረጥ ፡ መቅጨት ፤ ባጭር ፡ ማስቀረት ፤ የትክል ፡ የሰብል ፡ የሕፃን ። መግፈፍ ፡ መግለጥ ፤ ማስራቆት ፤ ዕራቍት ፡ ማስጣል ፤ ለመግረፍ ።

—፤ መግረፍ ፤ መጠብጠብ ፤ መምታት ፤ መቅጣት ፤ መዝለፍ ፡ መገሠጽ ። ዘይቀሥፍ ፡ ብዕራይሁ ። ይቀሥፎሙ ፡ ለአሕዛብ ። ቀሠፍከኒ ፡ ወተቀሠፍኩ ። እግዚኦ ፡ በመዐትከ ፡ ኢትቅሥፈኒ ፡ (ሚራ፴፰ ፡ ፳፭ ። ራእ፲፱ ፡ ፲፭ ። ኤር፳ ፡ ፯ ። መዝ ፡ ፯ ። ኢሳ፲፭ ፡ ፱) ።

**ቀሣፊ** ፤ (ፊት ፡ ፍያን ፡ ያት) ፤ የሚገርፍ ፤ ገራፊ ፤ ቀጪ ። ንበ ፡ ቀሣፌሁ ፡ (ኢሳ፱ ፡ ፲፫) ።

**አቅሠፈ ፤** አስቀሠፈ ፤ አስገረፈ ፤ አስገረፈ ፤ አስቀጣ ።

**ተቀሥፈ ፤** ተቀሠፈ ፤ ተመታ ፡ ተቀጣ ፤ ተገረፈ ። ሐቡል ፡ እንዘ ፡ ይትቀሠፍ ። በተቀሥፎ ፡ ወበተሞቅሖ ። ወኢተቀሥፉ ፡ ምስለ ፡ ሰብእ ። ተቀሥፈት ፡ ፀሓይ ፤ ተመታች ፡ (ሚራ ፲፱ ፡ ፳፭ ። ፪ቆሮ ፡ ፮ ፡ ፭ ። መዝ ፡ ፸፪ ። ራእ ፡ ፲፪) ።

**ቅሡፍ ፤ (ፋን ፡ ፋት ፡ ሥፍት) ፤** የተቀሠፈ ፤ የተገረፈ ፤ የተመታ ፡ (መዝ ፡ ፸፪ ። ኢሳ፶፫ ፡ ፫ ፡ ፬) ።

**ቅሥፈት ፤ (ታት) ፤** መገረፍ ፤ መገረፍ ፤ አገራረፍ ፤ ግርፊያ ፤ ግርፋት ፤ ቍስል ፤ ደዌ ፡ መከራ ። ወኀፀበሙ ፡ እምቅሥፈቶሙ ። በቅሥፈታቲሁ ። ወሐይወ ፡ ኢዮብ ፡ እምድኅረ ፡ ቅሥፈቱ ፡ (ግብ ፲፮ ፡ ፴፫ ። ደራሲ ። ኢዮ ፵፱ ፡ ፲፮) ።

—፤ መውጫ ፤ ውጭ ፤ ዕዳሪ ። ወቅሥፈቱ ፡ ብሒረ ፡ ምድያም ፡ (ክብ ፡ ነገ) ።

**መቅሠፍት ፤ (ታት) ፤** መገረፊያ ፤ ጅራፍ ፡ ዐለንጋ ፡ ከዘራ ፡ ጨንገር ፤ የመሰለው ፡ ኹሉ ። መቅሠፍት ፡ ወተግማጽ ። ቍስለ ፡ መቅሠፍት ፡ ይገብር ፡ ሕምግልተ ። ድምፀ ፡ መቅሠፍት ። ወገብረ ፡ መቅሠፍተ ፡ ጥብጣቤ ፡ ዘሐብል ፡ (ሢራ ፳፰ ፡ ፮ ። ፳፰ ፡ ፲፯ ። ናሖ ፡ ፫ ። ዮሐ ፡ ፲፭) ።

—፤ ግርፋት ፤ ቍስል ፤ ሰንበር ፤ በትር ፤ ቅጣት ። መጠውኩ ፡ ዘባንየ ፡ ለመቅሠፍት ። ምንትኑ ፡ ዝ ፡ መቅሠፍት ፡ ዘማእከለ ፡ እደዊከ ። ዘየአምር ፡ ፈቃደ ፡ እግዚኡ ፡ ወኢይገብር ፡ ብዙኀ ፡ መቅሠፍቱ ፡ (ኢሳ፶ ፡ ፮ ። ዘካ፲፫ ፡ ፮ ። ሉቃ፲፪ ፡ ፵፯) ።

—፤ በቊጣ ፤ የእግዚር ፡ ዐለንጋ ፤ መቻያ ፤ ፍርድ ፡ ቅጣት ፤ መከራ ፡ ሥጋ ። ዓዲ ፡ አሐተ ፡ መቅሠፍተ ፡ ኣመጽእ ፡ ዲበ ፡ ፈርዖን ፡ ወዲበ ፡ ኵሉ ፡ ግብጽ ። ሰብዐቱ ፡ መላእክት ፡ እለ ፡ ይጸውሩ ፡ ሰብዐተ ፡ መቅሠፍተ ። አርባዕቱ ፡ መቅሠፍት ፡ እኩያት ፡ (ዘፀ፲፩ ፡ ፩ ። ራእ፲፭ ፡ ፩ ። ሕዝ፲፬ ፡ ፳፩) ።

**ምቅሣፍ ፤ (ፋት) ፤** መገረፊያ ፤ መገረፊያ ፤ ማስገረፊያ ፡ ቦታ ።

**ቀሥፍ ፤ ቅሥፍ ፤** አፍአ ፤ ዕዳሪ ፤ ገጠር ፤ ከከተማ ፡ ውጭ ፡ ያለ ፡ አገር ፤ ከቤት ፡ ውጭ ፡ ያለ ፡ ዐዘቅት ፡ ኵሬሕ ፤ ሜዳ ። ይቁሙ ፡ ቅሥፈ ፡ እቶት ። አይሁድ ፡ እለ ፡ ተዘርዉ ፡ ውስተ ፡ ኵሉ ፡ በሓውርት ፡ ቀሥፍ ። ይኑብር ፡ ጽመ ፡ ቅሥፈ ፡ (ቀሌ ። አስቴ፱ ፡ ፲፱ ። መሳ፫ ፡ ፳፱) ።

**ቀሠፋይ ፤** አፍኣዊ ፤ ዘአፍኣ ። ይፍልጥ ፡ መንጦላዕት ፡ ውሳጤ ፡ ወቀሠፋየ ፡ (ዘፀ፳፯ ፡ ፴፫) ።

**ቅማር ፤ (ራት ። ዐረ ፡ ቈሽረት ። ዕብ ፡ ቃሽቈሼት) ፤** ገለፈት ፤ የዓሣ ፡ ቅርፍት ። ዘቦ ፡ ክንፍ ፡ ወቅማር ፡ (ዘሌ፲፩ ፡ ፱—፲፪ ። ዘዳ፲፬ ፡ ፱ ፡ ፲ ። ሕዝ፳፱ ፡ ፬) ።

**ቀሠት ፤—ማድጋ ፤—ቀሠወ ።**

**ቀሥት ፤—በቊሙ ፤—ቀስት ።**

**ቅሥት ፤—ክርክር ፤—ወቀሠ ።**

**ቋዕ ፤—ቍራ ፤—ቀዊዕ ፡ ቆዐ ።**

**ቃዕደወ ፤ (ዐደወ ፤ ቀደወ ። ዐረ ፡ ቀዐደ ፤ ተቀመጠ) ፤** አሻግሮ ፡ አየ ፡ ተመለከተ ፤ ዐይኑን ፡ አርቆ ፡ ጣለ ፤ አራመደ ፤ ፊት ፡ ለፊት ፡ ማደ ፡ ለማደ ። ቀ ፡ ከቀደወ ፡ መቆቆ ፡ በዐደወ ፡ ላይ ፡ ተደርቧል ።

**አንቃዕደወ ፤** አንጋጠጠ ፤ አሻቀበ ፤ ተንጋጠጠ ፤ ወደ ፡ ላይ ፡ ወደ ፡ ሰማይ ፡ አየ ፤ ዐይኑን ፡ ሰካ ፤ ጸለየ ፡ ለመነ ። (ተረት) ፤ ከመሮጥ ፤ ማንጋጠጥ ። ይትፈሣሕ ፡ በበርጉ ፡ ሰማያት ፡ ሶበ ፡ ያንቃዕዱ ። ጕዩ ፡ ኀበ ፡ ታቦት ፡ ወአንቃዕደዉ ፡ ኀበ ፡ ኖኅ ፡ ከመ ፡ ይንሥኦሙ ፡ ኀቤሁ ። ላዕለ ፡ ላዕለ ፡ እንዘ ፡ ያንቃዕዱ ፤ በነጽሮ ፡ ተሰብረ ፡ ክሳዱ ። አንቃዕደወ ፡ ሰማየ ፡ ኀቤከ ፡ ኀበ ፡ አቡሁ ። አልዐለ ፡ እደዊሁ ፡ ወአንቃዕደወ ፡ አዕይንቲሁ ፡ ወኅሊናቲሁ ፡ (መጽ ፡ ምስ ። ቀሌ ። ቅኔ ። ቅዳ ። ፊልክ ፡ ፳፫) ።

**አንቅዕድው ፤ (ዋን ፡ ዋት ፡ ዱት) ፤** ያንጋጠጠ ፤ የተንጋጠጠ ፤ ዐይኑ ፡ ልቡ ፡ የተመሠጠ ፤ ሰማይ ፡ ሰማይ ፡ የሚያይ ፡ (አርጋ) ።

**ቈዐለ ፤ (ይቈዕል ፡ ይቈዐል ። ቀዊዕ ፡ ቆዐ) ፤** ሠባ ፡ ወፈረ ፤ ሥጋ ፡ ኾነ ፤ አደገ ፡ አፈረጠመ ።

**መቍዐል ፤ (ብ ፡ መቋዕል ፡ ልት ። ዐረ ፡ ሙክል ፤ ሙቅለት) ፤** ሥብ ፡ ወፍር ፡ ሥጋ ። የሠባ ፡ የወፈረ ፡ ያፈረጠመ ፤ ወረሞ ፡ አውላድ ፤ መሐስዕ ። መቍዐለ ፡ ጠሊ ፡ ወላሕም ። እለ ፡ ይሴስዩ ፡ መቋዕለ ። ቍርባናተ ፡ ወመቋዕልተ ፡ (ዘዳ፴፪ ፡ ፲፬ ። ዓሞ፮ ፡ ፬ ። ፪ዜና ፡ ፯ ፡ ፯) ።

**ቅዓን ፤ ኖት ፤ (ቀዐነ ፡ ይቅዕን ፡ ይቅዐን ። ቀነየ) ፤** ማስጨነቅ ፡ ማስጠበብ ፤ ማጣበቅ ። መጨነቅ ፡ መጠበብ ፡ መጣበቅ ፤ የቦታ ።

**ተቃዐነ ፤** ተጣነቀ ፤ ተጨናነቀ ፤ ተጣበበ ፡ (ሉቃ፰ ፡ ፵፭) ።

**መቅዐን ፤ (ብ ፡ መቃዕን) ፤** የሚያስጨንቅ ፤ የሚያስጠብብ ፤ ጠባብ ። ጭንቅ ፡ ጥብ ፤ አጣብቂኝ ። ፍኖት ፡ እንተ ፡ ትወስድ ፡ ውስተ ፡ ሕይወት ፤ ጽዕቅት ፡ ወመቅዐን ፡ ይእቲ ። እስመ ፡ መቅዐን ፡ ወጠዋይ ፡ ምሕዋራ ፡ (አፈ ፡ ተ፳፱ ። ደራሲ) ።

**መቅዓን ፤ (ናት) ፤** የሥቃይ ፡ መጣሪያ ፤ የሚያጣብቅ ፤ የሚጠረቅቅ ፤ የሚያጦዝ ፡ የሚጠመዝዝ ። አዘዘ ፡ ንጉሥ ፡ ይደይዎ ፡ ውስተ ፡ መቅዓን ፡ እስከ ፡ ይነቅዐ ፡ መለያልዩሁ ፡ ወይጠወይ ፡ ሥጋሁ ፡ በእኩይ ፡ (ስንክ ፡ መጋ፲፯) ።

**ቃፍ ፤ (ዕብ ፡ ማጣራ) ፤** ጊጤ ፤ ዐላማ ፤ መጋፊያ ፤ ብራኳ ። የመጠራን ፡ ፍች ፡ ተመልከት ፤ ከዚህ ፡ ጋራ ፡ አንድ ፡ ነው ። ከመ ፡ ቃፍ ፡ (ኢዮ፲፯ ፡ ፲፪) ።

**ቃፍ ፤ (ዐረብ) ፤** ስመ ፡ ፊደል ፡ ቀ ። ጋፍ ፤ ወንቃፍ ፡ ማለት ፡ ከዚህ ፡ ወጥቷል ።

**ቀፋዲት** ፤ (ጽር ፡ ኳፋሪ ፡ ዕብ ፡ ክፎፊይ) ፤ ምንዛሀ ፤ ምዝራቅ ፡ የውሃ ፡ የጠበል ፡ መርጫ ፡ ንዝፀንና ፡ ዘረቀን ፡ ተመልከት ፡ (፩ዕዝ ፡ ፳ ፡ ፳፯) ፡ ባለብሉየች ፡ ጻሕል ፡ ጽዋ ፡ ይሉታል) ።

**ቀፎ** ፤ (ዐረ ፡ ቁፊት ፡ ዕብ ፡ ቁፋህ) ፤ እንቅብ ፡ ቅርጫት ፡ እንገልግል ፤ ከረር ። በቁሙ ፤ የንብቾ ፡ ቤት ፤ ማጥን ፡ ኹለት ፡ አፍ ፡ ያለው ፤ ወይም ፡ ጕድጓድ ፤ ማን ፡ ቀባ ፤ ዕው ፡ ያልሠራው ፤ ንባም ፡ ማሬም ፡ በታ ፡ ዛፍ ። ቀፎ ፡ ዘመዓር ፡ (፩ነገ ፡ ፲፱ ፡ ፳፭) ።



ቀፎ ፡

**ቀፈዋት** ፤ ቀፎዎች ። ክልኤ ፡ ቀፈዋተ ፡ (ገድ ፡ ተክ) ።

**ቄፋዝ** ፤ (ጽር ፡ ኬፋዝ) ፤ አፈዝ ፤ ጥሩ ፡ ወርቅ ፤ ምዝምዝ ። ርእሱ ፡ ወርቀ ፡ ቄፋዝ ፡ (ማሕ፭ ፡ ፲፩) ። ፎዘን ፡ ተመልከት ።

(ጥፊ) **ቀፈለ** ፤ ሎት ፤ (ቀፈለ ፡ ይቀፍል ፡ ይቅፍል ። ዕብ ፡ ቃፋል) ፤ ማጠፍ ፡ መደረብ ፤ ዕጥፍ ፡ ድርብ ፡ ማድረግ ፤ መጠምጠም ፤ ማልበስ ፡ መሸፈን ፤ መለበጥ ፡ ማስጌጥ ። በዐረብ ፡ ግን ፡ ቀፈለ ፡ ብሎ ፡ ቈለፈ ፡ ዘጋ ፡ ያሰኛል ። ከመ ፡ ብሩረ ፡ ተምያን ፡ ዘቀፈልዎ ፡ ባዕለ ፡ ንዋየ ፡ ሰብሓ ። ዘቀፈሎን ፡ በብሩር ። ቀፈልየ ፡ በዐረር ፡ (ምሳ፳፯ ፡ ፳፫ ። ዘፀ፴፰ ፡ ፲፱ ። ድር ፡ ሚካ) ።

**አቅፈለ** ፤ አስለበጠ ፤ አስለበሰ ። እሌኒ ፡ አቅፈለት ፡ (መስቀለ) ፡ በወርቅ ፡ ወበዕንቍ ፡ ክቡር ፡ (ድጓ) ።

**ተቀፍለ** ፤ ተለበጠ ፤ ተሸለመ ፤ ለበሰ ፡ አጌጠ ። ይትቀፈሉ ፡ ወርቀ ፡ (ዘፀ፳፯ ፡ ፳፱ ። ፳፯ ፡ ፲፩) ።

**ቅፉል** ፤ (ላን ፡ ላት ፡ ፍልት) ፤ የተለበጠ ፤ ልብጥ ። ቅፉለ ፡ ወርቅ ። እለ ፡ ቅፉላን ፡ በብሩር ፡ (አርጋ ፡ ፬ ። ኢሳ፴ ፡ ፳፪ ። ዘፀ፳፯ ፡ ፴፱ ። ፴፯ ፡ ፬ ፡ ፲፩) ።

**ቅፍሎ** ፤ (ብ ፡ ቀፋልው ፤ ሉት) ፤ ቅጽለ ፡ ወርቅ ፤ ሥሥ ፡ ረቂቅ ፤ ልብጣት ፤ ቅባት ። ቅፍሎ ፡ ወርቅ ፡ (ዘፀ፴፩ ፡ ፲፰ ። ፴ ፡ ፫ ፡ ፭) ።

**መቅፈል** ፤ ልት ፤ (ብ ፡ መቃፍልት) ፤ መለበጫ ፤ ልባጥ ፤ ሽልማት ፡ ጌጥ ። ወትገብር ፡ መቃፍልቲሃ ፡ ለታቦት ፡ በወርቅ ፡ ጽሩይ ፡ (ክብ ፡ ነገ) ።

**ቀፈፍ** ፤ (ቀፈ ፡ ዐረብ ። ሱር ፡ ቃፈፍ ። ዕብ ፡ ቃፋእ) ፤ መርጋት ፤ መጽናት ፤ እንደ ፡ ዳቦና ፡ እንደ ፡ ደንጊያ ፡ መኾን ፤ የፈሳሽ ፡ ነገር ፤ የውሃ ፡ የውርጭ ፡ የመሰለው ፡ ኹሉ ። መጨከን ፡ ልበ ፡ ደንጊያ ፡ መኾን ፤ እለመፈራት ፡ አለማዘን ፤ መወፈር ፡ መግዘፍ ፡ መታበይ ። በቁሙ ፤ መቅፈፍ ፡ መኮርኮም ፤ ማስተካከል ። (ዐማርኛ) ።

**ቀፈት** ፤ ማኅቃ ፡ ደንደስ ፤ ጥናት ፤ ድርቅና ፤ ጭካኔ ፤ ትዕቢት ፡ ግዘፍ ፡ ድንዳኔ ። ቀፈቶሙ ፡ ለጽኑ ፡ ዖሙ ። ይወዲ ፡ ርእሶ ፡ ዲበ ፡ ብረኪሁ ፡ ወያደንን ፡ ቀፈቶ ፡ ወያቴሕት ፡ ጎሊናሁ ። ኢያትሐትከ ፡ ቀፈተ ፡ ልብከ ። ቀፈተ ፡ ልብ ፡ ዘሥጋ ፡ (ቄር ። ቄድር ። መቃ ። ቅዳ) ።

**ቀፊጽ** ፤ ጾት ፤ (ቀፈጸ ፡ ይቀፍጽ ፡ ይቅፍጽ ። ዕብ ፡ ቃፋጽ ፤ ቀነጸ) ፤ መግለጥ ፤ መክፈት ፤ መግፈፍ ፤ ማስፈቂት ። ቀልዐን ፡ ተመልከት ፤ የዚህ ፡ መንቲያ ፡ ነው ። ቀፈጽኪ ፡ አቍያጽኪ ። ቀፈጽኪ ፡ ኀፍረተኪ ። መኑ ፡ ይቀፍጽ ፡ ገልባቤ ፡ ገጹ ። ይቀፍጾን ፡ እግዚ ፡ አልባሲሆን ፡ (ሕዝ፲፮ ፡ ፳፭ ፡ ፴፯ ። ኢዮ፵፱ ፡ ፬ ። ኢሳ፫ ፡ ፲፯) ።

**ቀፋጺ** ፤ (ጺት ፡ ጽያን ፡ ያት) ፤ የሚገልጥ ፤ ገላጭ ፡ ገፋፊ ።

**ተቀፍጸ** ፤ ተገለጠ ፤ ተገፈፈ ፤ ተከፈተ ። ወይትቀፈጽ ፡ ኀፍረቶሙ ፡ ለግብጽ ። ተቀፈጽኪ ፡ እምድኅሬኪ ። ይትቀፈጽ ፡ ሞኅት ፡ (ኢሳ፳ ፡ ፬ ። ኤር፲፫ ፡ ፳፪ ። ቅዳ) ።

**ቅፉጽ** ፤ (ጻን ፡ ጻት ፡ ፍጽት) ፤ የተገለጠ ፤ የተገፈፈ ፤ ግልጥ ፡ ክፍት ፤ ባዶ ።

**ቀፊር** ፤ ሮት ፤ (ቀፈረ ፡ ይቀፍር ፡ ይቅፍር) ፤ መቈፈር ፡ መፈልፈል ፤ መፈለቅ ፤ መኮርኮር ፤ የመሬት ፡ የንጨት ፤ የደጋን ፡ የሚዛን ። መቀፈር ፡ መቀቀር ፤ ማለብ ፡ መደገን ፤ የዦሮ ፡ የቀስት ፡ የንፍጥ ። መጠየቅ ፡ መመርመር ፤ ትንቢት ፡ መፈለግ ፤ ከነቢይ ፡ ከካህን ።

**ቀፈር** ፤ **ቅፍር** ፤ ኮርኮር ፤ ፍልቅ ፤ ፍልፍል ፤ የኾርማት ፡ መግቢያ ፡ የንጨት ፡ መጋጠሚያ ። ቀፈረ ፡ ሐጽ ። ቀፈረ ፡ ፀምድ ፡ (ማር፲ ፡ ፳፭ ። ዘፀ፳፯ ፡ ፳፱) ።

**መቅፈርት** ፤ (ዕብ ፡ ኤፎድ ። ጽር ፡ ሄፖሚዳ) ፤ ልብሰ ፡ ኤፉድ ፤ ከእልባሳ ፡ ከህነት ፡ አንዱ ፤ ትንቢት ፡ ማወቂያ ፤ መጠየቂያ ፡ መመርመሪያ ። አፈደን ፡ ተመልከት ። ትብልያ ፡ ዘመቅፈርት ፡ (ዘፀ፳፰ ፡ ፬) ።

**ቀፈት** ፤—ደንደስ ፤—ቀፈፍ ።

**ቀጺብ** ፤ ቦት ፤ (ቀጸበ ፡ ይቀጽብ ፡ ይቅጽብ ። ዐረ ፡ ቀጸበ ። ዕብ ፡ ቃጻብ ፤ ቈረጠ ፤ ወሰነ) ፤ መቅጸብ ፤ ዐይንን ፡ መክፈትና ፡ መክደን ። መጥቀስ ፤ በዐይንና ፡ በእጅ ፡ መጥራት ፡ ማመልከት ፤ ከንፈርን ፡ መንከስ ። (ተረት) ፤ ባይን ፡ ጥቅሻ ፡ በከንፈር ፡ ንክሻ ። ይቀጽብ ፡ በዐይን ። ይዋጽብ ፡ በእደዊሁ ። አን

በስብሶ ፡ በቀራንብት ፡ ወቀጺብ ፡ በአዕይንት ፡ ዘእን በለ ፡ ኀፍረት ። ወቀጸባ ፡ ከመ ፡ ታምጽእ ፡ (ምሳ፳ ፡ ፲፫ ። ኪዳ ። ፈ ፡ መ ፡ ፹፩ ፡ ፳ ። ገድ ፡ ተክ) ።

—፤ መመሰል ፤ መተረት ፤ ምሳሌ ፡ መስጠት ። መፍጠን ፤ መቀልጠፍ ፤ ማፈዝ ፡ ማላገጥ ።

**ተቃጸበ** ፤ ተጣቀሰ ፤ ተጠቃቀሰ ። የሐውራ ፡ እንዘ ፡ ይትቃጸባ ፡ በአዕይንቲሆን ። ዘይትቃጸብ ፡ በ አዕይንቲሁ ። ይሬእዩዎ ፡ ወይትቃጸቡ ፡ ቦቱ ፡ (ኢ. ሳ፫ ፡ ፲፮ ። ምሳ፲ ፡ ፲ ። ጥበ፲ ፡ ፲፰) ።

**ቅጽበት** ፤ መጥቀስ ፤ መጠቀስ ፤ አጠቃቀስ ፤ ጥ ቅሻ ፤ ንክሻ ። በቁሙ ፤ ፍጥነት ፤ ችኩላ ፤ ቅልጠፋ ፤ ወዲ ያው ፤ ቶሎ ፤ ድንገት ፤ ጥቂት ፡ ሳይቈይ ፡ ሳይዘገይ ። ይ ሔምር ፡ በቅጽበተ ፡ አዒብዕ ። ዘነበበ ፡ በጊዜሁ ፡ ይገ ብሮ ፡ ወዘንለየ ፡ በቅጽበት ፡ ይከውኖ ። በመጠነ ፡ አ ሐቲ ፡ ቅጽበት ። ኢተፈልጠ ፡ መለኮት ፡ እምትስብ እት ፤ ወኢከመ ፡ ቅጽበተ ፡ ዐይን ። ወበማልስ ፡ ንፍ ኅተ ፡ ቀርን ፡ ይትነሥኡ ፡ ሙታን ፡ ከመ ፡ ቅጽበተ ፡ ዐ ይን ፡ (ምሳ፳ ፡ ፲፫ ። ቅዳ ፡ ግሩ ። ጥበ፲፰ ፡ ፲፱ ። ሃይ ፡ አበ ። ቅዳ ፡ ያዕ) ።

—፤ ጥቅስ ፤ ምሳሌ ፤ ተረት ፤ አንጻር ። ነገረ ፡ ጠቢባን ፡ በቅጽበት ። ፈክሮ ፡ ቅጽበት ፡ (ምሳ፩ ፡ ፮ ። ጥበ፰ ፡ ፰) ።

**ቀጽበ** ፤ (ትግ ። ዕብ ፡ ቃጸፍ) ፤ ተቈጣ ፤ ተ ናደደ ፤ ወገሸ ፡ አበደ ፤ ቱግ ፡ አለ ፤ እሳት ፡ ኾነ ።

**ቀጸወ** ፤—ጣደ ፡ አበሰለ ፤—ቀፀወ ።

**ቈጺል** ፤ ሎት ፤ (ቈጸለ ፡ ይቈጽል ፡ ይ ቍጽል ። ሐመለ ፤ ለምለመ) ፤ ማቍጸል ፤ ቅ ጠል ፡ ማውጣት ፤ መለምለም ፤ ማቀጠል ፤ ማ፪ፍ፪ፍ ፤ ፀጽቃም ፡ ቅጠላም ፡ መኾን ። መጽሐፍ ፡ ግን ፡ በቈጸለ ፡ ፈንታ ፡ አቍጸለ ፡ ይላል ፤ ስሕተት ፡ ነው ፡ (አርጋ ፡ ፩) ።

**ቍጹል** ፤ (ላን ፡ ላት ፡ ጽልት) ፤ ያ፪ፈ ፪ፈ ፤ ቅጠላም ፤ ባለቅጠል ። ቈጽለ ፡ ዕፀ ፡ ቍጹል ፡ ለ ገቢረ ፡ ምጽላል ፡ (ነሐ፰ ፡ ፲፭) ።

**ቈጽል** ፤ (ላት ፤ አቍጽል) ፤ ቅጠል ፤ ቅ ጠላቅጠል ፤ የዛፍ ፡ የመጣፍ ፡ የወርቅ ፡ የብር ። ልጥ ፡ ሐረግ ። ከመ ፡ ቈጽለ ፡ ዕፀ ፡ ዘጽሩቅ ፡ ቈጽሉ ። በኀብ ስት ፡ ወማይ ፡ ወቈጽል ። ቈጽለ ፡ ወርቅ ፡ ረቃቅ ። ቈ ጽለ ፡ አሥርቅ ፡ (ሚራ፲፱ ፡ ፲፰ ። ቀሌ ። ዘፀ፳፰ ፡ ፴፮ ። ሚራ፲፭ ፡ ፴) ።

**አቍጸለ** ፤ አለመለመ ፤ ዐደሰ ፡ አረጠበ ፤ ፀጽ ቃም ፡ ቅጠላም ፡ አደረገ ። ዐምደ ፡ ቤትየ ፡ ዘአቍጸ ልከ ፡ (ድጓ) ።

**ቀጸለ** ፤ (ይቈጽል ፡ ይቀጽል ፤ ቀጽሎ) ፤ ቀጠለ ፡ ቀጣጠለ ፤ ጨመረ ፤ የቁመት ፡ የፍሬ ፡ የትምርት ።

**አቀጸለ ፤ አስተቀጸለ** ፤ አስቀጠለ ። አቀዳ፪ ፤ ማን ፡ አሸከመ ፤ አስጌጠ ፡ ሸለመ ። አክሊለ ፡ ትፍሥሕት ፡ ታስተቈጽለከ ። ትገብር ፡ አክሊላተ ፡ ወታስተቈጽሎ ፡ ለዮሳዕ ። አስተቀጸለ ፡ አረፍተ ፡ በሜላትራ ፡ (ሚራ፮ ፡ ፹፩ ። ዘካ፮ ፡ ፲፩ ። ፫ነገ ፡ ፮ ፡ ፱ ። ፯ ፡ ፵) ።

**ተቀጸለ** ፤ ተቀጠለ ፤ ተጨመረ ፡ ተቀጥላ ፡ ኾነ ፤ በሰው ፡ ራስ ፡ ላይ ፤ ያበባ ፡ ያክሊል ። ተቀዳ፪ ፤ ሰውየው ፡ በራሱ ፡ ደፋ ፡ ለበሰ ፡ ታሸከመ ፤ ጠመጠመ ። እንዘ ፡ ይ ትቈጸል ፡ አክሊለ ፡ ዘሦክ ። ንትቀጸል ፡ ጽጌ ፡ ረዳ ። ን ትቀጸል ፡ አሕባለ ፡ ውስተ ፡ አርእስቲነ ፡ (ዮሐ፲፱ ፡ ፭ ። ጥበ፪ ፡ ፰ ። ፫ነገ ፡ ፳ ፡ ፴፩) ።

**ቅጹል** ፤ (ላን ፡ ላት ፡ ጽልት) ፤ የተቀጠለ ፤ ቅጥል ። የተቀዳ፪ ፡ ቅድ፮ ።

**ተቅጺል** ፤ (ላት) ፤ ተቀጥላ ፤ የንጨት ፡ ዲ ቃላ ።

**ቀጸላ** ፤ (ላት) ፤ በቁሙ ፤ የራስ ፡ ልብስ ፡ ጌጥ ፡ ሽልማት ፤ ታናሹም ፡ ታላቁም ፤ ማናቸውም ፡ ኹሉ ፡ በ የስሙና ፡ በያይነቱ ። ወገሮ ፡ ሥልዕ ፡ ሠርመዲ ፡ ክሎታ ፤ አክሊል ፡ ዘውድ ፡ ሜትራ ፤ ሾፈት ፡ ቆብ ፡ መጠምጠ ሚያ ፤ ጠርቡሽ ፡ ባርኔጣ ፤ የመሰለው ፡ ኹሉ ። ዕጨጌዎ ችና ፡ አበ ፡ ምኔቶች ፡ በቆባቸው ፡ ላይ ፡ የሚለብሱት ፤ የ ሚከናነቡት ፡ ሻሽ ፡ ነጠላ ። ወህየንተ ፡ ዘወርቅ ፡ ቈጸ ላሃ ፤ ብርሐት ፡ ወፀአ ፡ ላዕሌሃ ፤ ወድማኅ ፡ ኢኮነት ፡ ድማኅ ። ወደበ ፡ ርእሶሙ ፡ ቦሙ ፡ ቀጸላ ፡ በአምሳለ ፡ ወርቅ ። ሰብዐቱ ፡ ቀጸላት ። ወተቀጸሊ ፡ ቈጸ ላኪ ፡ ደበ ፡ ርእስኪ ፡ ዘስብሐቲሁ ፡ ቅዱስ ። ቀጸላቲ ሆን ፡ ወባሕርያቲሆን ፡ (ቅኔ ። ራእ፱ ፡ ፯ ። ፲፱ ፡ ፲ ። ባሮ፭ ፡ ፱ ። ኢሳ፫ ፡ ፲፱) ።

**ቀጸላ** ፤ ቅጽል ፤ በስምና ፡ በግብር ፡ የሚጨመር ፡ ቃል ፤ የአካልንና ፡ የግብርን ፡ አኳኾን ፡ ጠባዩን ፡ መል ኩን ፡ የሚገልጥና ፡ የሚያስረዳ ። ንዋኅ ፡ ሠናይ ፡ ጸዐዳ ፡ እንደ ፡ ማለት ።

**ቀጺመት** ፤ (ቃት ። ዕብ ፡ ቅጺዓህ ፤ ቃኔ ። ዐረ ፡ ቀጸብ) ፤ ሽቱ ፤ የሽቱ ፡ ዕንጨት ፡ ስም ፤ ውስጠ ፡ ክፍት ፤ የመቃ ፡ የሸንበቆ ፡ ዐይነት ። ጽጌ ፡ ቀ ጺመት ፡ ወቀናንም ፡ (ስንክ ፡ ነሐ፳፯ ። ዘፀ፴ ፡ ፳፫ ። ማሕ፬ ፡ ፲፬) ።

**ቀጺዕ** ፤ ዖት ፤ (ቀጽዐ ፡ ይቀጽዕ ፡ ይቅ ጻዕ ። ዕብ ፡ ቃጻዕ ። ዐረ ፡ ቀጠዐ) ፤ መቅጨት መቅጸት ፤ እየለኩ ፡ እያስተካከሉ ፡ መቍረጥ ፡ ማጠፍ ፤ ማጕበጥ ፡ ማረቅ ፤ ማስጐንበስ ፤ ማስጨነቅ ። የማማ ፡ የብራና ፡ የማኅደር ፡ የልብስ ፤ የወገብ ፡ የደጋን ። እለ ፡ ይቀጽዑ ፡ ቀሚሰ ። ቀጽዕዋ ፡ ለነፍስየ ። ይቀጽዕ ፡ ዙሎ ፡ ሐቌ ። ያደነግፁ ፡ ልበ ፡ ወይቀጽዑ ፡ ከመ ፡ ማ ሕምም ፡ (ገድ ፡ አዳ ። መዝ ፡ ፶፮ ። ናሖ፪ ፡ ፲ ። ሚራ ፴፩ ፡ ፭) ።

—፤ ማወቅ ፤ ዐውቆ ፡ መሥራት ፡ መቅጣት ፤ መደልደል ፡ ማስተካከል ፡ መጥረግ ፡ መመድመድ ፤ የሰው ፡ የቦታ ፡ የ መንገድ ። አሠር ፡ ዘቀጻዕነ ። ፍኖትየ ፡ ወአሠርየ ፡ አ ንተ ፡ ቀጻዕከ ። ወቀጻዕከዋ ፡ በጾም ፡ ለነፍስየ ፡ (ኢ. ዮ፩ ፡ ፳፯ ። መዝ ፡ ፻፴፰ ፡ ፫፫) ። ዘቀጻዕነ ፡ በማለት ፡ ፈንታ ፡ ዘአቅጻዕነ ፡ ይላል ፤ ስሕተት ፡ ነው ። ባለብሉዮ ችም ፡ ያዕጋነው ፡ ወግ ፡ ያስተረከነው ፡ ታሪክ ፡ ብለው ፡ ይፈቱታል ።

**አቅጽዐ** ፤ አስቀጨ ፤ አስቀጣ ፤ አስጉበጠ ።

**ተቀጽዐ** ፤ ተቀጨ ፤ ተሠራ ፡ ተቀጣ ፤ ጉበጠ ፤ ፈራ ፡ ደነገጠ ። ወትትቀጻዕ ፡ ዘላ ፡ ነፍስ ። አረጋዊ ፡ ዘተቀጽዐ ፡ ዘባኑ ። ተቀጽዑ ፡ ወኢተርፈት ፡ ነፍሶሙ ፡ በላዕሌሆሙ ፡ (ሕዝ፳፮ ፡ ፯ ። አፈ ፡ ተ፳፫ ። ነሐ፯ ፡ ፩ ። ኢሳ፲፫ ፡ ፰) ።

**ቀጻዕ** ፤ **ቀጻ** ፤ **(ብ ፡ ቀጻት)** ፤ የእሳት ፡ እራት ፤ ጸባሕርይ ፡ ፈቃዱ ፡ የሚቀጣ ፡ የሚቃጠል ፤ ቅጣት ፡ የሚቀበል ፤ ኋላም ፡ ታድሶ ፡ የሚነሣ ፡ የትንሣኤ ፡ ሙታን ፡ አምሳል ። ዖፍ ፡ ዘይሰመይ ፡ ቀጻ ፡ (ሃይ ፡ አበ ፡ ኤጲ) ።

**ቀጽቀጸ** ፤ **(ቀጥቀጠ)** ፤ አንቈጨቈጨ ፡ ፈጨ ፡ ቈረጠመ ፤ ወዘወዘ ፤ አራደ ፡ አንቀጠቀጠ ፤ የደዌ ፡ የሐዘን ፡ የፍርሀት ። በእንተ ፡ ዝንቱ ፡ ይቀጸቅጸኒ ፡ ሐቌየ ፡ (ኢሳ፳፩ ፡ ፫) ።

**ቅጽቃጼ** ፤ **(ቅጥቃጤ)** ፤ መፍጨት ፤ መፈጨት ፤ መወዝወዝ ፤ መቈርጠም ። ቍርጥማት ፤ ቃንዛ ፤ የደዌ ፡ የሐዘን ፡ ስሜት ። ፈውስ ፡ ዘያሴስል ፡ ቅጽቃጼ ፡ ሕማም ፡ (አፈ ፡ ድ፳፩) ።

**ቀጺር** ፤ **ሮት** ፤ **(ቀጸረ ፡ ይቀጽር ፡ ይቅጽር ። ዐረ ፡ ቀጸረ ። ዕብ ፡ ቃጻር ፤ ዐጨደ ፤ አነሰ)** ፤ መቅጠር ፤ ማጠር ፤ መጀጐል ፤ ማረድ ፡ መመሸግ ፤ በቤት ፡ በከተማ ፡ ዙሪያ ፡ ዐጥር ፡ ቅጥር ፡ መሥራት ፤ መከበብ ፤ ዙሪያውን ፡ መያዝ ። ወቀጸሩ ፡ ላዕለ ፡ ሕሀጉር ፡ (ዮዲ፲ ፡ ፭) ። ሐጸረን ፡ ተመልከት ።

—፤ ቀጠሮ ፡ ማድረግ ፤ ቀን ፡ መቍረጥ ፤ መወሰን ፡ (ዐማርኛ) ። ዐደመን ፡ እይ ።

**ቀጻሪ** ፤ **(ሪት ፡ ርያን ፡ ያት ፤ ጻርት)** ፤ የሚያጥር ፡ የሚቀጥር ፡ ቀጣሪ ፤ ቅጥር ፡ ሠሪ ።

**አቅጸረ** ፤ አስቀጠረ ፤ ቅጥር ፡ አሠራ ፡ አስከበበ ።

**ተቀጽረ** ፤ ተቀጠረ ፤ ታጠረ ፤ ተከበበ ።

**ቅጹር** ፤ **(ራን ፡ ራት ፡ ጽርት)** ፤ የታጠረ ፤ የተቀጠረ ። ሀገር ፡ ቅጽርት ፡ (ኢሳ፩ ፡ ፰) ።

**ቅጽር** ፤ **(ራት)** ፤ በቁሙ ፤ ቅጥር ፤ ዐጥር ፤ መከበቢያ ፤ የቤት ፡ የከተማ ። ለእመ ፡ ፈቀደ ፡ ይሕንጽ ፡ ብእሲ ፡ ቅጽረ ፡ ይርሐቅ ፡ እምቢጹ ፡ አሐተ ፡ ምሥጋረ ፡ እግር ። ሀገር ፡ እንተ ፡ ባቲ ፡ ቅጽር ። ይጠቅሙ ፡ ለርእሰሙ ፡ ቅጽረ ። ኢያሪኮ ፡ እንተ ፡ የዐውዳ ፡ ሰብዐቱ ፡ ቅጽራት ፡ (ፍ ፡ ነ ፡ ፴፯ ። ዘሌ፳፭ ፡ ፳፱ ። ምሳ፳፰ ፡ ፱ ። ስንክ ፡ ሠኔ፳፯) ።

**ቈጼሩት** ፤ **(ዕብ ፡ ቅጹሮት)** ፤ ዐጫጭሮች ፤ ታናናሾች ፤ ጠባቦች ፡ (ሕዝ፵፮ ፡ ፳) ።

**ቈጺር** ፤ **ሮት** ፤ **(ቈጸረ ፡ ይቈጽር ፡ ይቍጽር ። ዕብ ፡ ቃሻር ፤ ቃጣር ። ሱር ፡ ቅጣር)** ፤ መቋጠር ፤ መቀጠል ፤ አንዱን ፡ ካንዱ ፡ ጋራ ፤ ወይም ፡ አንዱን ፡ ባንዱ ፡ ማሰር ፡ ማቈር ፤ ማጽናት ፡ ማጠንከር ፤ መሰገጥ ፡ መኰፍተር ፡ መጨምደድ ፤ የፊት ። ነሥአ ፡ ዲናረ ፡ ወርቅ ፡ ወቈጸሮ ፡ በጸርቅ ። ቈጸርዎ ፡ በልብሶሙ ። ቈጸሩ ፡ አማዑቶሙ ። ሐብል ፡ መንፈሳዊ ፡ ዘያዐርግ ፡ ልበ ፡ እምድር ፡ ወይቈጽሮ ፡ ውስተ ፡ ሰማይ ። ኢትቍጽሩ ፡ ገጸክሙ ። እፎ ፡ ክመ ፡ ዝ ፡ ይቈጽር ፡ ገጾ ። ትካዝ ፡ ወቈጺረ ፡ ገጽ ፡ (ስንክ ፡ ታኅ ፲ ። መጽ ፡ ምስ ። መዝ ፡ ፲፯ ። ፊልክ ፡ ፻፳፩ ። ፍ ፡ ነ ፡ ፵፩ ። አፈ ፡ ተ፳፱) ።

—፤ ክፉ ፡ ማሰብ ፤ መፅነስ ፤ መተንኰል ፤ ማታለል ፤ መሸንገል ። እመ ፡ ቦ ፡ ዘቈጸረ ፡ ከመ ፡ ይቅትል ። አንተሰ ፡ ትቈጽር ፡ በዘትትሜጠዋ ፡ ለነፍስየ ። ለመጋቢ ፡ ኢይደልዎ ፡ ከመ ፡ ይቍጽር ፡ ለአመጋቢሁ ፡ ውስተ ፡ ሠዪጥ ፡ ወተማይጦ ፡ (ዘፀ፳፩ ፡ ፲፬ ። ፩ነገ ፡ ፳፱ ፡ ፲፱ ። ፍ ፡ ነ ፡ ፴) ።

—፤ መቍጠር ፤ ቍጥር ፡ ሒሳብ ፡ ማድረግ ፤ አንድ ፡ ኹለት ፡ ሦስት ፡ ማለት ። ኈለቈ ፡ ሐሰበ ፡ አንዘ ፡ ብሎ ፡ ቈጠረ ፡ ማለት ፤ ዐማርኛው ፡ ከዚህ ፡ የወጣ ፡ ነው ።

**ቈጻሪ** ፤ **(ሪት ፡ ርያን ፡ ያት)** ፤ የሚቈጥር ፤ የሚቋጥር ፤ አሳሪ ፡ ቋጣሪ ፤ ዐሳቢ ፡ ቈጣሪ ።

**አቍጸረ** ፤ አስቈጠረ ፤ አስቋጠረ ። አስተንኰለ ፤ አሳተ ፡ አባበለ ፤ ሐሰት ፡ ሸንገላ ፡ አስተማረ ። አቍጸሩ ፡ ሎቱ ፡ ዕደወ ። ያቈጽሩ ፡ ሎቱ ፡ ሰማዕተ ፡ ሐሰት ፡ (ግብ፮ ፡ ፲፩ ። መጽ ፡ ምስ) ።

**ተቈጽረ** ፤ ተቈጠረ ፤ ተቋጠረ ፤ ተሰበሰበ ። በከመ ፡ ይትዐወቅ ፡ ንዋየ ፡ ሰብኣ ፡ ዘተሰብረ ፡ እምነ ፡ ዘኢተሰብረ ፡ በተቈጽሮ ፤ ከማሁ ፡ ብእሲኒ ፡ በንባቡ ፡ (ፈላስ) ።

**ቍጹር** ፤ **(ራን ፡ ራት ፡ ጽርት)** ፤ የታሰረ ፤ የተቋጠረ ፤ ቍጥርጥር ። ቍጹር ፡ ውስተ ፡ አሥዋክ ። እንተ ፡ ቍጽርት ፡ ውስቴታ ። ቍጹረ ፡ ገጽ ፡ (ፊልክ ፡ ፻፲፯ ። ክብ ፡ ነገ ። ገድ ፡ አዳ) ።

**ቍጽረት** ፤ መቋጠር ፤ መፅ(ፀ)ነስ ፤ አቈጣጠር ፤ እስራት ፤ ቍጥራት ፤ ቍጥርጥርነት ፡ መጋጠሚያ ። አመ ፡ ሰቡዑ ፡ ለነሐሴ ፡ ቍጽረታ ። መካነ ፡ ቍጽረቱ ። ቍጽረቱ ፡ ከመ ፡ እብነ ፡ ኰኵሕ ። ቍጽረተ ፡ ዐራዙ ፡ (አዋል ። ኢዮ፵፩ ፡ ፯ ። ዘፀ፳፰ ፡ ፴፩) ።

**ቈጻራ** ፤ ሽንገላ ፤ ስርቆት ፤ ቅጥፈት ። አግብአ ፡ ሎቱ ፡ ንዋየ ፡ ወሀቦ ፡ ዘእንበለ ፡ ቈጻራ ፡ ወርዲ ፡ (ቀሌ) ።

**ቍጽር** ፤ **(ራት)** ፤ በቁሙ ፤ ቍጥር ። እስራት ፤ ግርፋት ፤ ዐለንጋ ፡ ጅራፍ ፡ ጢጢ ፡ ሳንባ ፡ ጠለፍ ፤ ክፉ ፡ ምክር ፤ ሽንገላ ፡ ተንኰል ። ኢታጽንዑ ፡ ቍጽረክሙ ። እለ ፡ ይጼብእዎ ፡ በቍጽር ። ይመክሩ ፡ በቍጽር ፡ ያመንስዉኒ ፡ (ኢሳ፳፰ ፡ ፳፪ ። ፴ ፡ ፴፱ ። መዝ ፡ ፴፱ ። ፴፯) ።

**ቍጽሮ** ፤ ጥልፍ ፤ ግብረ ፡ መርፌ ። መልበስተ ፡ ቍጽሮ ፡ (ዘፀ፳፰ ፡ ፱) ።

—፤ ቋጠሮ ፤ ቋጨራ ፤ የታሰረ ፡ የማር ፡ የቅጠል ፡ ነዶ ፡ ችቦ ። ቍጣሮ ፡ አቍጣሮ ፤ የመቍጠሪያ ፡ ጸሎት ።

**መቍጸርት** ፤ ጕንጕን ፡ ሽርባ ፤ ቋድ ፡ ጥብጣብ ፤ የልብስ ፡ ማስጌጫ ፡ መዘምዘሚያ ፤ ዝምዝማት ፤

ቍልፍ ፡ ተከፈለ ። ወመቍጸርቱ ፡ ወርቅ ፡ ዘግቡር ፡ በዕንቍ ፡ (ሚራ ፺፩ ፡ ፲፩) ።

—፤ መቍጠሪያ ፤ መቋጠሪያ ፤ መቈጣጠሪያ ፤ የቍጥር ፡ መሣሪያ ።

**ተቋጸረ** ፤ ተቋጠረ ፤ ተቈጣጠረ ፤ ተሸናገለ ፤ ተሸነጋገለ ። ዘይከውን ፡ በውስቴቱ ፡ ተቋጽሮ ። ተቋጻር ያን ፡ ምስለ ፡ እሊኣሁ ፡ (ፍ ፡ ነ ፡ ፴) ።

—፤ ተባበረ ፤ አንድ ፡ ልብ ፡ አንድ ፡ ሐሳብ ፡ ኾነ ፤ ሚሬ ፡ ቈረጠ ፡ ተማማለ ፤ ለመግደል ፡ ለመወንጀል ። መጽሐፍ ፡ ግን ፡ ተቋጸረ ፡ በማለት ፡ ፈንታ ፡ አስተቋጸረ ፡ ይላል ፤ የጣፊ ፡ ስሕተት ፡ ነው ። አስተቋጸሩ ፡ ሎቱ ፡ በሽብሂ ፡ ማኅበሌት ፡ (፱ነገ ፡ ፲፱ ፡ ፳) ።

**አስተቋጸረ** ፤ አቋጠረ ፤ አቈጣጠረ ፤ አስተሳሰረ ።

**ቀጸጼ** ፤ (ቀጸቢ ፤ ቀጸበ) ፤ ገበሎ ፤ ጕበና ፤ እንቃቅላ ፤ የዕምሥምት ፡ ዐይነት ፡ (አዋል) ።

**ቀፂው ፤ ዎት** ፤ (ቀፀወ ፡ ይቀፁ ፡ ይቅፁ ። ዕብ ፡ ቃጸሀ ፤ ቈረጠ ፡ ለየ) ፤ መጣድ ፡ ማስረር ፤ መቀቀል ፡ ማንፈር ።

**መቅፀት** ፤ (ታት ፤ መቃፅው) ፤ ሸክላ ፤ ድስት ፡ ምንቸት ፤ ማስሮ ፤ የሸክላ ፡ የብረት ። በአይቴ ፡ ይትዐረክ ፡ መቅፀት ፡ ምስለ ፡ ጽሀርት ። መቅፀተ ፡ ብርት ፡ ዐቢይ ። ብሱል ፡ በመቅፀት ። ምንባሬ ፡ መቅፀት ፡ (ሚራ ፲፫ ፡ ፪ ። ዮሴፍ ። ዘሌ ፯ ፡ ፺ ። ፲፩ ፡ ፴፭) ።

**ቀቀበ** ፤ (ነቀበ) ፤ ሰገበ ፤ ሰፋ ፤ ሸፈፈ ፡ ደጐሰ ፤ አለበሰ ፤ የሰይፍ ፡ የጐራዴ ፡ የዓንሽ ፡ የጦር ።

**ቀቀብ** ፤ (ባት ። ዕብ ፡ ንዳን ፤ ታዓር) ፤ ሰገባ ፤ አፎት ፤ ሽፋፍ ፤ ድርቁ ፤ የሰይፍ ፡ ቤት ፤ ማኅደር ። ኣወፅአ ፡ ለመጥባሕትየ ፡ እምኔ ፡ ቀቀባ ። አግብኣ ፡ ለመጥባሕትከ ፡ ውስተ ፡ ቀቀባ ። በልዑ ፡ ማእሰ ፡ ቀቀበ ፡ አስይፍቲሆሙ ፡ (ሕዝ፳፩ ፡ ፫ ፡ ፴ ። መጽ ፡ ምስ ፡ ዮሴፍ) ።

**ቈቀወ** ፤ ቍቁ ፡ አለ ፡ (ዐማርኛ) ።

**አስቈቀወ** ፤ (ተቀ ፡ ግ) ፤ ጮኸ ፡ ዋይ ፡ አለ ፤ የወደደውን ፡ ሰላጣ ፤ እንደ ፡ ሕፃን ፡ ተንሰቀሰቀ ፤ አልቅሶ ፡ አስለቀሰ ፤ አሞሸ ፡ ቈዘመ ፤ ሙሾ ፡ አወጣ ፤ ተቀኘ ፡ ገጠመ ። ቀንየንና ፡ ነቀወን ፡ ሰንቀወን ፡ ተመልከት ፤ የዚህ ፡ ጎር ፡ ናቸው ። አስቈቅዉ ፡ በቈቃወ ። አስቈቀውነ ፡ ለክሙ ፡ ወኢበከይክሙ ። አንስት ፡ ይበክያሁ ፡ ወያስቈቅዋሁ ፡ ለተሙዝ ። እለ ፡ ይበክዩ ፡ ወያስቈቅዉ ፡ (ሚክ፪ ፡ ፬ ። ማቴ፲፩ ፡ ፲፯ ። ሕዝ፰ ፡ ፲፬ ። ቀሌ) ።

**መስቈቅው** ፤ (ቍት ፡ ቅዉት ፤ ዋን ፡ ዋት) ፤ ጮኸ ፡ የሚያለቅስ ፤ አልቃሽ ፡ አስለቃሽ ፤ ገጣሚ ፡ ቀንቃኝ ፤ ሙሾ ፡ አውጭ ፤ ባለሙሾ ። መስቈቅው ፡ ወቍጸር ። ጸውዕዎን ፡ ለመስቈቅዋት ። ኢይደሉ ፡ ተዓስቦተ ፡ ሕሩማት ፡ ዘከመ ፡ መስቈቅዋት ፡ ወሰብአ ፡ ምራይ ፡ (ገድ ፡ አዳ ። ኤር፱ ፡ ፲፯ ። ፍ ፡ ነ ፡ ፴፯) ።

**ሰቈቃው** ፤ ጩኸት ፡ ዋይታ ፤ ልቅሶ ፡ ሙሾ ፤ የልቅሶ ፡ ግጥም ፤ ኀይለ ፡ ቃል ። ሰቈቃወ ፡ ኤርምያስ ፡ ነቢይ ። ንሥኢ ፡ ሰቈቃወ ፡ በከናፍርኪ ። ንሣእ ፡ ሰቈቃወ ፡ ላዕለ ፡ መላእክተ ፡ እስራኤል ፡ (ሰቈ ፡ ፩ ። ኤር፯ ፡ ፳፱ ። ሕዝ፲፱ ፡ ፩ ። ማቴ፪ ፡ ፲፰) ።

**ቈቅሐ** ፤—አጠራ ፤—ቀይቅሐ ።

**ቈቀየ** ፤—ቀቀተ ፤—ቀይቀየ ።

**ቃቂል** ፤ ቃጭል ፤ ታናሽ ፡ መረዋ ። ዘሩ ፡ ቀዊል ፡ ነው ።

**ቀቀኖ** ፤ (ጽር ፡ ኪክኖስ ። ዕብ ፡ ቃአት ፤ ቂቅ ። ሱር ፡ ቃቃአ ። ዐረ ፡ ቁቅ) ፤ ርኩም ፡ (ዘሌ፲፩ ፡ ፲፱ ። ዘዳ፲፬ ፡ ፲፯) ። ጕንባሕንና ፡ አበ ፡ ጕንባሕን ፤ እድገ ፡ መረብን ፡ እይ ። ብዥው ፡ ቀቃንው ፤ በቤት ፡ አንቀጽ ፡ ሲኾን ፡ ቀቀኑት ፤ ቀቃኑት ፡ ያሰኛል ።



ቀቀኖ ፤

**ቈቍዖ ፤ ዖት** ፤ (ቈቍዐ ፡ ይቈቍዕ ፡ ይቈቍዕ ። ዕብ ፡ ቃዕቂዕ ፤ ወጋ ፡ በሳ ፡ ነቀለ) ፤ መንቋቋት ፤ ቋ ፡ ቋ ፡ ማለት ፤ ያጥንት ። መጕረብ ፤ ማጕብጕብ ፤ መላጥ ፡ መመለጥ ፤ መብለዝ ፡ መዝጐን ፤ መከክም ፡ መጣመን ፤ የእጅና ፡ የእግር ። መክሳት ፡ መድረቅ ፤ መጣጋት ፤ መጕስቈል ፤ ፊት ፡ መምሰል ፤ የሰውነት ። ይቈቍዕ ፡ ኵሉ ፡ አዕፅምቲሁ ። ቈቍዓ ፡ ወቈስላ ፡ አጻብዒሆሙ ። እፎ ፡ ቈቍዐ ፡ በሐዊረ ፡ ፍኖት ፡ መከየደ ፡ እግርኪ ። ቈቍዐ ፡ ማእሶሙ ፡ ዲበ ፡ አዕፅምቲሆሙ ፡ (ኢዮ፴፫ ፡ ፲፱ ። ድር ፡ መድ ። ደራሲ ። ሰቈ፬ ፡ ፰) ።

**አቈቍዐ** ፤ አንቋቋ ፤ አቈሰለ ፤ አከሳ ፤ አደረቀ ። እከየ ፡ ልቡ ፡ ያቈቍዕ ፡ አዕፅምቲሁ ። ትጋሁ ፡ ሉብዐል ፡ ያቈቍዕ ፡ አዕፅምት ፡ (ሚራ፲፱ ፡ ፱ ። ፴፱ ፡ ፩) ።

**ቃቈር** ፤ (ራት ። ዕብ ፡ ቁርቁር) ፤ እንቍራሪት ፤ ትል ፡ አሙኝት ፤ ሌሊት ፡ የሚጮኽ ፡ የሚንጫጫ ። ወይነቅዉ ፡ ከመ ፡ ቃቈራት ፡ (ገድ ፡ ተክ) ።

**ቃር** ፤ (ዐረ ፡ ቂር ፤ ቃር) ፤ ሙጫ ፤ የዛፍ ፡ ደም ። ቃር ፡ ወፒሳ ፡ ወተይ ፡ (ስንክ ፡ ሐም፳) ።

**ቍር** ፤—ብርድ ፤—ቈሪር ፤—ቈረ ።

**ቀርአ** ፤—ቈረመ ፤ መታ ፤—ቀርዐ ።

**ቍርእ** ፤—በቁሙ ፡ ቍር ፤—ቍርዕ ።

**ቍርአን** ፤ የሕግ ፡ መጽሐፍ ፤ መሐመድ ፡ ለወገኖቹ ፡ የጣፈው ፤ ርሱን ፡ ነቢይ ፡ ሐዋርያ ፡ ብለው ፡ የሚያምኑ ፡ እስላሞች ፡ ከሰማይ ፡ ወርዷል ፡ የሚሉት ። ፍ

ችው ፡ ንባብ ፡ ድጋም ፡ ማለት ፡ ነው ፤ ዋንኛ ፡ ስሙ ፡ ግን ፡ ፋርቃን ፡ ነው ፤ ፈረቀን ፡ እይ ።

**ቀረበ ፤ በት ፤ (ቀርበ ፡ ይቀርብ ፡ ይቅረብ ። ዕብ ፡ ቃሬብ ። ሱር ፡ ቅሬብ ። ዐረ ፡ ቀሪበ)** ፤ መቅረብ ፤ መጠጋት ፤ መድረስ ፡ መንካት ፤ መለጠቅ ፡ መጣበቅ ፡ ልጥፍ ፡ ማለት ፡ እንደ ፡ ሥጋና ፡ እንደ ፡ ቁርበት ፤ ወዳጅ ፡ ዘመድ ፡ ባለሟል ፡ መኾን ። ቅረብ ፡ ዝየ ። ወአልቦ ፡ ዘይክል ፡ ቀሪበ ፡ ኀቤሁ ። ይቀርቡኒ ፡ በክናፍሪሆሙ ። ቦ ፡ ዘመድ ፡ ዘይቀርብ ፡ እምኔየ ፡ (ሔኖ፲፰ ፡ ፩ ። ሃይ ፡ አበ ። ኢሳ፹፱ ፡ ፲፫ ። ሩትኛ ፡ ፲፪) ።

—፤ መቍረብ ፤ ቍርባን ፡ መቀበል ፤ መሳተፍ ። እለ ፡ ኢትቀርቡ ፡ ፃኡ ። ይባእ ፡ ወይትከነስ ፡ ወይቅረብ ። ይቅረቡ ፡ ቍርባነ ። ቅድመ ፡ ይቅረቡ ፡ ጳጳሳት ፡ ወእምድኅሬሁ ፡ ቀሳውስት ፡ (ኪዳ ። ቀሌ ። ፈ ፡ መ ፡ ፩ ፡ ፪ ። ቅዳ) ። ቀርበ ፡ ይቀርብ ፡ ይቅረብ ፡ በማለት ፡ ፈንታ ፡ ቀረበ ፡ ይቈርብ ፡ ይቅርብ ፡ ይላል ፤ የጸበለና ፡ የገረመ ፡ ቤት ፡ ነው ። እለ ፡ ይቈርቡ ፡ ለእግዚ ። እስመ ፡ እሙንቱ ፡ ይቈርቡ ፡ መሥዋዕተ ። እንዘ ፡ ይቈርብ ። አው ፡ ቀረበ ፡ ቍርባኖሙ ፡ (ዘፀ፲፱ ፡ ፳፪ ። ዘሌ፳፩ ፡ ፮ ፡ ፰ ። ኪዳ ። ቢኖ ደ) ። ዳግመኛም ፡ በቀርበና ፡ በቀረበ ፡ ፈንታ ፡ ተቀረበ ፡ ይላል ፤ ስሕተት ፡ ነው ። ለእመ ፡ ፈቀደ ፡ ይትቀረብ ፡ ቍርባነ ። እምዘይትቈረብ ፡ (ፈ ፡ መ ፡ ፲፪ ፡ ፬ ። ፍ ፡ ነ ፡ ፲፮) ። ሦስተኛ ፡ ደግሞ ፡ እንዳማርኛው ፡ ቈረበ ፡ አቍረበ ፡ ይላል ፤ ስሕተት ፡ ነው ፤ አያስኸም ። ለምንት ፡ ኢትቈርቢ ፡ ቍርባነ ፡ አፍርንጅ ፡ (ስንክ ፡ ኅዳ፲፯) ።

**ቀራቢ ፤ (ቢት ፡ ብያን ፡ ያት ፤ ረብት)** ፤ የሚቀርብ ፤ የሚጠጋ ፤ ቀራቢ ፤ ቈራቢ ።

**ቅሩብ ፤ (ባን ፡ ባት ፡ ርብት)** ፤ የቀረበ ፤ የቈረበ ፤ ቅርብ ፤ አጠገብ ፤ ዘመድ ፤ ዐጭር ፤ ጥቂት ። እለ ፡ ቅሩባን ፡ ኀበ ፡ ንጉሥ ። ቅሩብ ፡ ውእቱ ፡ ረኪቦታ ። ዘየኀድር ፡ ቅሩበ ፡ ቤታ ። ለቅሩብ ፡ ምናቤ ፡ ምታ ። እስመ ፡ ቅሩብ ፡ ዘመኑ ። ፍሥሓ ፡ ዝንቱ ፡ ዓለም ፡ ቅሩብ ፡ ወኅዳጥ ፡ (አስቴ፩ ፡ ፲፬ ። ሚራ፶፩ ፡ ፳፮ ። ፲፬ ፡ ፳፬ ። ዮዲ፲፮ ፡ ፳፬ ። ዮሴፍ ። ቀሌ) ።

**ቅርበት** ፤ መቅረብ ፤ አቀራረብ ፤ ቅርቢያ ፤ ቀረቤታ ፤ ቅርብነት ፡ (ቁር ፡ ጸላ) ።

**ቍርበት ፤ (ዐማርኛ)** ፤ በቁሙ ፤ ማእስ ፤ የሥጋ ፡ ልብስ ፤ ሥጋን ፡ ከናጥንቱ ፡ ከኹሮማቱ ፡ ለብስበ ፡ የሚይዝ ፡ የሚገንዝ ።

**ቀርብ ፤ (ዕብ ፡ ቈሬብ)** ፤ ቀርበታ ፤ ውስጥ ፤ ውሳጣዊ ፤ ሆድ ፤ መኻው ፡ ኹለንተናው ፤ በእግርና ፡ በራስ ፡ መካከል ፡ ያለው ፤ የንዋያተ ፡ ውስጥ ፡ ሣጥን ፡ አቅማዳ ። ግራብን ፡ ተመልከት ፤ የዚህ ፡ መንቲያ ፡ ነው ።

**ቍርባን ፤ (ናት ። ዕብ ፡ ቆርባን ። ሱር ፡ ቍርባና ። ዐረ ፡ ቍርባን)** ፤ በቁሙ ፤ መንፈሳዊ ፡ አምኃ ፤ ስለት ፤ መሥዋዕት ፤ መባእ ፤ ለአምላክ ፡ የሚቀርብ ፡ የሚሰጥ ፡ ገንዘብ ፤ ማናቸውም ፡ ኹሉ ። የመሥዋዕትን ፡ ፍች ፡ ተመልከት ። መሥዋዕተ ፡ ወቍርባነ ፡ ኢፈቀድከ ። አምጽኡ ፡ ቍርባኖሙ ፡ ቅድመ ፡ ምሥዋዕ ። መንፈቀ ፡ ለዲድርክም ፡ ቍርባን ፡ ለእግዚ ፡ (መዝ ፡ ፴፱ ። ዘኍ፯ ፡ ፲ ። ዘፀ፴ ፡ ፲፫ ፡ ፲፬) ።

—፤ መሥዋዕተ ፡ ወንጌል ፤ ጥሩ ፡ ስንዴና ፡ ወይን ፤ ከውሃ ፡ በቀር ፡ ሌላ ፡ ቅይጣሬ ፡ የሌለበት ፤ በቍርባንነቱ ፡ ዕሙቅ ፡ ጥልቅ ፡ ረቂቅ ፡ ምስጢር ፡ ያለበት ። በእንተ ፡ ሥርዐተ ፡ ቍርባን ። አኰቴተ ፡ ቍርባን ። አርአዮሙ ፡ ሥርዐተ ፡ ምስጢር ፡ ዘቍርባን ። አንቀጽ ፡ በእንተ ፡ ቍርባን ፤ ወኢያዐርጉ ፡ ላዕለ ፡ ምሥዋዕ ፡ ዘእንበለ ፡ ኅብስተ ፡ ሥርናይ ፡ ንጹሕ ፡ ወማየ ፡ ወይን ፡ ንጹሕ ፡ (ኪዳ ። ቅዳ ። ፍ ፡ ነ ፡ ፲፫) ።

**አቅረበ ፤ (ያቀርብ ፡ ያቈርብ)** ፤ አቀረበ ፤ አስቀረበ ፤ አስጠጋ ፤ አሳጠረ ። አቅርቦ ፡ መሥዋዕተ ። ናቈርብ ፡ ለከ ፡ ዘንተ ፡ ኅብስተ ፡ ወዘንተ ፡ ጽዋዐ ። አቅረቡ ፡ ሎቱ ፡ አምኃሁ ። ጠይቅ ፡ ዘሎ ፡ ዘአቅረቡ ፡ ለከ ። አቅረብክዎሙ ፡ ለቤተ ፡ እስራኤል ፡ ኀቤየ ። ወአቅረብኪ ፡ መዋዕለኪ ፡ (አፈ ፡ ድ፲፬ ። ኩፋ ፡ ፵፪ ። ሚራ ፴፩ ፡ ፲፩ ። ኤር፲፫ ፡ ፲፩ ። ሕዝ፳፪ ፡ ፬) ።

—፤ ማቍረብ ፤ ቍርባን ፡ መስጠት ፤ ማቀበል ። ኢታቅርብዎሙ ። ወያቅርብዎ ፡ ቍርባነ ፡ (ቀሌ ። ፈ ፡ መ ፡ ፬ ፡ ፪) ። በአቅረበ ፡ ፈንታ ፡ አስተቅረበ ፡ ይላል ፤ አንድ ፡ ወገን ፡ ነው ። ዘጠቢብ ፡ በርእሱ ፡ ያስተቈርብ ፡ ርእሶ ፡ (ሚራ፰ ፡ ፲፫) ።

**መቅረቢ ፤ ርብ** ፤ የሚቀርብ ፤ የሚያቀርብ ፤ የሚያስቀርብ ፤ አቅራቢ ። ሎቱ ፡ ናቈርብ ፡ ዘውእቱ ፡ መቅርብ ፡ (ቅዳ ፡ አት) ።

**መቅረብ ፤ (ብት)** ፤ ቀራቢ ፤ ዘመድ ፤ ወዳጅ ። አሐዱ ፡ እምአግዋሪሁ ፡ ወመቅረቡ ፡ (ቢኖ ደ) ።

**ተቃረበ** ፤ በቁሙ ፤ ተቀራረበ ፤ ተጣጋ ፡ ተጠጋጋ ፤ ተሳለፈ ፡ ተስባለፈ ። ኢይትቃረብ ፡ ወኢይኑም ፡ ምስለ ፡ ብእሲቱ ። እለ ፡ ይትቃረቡኒ ። እምተራክቦ ፡ ወተሳምኖ ፡ እንዘ ፡ ይትቃረቡ ። እንበለ ፡ ይትቃረቡ ፡ (ፈ ፡ መ ፡ ፲፬ ፡ ፬ ። መዝ ፡ ፶፬ ። ቄድር ። ማቴ፩ ፡ ፲፰) ። ቀረበ ፤ ቀርበ ፡ በማለት ፡ ፈንታ ፡ ተቃረበ ፡ ይላል ፤ ስሕተት ፡ ነው ። ንፍረት ፡ ተቃርቦ ፡ ለበሲዐ ፡ እክለ ፡ ባዕድ ። አው ፡ ይትቃረብ ፡ ኀበ ፡ ሃይማኖት ፡ ርትዕት ፡ (ሚራ፵፩ ፡ ፲፬ ። ፈ ፡ መ ፡ ፳፯ ፡ ፰) ።

**አስተቃረበ** ፤ አቃረበ ፤ አቀራረበ ። አሌ ፡ ሎሙ ፡ ለእለ ፡ ያስተቃርቡ ፡ ገራህተ ፡ ምስለ ፡ ገራህት ፡ (ኢሳ፭ ፡ ፰ ። ዲድ ፡ ፩) ። አቅረበ ፡ አስተቅረበ ፡ በማለት ፡ ፈንታ ፡ አስተቃረበ ፡ ይላል ፤ ስሕተት ፡ ነው ። ነሥአ ፡ ብእሴ ፡ ወኪያሁ ፡ አስተቃረቦ ፡ ለርእሱ ፡ (ቁር ፡ ጸላ) ።

**ምቅራብ ፤ (ባት)** ፤ መቅረቢያ ፤ ማቅረቢያ ፤ መቃረቢያ ፤ አዳራሽ ፡ ወልወል ፤ አይጸየፍ ። ነበሩ ፡ ውስተ ፡ ምቅራቡ ፡ ወአንበብዋ ፡ ለይእቲ ፡ መጽሐፍ ፡ (ዕዝ፫ ፡ ፲፬) ።

**ምቅራብ፤(ዕብ፡ ሚልቃሐይም)፤** የቀንዲል፡ መኖቀሻ፤ መኩስተሪያ፤ መቀስ። ጽዋዓት፡ ወምቅራብት፡(፪ዜና፡ ፬፡ ፳፪)።

**ቀረብ፤(ብ፡ አቅራብ)፤** የደጋ፡ የቈላ፡ እንቧይ፡ እሾኽም፤ ፍሬው፡ ክብ፡ እንክብል፤ ሎሚ፡ የሚያክክል። ምስክር፡ የለውም፤ ባለሐዲሶች፡ ግን፡(ሉቃ ፲፭፡ ፲፪)፡ ወእመኒ፡ እንቆቅሖ፡ ስእሎ፡ ፀቅራብኑ፡ ይሁብ፡ ያለውን፤ እንቧይ፡ ይሉታል፤ ስሕተት፡ ነው፤ እውነተኛ፡ ፍችው፡ አይደለም። የጽርኡ፡ አብነት፡ ከጽርእም፡ የተቀዳው፡ ኹሉ፤ እመኒ፡ ዓሣ፡ ሰአሎ፡ አርዌ፡ ምድርኑ፡ ይሁቦ፡ ባለው፡ አንጻር፡ ጊንጥ፡ እንደ፡ ማለት፡ በዐይን፡ ፀቅራብኑ፡ ይላል፡ እንጂ፤ እንቧዮች፡ እንደ፡ ማለት፡ በአልፍ፡ አቅራብ፡ አይልም።

**ቀራቢብ፤(ዐረብ)፤** ያልተሰፋ፡ ልብስ፤ ፈርጅ፡ መዳ፡ ጣቃ። ቁማስን፡ እይ፤ ከዚህ፡ ጋራ፡ አንድ፡ ነው።

**ቀርዱ፤** የተፉራ፡ ስም፤ ታላቅ፡ ተራራ፤ ከአራራት፡ ተራሮች፡ አንዱ።

**ቀርድ፤ ቅርድ፤(ዐረ፡ ቂርድ)፤** ዝንጀሮ፤ ጫላዳ፤ ነጯው፡ ጥቍሬው፡(ገድ፡ ተክ)።

**ቀራዲን፤(ናት)፤** ዝንጀሮች፤ ጫላዶች። ሆባይን፡ ተመልከት።

**ቅርዳን፤(ዐረ፡ ጊርደውን)፤** ያይጥ፡ ገመር፤ ታላቅ፡ ዐይጥ፤ ፍልፈል፡(አዋል)።

**ቂራዲስ፤(ጽር፡ ኪራዳስ። ዕብ፡ ቂርሔሬስ)፤** ስመ፡ ሀገር፤ የሞአብ፡ ክፍል፤ ከሞአብ፡ አገሮች፡ አንዲቱ። ዐደወ፡ ቂራዲስ፡(ኤርሚ፳፡ ፴፩። ኢሳ፲፮፡ ፲፩)።

**ቆራሕ፤—ገነት፤—ቀወራህ።**

**ቀርሐ፤ ሐት፤(ቀርሐ፡ ይቄርሕ፡ ይቀርሕ። ዕብ፡ ቃራሕ)፤** መንጨት፤ መላጨት፤ መምለጥ፤ የጠጕር። ይቄርሑ፡ ርእሶሙ፡ በእንቲኣኪ፡ ወይቀንቱ፡ ሠቀ፡(ሕዝ፳፯፡ ፴፩)። በርሐን፡ እይ።

—፤ መጨለጥ፤ ማንቀር፤ የውሃ። ጸወበን፡ ተመልከት፤ የዚህ፡ ወንድም፡ ነው።

(ጥሬ) **ቀራሕ፤** የሚነጭ፤ የሚጨልጥ፤ ጨላጭ፡ አንቃሪ። ልጩ፤ ነጩ፤ ምልጥ፡ መላጣ፤ በራ፤ ቡሓ።

**ቅርሐት፤** ልጭታት፤ ንጭታት፤ በራነት፤ በራ፡ መኾን። እንቃፊ፤ ጫላጭ፡(አዋል)።

**ቃርሐ፤(ዲቃ፡ ግ)፤** አቃረ፤ ተኰሰ፤ ፈላ፤ (ዐማርኛ)።

**ቃርሕ፤** ቃር፤ ትኵሳት፤ የምግብ፡ አለመስማማት።

**ቂራጥ፤(ዐረብ። ጽር፡ ኬራቲዎን)፤** የሚዛን፡ ስም፤ ታናሽ፡ ልክ፤ ክብደቱ፡ አራት፡ የወይራ፡ ፍሬ፡ የሚያኽል፤ ወይም፡ ከዚያ፡ የሚያንስ። የገንዘብ፡ ስም፤ ታናሽ፡ ገንዘብ፤ ፪፡ ሳንቲም፡ ተሩብ፤ ወይም፡ ፪፡ ሳንቲም፡ ብቻ፡ የሚኾን። ጸባሕት፡ ላዕለ፡ ኵሉ፡ ክርስቲያን፡ ለለ፡ ቂራጥ፡ በበ፡ ዓመት። ብእሲ፡ ዘይወቅር፡ አእባነ፡ በቂራጠ፡ ወርቅ፡ ኵሎ፡ ዕለተ። አስተዋፂኦሙ፡ ዘበበ፡ ክልኤቱ፡ ቂራጥ፡(አቡሻ፡ ፶። ስንክ፡ ግንቦ። ሠኔ፲፭)።

**ቅርጥብ፤(ዐረ፡ ቀርፀብ)፤** የሚነክስ፡ የሚገጥ፡ የሚያበላሽ፤ በልዩ፡ የማይጠግብ፤ እንዳይጥ፡ እንደ፡ ምሥጥ፡ ያለ፡ አጥፊ፡ ዘራፊ፡ ሌባ፡ ቀጣፊ። ባለመጽሐፎች፡ ግን፡ ጊንጥ፡ ዳሞትራ፡ ኰሽሽላ፡ ይሉታል። አባ፡ ወቅሪስኒ፡ ሰመዮ፡ አልቅርጥበ፡ እስመ፡ ይነስክ፡ እምዙሉ፡ ገቦ፡(ፊልክ፡ ፶፯)።

**ቀርጣሎን፡ ስ፤(ጽር፡ ከርታሎስ። ዕብ፡ ቃርጢል። ሱር፡ ቃርጣላ። ዐረ፡ ቂርጠለት)፤** ቅርጫት፡ የሪቅ፡ የጕታ፡ ዐይነት፤ የወይን፡ መልቀሚያ፤ ዘለላውን፡ በርሱ፡ እየከተቱ፡ የሚጭኑበት፡ የሚሸከሙበት፤ እንደ፡ ስፌት፡ ብዙ፡ ዐይነት፡ ያለው፤ ጕብ፡ መሶብ፡ እንቅብ፡ አገልግል፡ ቅንብቻ፡ የሚመስል። ከፈርንና፡ መሥየምትን፡ አስፈሬድንና፡ ክረቦን፡ እይ። ትነሥእ፡ እምፍሬ፡ ምድር፡ ወትወዲ፡ ውስተ፡ ቀርጣሎን። ወሤሙ፡ አርእስቲሆሙ፡ ውስተ፡ ቀርጣሎስ፡(ዘዳ፳፮፡ ፪፡ ፬። ፬ነገ፡ ፲፡ ፯)።

**ቀርይ፤ ዮት፤(ቀረየ፡ ይቀሪ፡ ይቅሪ። ዕብ፡ ቃራእ)፤** ማሸረት፡ መጠንቈል፤ አስማት፡ መድገም፤ ጋኔን፡ አሾክሿኪ፡ መጥራት፤ ቅኔ፡ ተመሪ፡ ከባለቅኔው፡ አፍ፡ እየሰማ፡ እንዲጮኽ፤ ወይም፡ እንዳስተርጓሚ፡ ከሾክሿኪው፡ አፍ፡ እየሰሙ፡ ማውራት፡ መለፍለፍ፡ መቀባጠር። ሰምንት፡ ሰረቅሙ፡ ገይበ፡ ብሩር፡ ዘይሰቲ፡ ወይቀሪ፡ ቦቱ፡ እግዚእየ፡(ዘፍ ፵፬፡ ፭)።

—፤ መቅረት፡ መትረፍ፤ ቀሪ፡ ትርፍ፡ ውዝፍ፡ መኾን፡ (ዐማርኛ)።

**ቀራዪ፤(ዪት፡ ይያን፡ ያት)፤** ሻርተኛ፤ አስማት፡ ደጋሚ፤ ጋኔን፡ ጠሪ፤ ባላሾክሿኪ።

**አቅረየ፤** አስሻረተ፤ ጋኔን፡ አስጠራ፤ አስማት፡ አስደገመ።

**አቃረየ፤** መሥዋዕት፡ ሠዋ፤ አቀረበ፤ አምኃ፡ ሰጠ። የእግዜርን፡ ቃል፡ ከነቢይ፡ ከካህን፡ ለመጠየቅ። ኢየአክል፡ ሊባኖስ፡ ለአንድዶ፡ ወኵሉ፡ እንስሳ፡ ለአቃርዮ፡(ኢሳ፵፡ ፲፮)።

**ቀርያሲም፤(ጽር፡ ካሪሲም)፤** ጣዖት፤ ስመ፡ ጣዖት፡(፪ዜና፡ ፴፩፡ ፲፱)።

**ቀሪም፤ሞት፤(ቀረመ፡ ይቀርም፡ ይቅርም። ዐረ፡ ቀረመ። ዕብ፡ ቃራም፤ ቍርበት፡ ሸፈነ፤ ቍርበታም፡ ኾነ)፤** መቃረም፡ መልቀም፤ ካማጅ፡ የቀረውን፡ የወደቀውን፡ እልፍ፡

እንቡጥ ፡ ዘላ ፡ ዘለላ ፡ መማረር ። ሀብኒ ፡ ክፍልየ ፡ እም ዘቀረምኪ ፤ አኀዘት ፡ ትቅርም ፡ (ድር ፡ ሚክ) ። ብዙው ፡ መጽሐፍ ፡ ግን ፡ በቀረመ ፡ ፈንታ ፡ ተቀረመ ፡ ይላል ፤ ስሕተት ፡ ነው ። ትትቈረሞሙ ፡ ዘከመ ፡ ተቀረምከ ፡ ኪያየ ። ተቅራመ ፡ ይትቈረምዎሙ ፡ ከመ ፡ ወይን ፡ ለተረፈ ፡ እስራኤል ። ኢትትቀረም ፡ ሕንባባተ ፡ ወይንከ ፡ (ስቈ፭ ፡ ፳፱ ። ኤር፮ ፡ ፱ ። ዘሌ፲፱ ፡ ፲) ።

**ቀራሚ ፤ (ሚት ፡ ምያን ፡ ያት ፤ ረምት) ፤** የሚቃርም ፤ ቃራሚ ፤ ለቃሚ ። በቀራሚ ፡ ፈንታ ፡ ተቀራሚ ፡ ይላል ፤ ስሕተት ፡ ነው ። ተቀራሚ ፡ በለስ ፡ አነ ፡ (ዓሞ፯ ፡ ፲፫) ።

**ቀርም ፤ (ማት ፤ አቅራም) ፤** በቁሙ ፤ ቃርሚያ ፤ ቅራሚ ፤ ከማጀቱ ፡ የቀረ ፡ ቅሬታ ። (ተረት) ፤ ሰው ፡ እንዳቅሙ ፤ እኽል ፡ እንደ ፡ ቀርሙ ። ወይተርፍ ፡ ቀርሙ ፡ ውስቴቱ ። ዘያስተጋብእ ፡ ቀርመ ፡ በማእረር ፡ (ኢሳ፲፯ ፡ ፮ ። ሚክ፯ ፡ ፩) ። በቀርም ፡ ፈንታ ፡ ቀሪም ፡ ይላል ፤ የጣፊ ፡ ስሕተት ፡ ነው ። ሠዊት ፡ ዘይወድቅ ፡ እምነ ፡ ቀሪሙ ፡ (ኢዮ፳፱ ፡ ፳፱) ።

**ተቀርመ ፤** ተቃረመ ፤ ተለቀመ ፤ እልፉ ፡ እንቡጡ ፡ ዛላው ።

**ቅሩም ፤ (ማን ፡ ማት ፡ ርምት) ፤** የተቃረመ ፤ የተለቀመ ፤ ቃርሞሽ ።

**ተቅራም ፤ (ማት) ፤** ቀርም ፤ ቃርሚያ ። ከመ ፡ ተቅራም ፡ አመ ፡ ቀሥም ። ተቅራመ ፡ ማእረር ። ዐቀብተ ፡ መቃብር ፡ አረሩ ፡ ኅጠተ ፡ ብሩር ፡ ጸዐዳ ፤ ወተቅራመ ፡ ብሩር ፡ መቃብረ ፡ አትረፉ ፡ ለእንግዳ ፡ (ሚክ፯ ፡ ፩ ። ስንክ ፡ መስ፲፩ ። ቅኔ) ።

**ተቃረመ ፤** ተቀራመተ ፤ ተቀረማመተ ፤ የሥጋ ፡ (ዐማርኛ) ።

**ተቃራሚ ፤** የሚቀራመት ፤ ተቀራማች ፤ ዐራጅ ፡ በጋማች ።

**ቅርመት ፤** መቃረም ፤ (ጥቃ) መቃረም ፤ አቀራረም ፤ ቅርሚያ ፡ ለቀማ ።

—፤ መቀራመት ፤ ቅርምቻ ፤ ቀረመት ፤ ቅርምት ፤ አንዱን ፡ ፍሪዳ ፡ ብዙ ፡ ኹኖ ፡ መግዛት ፡ ማረድ ፤ ሥጋውን ፡ ከፋፍሎ ፡ በዕፃ ፡ መውሰድ ።

**ቀርመዝ ፤ (ዐረ ፡ ቂርሚዝ) ፤** ቀይ ፡ ግምጃ ፤ እንድኪ ፡ ጃዊ ። ኳኳን ፡ ተመልከት ፡ (ኢሳ፩ ፡ ፲፰) ።

**ቀርሜሎስ ፤ (ጽር ፡ ከርሚሎን ። ዕብ ፡ ከርሜል) ፤** የተራራ ፡ ስም ፤ ተራራ ፤ በባሕር ፡ ዳር ፡ ያለ ፤ ኤልያስ ፡ የጸለየበት ፡ (፫ነገ ፡ ፲፰ ፡ ፵፪) ።

**ቀሬን ፤ ኖት ፤ (ቀረነ ፡ ይቀርን ፡ ይቅርን ። ዕብ ፡ ቃራን) ፤** (መቀርናት) ፤ ቀንድ ፡ ማብቀል ፡ ማውጣት ፤ ቀንዳም ፡ ቀንደኛ ፡ ባለቀንድ ፡ መኾን ። መውጋት ፡ ማናፈር ፤ በቀንድ ፡ መቈፈር ፤ የበሬ ። ማሰር ፡ ማቈራኘት ፤ ማጣመር ፡ ማቀናጀት ፤ የገበሬ ። ቅራና ፡ ቍራኛ ፡ ማለት ፡ የዚህ ፡ ዘር ፡ ነው ። ቀንድ ፡ መምሰል ፤ ቀንድ ፡ መኾን ፤ ቀንድ ፡ መባል ፤ ያገር ፡ ቀንድ ፡ እንዲሉ ። ማየል ፡ መበርታት ፤ መንገሥ ፡ መሠልጠን ፤ በላይ ፡ መኾን ። ቈንደየን ፡ ተመልከት ።

**ቀራኒ ፤ መቅርን ፤ (ብ ፡ መቃርንት) ፤** ቀንዳም ፡ የሚወጋ ፡ የሚቃወም ፤ ጠላት ፡ ደመኛ ፡ ወደረኛ ። እስመ ፡ እሉ ፡ እለ ፡ ይነሥኡ ፡ ርዴ ፡ መቃርንቲሁ ፡ ለእግዚ ፡ (ዲድ ፡ ፳፩) ።

**ቀርን ፤ (ብ ፡ አቅርንት ። ዕብ ፡ ቄሬን ። ሱር ፡ ቃርና ። ዐረ ፡ ቀርን) ፤** ቀንድ ፤ ጥኑ ፡ ጠንካራ ፡ ደረቅ ፤ እንደ ፡ ዐጽቅ ፡ ኹኖ ፡ በእንስሳት ፡ ራስ ፡ የሚወጣ ፤ የሚያድግ ፡ የሚረዝም ፤ ጠማማ ፡ ቈልማማ ። የቀንድ ፡ መጣሪያ ፤ ቱልቱላ ፡ ዋንጫ ፤ የቀንድ ፡ ዐይነት ፡ ቀንድ ፡ የሚመስል ፤ ቀንዳ ፡ መለከት ፤ የዝኆን ፡ ጥርስ ፡ የመሰለው ፡ ኹሉ ። አ ፡ ላሕም ፡ ዘኢይትኄየል ፡ በቀርኑ ። ክቡዳነ ፡ አቅርንት ። ንፍኁ ፡ ቀርነ ። ቀርነ ፡ ዝብጦ ። ቀርነ ፡ ነጌ ። ቀርነ ፡ ቅብዕ ። ንፍንተ ፡ ቀርን ። ቃለ ፡ ቀርን ፡ (ቅዳ ። መዝ ፡ ፵፱ ። ፹ ። ፺፮ ። ዓሞ፫ ፡ ፲፭ ። ፩ነገ ፡ ፲፮ ፡ ፩ ። ፩ተሰ ፡ ፬ ፡ ፲፮ ። ኢሳ፲፰ ፡ ፫) ። ባለቅኔዎች ፡ ግን ፡ ነጋሪት ፡ ይሉታል ፤ ፍችው ፡ አይደለም ። ኢትንፍኁ ፡ ቀርነ ፡ ዘእንበለ ፡ በሆሳዕና ፡ (ድጓ) ። ጥፍርም ፡ የጣት ፡ ቀንድ ፡ ይባላል ። ሰባም ፡ ለአጽፋረ ፡ እግርኪ ፡ አቅርንተ ፡ አዳብዕ ፡ ዐሠርቱ ፡ (ደራሲ) ።

ቀርን ፡

—፤ ጮራ ፡ ምዕዛር ፡ የፀሐይ ፡ እግር ፤ ለጋ ፡ ጨረቃ ፤ ማእዝን ። ቀርነ ፡ ወርኅ ። እስክንድር ፡ ይሰመይ ፡ ዘክልኤ ፡ አቅርንቲሁ ፤ እስመ ፡ ውእቱ ፡ ነግሠ ፡ በአቅርንተ ፡ ፀሓይ ፡ እምሥራቂሃ ፡ እስከ ፡ ምዕራቢሃ ፡ (አዋል ። አቡሻ ፡ ፵፰) ።

—፤ ኀይል ፤ ጽንዕ ፤ ሥልጣን ፤ ንጉሥ ፡ መስፍን ። አበቍል ፡ ቀርነ ፡ ለዳዊት ። ወያሌዕል ፡ ቀርነ ፡ መሲሑ ። አንሥአ ፡ ለነ ፡ ቀርነ ፡ መድኀኒት ። ይእቲ ፡ አሚረ ፡ ይበቍል ፡ ቀርን ፡ ለቤተ ፡ እስራኤል ። ተሰብረ ፡ ቀርነ ፡ ሞአብ ፡ (መዝ ፡ ፻፴፩ ። ፩ነገ ፡ ፪ ፡ ፲ ። ሉቃ፩ ፡ ፷፱ ። ሕዝ፳፱ ፡ ፳፩ ። ኤር፵፩ ፡ ፳፭) ። ዘአሐዱ ፡ ቀርኑ ፤ አውራሪሥ ። ቀርነ ፡ ኀብስት ፤ ቍርማሚ ፡ ሾለቅ ፡ (መዝ ፡ ፳፩ ። ሕዝ፲፫ ፡ ፲፱) ።

**አቅረነ ፤** አቀረና ፤ ቀንድ ፡ አስመሰለ ፤ ቀንዳም ፡ አደረገ ፤ አስወጋ ።

**ተቃረነ ፤** ተዋጋ ፤ ተተማተመ ፤ ተቀራሸመ ፤ ተጣላ ፡ ተቃወመ ፤ ተከራከረ ፤ የሰው ፡ የእንስሳ ። ተገሐሡ ፡

እምዝሉ ፡ ዘይትቃረን ፡ ተቃርኖ ፡ ምስለ ፡ ሕግ ። ቀዳሚ ፡ ዘይትቃረኒክ ፡ ተቃረኒ ፡ ምስሌነ ። ይትቃረኑ ፡ ምስለ ፡ ዝሉ ፡ ሰብእ ፡ (ዲድ ፡ ፴፫ ። ቀሌ ። ፩ተሰ ፡ ፪ ፡ ፲፭) ።

**ተቃራኒ** ፤ (ኒት ፡ ንያን ፡ ያት) ፤ ተዋጊ ፤ ተጣይ ፤ ወደረኛ ፤ ባለጋራ ። ዲያብሎስ ፡ ተቃራኔ ። ዝሉ ፡ ሕሡም ፡ ተቃራኒሁ ፡ ለሠናይ ። እስመ ፡ ፈውሰ ፡ ዝሉ ፡ ኀጢአት ፡ ይደሉ ፡ ከመ ፡ ይኩን ፡ ተቃራኔ ፡ ለኀጢአት ። ፀር ፡ ተቃራንያን ፡ (ስንክ ፡ ኅዳ፳፯ ። ፈላስ ። ፈ ፡ መ ፡ ፫ ፡ ፫ ። ጥበ፲፰ ፡ ፯) ።

**አስተቃረነ** ፤ አዋጋ ፤ አጣላ ፤ አከራከረ ፤ አወዳደረ ።

**መስተቃርን** ፤ (ንት ፡ ናን ፡ ናት) ፤ የሚያጣላ ፤ አጣይ ። የሚጠላ ፤ ተጣይ ፤ ባለጋራ ። ወእመሰ ፡ ተቃወመኒ ፡ መስተቃርን ። ዲያሁ ፡ ለመስተቃርን ። ዘይከውን ፡ መስተቃርነ ፡ ለዝንቱ ፡ (አፈ ፡ ተ፴፭ ። ማር ፡ ይሥሐ ፡ ፫ ። ስንክ ፡ መጋ፫) ።

**ቀርንብ** ፤ (ዐረ ፡ አርንብ ። ሱር ፡ አርንባ ። ዕብ ፡ አርኔቤት) ፤ ጥንቸል ፤ ሥርዋ ፡ እንደ ፡ ቀንድ ፡ የኾነ ፤ ቀንድ ፡ የሚመስል ፤ ረዝሙም ፤ ማር ፡ የምትበላ ፤ የምታመስኲ ፡ ያዝኮ ፡ ወገን ።

**ቀርንብ** ፤ (ብ ፡ ቀራንብት) ፤ ቅርንው ፤ ቀርናዊ ፤ ምርቅ ፡ ቂንድ ። ቅንድብ ፤ ሽፋሽፍት ፤ ከሽፋል ፡ በታች ፡ ያለው ፡ ያይን ፡ መክደኛ ፤ ከንፈሩ ፡ ላዩና ፡ ታቹ ። ቅንድብ ፡ ቍርበቱ ፡ ላንቃው ፤ ሽፋሽፍቱ ፡ ጠጕሩ ፡ ጠፈቃው ፡ ምርቁ ፡ እንደ ፡ ቀንድ ፡ ኹኖ ፡ የበቀለው ፤ አፍሬው ፡ ወደ ፡ ላይ ፡ ወደ ፡ ታች ፡ ያቆተለው ። ቂጽለ ፡ ወብርዐ ፡ ወሐሠረ ፡ ወቀርንበ ፤ ምርቅ ፡ ቂንድ ፡ (መቃ ፡ ፲፭) ። ሰላም ፡ ለቀራንብቲከ ፡ ከመ ፡ ክልኤ ፡ ከንፈ ፡ ኪሩብ ፤ እለ ፡ ይጼልላ ፡ ወትረ ፡ አዕይንቲከ ፡ ዘርግብ ። ጸጕረ ፡ ቀራንብቲሁ ። ነበስባስ ፡ ቀራንብት ። ወቀራንብቲሁኒ ፡ የሐተ ፡ ለዕጓለ ፡ መሕያው ። ቀራንብት ፡ ኀቤሁ ፡ ለዐይን ፡ እንዘ ፡ ቅሩባን ፤ ቀራንብተ ፡ ኢይኔጽር ፡ ዐይነ ፡ (ደራሲ ። ስንክ ፡ ግንቦ፲፫ ። መጽ ፡ ምስ ። መዝ ፡ ፲ ። ቅኔ) ። ሽፋልም ፡ ከሽፋሽፍት ፡ ጋራ ፡ ባንድነት ፡ ቅንድብ ፡ ይባላል ። ዕብራይስጡ ፡ ከንፈር ፡ ከናፍር ፡ ሲል ፤ ላፋ ፡ ስፋታይም ፡ ስፋቶት ፡ ይላልና ፤ ሽፋሽፍት ፡ ከዚህ ፡ ወጥቷል ፤ ፍችው ፡ ከንፈራዊ ፡ ሥዐርተ ፡ ከንፈር ፡ ማለት ፡ ነው ፤ ለአፍም ፡ ይኾናል ፤ ጽሕምን ፡ ተመልከት ። ሽፋልም ፡ የዕብራይስጥ ፡ ነው ፤ (ሻፋል) ፡ ፀጒር ፡ ቀጭን ፡ ኰሳሳ ፡ ደከማ ፡ ልም ፡ ልዝብ ፡ ማለት ፡ ነው ፤ የጠጕሩን ፡ ጠባይ ፡ ባሕርያዊ ፡ ሕጉን ፡ አለማደጉን ፡ ያሳያል ።

**ቀርነው** ፤ ቀርነለው ፤ ቀርናዊ ፤ ቀርን ፡ ላዊ ፤ ቀንዳም ፡ ቀንደ ፡ ቂልማማ ፤ ላዊን ፡ እይ ።

—፤ ቀርን ፡ ቅብዕ ፡ ወይም ፡ ቅብዐ ፡ ቀርን ። ከሌዊና ፡ ከይሁዳ ፡ ወገን ፡ ካህንና ፡ ንጉሥ ፡ የሚቀቡት ። ባለቅኔዎች ፡ ግን ፡ ሽቱ ፡ ይሉታል ፡ (ጥፊ ፡ ሰዋ) ።

**ቀሬናዊ** ፤ (ሱር ፡ ቁርያና ። ዐረ ፡ ቀሪይ) ፤ ቍርጩ ፡ ድኻ ፤ ባለጊ ፤ ባላገር ። እፎ ፡ እትለአክ ፡ ለዝንቱ ፡ ቀሬናዊ ፡ (ፍ ፡ ነ ፡ ፲) ።

**ቀሬናዊ** ፤ (ቀሬን ፤ ቄሬን ፤ ስመ ፡ ሀገር) ፤ የቀሬን ፡ ሰው ፡ አገሩ ፡ ቀሬን ፡ የሚባል ፤ የማብጽ ፡ አውራጃ ፤ የልብያ ፡ ቅርብ ፡ አጠገብ ። ብእሲ ፡ ቀሬናዊ ፡ ዘስሙ ፡ ስምዖን ፡ (ማቴ፳፯ ፡ ፴፪) ።

**ቀራንዮ** ፤ (ጽር ፡ ክራኒዮ) ፤ ርእሳዊ ፤ ድማኃዊ ፤ መካን ፡ ድማኅ ። ጎልጎታ ፡ ዘበትርጓሜሁ ፡ ቀራንዮ ፡ (ማቴ፳፯ ፡ ፴፫ ። ማር፲፭ ፡ ፳፪ ። ዮሐ፲፱ ፡ ፲፯) ። ድማኅንና ፡ ጎልጎታን ፡ እይ ።

**ቀርኔን** ፤ ቀሬን ፡ ስመ ፡ ሀገር ። ወእለሂ ፡ እምቀርኔን ፡ (ግብ፪ ፡ ፲) ።

**ቄርኔን** ፤ ቂሬን ፡ (ጽር ፡ ክሬኒ ። ዕብ ፡ ብሬክ) ፤ ዥሬ ፡ የውሃ ፡ መቋሚያ ፤ ጕድጓዳ ፡ ስፍራ ፡ (፪ነገ ፡ ፪ ፡ ፲፫ ። ፩ነገ ፡ ፳ ፡ ፳) ።

**ቄርኔን** ፤ (ጽር ፡ ከሬኒ ። ዕብ ፡ ሐዳሽ) ፤ ሐዲስ ፡ መማሪያ ፤ የጦር ፡ ልብስ ። ባለብሉዮች ፡ ግን ፡ ለይተው ፡ ቋዝመን ፡ ይሉታል ፤ ይኸውም ፡ እንደ ፡ ጩቤ ፡ ያለ ፡ ጋሻዎች ፡ የሚታጠቁት ፡ ታናሽ ፡ ካራ ፡ ነው ፡ (፪ነገ ፡ ፳፩ ፡ ፲፯) ።

**ቀርነናእ** ፤ (ዕብ ፡ ቅርናን) ፤ ቀንዳም ፡ ትል ፤ ተሳቦ ፤ ዝጕል ፡ ልብሱ ፤ ቀንዱ ፡ ብርንደ ፡ የኾነ ፤ ልሕሉሕ ፤ ልጋጋም ። ሐለዚዝንና ፡ ናእትን ፡ ተመልከት ።

**ቈርነናዕ** ፤ ናዓት ፤ (ዕብ ፤ ጽፋርዴዕ ። ዐረ ፡ ፀፋዲዕ ። ሱር ፡ ዑርድዓናያ) ፤ ጓጕንቸር ፤ እንቍራሪት ። ጪኺ ፡ አቅራሪ ፡ ጩፋፊ ፡ ነጩሬ ፡ ማለት ፡ ነው ፤ ቃቄርን ፡ እይ ። ይቀይእ ፡ ተከዚ ፡ ቈርነናዓተ ፡ (ዘፀ፰ ፡ ፪—፲፫) ።


ቀርነናእ ፡


ቈርነናዕ ፡

**ቀሪዕ** ፤ ዖት ፤ (ቀርዐ ፡ ይቀርዕ ፡ ይቅራዕ ። ዐረ ፡ ቀረዐ ። ዕብ ፡ ቃራዕ ፤ ቀደደ) ፤ ኰሪዕ ፤ መቍሬት ፡ መቈረም ፤ መኰርኰም ፡ መምታት ፤ ራስን ፡ በበትር ፡ ቋ ፡ ኳ ፡ ከሽ ፡ ማድረግ ። ኰርዐን ፡ ተመልከት ፡ የዚህ ፡ መንትያ ፡ ነው ።

**መቅርዕ** ፤ (ብ ፡ መቃርዕ ። ዐረ ፡ ሚቅረዐት) ፤ መቍሪያ ፤ መቈረሚያ ፡ በትር ፤ የራስጌ ፡ ዱላ ፤ ወይም ፡ የራስ ፡ በሽታ ፤ የራስ ፡ ምታት ። በቅሥፈት ፡ መቃርዕ ፡ (አቡሻ ፡ ፶) ።

**ቍርዕ** ፤ (ዓት) ፤ የራስ ፡ ቍር ፤ በርበርቲ ፤ የብረት ፡ ቆብ ፤ ጌራ ፡ (አዋል) ።

**ቀሪፍ፤ ፎት፤** (ቀረፈ፡ ይቀርፍ፡ ይቅርፍ። ዐረ፡ ቀለፈ። ሱር፡ ቅላፍ)፤ መቅረፍ፤ መላጥ። ቈለፈን፡ እይ፤ ስና፡ ረ፡ ተወራርሰዋል፤ ቀረፈ፡ ፀማርኛ፡ ነው። ቀረፈ፡ ሠሎ፡ ቅርፍት። ቅርፍ፡ ጸሕፀ፡ ዘንጢአት፡(ጥበ፲፫፡ ፲፩። ደራሲ)።

**ቅራፍ፤** (ፋት)፤ ቅራፊ፤ ልጥ። ሔልባዐ፡ ፈወሰ፡ በጣፀመ፡ ጼው፡ ማየ፡ ኢያሪኮ፡ ሕሙመ፤ ወበቅራፈ፡ ዕፀ፡ አውፀአ፡ ማሕጼ፡ ስጡመ፡(በንከ፡ ጥቅ፳)።

**ቅርፍት፤** (ታት)፤ በቁሙ፤ ቅርፊት፤ ልጥ፤ እንቡጥ፤ ቂንድ፤ ገለባ፡ ንፋሽ፤ ቍርበት፡ ጕለፊት። ቅርፍት፡ ዕፀ። ቅርፍት፡ ኅብስት። ቅርፍት፡ ሮማን። ቅርፍት፡ ተርሙስ። ቅርፍት፡ ሥጋ፡(፱ካ፡ ፯፡ ፯። እዋል። ማሕ፱፡ ፫። ስንክ፡ የካ፳፱። ቅዳ፡ ያዕ። ሕዝ፳፱፡ ፬)።

**ቋረፈ፤** ቈረፈ፤ ቈራረፈ፤ ቈራረጠ፤ በጣጠሰ። ይቋርፍ፡ አራዊት፡(እዋል)።

**ቋርፍ፤** የዋልድባች፡ ምግብ፤ ሥራሥር፤ እንደ፡ ድንችና፡ እንደ፡ ሽንኵርት፡ የሚላጥ፤ የሚቀረፍ።

**ቈሪፍ፤** (ዐማርኛ)፤ ጕፈማ፤ ጕፈም፤ ጕሮው፡ ታላላቅ፡ የኾነ፤ ከልክ፡ ያለፈ። ቀርፋፋ፡ ከርፋፋ፡ ማለት፡ ከዚህ፡ የወጣ፡ ነው።

**ቀሪጽ፤ ጾት፤** (ቀረጸ፡ ይቀርጽ፡ ይቅርጽ። ዐረ፡ ቀረጸ። ዕብ፡ ሐራጽ)፤ መቅረጥ፡ ማነጥ፤ ማንጠጥ፤ ምስል፡ መሥራት፤ መልክ፡ ማውጣት፡ ማስጌጥ፤ መብጣት፡ መክተፍ፡ መተፍተፍ። በዕፀ፡ ብንጺን፡ በስሌዳ፡ እብን፡ መጣፍ፡ መፈደል፤ መንደፍ፡ መፈልፈል፤ ፊደሉን፡ ማስመጥ፡ ወይም፡ ማሳበጥ። ለሠሎሙ፡ አሕዛብ፡ ሀለዎሙ፡ ምግባራት፡ ዘልማድ፡ ዘትሜኒ፡ በንቤሆሙ፤ ወቦ፡ ዘትከውን፡ ኀሳረ፡ በኀበ፡ ካልኣኒሆ፡ ከመ፡ ቀሪጸ፡ ገጽ፡ በኀበ፡ ኢትዮጵያ፡ ወኖባ፤ ወከመ፡ ተላጽዮ፡ ጽሕም፡ በኀበ፡ አፍርንጅ። ወረከበ፡ መጽሐፈ፡ ዘቀረጹ፡ ቀደምት፡ ውስተ፡ ኰኵሕ፡(ፍ፡ ነ፡ ፶፩። ኩፋ፡ ፰)።

**ተቀርጸ፤** ተቀረጠ፤ ተነጠጠ፤ ተጣፈ፡ ተነደፈ። ናሁ፡ ተአዘዘ፡ ወተቀርጸ። ወከመ፡ ዝ፡ ተጽሕፈ፡ ወተቀርጸ፡ በእንቲኣሁ። በንበተ፡ አይሁድ፡ እንተ፡ ተቀርጸት፡ በጽላተ፡ በማይ። ወሀበ፡ ሙሴ፡ በሰሌዳተ፡ አብላቅ፡ እለ፡ ተቀርጻ፡ በሆህያተ፡ ዕብራይስጢ፡(ኩፋ፡ ፲፯። ፳፱። መጽ፡ ምስ)።

**ቅሩጽ፤** (ጻን፡ ጻት፡ ርጽት)፤ የተቀረጠ፤ የተጣፈ፤ ያበጠ፡ የሰመጠ፤ መልክ፡ ያለው። ወረከብናሁ፡ ለበትር፡ ጽሑበ፡ በንባብ፡ ወቅሩጸ፡ በትርጓሜ፡ (ቅኔ። ሃይ፡ አበ፡ ሳዊ)።

**ቅርጸት፤** መቅረጽ፤ መቀረጽ፤ አቀራረጽ፤ ቅርጽ፤ ጥሬት፤ የፊደል፡ መልክ፤ እጅ፡ እግር፤ ኀርመት፡ ቅንጣት። ወጸሐፉ፡ ባፀሌሁ፡ በቅርጸት፡ ማኅተም። የውጣ፡ እንተ፡ አሐቲ፡ ቅርጸታ፡ (ዘፀ፴፯፡ ፴፱። ማቴ፳፡ ፲፰። ቀሌ)።

**ቀረፀ፤** (ዐረ፡ ቀረፀ። ሱር፡ ቅራጥ)፤ ቀረጠ፤ ቀረጥ፡ ተቀበለ፡ (ዐማርኛ)። ቈረጠ፤ ሸለተ፤ ላጨ፤ ከረከመ፤ የሕዋስ፡ የጠጕር፡ የጥፍር። ቀረፀ፡ እዝኖ፡ ዘፀጋም። ኢትቅርፀ፡ እምኔከ፡ አባለ፡ ዘርዕ። ኢይደሉ፡ እምድኅረ፡ ተመጥዎ፡ ቍርባን፤ ቀሪፀ፡ አጽፋር፡ ወተላጽዮ፡ ጸጕር። ኢይቅርፀ፡ ጽፈሪሁ። ኢታንኅ፡ ሥዕርተ፡ ርእስከ፡ ዳእሙ፡ ቅርፀ። ሖረ፡ ኀበ፡ ይቀርፀ፡ አበግዒሁ። ከመ፡ በግዐ፡ ዘኢይነብብ፡ በቅድመ፡ ዘይቀርፆ። እምነ፡ ቀዳሚ፡ ዘቀረፅኩ፡(ፊልክ፡ ፯። ፱፻፴። ቅዳ። ቄድር። ዲድ፡ ፩። ዘፍ፴፩፡ ፲፱። ኢሳ፶፫፡ ፯። ጦቢ፩፡ ፯)።

**ቀራፂ፤** (ፂት፡ ፅያን፡ ያት)፤ የሚቈርጥ፤ ቈራጭ፤ ቀራጭ፤ ሸላች፤ ላጭታ። ጸውዐት፡ ቀራፄ፡ ወቀረፀቶ። መላጼ፡ ቀራፂ፡(መሳ፲፮፡ ፲፱። ሕዝ፭፡ ፩)።

**አቅረፀ፤** አስቈረጠ፤ አስቀረጠ፤ ቀረጥ፡ አስጠ፡ አስቀበለ። አቀረጠ፤ ቀረጥ፡ ሰጠ።

**መቅረፅ፤** (ብ፡ መቃርፅ። ዐረ፡ ሚቅራፅ)፤ መቅረጫት፤ መቍረጫ፤ መላጫ፤ መቀስ፡ ምላጭ፤ የመሰለው፡ ኹሉ። ይቤሎ፡ ሰረድአ፡ ሀበኒ፡ መጥባሕተ፡ አው፡ መቅረፀ፡ ወመተረ፡ ባቲ፡ ልሳኖ፡ (ስንክ፡ ጳጕ፭)። ሙዳየ፡ ዔረግ፡ በማለት፡ ፈንታ፡ መቅረፅ፡ እንደ፡ ማለት፡ ቈረፅ፡ ይቈርፅ፡ ይላል፤ የተሳሳተ፡ ነው፡ (ዓሞ፰፡ ፩)።

**ተቀርፀ፤** (ተቀረጠ)፤ ተቈረጠ፤ ተሸለተ። እስከ፡ ተቀርፀ፡ ሥጋሁ። መራዕይ፡ እለ፡ ተቀርፃ። ተቀርፆ፡ ሥዕርት። አልቦ፡ ዘይትቀረፀ፡ ርእሶ፡ ዘእንበለ፡ ያእምር፡ አባስ፡(ስንክ፡ ግን፳፰። ማሕ፬፡ ፪። ስንክ፡ ሐም፳፩። ሥር፡ ጳኰ)።

**ቅሩፅ፤** (ፃን፡ ፃት፡ ፅት)፤ የተቈረጠ፤ ቍርጥ፡ ሽልት። ድኅረ፡ ወድቀ፡ መልዐልተ፡ ምድር፡ ርእሱ፡ ቅሩፀ። መራዕይ፡ ቅሩፃት፡(ስንክ፡ ሚያ፲፰። ደራሲ)።

**ቀረፅ፤** በቁሙ፤ ቀረጥ፤ ነጋዴ፡ ለመንግሥት፡ የሚያቀርጠው፡ ገንዘብ። ስሙ፡ ዕፅ።

**ቀርቀር፤** (ዕብ፡ ቃርቆር)፤ ስሙ፡ ሀገር፤ ከዮርዳኖስ፡ ማዶ፡ ያለ። ባለብሉዮች፡ ግን፡ ገዎቻ፡ ቋጥኝ፡ ይሉታል፡ (መሳ፰፡ ፲)።

**ቈርቋር፤ ሮት፤** (ቈርቈረ፡ ይቈረቍር፡ ይቈርቍር። ዐረ፡ ቀርቀረ። ዕብ፡ ቃርቄር)፤ መቈርቈር፤ መቀብቀብ፤ የጥሬ፤ ቃሕቅሕን፡ ተመልከት። መሬኸ፡ ማስከከት፤ ቍርቍሩ፡ ማለት፤ የደሮ፡ የንቍራሪት፤ ቃቈርንና፡ ቈርነናፀን፡ እይ፤ ዘሩ፡ ቈሪር፡ ቈረ፡ ነው።

—፤ በቁሙ፡ መቈርቈር፤ መጕርበጥ፡ አለመመቸት፤ ማሳዘን፡ ማስቈጣት። የሐዘንን፡ ፍች፡ ተመልከት። መመ

ሥረት ፤ መዠመር ፤ ለማቅናት ፡ ለመሥራት ፤ ያገር ፡ የከተማ ፡ (ዐማርኛ) ።

**ተቈርቈረ** ፤ በቁሙ ፤ ተቍረቍረ ፤ ዐዘነ ፤ ተቈጣ ፤ ተናወጠ ፤ ተንቀጠቀጠ ፤ ከሐዘን ፡ ከቍጣ ፡ የተነሣ ። ተመሠረተ ፡ ተዠመረ ፤ ሀገሩ ፡ ከተማው ።

**ቍርቁር** ፤ የተቈረቈረ ፤ ያዘነ ፡ የተቈጣ ፡ ቍጡ ።

**ቍርቍር** ፤ ቍርቈራ ፡ ሐዘን ፤ ቍጣ ፡ ብስጭት ፤ ክርክር ፡ ሙግት ፤ ጩኸት ፡ ፍጅት ። ኢንፌር ፤ ካሕድ ፤ ቍርቍር ፤ መዐት ፤ ሁከት ፡ (ኪዳ) ።

**አንቈርቈረ** ፤ (ዐማርኛ) ፤ አንቈረቈረ ፤ ተንቈረቈረ ፤ የውሃ ፡ የጥሬ ፤ ለዜማም ፡ ይኾናል ።

**ቈርቈሮ** ፤ በቁሙ ፤ ጪኺ ፤ ፈሳሽ ።

**ቈረቈር** ፤ በቁሙ ፤ ነጭ ፡ የራስ ፡ ቋቍቻ ። (ተረት) ፤ በቡሓ ፡ ላይ ፡ ቈረቈር ።

**ቀርቂስ** ፤ (ዕብ ፡ ቃርቃሽ ፤ ሻኩራ ፡ የቃጭል ፡ ቍላ) ፤ መክን ፤ ተውኔት ፤ ብዙ ፡ ዐይነት ፡ ሥጋዊ ፡ ጨዋታ ፡ ያለበት ። ለእመ ፡ ኮነ ፡ አሐዱ ፡ ዘየሐውር ፡ ኀበ ፡ ቀርቂስ ፤ ለይኅድግ ፡ አው ፡ ለይሰደድ ፡ (መጽ ፡ ቄስ ፡ ፳፯) ።

—፤ ገበጣ ፤ ሰንጠረዥ ። ካህን ፡ ዘአዝለፈ ፡ ተዋንዮ ፡ ቀርቂስ ፡ (ፍ ፡ ነ ፡ ፱) ።

**ቀርቂሳዊ** ፤ ገበጣ ፡ ዐዋቂ ፤ ተጫዋች ። ቀርቂሳዊ ፡ ዘይትዋነይ ፡ ቀርቂሰ ፡ (መጽ ፡ ቄስ ፡ ፳፱) ።

**ቂርቆስ** ፤ የሰው ፡ ስም ፤ ሰማዕት ፤ ከነናቱ ፡ እሳት ፡ የገባ ፤ አንጌቤንን ፡ እይ ። ቂርቆስ ፡ ሕንቀቅሖ ፡ ተሠርዐ ፡ ምስለ ፡ እሙ ፡ (ቅኔ ። ስንክ ፡ ጥር ፲፭ ። ሐም ፲፱) ።

**ቈሪር** ፤ ሮት ፤ (ቈረ ፡ ይቈርር ፡ ይቍርር ። ዕብ ፡ ቃራር ። ሱር ፡ ቃር ። ዐረ ፡ ቀረ) ፤ መቍረር ፤ መብረድ ፤ መቀዝቀዝ ፤ ከሙቀት ፡ መለየት ፤ በረድ ፡ ቀዝቃዛ ፡ መኾን ። ወናሁ ፡ አብርሃም ፡ ቈረ ፡ ከመ ፡ በረድ ፡ (ኩፋ ፡ ፳፫) ። ተመይጠ ፡ ተፈጸመ ፡ በማለት ፡ ፈንታ ፡ ቈረ ፡ ይላል ፤ የመላሽ ፡ ስሕተት ፡ ነው ። እስከ ፡ ይቈርር ፡ መዐተ ፡ እጉከ ፡ (ዘፍ ፳፯ ፡ ፵፬ ። ኢዮ ፲፩ ፡ ፲፫ ። ኢሳ ፭ ፡ ፳፱ ። ፲ ፡ ፳፭) ።

**ቈሪር** ፤ (ራን ፡ ራት ፡ ራር) ፤ የቈረረ ፤ የቀዘቀዘ ፤ ቀዝቃዛ ፤ በራዳ ። ነፋስ ፡ ቈሪር ። ማይ ፡ ቈሪር ። ፀሓይ ፡ ጥዒና ፡ ቈሪራን ፡ አዝርዕት ። ቈራር ፡ ወሙስንት ፡ ምክር ፡ (ሚራግ፫ ፡ ፳ ። ምሳ፳፭ ፡ ፳፭ ። ስንክ ፡ ሐም፲፪ ። ቄር ፡ ጸላ) ።

**ቍረት** ፤ በቁሙ ፤ መቀዝቀዝ ፤ መብረድ ፤ አቀዛቀዝ ፤ አበራረድ ። ቅዝቃዜ ፤ ብርድ ፤ ቈፈን ። ቍረቲ ፡ ቶሳሔ ፡ ዘርዕ ። ቍረተ ፡ ሥጋሁ ፡ ኢያጥፍኦ ፡ ለእሳተ ፡ መለኮቱ ። ቍረተ ፡ ኅሊና ፡ (ፈ ፡ መ ፡ ፲፪ ፡ ፭ ። ያዕ ፡ ዘእል ። አርጋ ፡ ፱) ።

**ቍር** ፤ በቁሙ ፤ ብርድ ፤ ቈፈን ፤ ቅዝቃዜ ። ይመውት ፡ በቍር ። ይርዕዱ ፡ በእንተ ፡ ቍር ፤ እስመ ፡ ክረምት ፡ ውእቱ ። ቍር ፡ ወበረድ ። እስመ ፡ ብዙኅ ፡ ቍራ ፡ ለይእቲ ፡ ሌሊት ፡ (ኢዮ፴፮ ፡ ፲፰ ። ፩ዕዝ ፡ ፱ ፡ ፮ ። ዘካ፲፱ ፡ ፮ ። ዮሐ፲፰ ፡ ፲፰) ።

**አቍረረ** ፤ አቀዘቀዘ ፤ አስቀዘቀዘ ፤ አበረደ ፤ አስበረደ ፤ አስታገሠ ። ሰትየ ፡ ማይ ፡ ያቈርር ፡ ላህበ ፡ ጽምእ ። ዝናም ፡ ያቈርሮ ፡ ለመርቄ ። አቍረረ ፡ ሙቀቶ ። አቍርር ፡ መዐተከ ፡ (አፈ ፡ ተ፪ ። ሚራ፲፰ ፡ ፲፯ ። ፊልክ ፡ ፶ ። ዘፀ፴፪ ፡ ፲፪) ።

—፤ አቀረረ ፤ ቀዳ ፤ ጨመረ ፤ አንቈረቈረ ፤ ባፉ ፡ ወይም ፡ በሌላ ። አቍረሩ ፡ ማየ ፡ በመንፈ ፡ ወኢቱክዕወ ፡ ማይ ። ኢያቍርርዎ ፡ ወኢይክዕውዎ ፡ ቍርባኖ ፡ በኀብስት ፡ እምቅድመ ፡ ሠርሖት ፡ (ገድ ፡ ዘሚ ። ፍ ፡ ነ ፡ ፲፫) ።

**መቍረሪ** ፤ (ሪት ፡ ርያን ፡ ያት) ፤ የሚያበርድ ፤ አብራጅ ፤ አቀዝቃዥ ።

**መቍረር** ፤ ርት ፤ ማቍረሪያ ፤ ማብረጃ ፤ ማቀዝቀዣ ፤ ማቅረሪያ ፤ ማንቈርቈሪያ ፤ ኰስኰስት ፤ ጡታም ፡ ብርት ፤ ልሕኵት ። ማየ ፡ መቍረር ፤ የኰስኰስት ፡ ውሃ ፤ የቅዳሴ ፡ ጠበል ። ወማየ ፡ መቍረርኒ ፡ ኢይንጥብ ፡ ምንትኒ ፡ እምአፍ ፡ (ፍ ፡ ነ ፡ ፲፫) ።

**አስቈረረ** ፤ (ተቀ ፡ ግ) ፤ አስጠየፈ ፤ አሸቈረረ ፤ አስጠያፊ ፡ ኾነ ፤ ለሌላው ። ተጠየፈ ፤ ተሸቈረረ ፤ ተጠያፊ ፡ ኾነ ፤ ጠላ ፡ ተሰቀቀ ፤ እንደ ፡ ርኩስ ፡ አየ ፤ ሌላውን ። ብእሴ ፡ ደም ፡ ወጕሕላዌ ፡ ያስቈርር ፡ እግዚ ። ታስቈርር ፡ ጣዖተ ። ጸሊአቶ ፡ ወአስቈርሮቶ ፡ (መዝ ፡ ፭ ። ሮሜ፪ ፡ ፳፪ ። ዮሴፍ) ።

**መስቈርር** ፤ (ርት ፡ ራን ፡ ራት) ፤ የሚያስጠይፍ ፡ አስጠያፊ ፤ አስቀያሚ ። የሚጠየፍ ፡ ተጠያፊ ፡ ተቀያሚ ፤ ተሰቃቂ ። አሕላማት ፡ መስቈርርት ፤ አስጠያፊ ፡ (ፊልክ ፡ ፻፳፱) ።

**ስቍሩር** ፤ የተጠላ ፡ የተነቀፈ ፤ የረከሰ ፡ ያስጡየፈ ። የተጠየፈ ፤ ሸቍራራ ፤ ጥይፍተኛ ። አክአብ ፡ ንጉሥ ፡ ወብእሲቱ ፡ ስቍርርት ፤ አስጠያፊ ፡ (ስንክ ፡ ጥር፯) ።

**ሰቈራር** ፤ (ቅጽልና ፡ ጥሬ) ፤ የሚያስጠይፍ ፤ የሚያስቅቅ ፤ ከባድ ፤ ግም ፤ ጽሉእ ፤ ርኩስ ፤ ቅጽል ። ጥይፍታ ፤ ስቅቅታ ፤ አልየው ፡ አልሰማው ፡ ማለት ፤ ጥሬ ። ሰቈራረ ፡ ኮንክሙኒ ። ገበርክምዎ ፡ ለጼናነ ፡ ሰቈራረ ። ሰቈራረ ፡ ነፍሱ ። ኢኮነ ፡ ሰቈራረ ፡ ሰብሳብ ፡ ዘበሕግ ፤ ቅጽል ፡ (ኢሳ፭ ፡ ፲፬ ። ዘፀ፭ ፡ ፳፩ ። ምሳ፯ ፡ ፲፯ ። ዲድ ፡ ፴፫) ። ግስንቱ ፡ ዲቃላና ፡ ቅጥይ ፡ ስለ ፡ ኾነ ፡ መንገድ ፡ ሊወጣል ፤ መስቈርርና ፡ አስቈራሪ ፤ ሰቈራርና ፡ ስቍሩር ፡ አንዳንድ ፡ ወገን ፡ ናቸው ።

**ቃሩራ** ፤ (ዐረ ፡ ቃሩረት ። ትግ ፡ ቈራረት) ፤ በቁሙ ፤ ቅዛዝ ፤ ጠርሙዝ ፤ የብርሌ ፡ የብርጭቆ ፡ ዐይነት ፤ ሥራው ፡ ቈሪር ፡ ውሃ ፡ የኾነ ፤ ከብረት ፡ ከልሕኵት ፡ ያይደለ ፡ (ዮሴፍ) ።

**ቆሮስ** ፤—መስፈሪያ ፤—ቀወሮስ ።

**ቅራስያ** ፤—(ዐረ ፡ እልቅራስያ) ፤ ፅፅ ፤

ፍሬ ፡ ዕፅ ፤ ፍሬነቱ ፡ እንደ ፡ እንኰይ ፡ ያለ ፤ ታናናሽ ፤ ፀጥነታም ፡ (ፍ ፡ ነ ፡ ፲፯) ።

**ቀስ ፤—ቄስ ፤—ቀሲስ ፡ ቀሰ ።**

**ቃስ ፤ (ዐረ ፡ ቂያስ ፤ ልክ ፤ መለኪያ) ፤** ገላ ፤ የገላ ፡ ልብስ ፤ ሱሪ ፡ ቀሚስ ፤ ልከኛ ፤ በልክ ፡ የተብፋ ፤ ረዘሙ ፡ ዐጠረ ፡ የማይሉት ፤ ድርማንቅ ። ልብሰ ፡ ቃስ ፡ (ዘፀ፳፰ ፡ ፴፱ ። ዘሌ፲፮ ፡ ፬) ።

—፤ የላይ ፡ ልብስ ፤ ጀባ ፡ ካባ ፡ መጐናጠፊያ ። ዘይትሞጣሕ ፡ ቃስ ። አስኬማ ፤ ልብሰ ፡ ቃስ ፡ አኮ ፡ ለአሮን ፡ ሰርጐ ፡ ዘባኑ ፡ (ደራሲ) ።

**ቄስጤ ፤—ቄሽት ፡ ጨጓራ ፤—ቀሠጠ ።**

**ቍስጥ ፤ (ዐረ ፡ ቁስጥ ። ዕብ ፡ ቆሽጥ) ፤** ሽቱ ፤ የሽቱ ፡ ስም ። ባለቅኔዎች ፡ ቀበርቾ ፡ ይሉታል ። ዝክረ ፡ ስምኪ ፡ ሐዋዝ ፡ እምነ ፡ ከልበኔ ፡ ወቍስጥ ፡ ወእምነ ፡ ሰንበልት ፡ ምዑዝ ፡ (ደራሲ) ።

**ቄስያ ፤ ያት ፤ (ዐረ ፡ ቁሽአ ። ዕብ ፡ ቂሹእ) ፤** የቅል ፡ የዱባ ፡ ወገን ፤ ያበሬ ፡ ያንኰሏ ፡ የሽክና ፡ ዐይነት ፤ ሞላላ ፤ ወጥ ፡ የሚኾን ፤ የሚቀቀል ፡ ቶሎ ፡ የሚበስል ፡ (ዘኍ፲፩ ፡ ፭) ። ባለብሉዮች ፡ ግን ፡ ቄሽት ፤ የበለስ ፡ ቋንጣ ፡ ይሉታል ።

**ቄሲል ፤ ሎት ፤ (ቄስለ ፡ ይቄስል ፡ ይቍሰል ። ዕብ ፡ ካሻል ፡ ተሰናከለ) ፤** መቍሰል ፤ መነካት ፤ መመታት ፤ ቍስለኛ ፡ ቍስላም ፡ መኾን ፤ በደዌ ፡ በበትር ፡ በሥራ ፡ በሐዘን ። አነ ፡ ጠቢብ ፡ ወእፈውሰሙ ፡ ለድዉያን ፡ እለ ፡ ቄስሉ ፡ በደዌ ። ቄሰልኩ ፡ በቤተ ፡ ዐርክየ ። ወናሁ ፡ አበዊነ ፡ ቄስሉ ፡ በኀጺን ፡ (ስንክ ፡ ግንቦ፳ ። ዘካ፲፫ ፡ ፮ ። ፪ዜና ፡ ፳፱ ፡ ፱) ።

**ቍሱል ፤ (ላን ፡ ላት ፡ ስልት) ፤** የቈሰለ ፤ የተነካ ፤ ንክ ፤ ውጋ ፤ ምት ። ቍሱላነ ፡ ልብ ፡ (ኢሳ፶፯ ፡ ፲፭ ። ፳፭ ፡ ፭) ።

**ቍስለት ፤** መቍሰል ፤ አቈሳሰል ፤ ቍስልነት ። ድካም ፤ ሐዘን ፤ ጭቅጭቅ ፡ (ዐማርኛ)

**ቍስል ፤ (ላት ፤ ቍሰል) ፤** በቁሙ ፤ የተነካ ፡ ገላ ፤ ደዌ ፡ በትር ፡ ያረፈበት ፤ ግርፋት ፡ ውግታት ፤ መከራ ፤ ቂም ፤ ሐዘን ፤ ኀጢአት ። ከመ ፡ ይትፈወስ ፡ እምቍስል ፡ ዘአቍሰልዎ ። ቍስለ ፡ ሕዝቡ ። እመ ፡ ብ ፡ ቍስል ፡ ከመ ፡ ቍስልየ ። ቍስለ ፡ ሞት ፤ (የሚገድል ፤ ለሞት ፡ የሚያበቃ) ። እምዙሉ ፡ ቍስል ፡ የአኪ ፡ ቍስለ ፡ ልብ ። ወቍስለ ፡ አማዑት ፡ (፪ዜና ፡ ፳፪ ፡ ፮ ። ኢሳ፴ ፡ ፳፮ ። ሰቈ፭ ፡ ፲፪ ። ራእ፲፫ ፡ ፫ ። ሚራ፳፭ ፡ ፲፫ ። ፍ ፡ ነ ፡ ፶) ።

**አቍሰለ ፤** አቈሰለ ፤ አስቈሰለ ፡ አሳዘነ ። ነደፍዎ ፡ ወአቍሰልዎ ። ትፍሥሕትከ ፡ ያቈስሎሙ ፡ ለጸላእትከ ። አነ ፡ አቍሰልኩ ፡ ነፍስየ ፡ (፪ዜና ፡ ፳፪ ፡ ፭ ። ሚራ፲፪ ፡ ፳ ። ዮሴፍ) ።

**አቍሳሊ ፤ መቍሰሊ ፤ (ሊት ፡ ልያን ፡ ያት) ፤** የሚያቈስል ፤ የሚያስቈስል ፤ አቍሳይ ፤ አስቈሳይ ፤ አሳዛኝ ፡ አስቀያሚ ። ትካዝ ፡ መቍሰሌ ፡ ልብ ፡ ውእቱ ፡ በከመ ፡ ደዌ ፡ ያቈስል ፡ ሥጋ ፡ (ፈላስ) ።

**ቀሰመ ፤—ለቀመ ፤—ቀሚም ፡ ቀሠመ ።**

(ጥስ) **ቀስሞ ፤ ሞት ፤ (ቀሰመ ፡ ይቄስም ፡ ይቀስም ። አው ፡ ቀሲም ፤ ቀሰመ ፡ ይቀስም ፡ ይቅስም ። ዐረ ፡ ቀሰመ ፤ ከፈለ) ፤** ማጣፈጥ ፡ ማጣፋፈጥ ፤ መመጠን ፤ መቀመም ፤ ሰብሰቦ ፡ ማዋሐድ ፤ ማዘመድ ፤ ለማጣፈጥ ። በምንት ፡ ይቄስምዎ ። ለቀሲመ ፡ ልሳንየ ፡ (ማር፱ ፡ ፵ ። አርጋ) ። ሲጠብቅ ፡ የቀደሰ ፤ ሲላላ ፡ የቀተለ ፡ ቤት ፡ ነው ፤ ስለዚህ ፡ በ፪ ፡ ይኼዳል ።

**ቀሳሚ ፤ (ሚት ፡ ምያን ፡ ያት) ፤** የሚያጣፍጥ ፡ አጣፋጭ ፤ ቀማሚ ፤ ወጥ ፡ ቤት ።

**መቅስም ፤ መቅሰም ፤ (ብ ፡ መቃስም ፤ ማት) ፤** ማጣፈጫ ፤ ጨው ፤ ቅመም ፤ እንደ ፡ ማር ፡ ከብዙ ፡ ተቀሥሞ ፡ አንድ ፡ የኾን ፤ ብዙ ፡ ዐይነት ፡ ወጥ ፤ በብዙ ፡ ቅመም ፡ የተሠራ ፤ ሽታውና ፡ ጣዕሙ ፡ ልብ ፡ የሚመሥጥ ፤ እጅ ፡ የሚያስመጥጥ ። ይትዐቀብ ፡ እመቃስማተ ፡ መብልዕ ፡ ወመስቴ ። እመ ፡ ቦ ፡ ዘጥዕመ ፡ ዘኮነ ፡ እመቃስማት ። ይኅድግ ፡ ኵሎ ፡ መቃስማተ ። ኢይብልዑ ፡ መቃስማተ ፡ (ቄድር ። ፍ ፡ ነ ፡ ፲፭) ።

**ቀስም ፤** ቅመም ፤ ቀመመን ፤ ጣዕም ፤ ጥፍጥነት ፤ አጠፋፈጥ ፤ የቅመም ፡ የወጥ ። ዘእንበለ ፡ ቀስም ። ወኢይብላዕ ፡ ቀስመ ፡ (ቀሌ ። ቄድር) ።

**ተቀስመ ፤ ተቀሰመ ፤** ተጣፈጠ ፤ ተቀመመ ። በምንት ፡ ይትቄሰም ፡ (ማቴ፭ ፡ ፲፫) ።

(ላ ፡ ጥ) **ቅሱም ፤ (ማን ፡ ማት ፡ ስምት) ፤** የተጣፈጠ ፤ ጥፍጥ ፤ ቅምም ። ነገሩ ፡ ቅሱም ፡ በጼው ፡ መሰኮት ። ተግማጽ ፡ ጥዑም ፡ ወዜና ፡ ቅሱም ፡ ከመ ፡ ጼው ። ቅሱም ፡ ማእድ ፡ (ድጓ ። ፈላስ ። ስንክ ፡ ጥር፲) ።

**ቅሳሜ ፤** ማጣፈጥ ፤ መጣፈጥ ፤ መቀመም ፤ አቀማመም ፤ ቅመማ ፤ ቅመምነት ። እምጽቡር ፡ ብሒባሒከ ፡ ወእምኔሁ ፡ ቅሳሜነ ፡ (ኢዮ፴፫ ፡ ፮) ።

(ላ) **ቀሰመ ፤ (ዕብ ፡ ቃሰም ። ሱር ፡ ቅሳም) ፤** አሟረተ ፤ ጠነቈለ ፤ ገመተ ፡ መላ ፡ ጣለ ። መጽሐፍ ፡ ግን ፡ በቀሰመ ፡ ፈንታ ፡ አስተቃሰመ ፡ ይላል ፤ አድራጊውን ፡ ባደራራጊ ፤ የመላሽ ፡ ስሕተት ፡ ነው ። በከመ ፡ ሐሰበ ፡ ወአስተቃሰመ ፡ ለአማስኖቶሙ ። አስተቃስሚ ፡ ሊተ ፡ (አስቴ፱ ፡ ፳፬ ። ፩ነገ ፡ ፳፰ ፡ ፰) ።

**አቅሰመ ፤ አስተቅሰመ ፤** አስሟረተ ፤ አስጠነቈለ ፤ መላ ፡ አስመታ ፤ ጨሌ ፡ ጠጠር ፡ አስጣለ ።

**አቅሳሚ ፤ መቅሰሚ ፤** አስጠንቋይ ፤ ጠንቋይ ፡ ጠያቂ ።

**መቅስም ፤ (ምት ፡ ማን ፡ ማት) ፤** ጠንቋይ ፤ ሟርተኛ ፤ መለኛ ፤ ነቢየ ፡ ሐሰት ። በመቅስም ፡ ፈንታ ፡ መስተቃስም ፡ ይላል ፤ አያሰኝም ። መስተቃስማን ፡ (አርጋ ፡ ፫ ። ቀሌ ። ገድ ፡ ተክ) ። መስተቅስም ፡ ቢል ፡ ግን ፡ አስጠንቋይ ፡ ያሰኛል ፤ ከአስተቅሰመ ፡ ይሰማማል ።

**መቅሰምት ፤ (ብ ፡ መቃስምት) ፤** የሕ ርት ፡ መማሪያ ፤ በየስሙና ፡ በያይነቱ ። ወነሥኡ ፡ መቃ ስምቲሆሙ ፡ ምስሌሆሙ ፡ (ዘኍ ፴፱ ፡ ፯) ።

**ምቅሳም ፤ (ማት) ፤** ማሕረቻ ፤ መጠንቈ ያና ፡ ማስጠንቈያ ፤ ቦታ ።

**ቀስም ፤ ቅስም ፤ (ማት) ፤** ሕርት ፤ ጥን ቈላ ፤ ነቢብ ፡ ግምት ፤ መላ ፤ ትንቢተ ፡ ሐሰት ። መጽሐፍ ፡ ግን ፡ በቀስም ፡ ፈንታ ፡ መቅስም ፡ መቅሰም ፡ መቃስም ፡ ይላል ፤ ኹሉም ፡ ስሕተት ፡ ነው ፤ አያሰኝም ። ሰብአ ፡ መቅስም ። በሰዐም ፡ ዘመቅስም ። ሕልም ፡ ወሰ ገል ፡ ወመቃስም ፡ ከንቱ ፡ ኵሉሙ ፡ (፩ነገ ፡ ፮ ፡ ፪ ። ኢያ፲፫ ፡ ፳፪ ። ሢራ፴፩ ፡ ፭) ።

**አስተቃሰመ ፤ (አደራረጊ) ፤** አጠናቈለ ፤ አጠንቃቈለ ፤ መላ ፡ አማታ ።

**መስተቃስም ፤** የሚያጠናቊል ፤ አጠናቋይ ፤ አጠንቋቋይ ።

**ቅስና ፤—ቄስነት ፤—ቀሲስ ፡ ቀሰ ።**

**ቄስቄስ ፤ (ብ ፡ ቄሳቍስ ፤ ሳት) ፤** የቤት ፡ ዕቃ ፤ ታናናሽ ፤ ሰባራ ፡ ሥንጥር ፤ ደጅ ፡ አፍ ፡ የመለሰው ፡ ማጀት ፡ የጕረሠው ፤ ማናቸውም ፡ ኹሉ ፤ በየስሙና ፡ በያይነቱ ። ኵሉ ፡ ንዋየ ፡ ወቄስቄሰ ፡ ማኅበረኩ ። ውብ ዙኅ ፡ ቄሳቍሳተ ። ወቄሳቍሳቲሁኒ ። ወበህየ ፡ ርኢኩ ፡ ዕፀወ ፡ ኵነኔ ፡ ፈድፋደ ፡ ቄስቄሰ ፡ መዐዛ ፡ (መቃ ። ገድ ፡ ተክ ። ዘፍ፴፩ ፡ ፲፰ ። ሔኖ፳፱ ፡ ፱) ። ቄስቄስ ፤ ቀሰ ቀሰ ፡ ማለት ፡ ከዚህ ፡ የወጣ ፡ ነው ። ቀና ፡ ክ ፡ ተወራራ ሾች ፡ ስለ ፡ ኾኑ ፤ በቄሳቍስ ፡ ፈንታ ፡ ኵሳዥስ ፡ ይላል ። ቈራታተ ፡ ወኵሳዝሳተ ፡ ወአጽሕልተ ፡ (ዲድ ፡ ፴፩) ።

**ቄሳር ፤—ስመ ፡ ንጉሥ ፤—ቀይሳር ።**

**ቀሲስ ፤ ሶት ፤ (ቀሰ ፤ ቀሰሰ ፡ ይቀስስ ፡ ይቅስስ ። ዕብ ፡ ቅሻሽ ። ሱር ፡ ቃሽ) ፤** ማር ጀት ፤ መሸምገል ፤ መቈሸሽ ፤ ቈሻሻ ፡ መኾን ፤ ቈሻሻ ፡ መልቀም ፤ ማጋበስ ፡ መሰብሰብ ። መቅሰስ ፤ ካህን ፡ ቄስ ፡ መኾን ፤ ቅስና ፡ መሾም ። ምሥዋዒሆሙ ፡ በኀበ ፡ ቀ ሲሱ ፡ ወዛቅኑ ፡ (ቀኖ ፡ ኒቅ ፡ ፸፱) ።

**ቀሲስ ፤ (ዐረ ፡ ቀሲስ ። ሱር ፡ ቃሺሻ) ፤** ቄስ ፤ ካህን ፤ ሽማግሌ ። ቀሲስ ፡ ወዲያቆን ። እምነ ፡ ቀሲስ ፡ (ቅዳ ። ፪ዮሐ ፡ ፩) ።

**ቀስ ፤ ቀይስ ፤ (ትግ ፡ ቀሽ) ፤** ዝኒ ፡ ከማሁ ፤ ቀሲስ ። አባ ፡ ገሪማ ፡ ቀስ ፡ ዘመደራ ። ወይቤልዎ ፡ ቀስ ፡ ወመኳንንት ፡ ለአባ ፡ ሊባኖስ ። ለእመ ፡ ብረቀ ፡ አክሊሮስ ፡ ዘውእቱ ፡ ቀይስ ፡ ገበዝ ፡ ንዋያተ ፡ ምሥ ዋዕ ፡ (መዋሥ ። ፈ ፡ መ ፡ ፲፯ ፡ ፯) ።

**ቀሲሳን ፤ ቀሳውስት ፤** ቄሶች ፤ ቀሳውስ ቶች ። ትሚም ፡ ቀሲሳን ። ይጸውዕ ፡ ቀሳውስተ ፡ (ቲቶ ፩ ፡ ፭ ። ያዕ፭ ፡ ፲፬) ። ኤጲስቆጶስ ፡ በማለት ፡ ፈንታ ፡ ቀሲስ ፡ ይላል ፤ የመላሽ ፡ ስሕተት ፡ ነው ። ምስለ ፡ ቀሳ ውስት ፡ ወዲያቆናት ፡ (ፊልጵ፩ ፡ ፩) ።

**ቅስና ፤** ቄስነት ፤ ቄስ ፡ መኾን ፤ የቄስ ፡ ማዕ ርግ ፤ የሹመቱ ፡ ስም ። ዘተሠይመ ፡ ሢመተ ፡ ቅስና ። ይነሥእ ፡ ሢመተ ፡ ቅስና ፡ በሕልያን ፡ (ፈ ፡ መ ፡ ፯ ፡ ፫ ። ፍ ፡ ነ ፡ ፯ ፡ ፳) ።

**አቅሰሰ ፤** አቀሰሰ ፤ አስቀሰሰ ፤ ቅስና ፡ ሾመ ፤ አሾመ ፤ ቄስ ፡ አደረገ ፤ አስደረገ ።

**ቀስት ፤ (ዕብ ፡ ቄሼት ። ሱር ፡ ቂሽታ ። ዐረ ፡ ቀውስ) ፤** በቊሙ ፤ ደጋን ፤ ጕባባ ፤ ጕባጣ ፤ የጦር ፡ መሣሪያ ። ቀስት ፡ ጠዋይ ። ቀስተ ፡ ብርት ፤ ቀስተ ፡ ደመና ። ቀስተ ፡ እግዚአብሔር ፡ (ሆሴ፯ ፡ ፲፮ ። መዝ ፡ ፲፯ ። ሕዝ፩ ፡ ፳፰ ። ኩፋ ፡ ፮) ።



ቀስት ፡

**ቀስተወ ፤** ቀስተ ፤ ቀስት ፡ ሠራ ፤ ቀስት ፡ አኵ መሰለ ፤ አጕበጠ ። ዐለበ ፤ ደገነ ፤ ሳበ ፡ ለጠጠ ፤ ነደፈ ፤ ፍላጻውን ፡ በቀስት ። ወቦአ ፡ ወቀስተወ ፡ ፍጽመ ፤ ኢ ዮአብ ፡ (፩ዜና ፡ ፲፩ ፡ ፯) ።

**ቀስታዊ ፤** ቀስት ፡ ሠሪ ፤ ቀስተኛ ፡ ባለቀስት ፤ ነዳፊ ፤ ወርዋሪ ።

**ቀስታም ፤ (ማት) ፤** መንደርቆ ፡ በትር ፤ ጕ መድ ፤ ዱላ ፤ ከቀስት ፡ ጋራ ፡ የሚያዝ ። በቀስታመ ፡ ኀ ይሉ ፡ አድከሞ ፡ ለአርዌ ፡ ርኩስ ። በትርከ ፡ ወቀስታ ምከ ። ገሠጽኮ ፡ ለዮናስ ፡ በቀስታመ ፡ ባሕር ፡ (ድጓ ። መዝ ፡ ፳፪ ። ቅኔ) ።



ቀስታም ፡

**ቀታ ፤ (ዐረ ፡ ቂሻእ) ፤** ቊስያ ፤ የዱባ ፡ ወገን ። እልቀታ ፡ ወሐምሐም ፡ (ፍ ፡ ነ ፡ ፲፯) ።

**ቀቲው ፤ ዎት ፤ (ቀተወ ፡ ይቀቱ ፡ ይ ቅቱ ። ዐረ ፡ ወቀተ ፤ ጊዜ ፡ ወሰነ) ፤** መገበር ፤ ግብር ፡ መስጠት ፤ ገባር ፡ ተገዥ ፡ መኾን ። ጋላ ፡ በሬ ፡ ገበሬ ፡ ቢል ፤ ቆቲዮ ፡ ቆቱ ፡ የሚለው ፡ ከዚህ ፡ ይስማ ማል ። መቈታቸት ፤ ቍትቻ ፡ ማድረግ ፤ መወራረድ ፤ የቍትቻን ፡ ዕዳ ፡ ውርርድን ፤ መክፈል ። በቀተወ ፡ ፈንታ ፡ ቀተተ ፡ ይልና ፤ ጥሬውን ፡ ደግሞ ፡ ቀቶት ፡ እንደ ፡ ማ ለት ፡ ቀተት ፡ ይላል ፤ የመላሽና ፡ የጣፊ ፡ ስሕተት ፡ ነው ። ከመ ፡ ይግበር ፡ ቀተተ ፡ ምስሌሁ ። ወእለ ፡ ይበትዩ ፡ በቀተት ፡ (ዳን፲፩ ፡ ፯ ። ፍ ፡ ነ ፡ ፲፩) ።

**ቀቶት ፤** ገባርነት ፤ ግብር ። ቍትቻ ፤ ውርርድ ፤ ውሽንብር ፤ የማጉስ ፡ የቍትቻ ፡ ዕዳ ፤ የውርርድ ፡ ገን ዘብ ። በእንተ ፡ ከመ ፡ ኢመፍትው ፡ ይበትዩ ፡ በቀ ተት ፡ አስተዋዲአሙ ። ወአንበሩ ፡ ቀተተ ፡ በዝንቱ ፡ (ቀኖ ፡ ሎዶ ፡ ፶፩ ። ገድ ፡ ተክ) ።

**አቅተወ ፤** አስገበረ ፤ ገባር ፡ አደረገ ፤ አስጨነቀ ። አቈታቸ ፤ አወራረደ ፤ ቍትቻ ፡ አስከፈለ ። ሚጡ ፡ በችረ ፡ እለ ፡ ይትፌደዩ ፡ ወዐለውዎሙ ፡ ለእለ ፡ ያቀትዉ ። እፎ ፡ ተስዕረ ፡ ዘያቀቱ ። አልቦ ፡ ምንትኒ ፡ ዘያቀት ውዎ ፤ አስገበረ ፡ (ኢሳ፲ ፡ ፬ ። ፲፬ ፡ ፬ ። ዘዳ፳፱ ፡ ፳፩) ።

**ቀቲል ፤ ሎት ፤ (ቀተለ ፡ ይቀትል ፡ ይቅትል ። ዕብ ፡ ቃጣል ። ሱር ፡ ቅጣል ። ዐረ ፡ ቀተለ) ፤** መግደል ፤ መውጋት ፡ ማቍሰል ፤ መቍረጥ ፤ ማጥፋት ፤ ማድከም ፡ መጕዳት ። ይመክሩ ፡ ለቀቲል ። ቀተለ ፡ ርእሶ ፡ ለሊሁ ። ዕፄ ፡ ቀተሎ ፡ ለዝኩ ፡ ሐም ሐም ። በጾም ፡ ሰብእናሆሙ ፡ ቀተሉ ፡ (ኢሳ፶፱ ፡ ፯ ። ዮሴፍ ። ዮናፀ ፡ ፯ ። ድጓ) ።

**ቀታሊ ፤ (ሊት ፡ ልያን ፡ ያት ፤ ተልት) ፤** የሚገድል ፤ ገዳይ ፤ አጥፊ ። ቀታሌ ፡ ነፍስ ። ኮነተኒ ፡ ቀታሊተ ። ኖሎት ፡ ቀታልያን ። ቀተልተ ፡ አበዊሆሙ ፡ (ሚራ፲፩ ፡ ፳፭ ። ሮሜ፯ ፡ ፲ ። ኤር፳፫ ፡ ፩ ። ፩ጢሞ ፡ ፩ ፡ ፱) ። በቅቱል ፡ ፈንታ ፡ ቀታሊ ፡ ይባል ፤ በሕተት ፡ ነው ። ኢትግበርዋ ፡ ቀታሊተ ፡ ለምድርክሙ ፡ (ዘኍ፴፭ ፡ ፴፫) ።

**ቀትል ፤ (ላት) ፤** ግድያ ፤ ሰልፍ ፤ ውጊት ፤ ጦርነት ። ቀትል ፡ በመጥባሕት ። ገብሩ ፡ ቀትለ ። ጸብእ ፡ ወቀትል ። በሕገ ፡ ቀትል ። ቀትላት ፡ በይጣናት ፡ (ዮሴፍ ። ፩ዜና ፡ ፲ ፡ ፩ ። ያዕ፬ ፡ ፩ ። ዮዲ፯ ፡ ፲፩ ። ፊልክ) ።

**መቅትል ፤ ተል ፤ (ብ ፡ መቃትል) ፤** መግደያ ፤ መግሪያ ። ገዳይ ፤ ባለመግሪያ ።

**ምቅታል ፤ (ላት) ፤** መግደያ ፤ መገደያ ፤ ማስገደያ ፡ ቦታ ። መልዕልተ ፡ ምቅታል ፡ (፪ነገ ፡ ፭ ፡ ፳) ።

**አቅተለ ፤** አስገደለ ፤ አስፈጀ ። በአቅትሎትከ ፡ ጽኑዓኒነ ፡ (ዮሴፍ) ።

**ተቀትለ ፤** ተገደለ ፤ ሞተ ፤ ተመታ ፤ ታረደ ፤ ተወጋ ፡ ቈሰለ ፤ ጠፋ ፡ ተበላሸ ፤ ረከሰ ። ረሰይከነ ፡ ለተቀትሎ ። ተቀትለት ፡ ሀገር ። እስመ ፡ ተቀተልከ ። ወተቀትለት ፡ ምድር ፡ በደም ፡ (ጦቢ፫ ፡ ፬ ። ሕዝ፴፫ ፡ ፳፩ ። ራእ፭ ፡ ፱ ። መዝ ፡ ፻፭) ።

**ቅቱል ፤ (ላን ፡ ላት ፤ ትልት) ፤** በሰው ፡ እጅ ፡ የሞተ ፡ የተገደለ ፤ የተወጋ ፤ የቈሰለ ፡ ቍስለኛ ፤ ግዳይ ፡ ሬሳ ። ወለእመ ፡ ተረክበ ፡ ቅቱል ፡ በውስተ ፡ ምድር ። ቅቱላን ፡ በኲናት ፡ (ዘዳ፳፩ ፡ ፩ ። ዕዝ፪ ፡ ፲፱) ። ዕጉት ፡ በማለት ፡ ፈንታ ፡ ቅቱል ፡ ይባል ፤ በሕተት ፡ ነው ። ሀገር ፡ ትልት ፡ (ኢሳ፩ ፡ ፯) ።

**ቅትለት ፤ (ታት) ፤** መግደል ፤ መገደል ፤ አገዳደል ፤ ግድያ ፤ ትግል ፡ ትግያ ፤ ጦርነት ። ወኢነሰሑ ፡ ዓዲ ፡ እምነ ፡ ቅትለቶሙ ። ዜና ፡ ቅትለቱ ፡ ለአልዓዛር ፡ ካህን ። ስፍጠታተ ፡ ሰይጣን ፡ ልባዊት ፤ ወቅትለታቲሁ ፡ ኅቡኣት ፡ (ራእ፱ ፡ ፳፩ ። ዮሴፍ ። ፊልክ ፡ ፱) ።

**ተቃተለ ፤** ተጋደለ ፤ ተገዳደለ ፤ ተዋጋ ፤ ተባለፈ ፤ ተጋጠመ ። ይጓልሑ ፡ በበይናቲሆሙ ፡ ወይትቃተሉ ። ይትቃተልዎ ፡ ለይሁዳ ። ተቃተሉ ፡ ለመንክስ ፡ ኅሊና ፡ ዝሙት ። ንትቃተል ፡ ክልኤነ ፡ በባሕቲትነ ፡ (ማቴ ፳፬ ፡ ፲ ። ኢሳ፱ ፡ ፳፩ ። ገድ ፡ ዳን ። ፩ነገ ፡ ፲፯ ፡ ፲) ።

**አስተቃተለ ፤** አጋደለ ፤ አገዳደለ ፤ አዋጋ ፡ አጣላ ፤ አፋጀ ፡ አሜረሰ ፤ አስተጣጠቀ ። ብዙኃነ ፡ አዕርክተ ፡ አስተቃተለ ። ከመ ፡ ያስተቃትሎሙ ፡ በኀጺን ፡ ወበረ ንብ ፡ (ሚራ፳፰ ፡ ፲፫ ። ራእ፯ ፡ ፰) ።

**መስተቃትል ፤ (ልት ፡ ላን ፡ ላት) ፤** የሚጋደል ፤ የሚያጋድል ፤ አጋዳይ ፡ አገዳዳይ ፤ ተጋዳይ ፤ ዐርበኛ ፤ ተዋጊ ፡ ሰልፈኛ ። ብእሲ ፡ መስተቃትል ፡ ወተባዐ ። እዴክ ፡ መስተቃትልት ፡ ወመዋኢት ። ሕዝብ ፡ መስ ተቃትላን ፡ (ሚራ፳፯ ፡ ፳፰ ። ጥበ፲ ፡ ፳ ። ኢሳ፲፫ ፡ ፬) ።

**ምስትቅታል ፤** መገደያ ፤ መገዳደያ ፤ ማገዳ ደያ ፤ ቦታ ።

(ጥ) **ቀትሮ ፤ ሮት ፤ (ቀተረ ፡ ይቄትር ፡ ይቀ ትር ። አው ፡ ቀቲር ፤ ቀተረ ፡ ይቀትር ፡ ይቅ ትር ። ዐረ ፡ ቀተረ) ፤** ማዋደድ ፤ ማዘመድ ፤ መቻን ከር ፤ መቀርቀር ፤ መደንቀር ፤ የነጮት ፡ የብረት ። መዝ ጋት ፡ መቈለፍ ፡ ማጕር ፤ መወርወር ፤ መሸጕር ፤ የመዝ ጊያ ። ፀጸወ ፡ ኖኅተ ፡ ወቀተረ ። ዕጽዉ ፡ ኖኅተ ፡ ወ ቅትሩ ። ወጸአነ ፡ ቀተርነ ፡ ኖኅተ ፡ (መሳ፫ ፡ ፳፫ ። ፪ነገ ፡ ፲፫ ፡ ፲፯ ። ሉቃ፲፩ ፡ ፯) ።

—፤ በቁሙ ፤ መቀተር ፤ ማሾል ፤ ሹል ፡ ማድረግ ፤ ለማ ዋደድ ። ቀትር ፡ መኸን ፤ የጊዜ ። ወቀቲሮ ፡ ጊዜ ፡ ሰሱ ፡ በዓት ፡ (ሉቃ፳፫ ፡ ፵፬) ።

—፤ ማጠን ፤ ማጤስ ፤ ማሽተት ፡ (ዕብ ፡ ወሱር ፤ ቃጣር ፤ ቅጣር ፤ ቋጠረ ፤ ዐጠነ) ። በእንተ ፡ ዕጣኑ ፡ ለአሮን ፡ እ ንተ ፡ አቍረረ ፡ መዐተ ፡ ሞት ፡ ሶበ ፡ ቀተረ ፡ (አዋል) ።

**ቀትር ፤** በቁሙ ፤ መንፈቀ ፡ መዓልት ፤ እኩለ ፡ ቀን ፤ ፮ኛ ፡ ሰዓት ፤ የፀሐይ ፡ አፍሬ ፡ ቀርኍ ፡ ምዕዛሩ ፡ ም ድርን ፡ ፊት ፡ ለፊት ፡ የሚወጋበት ። ይጼልለከ ፡ እም ፀሓዩ ፡ ቀትር ። ቀትረ ፡ መዓልት ። ጊዜ ፡ ቀትር ። ብ ርሃነ ፡ ቀትር ። ጋኔነ ፡ ቀትር ፡ (ሚራ፴፩ ፡ ፲፱ ። ፴፭ ፡ ፲፯ ። ማር፲፭ ፡ ፴፫ ። ኢሳ፲፰ ፡ ፬ ። መዝ ፡ ፺) ።

**ተቀትረ ፤ ተቀተረ ፤** ተዘጋ ፤ ተሸጐረ ፤ ተወጋ ፡ ተቻነከረ ። ታጠነ ፡ ጤሰ ፤ ሸተተ ፤ መዓዛ ፡ ኾነ ። ዘበ ዮርዳኖስ ፡ ተጠምቀ ፡ ወዘበመስቀል ፡ ተቀትረ ፡ (መጽ ፡ ምስ) ።

**ቅቱር ፤ (ራን ፡ ራት ፡ ትርት) ፤** የተዘጋ ፡ ዝግ ፤ ሸጕር ፡ ቅርቅር ። ቤተ ፡ ሞቅሕ ፡ ዝጉሕ ፡ ወቅ ቱር ፡ (ግብ፭ ፡ ፳፫) ።

**ቅታሬ ፤ ቅታር ፤** መጤስ ፤ መሸተት ። ሽቱ ፡ ዕጣን ፤ የተቀመመ ፡ የተጣፈጠ ፤ የደቀቀ ፡ የተወገጠ ። የዕ ጣን ፡ ሽታ ፤ መዐዛ ። ዕጣን ፡ ዘቅታሬ ፡ ደቂቅ ። ዕጣን ፡ ዘካልእ ፡ ቅታሬሁ ፡ (ዘፀ፴ ፡ ፯ ፡ ፱ ፡ ፴፬—፴፰) ።

**ቅትር ፤ (ራት) ፤** ችንካር ፤ ቀኖት ፡ ምስማር ፤ ወስፌ ፡ እፊ ፡ ምዣር ፤ ካስማ ፡ ችካል ፤ ማናቸውም ፡ ሹል ፡ የኾነ ፡ ኹሉ ። ኀጺን ፡ ብዙኅ ፡ ለቅትራት ፡ ኀዋ

ኀው ። ቅንው ፡ በቅትራት ፡ ኀጻውንት ። ቅትራት ፡ ር ሱን ። ከመ ፡ ቅትራት ፡ ለአድግ ፡ (፩ዜና ፡ ፳፱ ፡ ፫ ። መጽ ፡ ምስ ። መክ፲፱ ፡ ፲፩ ። ምሳ፳፮ ፡ ፫) ።

**ቀተተ** ፤—ቄተቸ ፤—ቀተወ ።

**ቆጽን** ፤—ኵፍ ፡ ጫማ ፤—ቀወጽን ።

**ቆጸረ** ፤—ቈረጠመ ፤—ቀውጸረ ።

**ቆጵሮስ** ፤—ስመ ፡ ሀገር ፤ ደሴት ፤—ቀውጵሮስ ።

**ቈጵርስስ** ፤ (ጵር ፡ ኪፓሪሶስ ። ዕብ ፡ ብሮሽ) ፤ የዛፍ ፡ ስም ፤ ጥድ ፤ የጥድ ፡ የዘግባ ፡ ዐይነት ፤ ግንዱ ፡ ነጭ ፤ ደቅማ ፡ የሚመስል ። ቈጵርስስ ፡ ወዠሉ ፡ ዕፀወ ፡ ገዳም ፡ (ኩፋ ፡ ፲፫ ። ሕዝ፳፯ ፡ ፭ ። ፴፩ ፡ ፰) ።



**ረ** ፤ ኻያኛ ፡ ፊደል ፤ በግእዝ ፡ አልፍ ፡ ቤት ፡ በአበገደ ፤ ስሙ ፡ ርእስ ፤ ቍጥሩ ፡ ኹለት ፡ መቶ ፤ አኃዝ ፡ ሲኾን ፡ ረ ፡ (፪፻) ክልኤቱ ፡ ምእት ፡ ይባላል ።

**ርእይ ፤ ዮት ፤ (ርእየ ፡ ይሬኢ ፡ ይርአይ ። ዕብ ፡ ራአህ ። ዐረ ፡ ረአይ)** ፤ ማየት ፡ መመልከት ፤ መትኰር ፤ ማስተዋል ፡ መመርመር ፤ ባይን ፡ መቈፈር ፤ ዐይንን ፡ ልብን ፡ ባንድ ፡ ነገር ፡ ላይ ፡ መጣል ፡ መትከል ፤ አይቶ ፡ ማወቅ ፡ መረዳት ፤ ልኩን ፡ ማግኘት ። ዐየንን ፡ ተመልከት ፤ የዚህ ፡ ወንድም ፡ ነው ። መኑ ፡ ይጸግብ ፡ እምርእየ ፡ ሠናይቱ ። ይርአዩ ፡ ዕዉራን ። ርእዩ ፡ እመ ፡ ኮነ ፡ ከመ ፡ ዝ ። ኢትርአያኒ ፡ እስመ ፡ አነ ፡ ጸላም ፡ (ሚራ፵፱ ፡ ፳፱ ። ኢሳ፳፩ ፡ ፩ ። ኤር፪ ፡ ፲ ። ማሕ፩ ፡ ፮) ።

—፤ መስማት ፡ ማድመጥ ፤ ልብ ፡ ማድረግ ። አጽንን ፡ እዝነከ ፡ ለርእየ ፡ ሕልመ ፡ አቡከ ። ወርእየ ፡ ሕልመ ፡ አቡሁ ፡ ገብአ ፡ ማቱሳላ ። ወርእያ ፡ ደንገፀት ፡ እምቃሉ ፡ (ሔኖ ። ሉቃ፩ ፡ ፳፱) ።

—፤ ማሰብ ፡ መመኘት ፤ መገምገም ፡ መገመት ፤ መጠኈቈል ፡ ማሾረት ፤ ትንቢት ፡ መናገር ፤ መላ ፡ መምታት ። ልብየ ፡ ርእየት ፡ ብዙኀ ፡ ጥበበ ። ርኢኩ ፡ ሎቱ ፡ ዐስቦ ፡ ለዝኩ ፡ ወልድ ። ትሬእዩ ፡ በከከበ ፡ ሰማይ ። ነቢያትኪ ፡ ርእዩ ፡ ለኪ ፡ ከንቶ ፡ (መክ፩ ፡ ፲፮ ። መቢ፲፱ ፡ ፩ ። ኢሳ፵፯ ፡ ፲፫ ። ሰቈ፪ ፡ ፲፬) ። ሰማ ፡ ዐሰበ ፡ ገመተ ፡ አሾረተ ፡ ቢል ፤ የማየትን ፡ ስልት ፡ መናገር ፡ ነው ፡ እንጂ ፤ ምስጢሩ ፡ ከማየት ፡ አይወጣም ፤ ለሥራና ፡ ለነገር ፡ ኹሉ ፡ በዐይን ፡ ሥጋ ፡ ወይም ፡ በዐይን ፡ ልብ ፡ የሚታይ ፡ ሕልማዊ ፡ መልክ ፡ አለው ።

**ረአዪ ፤ (ዪት ፡ ይያን ፡ ያት ፤ አይት)** ፤ የሚያይ ፡ የሚያስተውል ፤ የሚጠነቍል ፤ መሠሪ ፡ ኮከብ ፡ ቈጣሪ ፤ ነቢይ ፡ ሐላሚ ፤ ፈታሽ ፡ መርማሪ ። አ ፡ ልብዋን ፡ ረአይያን ፡ ናሁ ፡ እንኰሙ ፡ እኀሌ ፡ ስምዐ ፡ ለዛቲ ፡ ቃል ። ረአይያነ ፡ ከዋክብት ። ረአይተ ፡ ኮከብ ። ረአዩ ፡ ኀቡኣት ። ረበየ ፡ ለወልዱ ፡ ረአዩ ፡ ለቤተ ፡ መቅደስ ፡ (ግንዘ ። ሔኖ፰ ፡ ፫ ። ኪዳ ። አርጋ ፡ ፫ ። ዮሴፍ) ።

**ረአይ** ፤ ዝኒ ፡ ከማሁ ፤ ነቢይ ። ንሑር ፡ ኀበ ፡ ረአይ ፤ እስመ ፡ ይብልዎ ፡ ሕዝብ ፡ ለነቢይ ፡ ረአየ ። ቦኑ ፡ ረአይ ፡ ዝየ ። አይቴ ፡ ቤቱ ፡ ለረአይ ፡ (፩ነገ ፡ ፱ ፡ ፲፩ ፡ ፲፰) ።

**ራእይ ፤ (ያት)** ፤ በቁሙ ፤ ሕልም ፤ ትንቢት ፤ ጥንቈላ ፡ ኮከብ ፡ ቈጠራ ። ራእይ ፡ ዘርእየ ፡ ኢሳይያስ ። እለ ፡ ይሬእዩ ፡ ራእየ ። ኢርእዩ ፡ ራእየ ፡ በኀበ ፡ እግዚ ። ራእየ ፡ ኮከብ ፡ (ኢሳ፩ ፡ ፩ ። ፴ ፡ ፲፰ ። ሰቈ፪ ፡ ፱ ። ሔኖ፰ ፡ ፫) ። ራእይ ፡ ለንጓፊና ፡ ለመጻኢ ።

—፤ ማየት ፤ አስተያየት ፤ ዐይን ፡ አገላለጥ ። እምራእዩ ፡ ይትዐወቅ ፡ ብእሲ ፡ (ሚራ፲፱ ፡ ፳፱) ።

—፤ መልክ ፤ ፊት ፤ ቅርጽ ፤ ገጽ ፤ ዐይን ፡ የሚያርፍበት ። ተወበጠ ፡ ራእዩ ። እለ ፡ ሠናይ ፡ ራእዮን ። ጸሊም ፡ ከመ ፡ ሕመት ፡ ራእዮሙ ። ገጹ ፡ ከመ ፡ ራእየ ፡ መብረቅ ፡ (ማቴ፲፯ ፡ ፪ ። አስቴ፪ ፡ ፪ ። ሰቈ፬ ፡ ፰ ። ዳን፲ ፡ ፮) ።

**አርአየ ፤ አስተርአየ** ፤ አሳየ ፤ ገለጠ ፤ አበራ ፤ ነገረ ፤ አስተማረ ፤ አሳወቀ ፤ አስረዳ ። አርአዮሙ ፡ እኪተኒ ፡ ወሠናይተኒ ። ከመ ፡ አርኢ ፡ ኀይልየ ፡ ባዕሌክ ። እግዚ ፡ ያርኢ ፡ ገጾ ፡ ላዕሌክ ። ነገር ፡ ዘአርአይኩክ ። አርእየኒ ፡ ወአእምር ። ምንተ ፡ ይቤሎ ፡ ዘአስተርአዮ ። ዕፀ ፡ ዘያሬኢ ፡ ወያሌቡ ፡ ሠናየ ፡ ወእኩየ ፡ (ሚራ፲፯ ፡ ፮ ። ሮሜ፱ ፡ ፲፫ ። ዘኍ፮ ፡ ፳፮ ። ኤር፲፩ ፡ ፲፮ ። ፴፮ ፡ ፪ ። ሮሜ፲፩ ፡ ፬ ። ዘፍ፪ ፡ ፱) ።

**አርአያ** ፤ በቁሙ ፤ ሥዕል ፤ አምሳል ፤ ዐይነት ፤ መልክ ፤ አካል ፤ አብነት ፡ መምር ። ንግበር ፡ ሰብአ ፡ በአርኣያነ ። በበ ፡ አርኣያሁ ። አርኣያሁ ፡ ለእግዚ ። ታሜኒ ፡ ገጻ ፡ ወታበረኑ ፡ አርኣያሃ ። ብርሃነ ፡ ስብሐቲሁ ፡ ወአምሳለ ፡ አርኣያሁ ። ኮነ ፡ አርኣያ ፡ ለዓለም ፡ ከመ ፡ ይነስሑ ። እስመ ፡ አርኣያየ ፡ ወሀብኩክሙ ፡ (ዘፍ፩ ፡ ፲፪ና ፡ ፳፮ ። ፪ቆሮ ፡ ፬ ፡ ፬ ። ስንክ ፡ ጳጕ፭ ። ዕብ፩ ፡ ፫ ። ሚራ፵፬ ፡ ፲፮ ። ዮሐ፲፫ ፡ ፲፭) ።

—፤ ዐቢይና ፡ ደቂቅ ፡ አገባብ ፤ እንደ ። አርኣያ ፡ ይነውም ፡ ዘልፈ ። አርኣያ ፡ ብዙኀ ፡ ዝናም ። አርኣያ ፡ ከመዝ ፡ በረረ ፡ (ስንክ ፡ ጥር፳፩ ። ጥቅ፳፭ ። ደራሲ) ።

**ተርእየ ፤** ታየ ፤ ተገለጠ ። ወተርእየት ፡ ማይ ፡ ርግዕተ ። ኢትትረአይ ፡ ቅድሜየ ፡ ዕሩቀከ ። መፍትው ፡ ለአንስት ፡ ይትረአያ ፡ በአርአያ ፡ ህድአት ፡ ወበትሕትና ፡ ፍድፉድ ፤ (ጥበ ፲፱ ፡ ፯ ። ዘፀ ፳፫ ፡ ፲፭ ። ፊ ፡ መ ፡ ፴፱ ፡ ፰) ። በተርእየ ፡ ፈንታ ፡ አስተርአየ ፡ ይላል ፤ የስሕተት ፡ ስሕተት ፡ ነው ፤ አያሰኝም ። ገባሬ ፡ ሰማያት ፡ ወምድር ፡ ዘያስተርኢ ፡ ወዘኢያስተርኢ ። አስተርአየ ፡ ዘኢያስተርኢ ፤ እሙነ ፡ ኮነ ፡ አስተርእዮቱ ፡ (ጸሎ ፡ ሃይ ። ድጓ) ። በአርእየ ፡ ቦታ ፡ አስተርአየ ፡ ቢል ፡ ግን ፤ ሥርወ ፡ ቀለሙ ፡ ሳይለ ፡ ስለ ፡ ኾነ ፤ ርትዕ ፡ እንጂ ፡ ጸያፍ ፡ አይኾንም ፤ ስሕተት ፡ አይባልም ።

**ርኡይ ፤ (ያን ፡ ያት ፡ ኢት) ፤** የታየ ፡ የተገለጠ ፤ ግልጥ ፤ ጕልሕ ።

**ርእየት ፤** ማየት ፤ መታየት ፤ አስተያየት ፤ መልክ ፤ አምሳል ፤ ዐይነት ። እፎ ፡ እክል ፡ ርእየተ ፡ እኪቶሙ ። ተወለጠ ፡ ርእየተ ፡ ገጹ ። ሕዝቅኤል ፡ ዘርእየ ፡ ርእየተ ፡ ስብሐቲሁ ። ይገብሮ ፡ ከመ ፡ ርእየተ ፡ ዕጓለ ፡ መሕያው ። ከመ ፡ ርእየተ ፡ እሰቁጥሩ ፡ (አስቴ ፰ ፡ ፯ ። ዳንኤ ፡ ፲፱ ። ሢራ ፵፱ ፡ ፰ ። ኢሳ ፵፱ ፡ ፲፫ ። ሕዝ ፩ ፡ ፱) ።

**ምርአይ ፤ (ያት) ፤** ማያ ፤ ማሳያ ፤ መተያ ፤ ቦታ ፤ መስታዮት ፤ መነጽር ። ርእይ ፤ ራእይ ፤ ርእየት ፡ በማለት ፡ ፈንታ ፡ ምርኣይ ፡ ይላል ፤ የተሳሳተ ፡ ነው ። ምርኣየ ፡ አዕይንቲከ ፡ (ዘዳ ፳፰ ፡ ፴፱) ። ሞራ ፡ ማለት ፡ ከዚህ ፡ ወጥቷል ፤ ማያ ፡ መጠንቈያ ፡ ማለት ፡ ነው ፡ (ሕዝ ፳፩ ፡ ፳፩) ።

**ተራአየ ፤** ተያየ ፤ ተማሰለ ፤ ተመሳሰለ ፤ ተነጻጸረ ። ነዐ ፡ ንትራአይ ፡ ገጸ ፡ በገጽ ። የሐውሩ ፡ ክልኤቱ ፡ ኅቡረ ፡ እንዘ ፡ ኢይትራአዩ ፡ (፬ነገ ፡ ፲፬ ፡ ፰ ። ዓሞ ፫ ፡ ፫) ።

**አስተራአየ ፤** አስተያየ ፤ አነጻጸረ ፡ ፊት ፡ ለፊት ፤ ዐይን ፡ ለዐይን ።

**አስተርአየ ፤ (አርአየ) ፤** አሳየ ፤ ገለጠ ። ባለቅኔዎች ፡ ግን ፡ ታየ ፡ አሳየ ፡ ብለው ፡ በኹለት ፡ ጾታ ፡ ይፈቱታል ፤ ታየ ፡ ማለት ፡ ስሕተት ፤ አሳየ ፡ ማለት ፤ እውነት ። ወዘንተሰ ፡ አማነ ፡ ትዌሊ ፡ (ዮሐ ፱ ፡ ፲፰) ።

**ረአመ ፤—ሮመ ፤ ነገደ ፤—ርኢም ፡ ረዐመ ።**

**ርኤም ፤ (ማት ። ዕብ ፡ ርኤም ። ሱር ፡ ርማያ) ፤** ቀንዳም ፤ የበረሓ ፡ እንስሳ ፤ የዋሊያ ፡ ወገን ፤ ቀንደቹ ፡ ጠፍጣፎች ፤ ታላላቆች ፤ ባለብዙ ፡ ዐጽቆች ፡ የኾኑ ፤ ለያንዳንዱ ፡ ፯ ፡ ፰ ፡ ዐጽቅ ፡ ያላቸው ፤ ዐጽቆቻቸው ፡ የእጅ ፡ ጣቶች ፡ የዥላብ ፡ ዕንጨቶች ፡ የሚመስሉ ። የግእዝ ፡ መላሽ ፡ ግን ፡ ርኤም ፡ በማለት ፡ ፈንታ ፡ ሐርማዝ ፡ ሐሪሥ ፡ እንደ ፡ ማለት ፡ ዘአሐዱ ፡ ቀርኑ ፡ ይላል ፤ የተሳሳተ ፡ ነው ፡ (መዝ ፡ ፳፩ና ፡ ፳፰) ።



ርኤም ፡

**ረአሙት ፤ (ዕብ ፡ ራእሞት) ፤** ውስጠ ፡ ብዙ ። ውድ ፡ ክቡር ፡ ዕቃ ፤ ጥሩ ፡ ገንዘብ ፡ ሸቀጥ ፤ በውድ ፡ የሚሸጥ ፡ የሚለወጥ ፤ ወርቅ ፡ ዕንቍ ፡ ዘጺ ፡ ሕቍ ፤ የመሰለው ፡ ኹሉ ፡ (ሕዝ ፳፯ ፡ ፲፮) ።

**ርኢስ ፤ ሶት ፤ (ርእሰ ፡ ይርእስ ፡ ይርእስ ። ዐረ ፡ ረአሰ) ፤** መራስ ፤ ራስ ፡ መኾን ፤ ራስ ፡ መባል ፤ መሸምገል ፡ መላቅ ፡ መሠልጠን ፤ እንደ ፡ ጕልላት ፡ በላይ ፡ መኾን ። ተለአከ ፡ ለነግድ ፡ ከመ ፡ አብርሃም ፤ ወተተሐት ፡ ለዘትርእስ ፡ ላዕሌሁ ፡ ከመ ፡ ዳዊት ፡ (ፊልክ ፡ ፩ ። አርጋ ፡ ፩) ። በርእሰ ፡ ፈንታ ፡ ተርእሰ ፡ ይላል ፤ አያሰኝም ። ኅበ ፡ ይትረአስ ፡ መስቀል ፡ ህየ ፡ መዊእ ። አጽፋር ፡ ዘተርእሳ ፡ ዲበ ፡ መልዕልቴሆን ፡ ለአእዳው ። ዘያጸንዐ ፡ ተርእሶተ ፡ (ተረ ፡ ቄር ፲፩ ። በንክ ። አፈ ፡ ድ፴፬) ።

**ርኡስ ፤ (ሳን ፡ ሳት ፡ እስት) ፤** ራስ ፡ የኾነ ፤ የተሾመ ፤ የሠለጠነ ፤ ንጉሥ ። እግዚ ፡ ሥሉጥ ፡ ወርኡስ ፡ ዲበ ፡ ኵሉ ። እግዚ ፡ ልዑል ፡ ወርኡስ ። ርእሰ ፡ ርኡሳን ፡ መኳንንት ። ርእሰት ፡ አንቲ ፡ (አፈ ፡ ድ፱ ። ሃይ ፡ አበ ። አዋል ። ቅዳ) ።

**ራእስ ፤ (ሳን ። ዐረ ፡ ረኢስ) ፤** አለቃ ፤ ሹም ፤ አበ ፡ ማኅበር ፤ ኤጲስቆጶስ ። ራእሳኒሆሙ ፡ ለክርስቲያን ፡ (አዋል) ። ራእስ ፤ ርእስ ፡ በማለት ፡ ፈንታ ፡ ርኡስ ፡ ይላል ፤ የተሳሳተ ፡ ነው ። ርኡሳኒሆሙ ፡ ለኢሎፍሊ ። ርኡሳነ ፡ አእላፍ ። ርኡሳነ ፡ ምእት ፡ (፩ዜና ፡ ፲፪ ፡ ፲፱ና ፡ ፰ ። ፲፫ ፡ ፩ ። ፳፯ ፡ ፩) ።

**ርእስ ፤ (ዕብ ፡ ሮሽ ። ሱር ፡ ሬሻእ ። ዐረ ፡ ረእስ) ፤** በቁሙ ፤ ራስ ፤ መክብበ ፡ ሕዋስ ፤ ከንገት ፡ በላይ ፡ ያለ ፤ ዐናት ፡ ሞንቅላት ፤ የናላ ፡ ቅል ፤ መዠመሪያ ፡ ክፍል ፤ በሥጋዊና ፡ በደማዊ ፡ ኹሉ ። ርእስ ፡ ወዘነብ ። ለሊሁ ፡ ርእስ ፡ ወንሕነ ፡ አባል ። አልቦ ፡ ር



ርእስ ፡

እስ ፡ ዘየአኪ ፡ እምርእሰ ፡ አርዌ ፡ ምድር ፡ (ኢሳ ፱ ፡ ፲፬ ። ሢራ ፳፭ ፡ ፲፭ ። አፈ ፡ ድ፯) ።

—፤ ሥዕርት ፤ የራስ ፡ ቡቃያ ፤ ፀምሩ ፡ ጠጕሩ ፤ ባሕር

ያዊ፡ ማዕሩ። ፀፈረት፡ ርእሳ። ወተላጸየ፡ ርእሶ፡ (ዮዲ ፲፮፡ ፪። ግብ ፲፰፡ ፲፰። ዘኁ ፮፡ ፲፱)።

—፤ ጫፍ፤ ቍንጮ፤ መጨረሻ፤ መደምደሚያ፤ የዛፍ፡ የቤት፡ የሕንጻ፡ የተራራ። አርዝ፡ ዘነዋኀ፡ ቆሙ፡ ወይበጽሕ፡ ደመናተ፡ ርእሱ። ማዕርግ፡ ትክልት፡ ውስተ፡ ምድር፡ ወርእሳ፡ ይበጽሕ፡ ሰማየ። ርእሰ፡ ማእዘንተ፡ ምሥራቅ። ሕፅነ፡ ርእሰ፡ ደብር፡ (ሕዝ ፴፩፡ ፫። ኩፋ ፳፯። ሉቃ ፬፡ ፳፱)።

—፤ የፊደል፡ ስም፤ ካያኛ፡ ፊደል፡ ረ። ሬስን፡ ተመልከት።

—፤ ነፍስ፤ ሰውነት፤ ሥጋ፡ ገላ፤ መላው፡ ኹለንተናው፤ ከራስ፡ ጠጕር፡ እስከ፡ እግር፡ ጥፍር፡ ያለው፡ ባንድነት፤ እኔ፡ የሚል፤ አካል፤ ቁመት፤ ርስ፡ ቅል፤ ባለቤት። ሬሳ፡ ማለት፡ ከዚህ፡ የወጣ፡ ነው፤ ለልንና፡ ኪያን፡ አካልን፡ ተመልከት። ሰለየ፡ በበሕኩ፡ ርእስየ። እቄድስ፡ ርእስየ። ከመ፡ ያርኅሱ፡ ርእሶሙ። አአምር፡ ርእስየ፡ ከመ፡ መሬት፡ አነ። ኢታዕቢ፡ ርእሰከ። ያገብኡ፡ ርእሶሙ፡ ኀቤከ፡ (ዮሐ ፲፯፡ ፲፱። ፲፯፡ ፲፱። ሮሜ ፩፡ ፳፬። ኢዮ ፵፪፡ ፮። ሚራ ፩፡ ፬። ዮዲ ፪፡ ፲)።

—፤ ሥር፡ መሠረት፤ መዠመሪያ፡ ጥንት፤ መግቢያ፡ መባቻ፤ ንጉሥ፤ በኵር፡ አለቃ። ርእሱ፡ ለነገረ፡ ጥበብ። አነ፡ ርእስ፡ ወማኅለቅት። ርእሰ፡ መጽሐፍ። አመ፡ ርእሰ፡ ሠርቅ። ትሠይመኒ፡ ርእሰ፡ ሕዝብ። ርእሰ፡ ካህናት፤ ርእሰ፡ ዲያቆናት። ጴጥሮስ፡ ርእሰ፡ ሐዋርያት፡ (ሔኖ ፴፯፡ ፪። ራእ ፳፪፡ ፲፫። መዝ ፴፱። ሕዝ ፳፱፡ ፩። መዝ ፲፯። ፍ፡ ነ፡ ፬። ስንክ፡ ነሐ ፲፯)።

አርእስት፤ (ታት)፤ ራሶች፤ ጫፎች፤ መዠመሪያዎች፤ አለቆች። ቀጥቀጥከ፡ አርእስቲሁ፡ ለከይሲ። መካን፡ ዘይመትሩ፡ ውስቴቱ፡ አርእስታተ። አርእስተ፡ ጥቅም። አርእስተ፡ ነገር። አርእስተ፡ ምንባብ። አርእስተ፡ ዐሠርቱ፡ ምእት። አርእስተ፡ መላእክት፡ (መዝ ፸፫። ስንክ፡ ሐም ፳። ምሳ ፬፡ ፳፩። መቅ፡ ወን። ግንዘ። ሔኖ። ኪዳ)።

ርእስና፤ ራስነት፤ ብኵርና፤ አለቅነት። ሠናየ፡ ርእስና። አመ፡ ርእስና፡ (ስንክ፡ ሐም ፲። ነሐ ፲፩)።

አርአሰ፤ ሾመ፡ አላደገ፤ ራስ፡ አደረገ፤ አላቀ፤ አበለጠ፤ በላይ፡ አስቀመጠ። ካህነ፡ እግዚ፡ ዘአርአሶ፡ ህየንቴሁ። ወአርአሶ፡ ላዕለ፡ ኵሉ፡ (ፈ፡ መ ፲፯፡ ፩። ኢፌ ፩፡ ፲)።

አርአሰ፤ አንተራስ፤ አቀና፤ ደገፈ፤ የድውይ።

ተርአሰ፤ ተንተራስ፤ ተጠጋ፤ ተደገፈ። መጽሐፍ፡ ግን፡ እንዳማርኛው፡ ተተርአሰ፡ ይላል፤ አያሰኝም። ተተርኢሶ፡ ኖመ። ያዕቆብ፡ ቅዳሴ፡ ተተርአሰ፡ እብነ፡ (ማር ፬፡ ፴፰። ቅኔ)።

ትርአስ፤ (ሳት)፤ ትራስ፤ መከዳ፤ ራስጌ፤ የመከዳ፡ ቦታ፤ የራስ፡ ቦታች፤ ቅርብ፡ አጠገብ። መንገለ፡ ትርአሲሁ። ሖረት፡ ውስተ፡ ምስካቡ፡ መንገለ፡ ትርአሱ። ይነብሩ፡ አሐዱ፡ ትርአሰ፡ ወአሐዱ፡ ትርጋፀ። ረከበ፡ ትርአሶ፡ ኅብስተ፡ (፩ነገ ፳፮፡ ፯። ዮዲ ፲፫፡ ፯። ዮሐ ፳፡ ፲፪። ፫ነገ ፲፱፡ ፯)።

መተርእስት፤ መንተራሻ፤ ማንተራሻ፤ ትራስ፤ ብርኵማ። የራስጌ፡ ሰይፍ፤ ዱላ፡ ሽጕጥ፤ የመሰለው፡ ኹሉ። መተርእስቱ፡ እንተ፡ በዲቤሃ፡ ያሰምክ። መልእት፡ መተርእስተ፡ ወዘበጠት፡ ክሣደ፡ ወመተረት፡ ርእሶ፡ እምኔሁ፡ (ዮዲ ፲፫፡ ፮ና፡ ፰፡ ፲፮)።

ረቢብ፤ በት፤ (ረበ፤ ረበበ፡ ይረብብ፡ ይርብብ። ዕብ፡ ራባብ። ዐረ፡ ረበ)፤ መብዛት፡ መፈድፈድ፤ መላቅ፡ መብለጥ፡ ማደግ፡ መግነን፤ መጕልበት፡ መሠልጠን፤ እጅግ፡ ብዙ፡ እጅግ፡ ታላቅ፡ መኾን፤ በቍጥር፡ በክብር፡ በጌትነት። ረቢ፡ ረባን፡ ረበዋት፡ አርባብ፡ የዚህ፡ ዘሮች፡ ናቸው።

—፤ መርበብ፤ መዘርጋት፤ መዘረር፤ መሰተር፤ መወጠር፡ መገተር። መነስነስ፡ መረብረብ። ይኩና፡ ኪኑቤን፡ እንዘ፡ ይረብባ፡ ክነፊሆን። ወረበብኩ፡ ለሰማይ፡ ከመ፡ ሠቅ። ይረብቡ፡ መሣግረ። አዘዘ፡ ያምጽእ፡ ሐመደ፡ ወረበቦ፡ ውስተ፡ ኵሉ፡ ቤት፡ (ዘፀ ፳፭፡ ፳። መዝ ፻፫። ሕዝ ፳፯፡ ፲፬። ዳን ፲፬፡ ፲፬)።

ረባቢ፤ (ቢት፡ ብያን፡ ያት)፤ የሚዘረጋ፡ ዘርጊ፤ ነስናሽ።

መረብ፤ (ዕብ፡ ሚድባር)፤ በረሓ፤ ምድረ፡ በዳ፤ ያደገ፡ የወጥመድ፡ ስፍራ፤ የእንስሳት፡ የአራዊት፡ ወጥመድ፤ አሽክላ። ወኮንኩ፡ ከመ፡ አድግ፡ መረብ፡ ዘገዳም፡ (መዝ ፻፩)።

መረብ፤ (ዕብ፡ ሙራሕ። ዐረ፡ መራእ)፤ የአዕዋፍ፡ ፊኛ፤ ያንገታቸው፡ ኪስ፡ ከረጢት፡ በስተታች፡ በደረት፡ ያለው፤ ጥሬ፡ መቋጠሪያው።

—፤ በቁሙ፤ መረበ፡ የሚባል፡ አሞራ፡ ባለታላቅ፡ ፊኛ፤ መጠኑ፡ የርኩም፡ እግሩ፡ የሽመላ፤ ላባው፡ ክቡር፡ በውድ፡ የሚሼጥ። በቀቀኖ፡ ፈንታ፡ አድግ፡ መረብ፡ እንዲል፡ (መዝ፡ ፻፩)። አድግን፡ እይ።

መርበብት፤ (ብ፡ መራብብት)፤ በቁሙ፤ መረብ፤ መርበብ፤ ያጣ፡ ወጥመድ፤ የሌላውም፡ ኹሉ፤ ወስከምት፤ ማንቆ፡ ሸምቀቆ። ይወድዩ፡ መርበብተ፡ ውስተ፡ ባሕር። ተከለ፡ መርበብተ፡ ከመ፡ ያሥግር፡ ባቲ፡ አራዊተ። መርበብተ፡ ሕይወት፡ (ማቴ ፬፡ ፲፰። ስንክ፡ ሚያ ፲፰። ቅዳ፡ ዮሐ)።



መርበብት፡

**አርበበ፤(ሱር፡ራውርበ)፤** አበዛ፤ አረባ፤ አከበረ። ረበበ፤ ቈለለ፡ ከመረ፤ አላቀ፡ ታላቅ፡ አደረገ።

**ተረበ፤** ተዘረጋ፤ ተዘረረ። እምቅድመ፡ ይትረበባ፡ ሰማያት፡ (ቅዳ፡ አፈ። ዲዮስ)።

**ርቡብ፤(ባን፡ ባት፡ ብብት)፤** የተዘረጋ፤ ዝርግ፤ ሰፋሕ። እደዊሁ፡ ርቡባቲሆን፡ (ዘፀ፲፯፡ ፲፪)።

**ርበት፤** መዘርጋት፤ ዝርግነት። ርበተ፡ ደመና፤ ርበተ፡ ገሚ፡ (አርጋ፡ ፩)።

**ረብ፤(ዐረብ)፤** ጌታ፤ አግዜር። ሰፊ፡ ታላቅ፤ ብዙ፡ እጅግ። ሲያበዛ፡ ረበዋት፡ አርባብ፡ ይላል።

**አርባብ፤** የኪሩቤል፡ ስም፤ ጌቶች፡ አለቆች፤ ደምባሮች። አርባብ፡ ኪሩቤል። ንበር፡ ዲበ፡ ባሬል፡ ወዲበ፡ አርባዕቱ፡ አርባብ፡ (ቀሌ። አርጋ፡ ፫። ማሕ፱፡ ፲፯)።

**ረበዋት፤(ዐረ፡ ሪብወት፤ ሩበት። ዕብ፡ ሪበ፤ ርበበ። ሱር፡ ሪቡ)፤** እልፍ፤ ወይም፡ ዐሥር፡ ሺሕ። በዐረብና፡ በዕብራይስጥ፡ በአራም፡ ቋንቋ፡ ግን፡ ዐሥር፡ እልፍ፤ ወይም፡ አእላፍ፡ ይባላል። ተስዐቱ፡ ምእት፡ ረበዋት፤ ፱፻—፻፤ ፱፡ ሚልዮን፡ (ጦማር)።

—፤ እጅግ፡ ብዙ፤ የብዙ፡ ብዙ፤ ብዛቱ፡ እንዳሸዋና፡ እንደ፡ ኮከብ፡ ያለ። አለፈንና፡ ምእልፊትን፡ እይ። ረበዋተ፡ ረበዋት፡ ይሰግዱ፡ ሎቱ፡ (ቅዳ፡ ያዕ)።

**ረቢ፤(ዕብ፡ ራቢ)፤** የከበሬታ፡ ስም፤ ጌታዬ። ጌታ፤ አለቃ፤ ሹም፤ መምር፤ ሊቅ፤ ሽማግሌ፤ ቢ፡ ዝርዝር፡ ነው። ኢትሰመዩ፡ ረቢ። ሰነሁ፡ እንጋ፡ ረቢ። በሓ፡ ረቢ። ወይቤልዎ፡ ረቢ፡ ዘበትርጓሜሁ፡ ሊቅ፡ (ማቴ፳፫፡ ፯። ፳፯፡ ፳፭፡ ማ፱። ዮሐ፩፡ ፴፱)።

**ረቡኒ፤(ዕብ፡ ራቡኒ)፤** እግዚእየ፤ አምላኪየ፤ ሊቅየ፤ መምህርየ፡ (ዮሐ፳፡ ፲፮። ማር፲፡ ፶፩)።

**ረባን፤(ዕብ፡ ራባን)፤** ስሙ፡ ሊቃናት፤ ጌታ፤ አለቃ፤ መምር፤ መኰንን፡ ወይዘር፡ የነገሥታት፡ ዘር። ጊዮርጊስ፡ ራባን፡ ሰባኬ፡ ትንሣኤሁ፡ ለመድኀን፡ (ድጓ)።

**ረበናት፤(ዕብ፡ ራበናን)፤** ጌቶች፡ አለቆች፤ ብልጦች፡ ዐዋቆች፤ ሽማግሎች፤ መምህራን፡ ሊቃውንት፤ ሹማምት። ረበናተ፡ ካህናት። ረበናቲሆሙ፡ ለሕዝብ። ሥርዐተ፡ ረበናት። ረበናተ፡ ገዳመ፡ አስቄጥስ፡ (ኢሳ፴፯፡ ፱። ኤር፲፱፡ ፩። ማር፯፡ ፫። ስንክ፡ ጥር፰። ግንቦ)።

**ረቢሕ፤ ሖት፤(ረብሐ፡ ይረብሕ፡ ይርባሕ። ዐረ፡ ረቢሐ። ዕብ፡ ራባሀ። ሱር፡ ርባእ)፤** መርባት፤ መብዛት፤ መውለድ፡ መክበድ፡ መፋፋት፤ መንጋ፡ እንግልጋ፡ መኾን። የሰው፡ የከብት፡ የገንዘብ፤ ለግስም፡ ይኾናል። ምናን፡ ዘበዝኀ፡ ወመክሊት፡ ዘረብሐ፡ (ቅዳ። ሳታ)።

—፤ መርባት፤ መጥቀም፤ ማገልገል፤ ሥራ፡ መያዝ፤ ጕዳይ፡ መምላት። ብእንተ፡ ዙሉ፡ ዘይረብሐክ፡ ወይበቍዐክ። ምንት፡ ይረብሖ፡ ለእመ፡ አንተ፡ አርታዕክ፡ ፍናዊከ። ይሜህሩ፡ በዘይረብሖሙ። ከመ፡ እርብሖ፡ ለክርስቶስ፡ (ሚራ፵፱፡ ፳። ኢዮ፳፱፡ ፫። ቲቶ፩፡ ፲፩። ፊልጵ፫፡ ፰)።

—፤ መግዛት፤ ገንዘብ፡ ማድረግ፤ መኼጥ፤ መነገድ፡ ማትረፍ፤ ትርፍ፡ ጥቅም፡ ማግኘት፡ (ማቴ፲፮፡ ፳፮። ፳፭፡ ፲፯)። ሌጂስቀጵስ፡ ኢያፍቅር፡ ይርባሕ። እመ፡ ረብሑ፤ ትንሣአ፡ ብእሲት፡ መንፈቀ፡ ረባሖሙ። ምንተ፡ ረባሕነ፡ ዘዐቀብነ፡ ትእዛዞ። አንትሙ፡ ትረብሑ፡ በመዊአቶሙ፡ ስመ፡ ክቡረ፡ (ሲኖዶ። ፍ፡ ነ፡ ዓ፱፡ ፫። ሚል፫፡ ፲፬። ዮሴፍ)። በረብሐ፡ ፈንታ፡ ተረብሐ፡ ይላል፤ ስሕተት፡ ነው። እንዘ፡ ኢትትረብሕዎሙ፡ (፩ጴጥ፡ ፭፡ ፪)።

**ረባሒ፤(ሒት፡ ሕያን፡ ያት)፤** የሚረባ፤ የሚጠቅም፤ ጠቃሚ። ምጽኢት፡ ተናግዶ፡ አምላካዊት፡ ማእምንት፡ ረባሒት፡ ይእቲ፡ (ፍ፡ ነ፡ ፲፭)።

**አርብሐ፤** አስገዛ፤ አረባ፤ አስረባ፤ አበዛ፤ አስጠቀመ። እግዚአብሔር፡ ዘአርባሕከነ፡ ሡሎ፡ ፍጥረተ፡ ዘዘ፡ ዚአሁ፡ ፍሬ። አርባሕከ፡ ትምክሕተ፡ በርእስከ፡ ወበሰብእከ፡ ኅሳረ፡ ወዝንጓጌ። ሐዘን፡ በእንተ፡ እግዚ፡ ያረብሕ፡ ሕይወተ፤ ወሐዘን፡ በእንተ፡ ዓለም፡ ያረብሕ፡ ሞተ። በሊዕኒ፡ ኢያረብሐነ፡ (ቄስጠ። ዮሴፍ። ፍ፡ ነ፡ ፳፱። ፪ቆሮ፡ ፯፡ ፲)።

**ተረብሐ፤** ተገኘ፤ ተወለደ፤ ትርፉ፡ ጥቅሙ፡ ዐራጣው። ዘተረብሐ፡ (ቄር፡ ጸላ)።

**ርቡሕ፤(ሓን፡ ሓት፡ ብሕት)፤** የረባ። የበዛ፤ የተረባ፡ የተጠቀመ፤ ብዙ፡ ትርፍ፡ ያገኘ።

**ርባሕ፤** ርባ፤ ርባታ፤ የሰዋሰው፡ ትምርት፤ አንዱን፡ ቃል፡ ባሥር፡ ሕዝብ፡ ባሥር፡ ንባብ፡ በዥ፡ መደብ፡ መዘርዘር፡ ማርባት።

**ረብሕ፤ ረባሕ፤(ሓት)፤** ብዙ፡ ትርፍ፤ ወለድ፤ ዐራጣ፤ ርቢ፤ ጥቅም፡ ጠቀሜታ። እለ፡ ያፈቅሩ፡ ረባሐ። ፍትወተ፡ ረባሕ። ረባሕ፡ ርኵስት። ኢትት ማከር፡ እንበይነ፡ ረባሕ፡ ምስለ፡ ሠያጢ። ረብሐ፡ ነፍስከ። አይኑ፡ ረባሕ፡ ለነ፡ በቀቲለ፡ ነፍሳቲነ። ፈልፈለ፡ ረባሕ። ረባሓተ፡ ጾም፡ (፩ጢሞ፡ ፫፡ ፰። ጥበ፲፬፡ ፪። ፈ፡ መ፡ ፲፰፡ ፩። ሢራ፴፯፡ ፲፩። ስንክ፡ ታኅ፳፭። ዮሴፍ። ቅዳ። ፍ፡ ነ፡ ፲፭)። በረባሕ፡ ፈንታ፡ ርቡሕ፡ ይላል፤ ስሕተት፡ ነው። ርቡሕ፡ ቢተ፡ (ፊልጵ፩፡ ፳፩)።

**ረብሓዊ፤(ዊት፡ ውያን፡ ያት)፤** የሚያተርፍ፤ አትራፊ፤ ሸቃጭ፡ ቸርቻሪ፤ አበዳሪ። ነጋዴ፡ ወረብሓዊ፡ (አፈ፡ ተ፲፯)።

**ያርብሕ፤(ሓን)፤** ሐርበኛ፤ ኀይለኛ፤ የወንዶች፡ ባል፤ ዝግና፡ ስሙዐ፡ ዜና፤ መጠኑ፡ ቁመቱ፡ ኀይሉና፡ ጕልበቱ፡ ከሰው፡ ልክ፡ ያለፈ፡ የተረፈ፤ እንደ፡ ዔናቅ፡ ልጆች፡ ያለ። ጢጣኖስንና፡ ናፊልን፡ ተመልከት። ኀይለ፡ ያርብሕ። ሥጋ፡ ያርብሕ። በንእሱ፡ ቀተለ፡ ያርብሐ። ከመ፡ ያርብሕ፡ ዘይሜርድ፡ ፍ

ዮት ፡ (ኢሳ ፲ ፡ ፱ ። ሕዝ ፴፱ ፡ ፲፰ ። ሚራ ፵፯ ፡ ፱ ። መዝ ፡ ፶፰) ። ኀያላን ፡ ያርብሖን ፡ በማለት ፡ ፈንታ ፡ እለ ፡ ያር ብሕ ፡ ይላል ፤ አያሰኝም ፡ (ዘፍ ፮ ፡ ፱ ። ፲፱ ፡ ፭ ። ዘኍ ፲፫ ፡ ፴፱) ።

**ያርብሓዊ** ፤ ዝኒ ፡ ከማሁ ። ዔናቃዊ ፤ የዔናቅ ፡ ወገን ፤ ሐርበኛ ። ወናሁ ፡ ያርብሓዊ ፡ (፭ነገ ፡ ፲፯ ፡ ፳፫) ።

**ተራብሐ** ፤ ተራባ ፤ ተባዛ ፤ ተጠቃቀመ ፤ ተገበ ያየ ፤ ተሻሻጠ ። ንትራባሕ ፡ በትግብርት ፡ እክልነ ፡ (ዓ ሞ፰ ፡ ፭) ።

**አስተራብሐ** ፤ አራባ ፤ አባዛ ፤ አጠቃቀመ ። አስተራብሖ ፡ ንዋይ ፡ (ፍ ፡ ነ ፡ ፴፱) ።

**መስተራብሕ** ፤ (ሒት ፡ ሓን ፡ ሓት) ፤ የሚያራባ ፤ የሚያባዛ ። ወኢመስተራብሒት ፡ (ዲድ ፡ ፲፱) ።

**ረብዮ** ፤ **ዮት** ፤ (**ረብዐ ፡ ይሬብዕ ፡ ይረ ብዕ ። ዕብ ፡ ራቤዕ**) ፤ አራት ፡ ማድረግ ፤ ካራት ፡ መክፈል ፤ አራት ፡ ማለት ። ዘያማስን ፡ ሥላሴ ፡ ወይሬ ብዕ ፡ ጥምቀተ ፡፡ ዘይሬብዮን ፡ ለክንትሮሳተ ፡ ዓመ ታት ፡ ከመ ፡ ይኩና ፡ ለሐጋይ ፡ ወለክረምት ፡ ለመ ፀው ፡ ወለተወን ፡ (ተረ ፡ ቄር ። መጽ ፡ ምስ) ።

**ረባዒ** ፤ (**ዒት ፡ ዕያን ፡ ያት**) ፤ አራት ፡ የሚ ያደርግ ፤ የሚል ፤ የሚከፍል ። ሰብአ ፡ ልዩን ፡ ይሰመዩ ፡ ረባዕያነ ፡ ወአከ ፡ ሠላስያነ ፡ (መጽ ፡ ምስ) ።

**መረብዕ** ፤ (**ዕት ፡ ዓን ፡ ዓት**) ፤ ዝኒ ፡ ከማሁ ፤ ረባዒ ።

**መርብዕት** ፤ አራት ፡ ጕን ፡ ወገን ፤ ገጽ ፡ ማእ ዝን ፤ ላንድነቱ ፡ አራት ፡ ክፍል ፤ ቅርጽ ፡ ገጽ ፡ ያለው ። እንተ ፡ መርብዕት ፡፡ መርብዕተ ፡ ማኅፈድ ፡፡ መርብ ዕተ ፡ መኣዝኒሃ ፡ ለዓለም ፡ ያንቀለቅል ፡፡ አሠረ ፡ ልቡ ፡ ለብእሲ ፡ መርብዕተ ፡ ያስተርኢ ፡ (፫ነገ ፡ ፯ ፡ ፴ ። ኩፋ ፡ ፵፰ ። ኪዳ ። ሚራ ፴፯ ፡ ፲፰) ።

**ተረብዐ** ፤ አራት ፡ ኾነ ፤ አራት ፡ ተባለ ፤ ካራት ፡ ተከፈለ ።

**ርቡዕ** ፤ (**ዓን ፡ ዓት ፡ ብዕት**) ፤ አራት ፡ የኾነ ፤ አራት ፡ ገጽ ፡ ያለው ፤ ምእዙን ፤ ዕሩየ ፡ ማእዝን ። ርቡ ዓዘ ፡ ገጽ ፡፡ መለኮተ ፡ አምላክ ፡ ኢርቡዕ ፡ አላ ፡ ሥሉስ ፡፡ ኀበ ፡ አርባዕቱ ፡ ርቡዓቲሁ ፡፡ ርብዕተ ፡ ትገብሩ ፡፡ ወ ርብዕት ፡ ይእቲ ፡ ሀገር ፡ በአምጣነ ፡ ኑኃ ፡ ወግድማ ፡ (አርጋ ፡ ፫ ። መጽ ፡ ምስ ። ሕዝ፵፫ ፡ ፲፯ ። ፵፰ ፡ ፳ ። ራእ፳፩ ፡ ፲፮) ።

**ርባዔ** ፤ አራት ፡ መኾን ፤ አራትነት ። ኢኮነ ፡ በ ሥላሴ ፡ ዘነአምን ፡ አላ ፡ በርባዔ ፡፡ እመ ፡ ቦ ፡ ዘያበ ውእ ፡ ርባዔ ፡ ውስተ ፡ ሥላሴ ፡ ውጉዝ ፡ ውእቱ ፡ (ተረ ፡ ቄር፲፰ ። ያዕ ፡ ዘእል) ።

**ሩባዔ** ፤ (**ዕያት**) ፤ ሩብነት ፤ ሩብ ፤ ካራት ፡ አ ንድ ፡ (አቡሻ ፡ ፴፯) ።

**ትርብዕት** ፤ አራትነት ፤ አራት ፡ እጅ ፤ አራት ፡ ቁጥሩ ፤ አራት ፡ ማእዝን ። ትርብዕተ ፡ ርቡዓን ፡ ኪሩ ቤል ፡ ወትሥልስተ ፡ አምላክ ፡ ዋሕድ ፡፡ ወሀበ ፡ ሎቱ ፡ ህየንተ ፡ አሐዱ ፡ ትርብዕተ ፡፡ ውስተ ፡ ትርብዕተ ፡ ዓ ለም ፡፡ በገበዋተ ፡ ጎል ፡ ዘበትርብዕት ፡ (ደራሲ ። ፊ ልክ ፡ ፫ ። ቅዳ ። አርጋ ፡ ፩) ።

**ረቡዕ** ፤ የዕለት ፡ ስም ፤ ቍጥር ። አራተኛ ፤ አ ራት ። ጾመ ፡ ረቡዕ ፡፡ አመ ፡ ዕለተ ፡ ዐሡሩ ፡ ወረቡዑ ፡፡ ረቡዐ ፡ መዋዕለ ፡ (ዘካ፰ ፡ ፲፱ ። ዘሌ፳፫ ፡ ፭ ። መሳ ፲፩ ፡ ፵) ።

**ራብዕ** ፤ (**ዕት**) ፤ አራተኛ ፤ ካራት ፡ አንድ ፤ ሩብ ፤ ርቦ ። ወራብዮሙ ፡ ይብዕል ፡፡ በራብዕት ፡ ዓ መተ ፡ መንግሥቱ ፡ ለኢዮአቄም ፡፡ ራብዕታ ፡ ለኢን ፡ (ዳን፲፩ ፡ ፪ ። ኤር፳፭ ፡ ፩ ። ዘፀ፳፱ ፡ ፵) ።

**ራብዓዊ** ፤ **ይ** ፤ (**ዊት ፤ ዪት ፤ ዒት**) ፤ ዝኒ ፡ ከማሁ ፤ አራተኛ ። ራብዓይ ፡ አርዌ ፡ (ዳን፯ ፡ ፲፱) ።

**ራብዒት** ፤ የቍጥር ፡ መደብ ፤ የኬክሮስ ፡ አራ ተኛ ፤ አንዱ ፡ ራብዒት ፡ ፰ ፡ ኃምሲት ፡ ይኾናል ፡ (አቡ ሻ ፡ ፲፩) ።

**ርብዕ** ፤ የጊዜ ፡ ቍጥር ፤ አራት ፤ ለስፍርም ፡ ይ ኾናል ። ርብዐ ፡ ለለ ፡ ዓመት ፡፡ ርብዐ ፡ በእመት ፡ (ኩፋ ፡ ፳፱ ። ዘፀ፳፯ ፡ ፰) ። በአርባዕቱ ፡ ፈንታ ፡ ርብዕ ፡ ይላል ፤ አያሰኝም ። ዕሥራ ፡ ወርብዐ ፡ (ስንክ ፡ ነሐ፴) ።

**አርባዕ** ፤ (የሴቶች) ፡ አራት ። አርባዐ ፡ አዋ ልድ ፡ ደናግል ፡፡ አርባዐ ፡ አህጉር ፡፡ ዘየሐውር ፡ በአ ርባዕ ፡ (ግብ፳፩ ፡ ፱ ። ኢ.ያ፳፩ ፡ ፲፰ ። ዘሌ፲፩ ፡ ፳) ። በ ራብዕ ፡ ፈንታ ፡ አርባዕ ፡ ይላል ፤ አያሰኝም ። ወበእንተ ፡ አርባዕሰ ፡ (ዓሞ፩ ፡ ፫) ።

**አርባዕቱ** ፤ **ት** ፤ (የወንዶች) ፡ አራት ፤ አራቱ ፤ አ ራተኛው ። ቱ ፡ አርቲክል ፡ ነው ። አርባዕቱ ፡ መኣዝነ ፡ ዓ ለም ፡፡ አርባዕቱ ፡ ነፋሳት ፡፡ አርባዕቱ ፡ አፍላጋት ፡፡ አርባዕቱ ፡ ጠባይዓት ፡፡ አርባዕቱ ፡ ወንጌላውያን ፡ (ፍ ፡ ነ ፡ ፱) ። በአኃዝ ፡ ብቻ ፡ ወይም ፡ እያቀናጀ ፤ ፬ ፡ ፬ቱ ፡ እያለ ፡ ይጥፋል ፤ አይገባም ፤ የጣፊ ፡ ስሕተት ፡ ነው ። ኹለተኛም ፡ አርባዕት ፡ በማለት ፡ ፈንታ ፡ አርባዕቱ ፡ ይ ላል ። አርባዕቱ ፡ እንስሳት ፤ አርባዕቱ ፡ ገጻት ፡፡ አርባ ዕቱ ፡ ምእት ፡ (ሕዝ፩ ፡ ፭ ፡ ፮ ። ዘፍ፳፫ ፡ ፲፮) ። ከአሐዱ ፡ እስከ ፡ ዐሠርቱ ፡ ያለ ፡ ቍጥር ፤ ኹሉ ፡ እንደዚህ ፡ ነው ፤ በገቢር ፡ ጊዜ ፡ ግን ፡ ካዕብነቱን ፡ ግእዝ ፡ ይወርሰዋል ። ይነብሩ ፡ ፈላስያነ ፡ አርባዕተ ፡ ምእተ ፡ ዓመተ ፡፡ ወር ኢኩ ፡ አርባዕተ ፡ አቅርንተ ፡ (ዘፍ፲፭ ፡ ፲፫ ። ዘካ፩ ፡ ፲፰) ።

**አርባዕት** ፤ የዜማ ፡ ቃል ፡ ትምርት ፤ አራተኛ ፡ ክፍል ፤ ከውዳሴ ፡ ማርያም ፡ (ድጓ) ።

**አርብዓ** ፤ (**፵** ፤ **መ**) ፤ የቍጥር ፡ ስም ፤ አርባ ፤ አራት ፡ ዐሥር ፡ ወይም ፡ ዐሥር ፡ ጊዜ ፡ አራት ። አርብዓ ፡ መዋዕለ ፡ ወአርብዓ ፡ ለያልየ ፡፡ አርብዓ ፡ ምእት ፡፡ አ ርብዓ ፡ ዓመት ፡ (ማቴ፬ ፡ ፪ ። ፲፭ ፡ ፴፰ ። መዝ ፡ ፺፬) ።

**አርብዓዊ** ፤ አርባኛ ፤ ካርባ ፡ አንድ ።

**ረጊብ** ፤ **በት** ፤ (**ረገበ ፡ ይረግብ ፡ ይር ግብ ። ዐረ ፡ ረጀበ**) ፤ መፍራት ፤ መሥጋት ፤ መታ

ወክ ፤ መርገብገብ ፤ መሽቈጥቈጥ ። መርገብ ፡ መላላት ፤ ጽንዕ ፡ ማጣት ፡ (ዐማርኛ) ።

**ርግብ** ፤ (ብ ፡ አርጋብ) ፤ በቁሙ ፤ የቤት ፡ ወፍ ፤ እንደ ፡ ደሮ ፡ የሚያረቧት ፡ ፈሪ ፡ ሥጉ ፤ ገር ፡ የዋህት ፡ ንጽሕት ፤ ሰላማዊት ። ኩኑ ፡ የዋሃነ ፡ ከመ ፡ ርግብ ። ይወርድ ፡ መንፈስ ፡ በአምሳለ ፡ ርግብ ። ርግብ ፡ ውእቱ ፡ መንፈስ ፡ ቅዱስ ፤ ለዘመዱ ፡ ኢየሱስ ፡ ክርስቶስ ። ማኅበረ ፡ አርጋብ ። እለ ፡ ይሠይጡ ፡ አርጋበ ፡ (ማቴ፳ ፡ ፳፮ ። ዮሐ፩ ፡ ፴፪ ። ቅኔ ። ሥር ፡ ጳኾ ። ዮሐ፪ ፡ ፲፬) ።



ርግብ ፡

**ረገደ** ፤—በቁሙ ፤—ረገፀ ።

**ረጊዝ** ፤ ዘት ፤ (ረገዘ ፡ ይረግዝ ፡ ይርግዝ ። ዐረ ፡ ረከዘ ፤ ቸከለ ፡ መደረ ። ዕብ ፡ ራጋዝ ፤ ተቈጣ ፡ ወገሸ) ፤ መውጋት ፤ መዘርከት ፤ መደደቅ ፡ መትከል ፤ መብሳት ፡ መንደል ፤ መቸከቸክ ፤ መግደል ። (ተረከዝ ፡ ማለት ፡ የረከዘ ፡ ዘር ፡ ነው) ። ረገዘ ፡ ውስተ ፡ ከርሡ ። እለ ፡ በኲናት ፡ ረገዝዎሙ ። አምጽእዎሙ ፡ ወርግዝዎሙ ፡ በቅድሜየ ፡ (መሳ፫ ፡ ፳፩ ። ኤር፲፭ ፡ ፫ ። ሉቃ፲፱ ፡ ፳፯) ።

—፤ ዘር ፡ መስጠት ፤ ማስረገዝ ፤ ማጥገብ ፡ ማንጠርዘዝ ፡ (ዐማርኛ) ።

—፤ ይዞ ፡ ማቆም ፤ መግታት ። መጽሐፍ ፡ ግን ፡ በረገዘ ፡ ፈንታ ፡ አርገዘ ፡ ይላል ፤ አያሰኝም ። ከመ ፡ ናርግዝ ፡ ሐመረነ ፡ (ግብ፳፯ ፡ ፲፯) ። ሐገዘን ፡ ተመልከት ፤ የዚህ ፡ ጎረ ፡ ቤት ፡ ነው ።

**አርገዘ** ፤ (ዐማርኛ) ፤ አረገዘ ፤ ተነፋ ፡ ዐበጠ ፤ ተንዘረጠጠ ።

**ተረግዘ** ፤ ተወጋ ። ነሥአ ፡ ሰይፈ ፡ ወተረግዘ ፡ ለሊሁ ፡ (፩ነገ ፡ ፴፩ ፡ ፬ ፡ ፭ ። ግብ፲፮ ፡ ፳፯) ።

**ርጉዝ** ፤ (ዛን ፡ ዛት ፡ ግዝት) ፤ የተወጋ ፤ ውግ ። ኢየሱስ ፡ ርጉዘ ፡ ገቦ ፡ (ደራሲ) ። ሕሩድ ፡ ጥቡሕ ፡ በማለት ፡ ፈንታ ፡ ርጉዝ ፡ ይላል ፤ ስሕተት ፡ ነው ። በገዐ ፡ ከመ ፡ ዘርጉዝ ፡ (ራእ፭ ፡ ፮) ።

—፤ በቁሙ ፤ ያረገዘ ፤ የተረገዘ ። (ተረት) ፤ የጨነቀው ፡ እርጉዝ ፡ ያገባል ። የታዘለ ፡ በለምድ ፤ የተረገዘ ፡ በሆድ ።

**ርግዘት** ፤ መውጋት ፤ መወጋት ፤ አወጋግ ፤ ውግታት ፤ ቍስል ፤ ዕትራት ። አርአየኒ ፡ ርግዘተ ፡ ገቦሁ ፡ ዘየማን ፡ (ዲድ ፡ ፴ ። ቅዳ ፡ ማሩ) ። ማርገዝ ፤ መረገዝ ፤ እርግዝና ፡ (ዐማርኛ) ።

**ተራገዘ** ፤ ተዋጋ ፤ ተዘራከተ ፤ በሰይፍ ፡ ተማታ ፤ ተራረደ ፤ ተቀራደደ ። ይትራገዙ ፡ ውሉደሙ ፡ (ሔኖ፲ ፡ ፲፱ ። ዳን፱ ፡ ፳፮) ።

**ራግዝ** ፤ ዛት ፤ መቃን ፤ መቃኖች ፤ የግራና ። የቀኝ ፤ ቀንአን ፡ እይ ። ራግዛተ ፡ ሙባእየ ። ሕቅፉ ፡ ራግዛቲሃ ፡ ወኅዋኅዊሃ ። እምደምከሙ ፡ ንዝሁ ፡ ራግዛተ ፡ ኆኅትየ ፡ ቤት ፡ (ምሳ፰ ፡ ፴፬ ። ቀሌ ። ደራሲ ። ዘፀ፲፪ ፡ ፯) ።



ራግዛት ፡

**ምርጕዝ** ፤ (ብ ፡ መራጕዝ) ፤ በቁሙ ፤ ደጋፋ ፡ በትር ፤ እንደ ፡ ባላና ፡ እንደ ፡ መቃን ፡ ኹኖ ፡ የሚደግፍ ። ምርጕዞሙ ፡ ውስተ ፡ እዴሆሙ ። ምርጕዘ ፡ ጻድቃን ። ምርጕዝ ፡ ለርሥኣንየ ፡ (ዘካ፰ ፡ ፬ ። ኪዳ ። ድጓ) ።

**ተመርጐዘ** ፤ ተመረ(ኰ)ጐዘ ፤ በትር ፡ ያዘ ፤ ተደገፈ ። ተመርጕዘ ፡ ባቲ ። አእዳዊከ ፡ እለ ፡ ይትመረጐዛ ፡ በትረ ፡ ወርቅ ። ዘእንበለ ፡ በትር ፡ ወተመርጕዞ ። እንዘ ፡ ይትመረጐዙ ፡ ሕገ ፡ ኦሪት ፡ ዘሙሴ ፡ (፪ነገ ፡ ፲፰ ፡ ፳፩ ። ደራሲ ። ቀሌ ። ተረ ፡ ቄር፳፪) ።

**ምርጕዝ** ፤ (ዛን ፡ ዛት ፡ ጕዝት) ፤ በትር ፡ የያዘ ፤ የተደገፈ ፤ የተመረጐዘ ፤ ባለምርጕዝ ፤ ድውይ ፡ ዐንካሳ ፡ ደካማ ።

**ረግሐ** ፤ (ትግሬ) ፤ መላ ፡ ተመላ ፤ ምሉእ ፡ ኾነ ፡ ቱደለደለ ፤ የጕድጓድ ፡ የመንገድ ። ረጋ ፡ ጸና ፡ ከረረ ፤ ደነገየ ፤ ድንጋይ ፡ ኾነ ። ረግዐን ፡ እይ ፤ የዚህ ፡ ጎር ፡ ነው ።

**መርግሕ** ፤ (ሓት ፤ መራግሕ) ፤ መርግ ፤ ቋጥኝ ፤ ናዳ ፡ ናደት ፤ ታላቅ ፡ ደንጊያ ። ወውእቱሂ ፡ መርግሐ ፡ እሳት ፡ ይወድቅ ፡ ዲቤሆሙ ፡ (ራእ ፡ ባሮ) ።

**አመርግሐ** ፤ ናደ ፡ ፈንቀለ ፤ አንከባለለ ፤ ገፋ ፡ መርግ ፡ ሰደደ ። አመርግሑ ፡ እብነ ፡ ላዕሌሆሙ ፡ (ዮዲ፯ ፡ ፲፪) ።

**ረጊም** ፤ ሞት ፤ (ረገመ ፡ ይረግም ፡ ይርግም ። ዕብ ፡ ራጋም ። ሱር ፡ ርጋም ፤ ወገረ ። ዐረ ፡ ረገመ ፤ ዐማ ፡ ነቀፈ) ፤ መርገም ፤ መስደብ ፤ ማሳደፍ ፡ ማርከስ ፤ ማቅለል ፡ ማኰሰስ ፤ ክፉ ፡ መመኘት ፤ ከበረከት ፡ ማውጣት ። ደንኑ ፡ ወኢትርግሙ ። ለምንት ፡ ይረግሞ ፡ ለእግዚእየ ። ዘይዘብጥ ፡ ወይረግም ፡ (ሮሜ፲፪ ፡ ፲፬ ። ፪ነገ ፡ ፲፮ ፡ ፱ ። ሲኖ ደ) ።

**ረጋሚ** ፤ (ሚት ፡ ምያን ፡ ያት) ፤ በቁሙ ፤ የሚረግም ፤ የሚሰድብ ፤ ሰዳቢ ። ረጋሚ ፡ ሰው ፡ ሰካሪ ፡ (፩ቆሮ ፡ ፭ ፡ ፲፩) ።

**መርገም** ፤ (ማት) ፤ በቁሙ ፤ ርግማን ፤ በ ድብ ፤ ክቡድ ፡ ቃል ። መጽአ ፡ መርገም ፡ ላዕሌነ ፡ ወመሐላ ። መሪር ፡ አፉሆሙ ፡ ወምሉእ ፡ መርገመ ። ኢይፃእ ፡ እምአፉሁ ፡ ቃለ ፡ መርገም ። ቡራኬ ፡ ወመርገም ፡ (ዳንኤ ፡ ፲፩ ። ሮሜ ፡ ፲፱ ። ዲድ ፡ ፲፯ ። ያዕ ፡ ፲) ።

**ተረግመ** ፤ ተረገመ ፤ ተሰደበ ፤ ማለ ፡ ተገዘተ ። ረገምኩ ፡ ወተረገምኩ ። አፍቅሮ ፡ ወኢትትረገም ፡ ላዕሌሁ ። ወእንዘ ፡ ይትረገም ፡ ወይምሕል ፡ (አዋል ። ቀሌ ። ማር፲፬ ፡ ፸፩) ። ተርጕመን ፡ እይ ፤ የዚህ ፡ ዲቃላ ፡ ነው ።

**ርጉም** ፤ (ማን ፡ ማት ፡ ግምት) ፤ በቁሙ ፤ የተረገመ ፤ ክፉ ፡ መጥፎ ፤ ውጉዝ ። ርጉመ ፡ ይኩን ። እመ ፡ ኢያውፃእክሙ ፡ እምኔክሙ ፡ ዘርጉም ። ሑሩ ፡ ርጉማን ፡ (ሚል፩ ፡ ፲፬ ። ኢያ፯ ፡ ፲፱ ። ማቴ፳፭ ፡ ፵፩) ።

**ርግመት** ፤ መርገም ፤ መረገም ፤ ርግማን ፤ ር ጉምነት ፡ (ሔኖ፭ ፡ ፮ ፡ ፯) ።

**ተራገመ** ፤ በቁሙ ፤ ተረጋገመ ፤ ተሳደበ ፤ ተሰ ዳደበ ፤ ተማማለ ። ተራገሙ ፡ ወተማሐሉ ፡ ወቦኡ ፡ ኪዳነ ፡ (ነሐ፲ ፡ ፳፱) ።

**ተርጐመ** ፤—በቁሙ ፤—ተረጐ ፡ ተ ።

**ረጊን** ፤ ኖት ፤ (ረገነ ፡ ይረግን ፡ ይር ግን ። ዐረ ፡ ረጀነ ፤ ረኩነ) ፤ አጥብቆ ፡ ማሰር ፤ መ ሳብ ፡ መገተር ፤ ማጥናት ፡ ማጠንከር ፤ የመርከብ ፡ የሸራዕ ። የረገዘን ፡ ፍች ፡ ተመልከት ፤ ባለቅኔዎች ፡ ግን ፡ ቀዘፈ ፡ ይሉታል ። ኵርጕነን ፡ እይ ፤ የዚህ ፡ ዲቃላ ፡ ነው ።

**ረግን** ፤ **ራግን** ፤ **አው ፡ ራግንት ፡ ናት** ፤ ታንኳ ፤ ፍልኳ ፤ ጀልባ ፤ ታናሽ ፡ መርከብ ። ራግንና ፡ ራ ግናት ፡ እንደ ፡ ራግዛት ፡ የብዙ ፡ ነው ፤ መጽሐፍ ፡ ግን ፡ ረግን ፡ ራግንት ፡ በማለት ፡ ፈንታ ፡ ራግናት ፡ ይላል ፡ (ግብ ፳፯ ፡ ፴ ፡ ፴፪) ። ውስተ ፡ ዘመጠነ ፡ ዝ ፡ ዐበየ ፡ ሠርም ከሙ ፡ ራግናተ ፡ ቃላትየ ፡ እጽሕቅ ፡ አሑር ። ያዐ ድዉ ፡ በድነ ፡ በራግናት ፡ (ተረ ፡ ቄር፬ ። ሥር ፡ ጳዣ) ።



ረግን ፡

—፤ የመርከብ ፡ ገመድ ፤ ሸራ ፤ ከምሰሶው ፡ ጋራ ። ራግ ናቲሃ ፡ ለሐመር ፡ ሑበለ ፡ ሥላሴ ፡ ዘኢይትበተክ ። ዘበራግናተ ፡ ወንጌሉ ፡ ቅዱስ ፡ (አርጋ ፡ ፩ና ፡ ፮) ።

**ረጊዕ** ፤ ዖት ፤ (ረግዐ ፡ ይረግዕ ፡ ይር ጋዕ ። ዕብ ፡ ራጋዕ) ፤ መርጋት ፤ መጽናት ፤ መግዘፍ ፤ እንደ ፡ ሞቃና ፡ እንደ ፡ ዳቦ ፡ እንደ ፡ ደንጊያ ፡ መኾን ፤ የፈሳሽ ። መጨመት ፡ ዝም ፡ ዕከም ፡ ጸጥ ፡ ማለት ፤ አለ መታወክ ፤ የልብ ፡ የሐሳብ ። ረግዐ ፡ ከመ ፡ ሐሊብ ፡ ል ቦሙ ። ይረግዕ ፡ ከመ ፡ ሠምዕ ። እምከመ ፡ ረግዐ ፡ አስሐትያ ። ይረግዕ ፡ ማይ ፡ ወይከውን ፡ ከመ ፡ እ ብን ፡ (መዝ ፡ ፻፲፰ ። ሚራ፵፫ ፡ ፲፱ ። ስንክ ፡ ኅዳ፲፱) ።

**ርጉዕ** ፤ (ዓን ፡ ዓት ፡ ግዕት) ፤ የረጋ ፤ የጠና ፤ የማይፈስ ፤ የማይታወክ ፤ ርጎ ፡ ዐይብ ። ደብር ፡ ርጉዕ ። አድባሪሃ ፡ ርጉዓን ። ነበርኩ ፡ ርጉዐ ፡ በደም ፡ ፀሠ ርተ ፡ አውራኅ ፡ እምዘርዐ ፡ ብእሲ ። በጽሐ ፡ ኀበ ፡ ዐ ቢይ ፡ ፈለግ ፡ ወረከቦ ፡ ርጉዐ ፡ (መዝ ፡ ፷፯ ። ድጓ ። ጥበ፯ ፡ ፪ ። ዮሴፍ) ።

**ርግዐት** ፤ መርጋት ፤ አረጋግ ፤ ርጋታ ፤ ጸጥታ ፤ ዕረፍት ፤ ሀድአት ፡ ጭምትነት ፡ (አዋል) ።

**አርግዐ** ፤ አረጋ ፤ አስረጋ ፤ አጸና ። አርጋዐከኒ ፡ ከመ ፡ ግብነት ። የዐቍር ፡ ማየ ፡ በማሕፀን ፡ ወያረ ግዕ ፡ ከመ ፡ ይኩን ፡ ሥጋ ። ናረግዖሙ ፡ ለማያት ፡ በ ውስተ ፡ ደመናት ፡ ወንፈኑ ፡ በረደ ፡ ወአስሐትያ ፡ ዲበ ፡ ምድር ፡ (ኢዮ፲ ፡ ፲ ። ቅዳ ፡ ግሩ ። ቀሌ) ።

**መርግዕ** ፤—መርግ ፡ ናደት ፤—ረግሐ ፡ መርግሕ ።

**ረጊፍ** ፤ ፎት ፤ (ረግፈ ፤ ረገፈ ፡ ይረ ግፍ ፡ ይርግፍ ። ረቀመ ፤ ሰርገወ) ፤ መርገፍ ፤ ማርገፍ ፤ ማውረድ ፤ የፍሬ ፡ የቅጠል ። መሣል ፡ መመ ስል ፤ አምሳል ፡ መርገፍ ፡ መሥራት ፤ አበባና ፡ ፍሬ ፡ ሐ ረግና ፡ ዛፍ ፡ እያስመሰሉ ፡ መበገር ፡ መንደፍ ፤ መታታት ፡ መጥለፍ ፤ በስፌት ፡ በቀለም ፡ ማስጌጥ ።

**ርጉፍ** ፤ (ፋን ፡ ፋት ፡ ግፍት) ፤ የረገፈ ፤ የተነጠፈ ፤ የተሸለመ ፡ የተጌጠ ፤ ዘፋም ፡ ቅጠላም ፤ ል ብስ ፡ ምንጣፍ ፡ ጸፍጸፍ ። ንጹፍ ፡ ወርጉፍ ፡ በሜላት ። ይነውም ፡ ውስተ ፡ ምስካቢሁ ፡ ፊላስ ፡ ዘርጉፍ ፡ በ ልብሰ ፡ ሜላት ፡ (አስቴ፩ ፡ ፮ ። ዮዲ፲ ፡ ፳፭) ።

**መርገፍ** ፤ (ዐማርኛ) ፤ ቀጭን ፡ ልብስ ፤ ጥሩ ፡ ግላስ ፤ በብዙ ፡ ዐይነት ፡ ሐር ፡ የተሠራ ፤ የተጠለፈ ፤ ሻሁራ ፡ አጣዋች ። (ግጥም) ፤ አባቶቻችን ፡ ለበቅሏቸው ፤ ኮርቻ ፡ ነበር ፡ ዐሳባቸው ፤ የዛሬ ፡ ልጆች ፡ እጅግ ፡ ኩሩ ፤ ለመርገፉ ፡ ነው ፡ የሚጥሩ ።

**ረጊፅ** ፤ ፆት ፤ (ረገፀ ፡ ይረግፅ ፡ ይር ግፅ ። ዐረ ፡ ረከፀ ። ዕብ ፡ ራቃድ ። ሱር ፡ ራቄድ) ፤ መርገጥ ፤ ማስረገጥ ፤ ማሸብሸብ ፤ ዳንኪራ ፡ መምታት ፤ መዝለል ፡ መፈንጨት ፤ መርገድ ፡ ማርገድ ፤ መርገድገድ ፤ እስክታ ፡ መውረድ ፤ መወዝወዝ ፡ መቅመ

ድመድ ። አስረጋጭ ፡ እንዲሉ ። ፀሐዩን ፡ ተመልከት ፤ የዚህ ፡ ጎረ ፡ ቤት ፡ ነው ።

—፤ መረጋገጥ ፡ መጠቅጠቅ ፤ ማልፋት ፡ ማበራየት ፤ በር ግጫ ፡ መምታት ፤ መሻለጥ ፤ የጭቃ ፡ የልብስ ፡ የነደ ፡ የቍርበት ፤ ለሰውም ፡ ይኸናል ። ባጥ ፡ ፊናጥ ፡ እንጣጥ ፡ ማለት ፤ ለመርገጥ ፡ የክብት ። ረገፀ ፡ ምድረ ። ረገፅ ፡ ውስተ ፡ ቀኖት ፡ በሊኅ ። ቦ ፡ ለዘረገፆ ፡ ወቦ ፡ ለዘወገሮ ። ረገፆ ፡ በእገሪሁ ፡ ወወድቀ ፡ ዲበ ፡ ምድር ፡ ወሞተ ። አው ፡ አብቅልተ ፡ ዘይረግፆ ፡ (ቀሌ ። ግብ፪ ፡ ፩ ። ክብ ፡ ነገ ። ስንክ ፡ የካ፲፪ ። ፍ ፡ ነ ፡ ፵፯) ።

ረጋጺ ፤ (ጺት ፡ ዕያን ፡ ያት) ፤ የሚረግጥ ፤ ረጋጭ ፤ ረጋጅ ፡ አርጋጅ ።

አርገፀ ፤ (ዐማርኛ) ፤ አስረገጠ ፤ መላልሶ ፡ ጠየቀ ፤ ወይም ፡ ተናገረ ፤ እውነቱን ።

ተረግፀ ፤ ተረገጠ ፤ በርግጫ ፡ ተመታ ፤ ተናቀ ፡ ተጠቀጠቀ ። እውነት ፡ ኾነ ፤ ልኩ ፡ ተገኘ ።

ርጉፅ ፤ (ፃን ፡ ፃት ፡ ግፀት) ፤ የተረገጠ ፤ ርግጥ ፤ እውነት ፤ ድርስ ፤ የነገር ፡ ልክ ።

ርግፀት ፤ መርገጥ ፤ መረገጥ ፤ አረጋገጥ ፤ ር ግጫ ። ኢያንትጉ ፡ እምሐቌሆሙ ፡ ርግፀተ ፤ እስከ ፡ መጠዉ ፡ ነፍሶሙ ፡ ክብርተ ፡ (ስንክ ፡ ሐም፴) ።

ተራገፀ ፤ ተራገጠ ፤ ተረጋገጠ ፤ በርግጫ ፡ ተ ማታ ። (ተረት) ፤ አህያ ፡ ላህያ ፡ ቢራገጥ ፡ ጥርስ ፡ አይሳበር ።

—፤ ተፈራገጠ ፤ ፍርግጥግጥ ፡ አለ ፤ የጻዕር ፡ (መሳ፪ ፡ ፳፭ ። ፩ ፡ ፳፮ ። አቡሻ ፡ ፵፮) ።

አስተራገፀ ፤ አራገጠ ፤ አፈራገጠ ፤ የጋኔን ። ይነፅኖ ፡ ወያስተራግፆ ፡ (ማር፩ ፡ ፳፮ ። ፱ ፡ ፲፰ ፡ ፳) ።

ትርጋፅ ፤ እግርጌ ፤ የእግር ፡ ቦታ ፤ መዘርጊያ ፤ መረጋገጫ ። ትርኣስ ፡ ወትርጋፀ ። ግበሩ ፡ ሎሙ ፡ ቅ ድመ ፡ በድኖሙ ፡ አርባዕተ ፡ መስቀለ ፤ በትርኣስ ፡ ወበትርጋፀ ፡ በየማን ፡ ወበፀጋም ፡ (ዮሐ፳ ፡ ፲፪ ። ግንዘ) ።

መርገፅ ፤ በቁሙ ፤ መርገጥ ፤ የበሬ ፡ ዕቃ ፡ ስም ፤ የወገል ፡ ወይም ፡ የከርፈስ ፡ ጠፍር ፤ ገበሬ ፡ ድግሩን ፡ ማረሻውን ፡ ከሞፈር ፡ ጋራ ፡ እየረገጠ ፡ የሚያስርበት ።

—፤ ርከብ ፤ የርካብ ፡ ጠፍር ። ተጽዕነ ፡ ላዕለ ፡ ፈረስ ፤ ወበጊዜሃ ፡ ተመትረ ፡ መርገፁ ፡ (ድር ፡ ሚካ) ።

መረግዕ ፤ መረግድ ፤ ርግድ ፤ ረገዳ ፤ ሽብ ሽባ ፤ ውዝወዛ ፤ ዳንኪራ ፡ እስክስታ ፤ ከበሮ ፡ ጭብጨባ ፡ ያለበት ። የፀሐይ ፡ ፀ ፡ አጠራር ፡ በዐረብ ፡ እንደ ፡ ምድ ራዊ ፡ ድ ፡ ስለ ፡ ኾነ ፤ መረግዕ ፡ በማለት ፡ ፈንታ ፡ መረ ግድ ፡ ይላል ። ንኡስ ፡ መረግድ ፤ ፀቢይ ፡ መረግድ ። መ ረግድስ ፡ አምሰለ ፡ ኪደተ ፡ ላሕም ፡ (ገድ ፡ አብርሀ) ።

ምርጋፅ ፤ መርገጫ ፤ መረገጫ ፤ ማስረገጫ ፤ ማርገጃ ፤ ማመርገጃ ፡ ቦታ ።

ረግረግ ፤ (ዐረ ፡ ሪግሪገት) ፤ በቁሙ ፤ ዐ ምዓም ፤ ውሃማ ፡ ቦታ ፤ ሲረግጡት ፡ የሚውጥ ፡ የሚያ ሠርግ ፡ የሚያረገርግ ፤ ፈሳ ፡ ቂጠማ ፡ ያለበት ፡ (ዐማርኛ) ። ከሐረገና ፡ ከመረገ ፡ ከ፪ቱ ፡ የወጣ ፡ ስም ፡ ነው ።

ረግረገ ፤ አ ፤ ተ ፤ ረገረገ ፤ አረገረገ ፤ ተረገ ረገ ። ኹሉም ፡ ዐማርኛ ፡ ነው ።

ረዳ ፤ (ዐረ ፡ ወርድ ። ዕብ ፡ ዌሬድ ። ሱር ፡ ዋርዳ ፤ ሮዳ ። ጽር ፡ ሮዶን) ፤ ያበባ ፡ ዕን ጨት ፤ አበባው ፡ እጅግ ፡ የሚያምር ፤ ደስ ፡ የሚያሰኝ ፤ ሽታው ፡ የሚጣፍጥ ፤ ልብ ፡ የሚመሥጥ ። ጽጌ ፡ ረዳ ። ንትቀጸል ፡ ጽጌ ፡ ረዳ ። ማርደም ፡ ድንግል ፡ ምዕ ዝት ፡ እምጽጌ ፡ ረዳ ፡ (ሢራ፳፬ ፡ ፲፬ ። ፶ ፡ ፰ ። ጥበ ፪ ፡ ፰ ። ደራሲ) ።

ረዲእ ፤ አት ፤ (ረድአ ፡ ይረድእ ፡ ይር ዳእ ። ዐረ ፡ ረደአ ። ዕብ ፡ ዓዘር ። ሱር ፡ ዕዘር) ፤ መርዳት ፤ ማገዝ ፤ መደገፍ ፤ ዋስ ፡ ጠበቃ ፡ መኾን ፤ አይ ዞኽ ፡ ማለት ፤ ማጽናት ፡ ማበርታት ፤ ማዳን ፡ መፈወስ ፤ መቤዠት ። ነጽር ፡ ውስተ ፡ ረዲኦትየ ። መጽአ ፡ ይር ድአኒ ። ዘረድአኒ ፡ ትምትሪ ፡ ርእሶ ። እረድኦ ፡ ለ ዛቲ ፡ ሀገር ። መጽአ ፡ ወረድኦሙ ፡ ለእለ ፡ ይትዓገ ሉሙ ፡ ሰይጣን ፡ (መዝ ፡ ፳፩ ። ዳን፲ ፡ ፲፫ ። ዮዲ፲፫ ፡ ፲፰ ። ኢሳ፴፩ ፡ ፩ ። ግብ፲ ፡ ፴፰) ። በረድአ ፡ ፈንታ ፡ አር ድአ ፡ ይላል ፤ ስሕተት ፡ ነው ። ዘአርድኦ ፡ ለጴጥሮስ ፡ አርድአኒ ፡ ሊተኒ ። በላኬ ፡ ታርድአኒ ። ያቃልሉከ ፡ ወያረድኡከ ። ታረድእ ፡ ምስሌሁ ፡ (ገላ፪ ፡ ፰ ። ሉቃ፲ ፡ ፵ ። ዘፍ፲፰ ፡ ፳፱ ። ፳፫ ፡ ፩) ።

ረዳኢ ፤ መርድኢ ፤ (ኢት ፡ እያን ፡ ያት) ፤ የሚረዳ ፤ የሚያግዝ ፤ ዐጋዥ ፡ ረዳት ፤ አይዞኽ ፡ ባይ ። ዘአልቦ ፡ ረዳኢ ። እስመ ፡ ረዳኢቱ ፡ ይእቲ ። ረዳእያን ፡ በቀትል ፡ (ኢዮ፳፱ ፡ ፲፪ ። ሢራ፴፯ ፡ ፳፱ ። ፩ዜና ፡ ፲፪ ፡ ፩) ። በመርድኢ ፡ ፈንታ ፡ መርዳኢ ፡ ይላል ፤ የተሳሳተ ፡ ነው ። መርዳእያኒሁ ፡ (ፍ ፡ ነ ፡ ፵፫ ፡ ፫) ።

መርድእ ፤ (እት ፡ አን ፡ አት) ፤ ዝኒ ፡ ከ ማሁ ። ንግበር ፡ ሎቱ ፡ መርድአ ፡ ዘከማሁ ። ኢየኃሥሥ ፡ መርድአ ። እስመ ፡ ዓለም ፡ መርድእ ፡ ውእቱ ፡ ለጻድቃን ፡ (ኩፋ ፡ ፫ ። ቅዳ ፡ ኢ.ጺ. ። ጥበ፲፯ ፡ ፲፯) ። ረድ ኤት ፡ በማለት ፡ ፈንታ ፡ መርድእ ፡ ይላል ፤ ስሕተት ፡ ነው ። በመርድእ ፡ እግዚአብሔር ። አዘዘ ፡ ይኀድግ ፡ መርድአ ፡ ህርቃኖስ ፡ (ፊልክ ፡ ፯ ። ዮሴፍ) ።

ረድእ ፤ (እት) ፤ ዝኒ ፡ ዓዲ ፡ ከማሁ ፤ በቁሙ ፤ አገልጋይ ፤ ተማሪ ፤ ደቀ ፡ መዝሙር ፤ ትምርትን ፡ የሚ ረዳና ፡ የሚያስረዳ ፤ አማኒ ፡ ምእመን ፤ እውነተኛ ፡ ክር ስቲያን ፤ የክርስቶስ ፡ ትምርት ፡ በጣም ፡ የገባው ፤ የተረ ዳው ። ጕንደየ ፡ ረድኡ ፡ ለአባ ፡ ሲሶይ ፡ ዐሠርተ ፡ አ ውራኀ ። ረድእ ፡ ዘያፈቅሮ ፤ ወውእቱ ፡ ረድእ ፡ ዘ ክነ ፡ ሰማዕተ ። ረድእሙ ፡ ለሐዋርያት ። አሐቲ ፡ ረድ እት ፡ እንተ ፡ ስማ ፡ ጣቢታ ፡ (ፊልክ ፡ ፵፯ ። ዮሐ፳፩ ፡ ፳፬ ፡ ፳፱ ። ሃይ ፡ አበ ። ግብ፱ ፡ ፴፮) ። ለመደን ፡ እይ ።

አርዳእ ፤ አርድእት ፤ ረደች ፤ ረዳቶች ፤ አ ገልጋዮች ፤ ተማሮች ፤ ደቀ ፡ መዛሙርት ፤ ምእመናን ።

ይቤልዎ፡አርዳኢሁ፤ወይቤሎሙ፡ለቢጹ፡አርዳእ። ሰብዓ፡ ወክልኤቱ፡ አርድእት። ወተሰምዩ፡ አርድ እት፡ ክርስቲያነ፡(ዮሐ፲፭፡ ፲፱፡ ፲፯። ቅዳ። ግብ፲፩፡ ፳፮)። በአግብርት፡ ፈንታ፡ አርድእት፡ ይላል፤ ስሕተት፡ ነው። ወቀሪቦሙ፡አርዳኢሁ፡ለበዓለ፡ገራህት፡(ማ ቴ፲፫፡ ፳፯)።

**አርድአ** ፤ አረዳ፤ አማጠነ፤ ርዱኝ፡ አለ፤ ረ ዳት፡ ለመነ፤ ቡታ፡ ሰደደ። ነሃቢ፡አርድአ፡ነሀብተ፡ ብሩር፡(ስንክ፡ ጥር፲፭)።

—፤ አስረዳ፤ ረዳት፡ ሰጠ፤ ርዱ፡ አለ፤ አስደራጊ።

—፤ አረዳ፤ አስረዳ፤ ገልጦ፡ ነገረ፤ አድራጊ። ጠየቀን፡ ተመልክት።

**አርዳኢ** ፤ አርጂ፤ አርጅ፤ አስረጅ።

**ተረድአ** ፤ ተረዳ፤ ታገዘ፤ ተጠረ፤ ጡረተኛ፡ ኾነ። ዘይትረዳእ፡በመኳንንተ፡ዝ፡ዓለም። እለ፡ ይትረድኡ፡በክልኤ፡ፍና፡(ሲኖ ዶ። ማር፡ ይሥ፯፡፱)።

—፤ ተረዳ፤ የሞት፡ ወሬ፡ ሰማ። ትምርት፡ ገባው፤ ዘ ለቀው፤ ተረዳው፡ (ዐማርኛ)።

—፤ ተረዳ፤ ታወቀ፤ ጕላ፡ ተገለጠ፤ ርግጥ፡ ኾነ፤ ወ ሬው፡ ትምርቱ።

**ርዱእ** ፤ (ኣን፡ ኣት፡ ድእት)፤ የተረዳ፡ የ ተረዳው፤ ትምርት፡ ነገር፡ የገባው፤ ዐጋዥ፡ ረዳት፡ ያ ለው። ዘየሐውር፡በጽድቅ፡ርዱእ፡(ምሳ፳፰፡፲፰)።

**ርድእት** ፤ መርዳት፤ መረዳት፤አረዳድ፤ረዳት ነት፤ ርዳታ፤ ዕገዛ፤ አይዞኽታ። መጽሐፍ፡ ግን፡ ርድ እት፡ ረዲኦት፡ በማለት፡ ፈንታ፡ ረድኤት፡ ይላል፤ አ ያሰኛም። በእንተ፡ ረድኤት፡ ሕሙም። ዘወፅአ፡ ለረድኤትክሙ፡(ግብ፱፡ ፱። ኤር፴፯፡ ፯)።

**ረድኤት** ፤ በቁሙ፤ርዳታ፤መልካም፡ ሥራ። በረድኤተ፡ኀይሉ። በረድኤተ፡እግዚ፡(መዝ፡ ፻፳። ኤፌ፫፡ ፯። ቈላ፱፡ ፲፱)።

—፤ ረዳት፤ ዐጋዥ፤ ባልንጀራ። እስ፡ መጽኡ፡ ረድ ኤተ፡ ለዳዊት። ረድኤትነ፡ በትምህርት። ወእሉ፡ ዳእሙ፡ ረድኤትየ። ረድኤቱ፡ ዘከማሁ፡ (፩ዜና፡ ፲፱፡ ፴፫። ፩ተሰ፡ ፫፡ ፱። ቈላ፬፡ ፲፩። ዘፍ፱፡ ፳)። ኀይል፡ ጽንዕ፡ ኵኵሕ፡ በማለት፡ ፈንታ፡ ረድኤት፡ ይላል፤ የመ ላሽ፡ ስሕተት፡ ነው። ወትበሊ፡ ረድኤቶሙ፡ በሲ ኦል፡እምክብሮሙ፡(መዝ፡ ፵፰)።

**ተራድአ** ፤ ተራዳ፤ ተረዳዳ፤ ተጋገዘ። ተራ ድኡ፡በበይናቲሆሙ። እኍ፡ምስለ፡እኍ፡ዘይት ራዳእ። ትትራድኦ፡ለምታ። ከመ፡ይትራድኡ፡ኅ ቡረ፡በየብስ፡ወበባሕር፤ወከመ፡ኢይትራድኡ፡ዘ ልፈ፡ ፀረ፡ ሮም፡ ላዕሌሆሙ፡ (አስቴ፱፡ ፲፯። ምሳ ፲፰፡ ፲፱። ፳፱፡ ፴። ዮሴፍ)።

**አስተራድአ** ፤ አራዳ፥ አረዳዳ፤ አስተጋገዘ።

**ሬዶን** ፤ (ጽር፡ ሬዶን)፤ ሠረገላ። ባለሐዲ ሶች፡ ግን፡ በቅሎ፡ ይሉታል። አፍራስ፡ ወሬዶን፡(ራ እ፲፰፡ ፲፫)።

**ረድይ** ፤ዮት፤(ረደየ፡ ይረዲ፡ ይርዲ። ዐረ፡ ረደይ፤ አበዘ)፤ ማበደር፡ ማለቃት፤ ባራጣ፡ በወለድ፡ መስጠት።

**ረዳዪ** ፤ (ዪት፡ ይያን፡ ያት፤ ደይት)፤ ባራጣ፡ አበዳሪ፤ ትርፍ፡ ፈላጊ።

**ተረድየ** ፤ ባራጣ፡ ወሰደ፤ ተበደረ። ወይም፡ ዐራጣውን፡ ተቀበለ፤ አበዳሪ። ኢትትረደይ፡እምኀበ፡ ቢጽከ፡ ኢርዴ፡ ወርቅ፡ወኢርዴ፡ እክል፡ (ዘዳ፳፫፡ ፳፡ ፳፩)።

**ተረዳዪ** ፤ ተበዳሪ፤ ዐራጣ፡ ከፋይ። ወይም፡ ተቀባይ፤ ባላራጣ።

**ርዱይ** ፤ (ያን፡ ያት፡ ዲት)፤ የተበደረ፤ ዐ ራጣ፡ ያለበት፤ ልቃኛ።

**ርድየት** ፤ ባራጣ፡ ማበደር፤ መበደር፤ ተበዳሪ ነት።

**ርዴ** ፤ ዐራጣ፤ የብድር፡ ወለድ፤ ፍድፋጅ፤ አ ታት፡ እልፍ፤ ትርፍ። ኢትንሣእ፡እምኔሁ፡ርዴ። ኢ ኀደጉ፡ነሚአ፡ርዴ። ወዘኢለቅሐ፡ወርቀ፡በርዴ፡ (ዘሌ፳፭፡ ፴፮። ኤር፲፭፡ ፲። መዝ፡ ፲፬)።

**ተራደየ** ፤ ተበዳደረ፤ ባራጣ፡ በወለድ፡ ተስ ማማ። ኢትትራደዮ፡(ዘፀ፳፪፡ ፳፭)።

**ረድፈ** ፤ረደፈ፤(ረዲፍ። ዕብ፡ ራዳፍ፤ ዴገነ)፤ ተከተለ፤ ተከታተለ፤ ተራደፈ፤ በሩጫ፡ በተራ።

**አርደፈ** ፤ አራደፈ፤ አከታተለ።

**ረድፍ** ፤ በቁሙ፤ ተራ፡ ጾታ፡ ዕርከን፡ ደራጃ።

**ራህርህ** ፤—ራራ፤—ራኅርኅ።

**ረዊድ** ፤ ዶት፤ (ሮደ፡ ይረውድ፡ ይ ሩድ። ዐረ፡ ራደ። ዕብ፡ ሩድ፤ ምልስ፡ ቅ ልስ፡ አለ፤ ታወከ፥ ተሸበረ)፤ መዝመት፤ መ ውጋት፤ አደጋ፡ መጣል፤ ማሸነፍ፤ መውረር፡ መዝረፍ፤ መከበብ፡ ከቦ፡ መያዝ፡ ማሰር፤ ቢያመልጥም፡ መከ ተል፡ ማሳደድ፡ ማባረር። ይረውዱ፡ወኢይክልዎሙ። ሮዱ፡ወቀተሉ፡ በይሁዳ። ወኢሎፍሊ፡ በጽሑ፡ ወሮዱ፡አህጉረ። ሮድዎ፡ወሰሐብዎ። ወደፈኖሙ፡ ማይ፡ለእለ፡ሮድዎሙ። እስመ፡ሮዳ፡ጸላኢ፡ለነ ፍስየ፡(ዘክ፲፡ ፩። ፪ዜና፡ ፳፰፡ ፲፰፡ ፲፰። ግብ፰፡ ፲፱። መዝ፡ ፻፩። ፻፵፪)።

**ረዋዲ** ፤ (ዲት፡ ድያን፡ ያት)፤ ዘማች፤ አ ጥፊ፤አሸናፊ፤ወራሪ፡ ዘራፊ፤ አባራሪ፤ ዠማና። ረዋዴ፡ በግዕ። ወረዋድያን፡ ኢይክሉ፡ ጸቢኦቶ፡ (አዋል። ድጓ)።

**ተሮደ** ፤ ተረውደ፤ ተያዘ፤ ተከበበ፤ ተወረረ፡ ተዘረፈ፤ ተዠመተበት።

**ርዉድ** ፤ (ዳን፡ ዳት፡ ውድ)፤ የተያዘ፡ የ ተከበበ፤ ድል፡ የኾነ፤ የተማረከ፡ ምርኮ።

**ሩደት** ፤ መዝመት፤መከበብ፤መከበብ፤ዘመቻ፡ ግሥገሣ፤ ወረራ፡ ዘረፋ፡ (አርጋ፡ ፯)።

**ሮዳስ**፤ የቀኖት ፡ ስም ፤ ዐምስተኛ ፡ ቀኖት ፤ ኊናተ ፡ ሐራዊ ፤ ወይም ፡ ዐምስተኛው ፡ ስቍረት ፤ ርግ ጃተ ፡ ገበ ። ሮዳስ ፡ ዘበትርጓሜሁ ፡ ኃምስ ፡ (መጽ ፡ ምስ) ። የሮዳስ ፡ ምስጢር ፡ መክበብ ፡ ስለ ፡ ኾነ ፤ ከሳ ደር ፡ ጋራ ፡ ይስማማል ፤ የሳደርን ፡ ፍች ፡ ተመልከት ።

**ሩዝ**፤ (ዐረ ፡ ሩዝ ፤ አሩዝ ። ሱር ፡ ሩዛ ። ዕብ ፡ አሬዝ) ፤ በቂመ ፤ ነጭ ፡ ጥሩ ፡ እኽል ፤ የነሬሞች ፡ ምግብ ፤ በእስያና ፡ በኤውሮፓ ፡ በዝቶ ፡ የሚዘራ ፡ የሚ በቅል ፤ ቈላ ፡ ሙቀት ፡ ውሃማ ፡ መሬት ፡ የሚወድ ።

**ራዛ**፤ ሩዛዊ ፤ ንጣቱ ፡ እንደ ፡ ሩዝ ፡ የኾነ ፤ ሩዝ ፡ የሚመስል ፡ አሞራ ፤ አንጭታ ፤ ሳቢሳ ፤ አንበጣ ፡ በል ፤ ሽመላ ፤ ወይም ፡ ሌላ ። ለእመ ፡ ጻዐደዉ ፡ ቋ ዓት ፡ ከመ ፡ ራዛ ። ተንዒቦ ፡ ይጻዐዱ ፡ እምራዛ ። ን ህብ ፡ ወራዛ ፡ (ኵፉ ፡ ፹፯ ። ስንክ ፡ ኀዳ፳፱ ። ፍ ፡ ነ ፡ ፵፩ ፡ ፪) ።



ራዛ ፡

**ሮዛ**፤ (ሮማይ) ፤ ረዳ ፤ ጽጌ ፡ ረዳ ።

**ረዊሕ**፤ ሖት ፤ (ሮሐ ፡ ይረውሕ ፡ ይ ሩሕ ። ዕብ ፡ ራዋሕ ። ዐረ ፡ ራሐ ፤ ዐረፈ ፤ ተነፈሰ) ፤ ማራገብ ፤ ማርገብገብ ፤ ማናፈስ ፡ መነስነስ ፤ መርጨት ፤ ማቃጨል ፤ የማርገቢያ ፡ የክንፍ ፡ የምንዛህ ፡ የጭራ ፡ የናብሊስ ፡ የመነሳንስ ። ዲያቆን ፡ ይረውሕ ። ዲያቆናት ፡ የዐውዱ ፡ ወይረውሑ ፡ በመራውሓት ፡ በአምሳለ ፡ አክናፈ ፡ ኪሩቤል ፡ (ኪዳ ። ፍ ፡ ነ ፡ ፲፪) ።

**ረዋሒ**፤ (ሒት ፡ ሕያን ፡ ያት) ፤ የሚያራ ግብ ፤ የሚያናፍስ ፤ የሚረጭ ፤ ነስናሽ ፤ አናፋሽ ።

**መርውሕ**፤ (ሕት ፡ ሓን ፡ ሓት) ፤ ዝኒ ፡ ከማሁ ፤ አናፋሽ ።

**ረውሕ**፤ (ዕብ ፡ ወዐረ ፡ ሩሕ) ፤ ነፋስ ፤ እ ስትንፋስ ፤ ነፍስ ፡ መንፈስ ፤ ዕረፍት ፡ ህድአት ። ዕሩፍ ፡ ህዱእ ፡ ወይም ፡ ርዉሕ ፡ በማለት ፡ ፈንታ ፡ ረውሕ ፡ ይ ላል ። እንጦንዮስ ፡ ረውሕ ፡ (ስንክ ፡ የካ፳፩) ።

**መረውሕ**፤ (ብ ፡ መራውሕ ፤ ሓት ። ዐረ ፡ ሚርወሕ ፤ ሚርወሐት ። ሱር ፡ ማርዋ ሕታ) ፤ ማርገቢያ ፤ ማናፈሻ ፤ መነሳንስ ፤ ጭራ ፤ የጭራ ፡ ዐይነት ፡ ኹሉ ። ይቅሙ ፡ ክልኤቱ ፡ ዲያቆናት ፡ በገበ ዋተ ፡ ምሥዋዕ ፡ ወየአኀዙ ፡ መራውሓተ ፡ ዘግቡራት ፡ እምግብር ፡ ልሙጽ ፡ ወይስድዱ ፡ ጽንጽንያተ ፡ (ፍ ነ ፡ ፲፪) ።



መረውሕ ፡

**መርዋሕት**፤ (ታት ። ቅብጥ) ፤ መረዋ ፤ መረዋት ፤ ቃጭል ፤ ታላቅ ፡ ታናሽ ፡ መካከለኛ ፡ በያይነቱ ። መርዋሕት ፡ ዘይሰማዕ ፡ ድምፁ ፡ እስከ ፡ ነዋኅ ፡ (አዋል) ።



መርዋሕት ፡

**ምርዋሕ**፤ (ሓት) ፤ ምዝራቅ ፤ ምንዛህ ፡ የ ውሃ ፡ መርጫ ፤ መፈንጠቂያ ። ይሰድዎ ፡ ኀበ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ በመኃትው ፡ ወበመጻውዕት ፡ ወበምር ዋሕ ፡ ወበድባብ ። ወትረቂ ፡ መቃብሪሁ ፡ በማይ ፡ (ግንዘ) ።

**ተሮሐ**፤ ተራገበ ፤ ተርገበገበ ፤ ተነሰነሰ ፤ ተረጨ ። መጽሐፍ ፡ ግን ፡ ተሮሐ ፡ ተረውሐ ፡ በማለት ፡ ፈንታ ፡ ተራውሐ ፡ ይላል ፤ አያሰኝም ። ዘተጸፍዐ ፡ መልታሕቱ ፡ ተሰፅለ ፡ ወነበረ ፡ በየማነ ፡ አቡሁ ፡ እንዘ ፡ ይትራዋሕ ፡ ሎቱ ፡ አክናፈ ፡ እሳት ፡ ዘሐራ ፡ ሰማይ ፡ (መጽ ፡ ምስ) ።

**ረውይ**፤ ዮት ፤ (ረወየ ፡ ይረዊ ፡ ይር ወይ ። ዕብ ፡ ራዋህ ። ዐረ ፡ ረዊየ ። ሱር ፡ ር ዊይ) ፤ መርካት ፤ ጠጥቶ ፡ መጥገብ ፤ አብዝቶ ፡ መጠ ጣት ፤ መራስ ፤ ጥምን ፡ ማብረድ ፤ ማራቅ ፡ ማስወገድ ። ትሰትዩ ፡ ወኢትረውዩ ። እለ ፡ ይሰትዩኒ ፡ ኢይረው ዩኒ ። እምከመ ፡ ረወየት ፡ መሬት ። ወይረውዩ ፡ እ ምጠለ ፡ ቤትከ ። ይረውዩ ፡ አድባረ ፡ በድው ፡ (ሐጌ ፩ ፡ ፮ ። ዓሞ፬ ፡ ፰ ። ሚራ፳፬ ፡ ፳፩ ። መቃ ። መዝ ፡ ፴፭ና ፡ ፷፬) ። በረወየ ፡ ፈንታ ፡ ተረወየ ፡ ይላል ፤ ስሕተት ፡ ነው ። ሀሰዉ ፡ እለ ፡ ኢተረወዩ ። ንትረወይ ፡ እምዘመድ ኅን ፡ አንቅዕት ። እለ ፡ ይትሬወዩ ፡ ሕገ ፡ (ተረ ፡ ቄር ። ሚራ፪ ፡ ፲፯) ።

**ረዋዪ**፤ (ዪት ፡ ይያን ፡ ያት) ፤ የሚረካ ፤ ረኪ ፤ ብዙ ፡ የሚጠጣ ፤ ጠጭ ።

**አርወየ**፤ አረካ ፤ አብዝቶ ፡ አጠጣ ፤ አጠገበ ፤ አራስ ፡ አረሰረሰ ፤ አጨቀየ ፤ ነከረ ። ጽዋዕከኒ ፡ ጽኑዕ ፡ ወያረዊ ። ሐወጽካ ፡ ለምድር ፡ ወአርወይካ ፤ አር ውዮ ፡ ለትለሚሃ ። ያረዊ ፡ ነፍሶ ፡ እምቃለ ፡ እግዚ ። ፈትለ ፡ አርዊ ፡ (መዝ ፡ ፳፪ ። ፷፬ ። ስንክ ፡ ጥቅ፲፯) ።

**መርወይ ፤** (ብ ፡ መራውይ) ፤ የውሃ ፡ ዕቃ ፤ መጠጫ ፤ ማጠጫ ፤ ቅል ፡ መንቀል ። እምብዝኀ ፡ ንዋይ ፡ ጽድቀ ፡ ዘአፍቀርከ ፤ ሐወ ፡ ዘዐቈርከ ፡ በመርወይ ፡ (ድጓ) ።

**ተረውየ ፤** ተጠጣ ፤ ተጠገበ ፤ ዝናሙ ፡ ጠሉ ፡ ውሃው ፡ ጠበሉ ።

**ርዉይ ፤** (ያን ፡ ያት ፤ ዊት ፡ ውይት) ፤ የረካ ፡ የጠገበ ፤ የተጠገበ ። ርዉይ ፡ ውእቱ ፡ ዘሉ ፡ ምድር ። ገነት ፡ ርውይት ። ሜስ ፡ ወምዝር ፡ እለ ፡ ርዉያን ፡ ኀበ ፡ ፆኩር ፡ (ዘፍ፲፫ ፡ ፲ ። ኢሳ፶፰ ፡ ፲፩) ።

**ርውየት ፤** መርካት ፤ ማርካት ፤ አረካካ ፤ ርካታ ፤ የውሃ ፡ ጥጋብ ።

**ሩማ ፤ አው ፡ አሩማ ፤** ስመ ፡ ሀገር ፤ በይሁዳ ፡ ክፍል ፡ ያለች ፤ የቡኬም ፡ አጠገብ ፡ (፱ነገ ፡ ፳፫ ፡ ፴፮ ። መሳ፱ ፡ ፵፩) ።

**ሮም ፤ ሮሜ ፤ ሮምያ ፤** የመዲና ፡ ስም ፤ የሮማውያን ፡ ከተማ ፤ ሮምሎ ፡ ያቀናት ፡ የቈረቈራት ።

**ሮማን ፤** (ናት ። ዕብ ፡ ሪሞን ። ሱር ፡ ሩማና ። ዐረ ፡ ሩማን) ፤ በቁሙ ፤ የተክል ፡ ዕንጨት ፡ ስም ፤ ሕንባቡ ፡ ቅርፍቱ ፡ ቀይ ፡ ደባባ ፤ ውስጡ ፡ ጽፍቅ ፤ ፍሬ ፡ የተመላ ፤ ቅንጣቱ ፡ የበቈሎ ፡ ዐይነት ። ታሕተ ፡ ሮማን ። በለስ ፡ ወሮማን ፡ ወዘይት ። ፈረየ ፡ ሮማን ፡ (፩ነገ ፡ ፲፬ ፡ ፪ ። ሐጌ፪ ፡ ፲፱ ። ማሕ፯ ፡ ፲፭ ። ፮ ፡ ፲፫) ። በሮማን ፡ አምሳል ፡ የተሠራ ፡ ሌላውም ፡ ኹሉ ፡ ስለ ፡ መልኩ ፡ ሮማን ፡ ይባላል ። ሮማን ፡ ዘያክንት ። ሮማነ ፡ ወርቅ ። ወሮማናት ፡ ባዐለ ፡ ከታፊት ፡ (ዘፀ ፳፰ ፡ ፴፫ ፡ ፴፱ ። ኤር፶፪ ፡ ፳፪ ፡ ፳፫) ።

ሮማን ፡

**ረዊጽ ፤ ጾት ፤** (ሮጸ ፡ ይረውጽ ፡ ይሩጽ ። ዕብ ፡ ራጽ ። ሱር ፡ ርሄጥ) ፤ መሮጥ ፤ መፈርጠጥ ፤ መሸሽ ፡ መኰብለል ፤ ማምለጥ ፤ መብረር ፡ መክንፍ ፤ መፍጠን ፡ መቀልጠፍ ፤ መቸኰል ፡ መጣደፍ ፤ ቶሎ ፡ ማለፍ ፤ ባክኜ ፡ በሥራ ፡ ፈጣን ፡ መኾን ። አእጋርኪ ፡ እለ ፡ ጻመዋ ፡ በረዊጽ ። ይረውጹ ፡ ከመ ፡ ሀየል ። ወሮጸ ፡ ኀቤሁ ፡ በኀይል ። ሩጹ ፡ ወኢትቁሙ ። ንሩጽ ፡ በትዕግሥት ። ወሮጸ ፡ አብርሃም ፡ ኀበ ፡ ላሕ ፡ (ደራሲ ። ኢሳ ፵፩ ፡ ፯ ። ዳን፰ ፡ ፯ ። ኤር፬ ፡ ፯ ። ዕብ፲፪ ፡ ፩ ። ዘፍ፲፰ ፡ ፯) ። ሰሮጸን ፡ ተመልከት ፤ የዚህ ፡ ዘር ፡ ነው ፤ ስንቀው ፡ የነቀው ፡ ዘር ፡ እንደ ፡ ኾነ ።

**ረዋጺ ፤** (ጺት ፡ ጽያን ፡ ያት) ፤ የሚሮጥ ፤ ሯጭ ፤ ፈጣን ፤ ቀልጣፋ ። ኢይክል ፡ ረዋጺ ፡ አምሥጦ ። አፍራስ ፡ ረዋጽያን ። ኄር ፡ ረዋጺ ። መላእክት ፡ ረዋጽያን ፡ (ዓሞ፪ ፡ ፲፬ ። ፮ ፡ ፯ ። ምሳ፳፬ ፡ ፵፱ ። ኢሳ፲፰ ፡ ፪) ።

**ርዉጽ ፤** (ጻን ፡ ጻት ፡ ውጽት) ፤ የሮጠ ፤ የሚሮጥ ፤ ችኩል ፤ ፈጣን ። ለኵሉ ፡ ህላዌ ፡ ርዉጽ ። ውስተ ፡ ሚጠት ፡ በሕቁ ፡ (ቄር) ። ርዉጸ ፤ ሩጦ ፡ ገሥግሦ ፤ ፈጥኖ ፡ ቸኵሎ ፤ እየሮጠ ፡ እየጋለበ ። ይመጽኡ ፡ መላእክት ፡ ርዉጸ ፡ (ሕዝ፩ ፡ ፲፬) ።

**ሩጸት ፤** መሮጥ ፤ አሯሯጥ ። ሩጫ ፡ ፍጥነት ፤ ኀይል ፡ ትሩፋት ፤ መልካም ፡ ሥራ ። ሩጸተ ፡ አፍራስ ። ሩጸተ ፡ እንስሳ ። መጠነ ፡ ሩጸተ ፡ መብርቅት ። እለ ፡ ትጋደሉ ፡ ሠናየ ፡ ገድለ ፡ ወፈጸሙ ፡ ሩጸቶሙ ፡ ወሞቱ ። ሠናየ ፡ ሩጸት ፡ (ኤር፰ ፡ ፲፯ ። ጥበ፲፯ ፡ ፲፰ ። መጽ ። ምክ ። ዲድ ፡ ፳፯ ። አርጋ ፡ ፩) ። በሩጸት ፡ ፈንታ ፡ ምርዋጽ ፡ ይባል ፤ ስሕተት ፡ ነው ። ፈጸምከ ፡ ምርዋጸከ ። ተፈጸመ ፡ ምርዋጺ ። ረበየ ፡ ምርዋጸ ፡ ለምህሮ ፡ ወለገሥጾ ፡ (ግንዘ ። ስንክ ፡ መጋ፳ ። ነሐ፯) ።

**አሮጸ ፤** አሮጠ ፤ አስሮጠ ፤ አስቸኰለ ፤ አጣደፈ ፤ ነዳ ፡ አባረረ ። አሮጺ ፡ አፍራሲሆሙ ። ያረውጾ ፡ ጋኔኑ ። ያረውጸሙ ፡ ለሐንካሳን ። ይትራድኡ ፡ ለአርውጾ ፡ ሐመር ፡ (፩ዕዝ ፡ ፪ ፡ ፴ ። ሉቃ፰ ፡ ፳፱ ። ቀሌ ። መጽ ፡ ምክ) ።

**መርወጺ ፤** የሚያሮጥ ፤ የሚያስሮጥ ፤ አሯሯጭ ፡ አስሯጭ ፤ ጋላቢ ። መርወጼ ፡ አፍራስ ፡ (ቄስጠ) ።

**ምርዋጽ ፤** (ጻት) ፤ መሮጫ ፤ ማስሮጫ ፤ የሩጫ ፡ ቦታ ፤ ሜዳ ፡ ስታታ ። ምርዋጸ ፡ ብእሲ ። ምርዋጸ ፡ ፈረስ ። ሖሩ ፡ ኀበ ፡ ምርዋጻት ፡ (ግብ፩ ፡ ፲፪ ። ዲድ ፡ ፴፫ ። አፈ ፡ ተ፯) ።

**ተራወጸ ፤** ተራወጠ ፤ ተሯሯጠ ፤ ተሽቀዳደመ ። እምከመ ፡ መጽአ ፡ ድምፀ ፡ ጸባኢት ፡ የኀድጉ ፡ ኵሎ ፡ ወይትራወጹ ፡ ለቀትል ። ሕፃናት ፡ እለ ፡ ይትራወጹ ፡ ማእከለ ፡ ጉባኤ ። አ ፡ አንስት ፡ ዐቀባ ፡ ውሉደክን ፡ ከመ ፡ ኢይትራወጹ ፡ ዝየ ፡ ወዝየ ፡ (አፈ ፡ ተ፭ና ፡ ፯ ። ቄስጠ ። ማር፱ ፡ ፳፭) ።

**ረዋቅ ፤** (ዕብራ ፡ ወዐረ) ፤ ባሕታዊ ፡ ፈላስፋ ፤ ሚስት ፡ የሌለው ፤ ስመ ፡ ጥር ፡ ታላቅ ፤ የፈላስፎች ፡ ሊቅ ።

**ረዋቃዊ ፤ ዪ ፤** (ውያን ፤ ይያን ። ዐረ ፡ እሩዋቂዩን) ፤ የረዋቅ ፡ ወገን ፤ ደቀ ፡ መዝሙር ፤ ወይም ፡ ትምርት ፡ ሕግ ፡ ሥርዐት ። ወካልኣን ፡ ይብሙዩ ፡ ረዋቃውያነ ፡ (ግብ፲፯ ፡ ፲፰) ።

**ሮስ ፤**—ወንድ ፡ ልጅ ፤—ኀሪስ ፡ ኀረሰ ።

**ረዊት ፤ ቶት ፤** (ሮተ ፡ ይረውት ፡ ይሩት ። ዐረ ፡ ረተ ፤ ዐረተ) ፤ መወልወል ፤ መጥረግ ፤ ማሸት ፡ መፈግፈግ ፤ ማጠብ ፡ መፈተግ ፤ ንጹሕ ፡ ጥሩ ፡ ማድረግ ። በማይ ፡ ኢኀፀቡኪ ፡ ወበጼው ፡ ኢሮቱኪ ፡ (ሕዝ፲፮ ፡ ፬) ።

**ሮጸሊም** ፤ (ጽር፡ ሮፖፖሊ። ዕብ፡ ሮክሊም) ፤ ነጋዶች ፤ የንጋዴ፡ ዐጣሮች ፤ አገር፡ ላገር፡ መንደር፡ ለመንደር፡ እየዞሩ፡ ታናናሽ፡ ነገር፡ የሚሼጡ ፤ የሚሸቅጡ፡ (ንሐሮ፡ ፴) ።

**ራዛ** ፤—ነጭ፡ **አሞራ** ፤—ሩኀ፡ ረወዘ።

**ረዚም** ፤ **ሞት** ፤ (ረዝመ፡ ይረዝም፡ ይርዘም። ዕብ፡ ራዛም። ሱር፡ ርማዝ። ዐረ፡ ረመዘ) ፤ ቀጺብ ፤ መጥቀስ ፤ ባይን፡ ማመልከት። መርዘም፡ ማደግ፡ መግነን ፤ መክበድ፡ መታበይ፡ መኰራት፡ መቈነን ፤ ራስ፡ መዞር ፤ መስከር፡ እንዑዝ፡ መኾን። በመጥቀስም፡ የመርዘም፡ ምስጢር፡ አለበት ፤ (ተረት) ፤ ቀንዱ፡ ሰማይ፡ ጠቀስ ፤ ጭራው፡ ምድር፡ አበስ። ደመና፡ ጠቅሶ ፤ ከሰበው፡ ደርሶ። እለ፡ ይገፈትዑ፡ ደመናተ፡ (አዋል) ።

**ረዛሚ** ፤ (ሚት፡ ምያን፡ ያት) ፤ የሚጠቅስ ፤ ጠቃሽ ፤ ረዥም ፤ ትቢተኛ ፤ ሰካር ።

**ርዙም** ፤ (ማን፡ ማት፡ ዝምት) ፤ የረዘመ ፤ ረዥም ፤ መለሎ ፤ ቁመታም ፤ ምጡቅ። ስኩር ፤ እንዑዝ። በርዙም፡ ፈንታ፡ መርገዝም፡ ይላል ፤ አያስኝም። በአ፡ ኀቤየ፡ ሰይጣን፡ ወረሰየ፡ ከመ፡ መርዝመ፡ ወይን፡ ወአርስየ፡ ዐቲበ፡ ገጻ፡ ወሆከ፡ ኀሊናየ፡ (ቀሌ) ።

**ርዝመት** ፤ በቁሙ ፤ መርዘም ፤ አረዛዘም ፤ ረዥምነት ፤ ርዝማኔ ፤ ልዕልና ፤ ቁመት፡ (ዐማርኛ) ።

**መርዘም** ፤ ትዕቢት ፤ ኵራት ፤ ነቀጥቃጥ ፤ እንባዜ ፤ እስክታ ፤ ፃሕስ ፤ ሑሰተ፡ ርእስ። እምስካር፡ ይትወለድ፡ ምርዓት፡ ወዝሙት፡ ወሥሥዕት፡ ፅርፈት፡ ወትዕቢት፡ ወመሐላ፡ በሐሰት፡ ወኢያሠንዮ፡ በዝንጋዔ፡ ወመርዘመ፡ ርእስ። ቅንአት፡ ወፍትወት፡ አንስት፡ ልበ፡ ጠቢባን፡ ያማስን ፤ ወዓዲ፡ ስካር፡ ወዘፈን፡ ወመርዘመ፡ ርእስ፡ (ቀሌ) ።

**አርዘመ** ፤ አረዘመ ፤ አስረዘመ ፤ ረዥም፡ ምጡቅ፡ አደረገ ፤ አስደረገ። ርዝመት፡ ለቁመትም፡ ለሞላልነትም፡ ይነገራል ፤ ምጥቀት፡ ግን፡ ለቁመት፡ ብቻ፡ ነው።

**ርሒብ** ፤ **ቦት** ፤ (ርሕበ፡ ይርሕብ፡ ይርሐብ። ዕብ፡ ራሐብ። ዐረ፡ ረሒበ) ፤ መስፋት ፤ መዘርጋት ፤ ሰፊ፡ ዝርግ፡ ሜዳ፡ ወርዳም፡ ጕናም፡ መኾን። ርሕበት፡ አረፍት፡ ባቢሎን። ከመ፡ ይርሐብ፡ እምላዕሉ። ርሕበ፡ አፉየ። ሠብሐ፡ ወገዝፈ፡ ወርሕበ፡ (ኤርሸ፰፡ ፶፰። ሕዝ፴፩፡ ፯። ፩ነገ፡ ፪፡ ፩። ዘዳ፴፪፡ ፲፭)። በርሕበ፡ ፈንታ፡ ተርሕበ፡ ይላል ፤ ስሕተት፡ ነው። እምቅድመ፡ ይትረሐብ፡ ኑኀ፡ አየራት። ስፍሐ፡ ምድር፡ እምቅድመ፡ ይትረሐብ፡ (ቅዳ፡ አፈ። መጽ፡ ምስ። ኤርሸ፡ ፳፪) ።

**ርሒብ** ፤ (ባን፡ ባት፡ ሕብት ፤ ረሓብ) ፤ ስፉሕ ፤ ሰፊ ፤ ዝርግ ፤ ወርዳም ፤ ጕናም ፤ ወርድ፡ ትልቅ። ምድር፡ ርሒብ። ርሒበ፡ ልብ። ወትእዛዝከሰ፡ ርሒብ፡ ፈድፋደ። ፍኖት፡ እንተ፡ ትወስድ፡ ውስተ፡ ሀጕል፡ ርሕብት፡ ይእቲ። በምሕረቱ፡ ርሒብት። ወምድርሰ፡ ረሓብ። ዛቲ፡ ባሕር፡ ዐባይ፡ ወረሓብ፡ (ኢሳ፴፡ ፱። አፈ፡ ተጸዋና፡ ፸፪። መዝ፡ ፻፲፰፡ ፺፮። ፻፫፡ ፳፭። ዘፍ፴፬፡ ፳። መሳ፲፰፡ ፲) ።

**ርሕበት** ፤ መስፋት ፤ አሰፋፍ ፤ ሰፊነት ፤ ወርዳምነት ፤ ስፋት ፤ ወርድ። ፈቂዶ፡ ርሕበተ፡ መካን፡ ለጸብእ። ትዕግሥት፡ ወርሕበተ፡ እንግድዓ፡ (ዮሴፍ። ፈላስ) ።

**ርሕብ** ፤ **ራሕብ** ፤ ስፋት ፤ ወርድ ፤ ጕን። ኑኃ፡ ወርሕባ። ርሕበ፡ ምድር። ርሕበ፡ ዓለም፡ ኢያገምራ። ምንትኑ፡ ራሕቡ፡ ወኑኁ። በራሕቡ፡ ለቅሊም። ራሕበ፡ ዘባኑ። ውስተ፡ ራሕበ፡ ልብከ፡ (ዘፍ፲፫፡ ፲፯። ፲፫፡ ፲፯። ኢሬሮ፡ ፲፰። ሰንክ፡ የካ፳። ኢዮ፲፩፡ ፰፯። ምሳ፯፡ ፫) ።

**አርሐበ** ፤ አሰፋ ፤ ዘረጋ ፤ ሰፊ፡ አደረገ ፤ አበዛ። ለያርሕብ፡ ብሔረ። አርሐበ፡ ለከ፡ ደወለከ። አርሕቢ፡ መታክሊ፡ ዘደብተራኪ። ከመ፡ ያርሕቡ፡ ንኀሳተ። አርሐበት፡ ሎቱ፡ ብእሲ፡ እምዳማሁ፡ (ዘፍ፱፡ ፳፯። ዘዳ፴፪፡ ፳። ኢሳ፶፬፡ ፪። ዮሴፍ። ጥበ፲፡ ፲) ።

**አርሓቢ** ፤ **መርሐቢ** ፤ (ሕብ) ፤ የሚያሰፋ ፤ አስፊ ፤ ሰፊ፡ አድራጊ።

**መርሕብ** ፤ (ብ፡ መራሕብት) ፤ ሰፊ፡ ቦታ ፤ ሜዳ ፤ ስታታ ፤ ገባያ፡ ጉባይ ፤ አደባባይ። ወአውፅአኒ፡ ውስተ፡ መርሕብ። ነገድር፡ ውስቴ፡ መርሕብ። መኳዝንኒ፡ መራሕብት፡ (መዝ፡ ፲፯። ዘፍ፲፱፡ ፪። ማቴ፮፡ ፭) ።

**ርሕበ** ፤—ተራበ ፤—ርኅብ፡ ርኅበ።

**ርሒይ** ፤ **ዮት** ፤ (ርሕየ፡ ይርሒ፡ ይርሐይ። ዕብ፡ ሪያሕ። ሱር፡ ራያሕ። ዐረ፡ ራሐ) ፤ መሽተት ፤ ማሽተት ፤ ማነፍነፍ ፤ ማፈንፈን ፤ ባፍንጫ፡ መሳብ ፤ መማግ።

**ረሓዪ** ፤ (ዪት፡ ይያን፡ ያት) ፤ የሚሸት ፤ የሚያሸት ፤ ሸታች ፤ አሽታች።

**ርሔ** ፤ (ሕያት) ፤ መልካም፡ ጥሩ፡ ሽታ ፤ የሽቱ፡ መዐዛ ፤ ልብ፡ የሚመሥጥ ፤ ላፍንጫ፡ የሚጥም፡ የሚጣፍጥ። ወጼና፡ መዐዛ፡ ሠናይ፡ ዘይጼኑ፡ እምኵሉ፡ ርሔ፡ አፈው፡ (ቀሌ። አርጋ። መጽ፡ ምስ)። መደብ፡ ወይን፡ በማለት፡ ፈንታ፡ ርሒ፡ ይላል ፤ የተሳሳተ፡ ነው። መላትሒሁ፡ ከመ፡ ርሔ፡ አፈው። ኣበትየከ፡ እምርሔ፡ አፈውየ፡ (ማሕ፭፡ ፲፫። ፰፡ ፱) ።

**ርሔ** ፤ (ዕብ፡ ሬሓን። ዐረ፡ ረይሐን) ፤ ሽቱ ፤ የሽቱ፡ ስም ፤ ሬሓን ፤ ስታናናሽ፡ ሽክላ፡ ዐፈር፡ እየመሉ፡ የሚተክሉት ፤ ጥሩ፡ ሽታ፡ ያለው። ዝክረ፡ ስምኪ፡ ዘይምዕዝ፡ እምርሔ፡ (ደራሲ) ።

**ርሒን** ፤ **ኖት** ፤ (ረሐነ፡ ይርሕን፡ ይርሐን። ዐረ፡ ረሐለ) ፤ መማስ ፤ ማሸከም ፤ መጕጐዝ

ጕገ፤ የኮርቻ ። ተንሥአ ፡ በጽባሕ ፡ ወረሐነ ፡ አድጎ ። ወረሐኑ ፡ አልባሲሆሙ ፡ ላዕሌሆን ፡ (ዘፍ፳፪ ፡ ፫ ። ማቴ፳፩ ፡ ፯) ።

**ራሕን፤** ኮርቻ ፤ ምቹ ፤ ግላስ ፤ የጭነት ፡ ዕቃ ፤ ጭነት ።

**ርሒፅ ፤ ፆት ፤ (ርሕፀ ፡ ይርሕፅ ፡ ይርሐፅ ። ዐረ ፡ ረሐፀ ። ዕብ ፡ ራሐጽ)** ፤ ማጠብ ፤ መታጠብ ፤ በውሃ ፡ መነከር ፤ መዘፈቅ ። መውዛት ፡ መላብ ፤ መረስረስ ፡ መርጠብ ፤ መቅለጥ ፤ መቅለጥለጥ ፤ ወፍራም ፡ ቀለጤ ፡ መኾን ። ይርሕፁ ፡ አፍራስ ፡ እምጽንዐ ፡ ኀይሎ ። ረሐፀከኒ ፡ ወለምለምከኒ ፡ (ገድ ፡ ተክ ። ዘዳ፴፫ ፡ ፶፬) ።

—፤ መታወክ ፤ መደረጥ ፤ መናወጥ ፤ መቈጣት ፤ መወገሸት ፤ መጮኽ ፤ የባሕር ፡ የዘፍ ፡ ከዐውሎ ፡ ነፋስ ፡ የተነሣ ፤ ለሰውም ፡ ይኾናል ። ወርሕፀት ፡ ነፍሱ ፡ ለንጉሠ ፡ ሶርያ ፡ (፬ነገ ፡ ፮ ፡ ፲፩) ።

**ርሑፅ ፤ (ፃን ፡ ፃት ፡ ሕፅት ፤ ረሓፅ)** ፤ የታጠበ ፤ የላበ ፡ የወዛ ፤ ወዛም ፡ ላበታም ፤ የታወከ ፤ ሀጩከ ፤ ሾሩ ፡ ወፍራም ፡ ቀለጤ ፤ ድልድል ፡ ቅምጥል ። አንተ ፡ ረሓፅኒ ፡ ወአንተኒ ፡ ድክምት ፡ (ዘዳ፴፫ ፡ ፶፯) ።

**ራሕፅ፤** ወዝ ፡ ላበት ፤ ከገላ ፡ የሚፈልቅ ፤ የሚመነጭ ። ሁከት ፡ መታወክ ። ይጼውዕ ፡ በጊዜ ፡ ራሕፁ ፡ (ደራሲ) ።

**አርሐፀ፤** አወዛ ፤ አስወዛ ፤ አቅለጠለጠ ።

**መርሕፅ ፤ መርሐፂ፤** የሚያልብ ፤ የሚያወዛ ፡ የሚያስወዛ ።

**ርሒቅ ፤ ቆት ፤ (ርሕቀ ፡ ይርሕቅ ፡ ይርሐቅ ። ዕብ ፡ ራሐቅ ። ሱር ፡ ርሔቅ)** ፤ መራቅ ፤ መወገድ ፤ መነጠል ፤ መለየት ፤ መቈረጥ ፤ ተለይቶ ፡ መኼድ ፤ ገለል ፡ ፈቀቅ ፡ ማለት ፤ ብታን ፡ ዘመድን ፡ መተው ፡ መልቀቅ ፤ ባዕድ ፡ መኾን ። ርሕቀ ፡ እምኔየ ፡ ረድኤቱ ። ነዋኅ ፡ ይርሕቁ ፡ እምኔየ ። ረሐቁ ፡ ረሐቁ ፡ ወፃኡ ፡ እምህየ ። ረሐቂ ፡ እምዐመፃ ። እምእግዚ ፡ ይርሕቅ ፡ ልቡ ፡ (ኢዮ፳ ፡ ፲፫ ። ኢሳ፶፪ ፡ ፲፫ ። ፶፱ ፡ ፲፩ ። ፶፱ ፡ ፲፱ ። ኤር፲፯ ፡ ፭) ። በርሕቀ ፡ ፈንታ ፡ ተርሕቀ ፡ ይላል ፤ ስሕተት ፡ ነው ። አለ ፡ ይትረሐቁ ፡ እምእግዚ ፡ አብሔር ፡ (ኢሳ፵፭ ፡ ፳፱) ።

**ረሓቂ ፤ (ቂት ፡ ቅያን ፡ ያት)** ፤ የሚርቅ ፤ የሚሸሽ ፤ ፈሪ ፤ እንቢተኛ ። ርኩሳን ፡ ወረሓቅያን ፡ እምስብሐተ ፡ እግዚአብሔር ፡ (ቄር ፡ ጸላ) ።

**ርሑቅ ፤ (ቃን ፡ ቃት ፡ ሕቅት)** ፤ የራቀ ፤ የወገደ ፤ ሩቅ ፤ ረዥም ፤ ብዙ ። ርሑቀ ፡ መዐት ። ርሑቅ ፡ ብሔር ። ርሑቅ ፡ ፍኖት ። ጊዜያት ፡ ርሑቃት ፡ (ዘፀ፴፬ ፡ ፮ ። ኢሳ፲፫ ፡ ፭ ። ፩ነገ ፡ ፰፮ ፡ ፲፫ ። ሕዝ፲፪ ፡ ፳፯) ።

**ርሕቀት፤** መራቅ ፤ አራራቅ ፡ ርቀት ፤ ሩቅነት ፤ ብዛት ፤ ርዝመት ። አበስኩ ፡ ላዕለ ፡ ነፍስየ ፡ በሑረትየ ፡ ኀበ ፡ ሮምያ ፡ ወርሕቀትየ ፡ እምህላዌ ፡ ንጉሥ ። ርሕቀተ ፡ ፍኖት ። ርሕቀተ ፡ መዋዕል ፡ (ዮሴፍ ። አፈ ፡ ተ፲፱ ። ጥበ፲፱ ፡ ፲፮) ።

**ርሕቅ፤** ርቀት ፤ ርቆሽ ፤ አራራቅ ፡ (አርጋ) ።

**ርሕቅና፤** ሩቅነት ፤ ርሕቀት ፤ ልዩነት ። ለይእቲ ፡ ኢያፀርዓ ፡ ርሕቅና ፡ ዘመን ። ረከበ ፡ ማእከሌሆሙ ፡ ርሕቅና ፡ ዐቢየ ፡ (ስንክ ፡ ጳጕ፪) ።

**አርሐቀ፤** አራቀ ፤ አስራቀ ፡ አሶገደ ፤ ለየ ፤ ቈረጠ ። ከመ ፡ ያርሕቁኒ ፡ እመቅደስየ ። አርሕቅ ፡ መዐተ ፡ እምልብከ ። አርሕቃ ፡ ለሐዘን ፡ እምኔከ ። ጌጋይክሙ ፡ አርሐቀ ፡ ሠናይተ ፡ እምኔክሙ ። አርሐቀኒ ፡ እምሕይወትየ ፡ (ሕዝ፰ ፡ ፮ ። መክ፲፩ ፡ ፲ ። ሚራ፴፰ ፡ ፳ ። ኤር፭ ፡ ፳፭ ። ኢዮ፴ ፡ ፳፪) ። በአርሐቀ ፡ ፈንታ ፡ አስተርሐቀ ፡ ይላል ፤ ፍችው ፡ አንድ ፡ ነው ። እፎ ፡ ታስተርሕቆ ፡ ለዘኢይትረሐቅ ። እምደሪበ ፡ ድርሳን ፡ አስተርሐቀ ። ወአስተርሐቅዋ ፡ ለኀጢአቶሙ ፡ (መጽ ፡ ምስ ። ስንክ ፡ ታኅ፰ ። መዝ ፡ ፻፫፰) ።

**መርሐቂ ፤ መርሕቅ ፤ (ቅት ፡ ቃን ፡ ቃት)** ፤ የሚያርቅ ፤ የሚያሶግድ ፤ አራቂ ። ትሕትና ፡ መርሕቅኒ ፡ ወመድኅንኒ ፡ እመሥገርተ ፡ ሰይጣን ፡ (ፊልክ ፡ ፻፶፪) ። ኹለተኛም ፡ ማራቂያ ፡ ማስራቂያ ፡ ማሶገጃ ፡ ተብሎ ፡ በማድረጊያነት ፡ ይፈታል ።

**ተራሐቀ፤** ተራራቀ ፤ ተለያየ ። ጊዜ ፡ ለተራሕቆ ። ኢይትራሐቁ ፡ አሐዱ ፡ እምካልኡ ። ተራሕቆ ፡ እምዓለም ፡ (መክ፫ ፡ ፭ ። ዮኤ፪ ፡ ፰ ። ፊልክ ፡ ፬) ።

**አስተራሐቀ፤** አራራቀ ፤ አለያየ ፤ ገላገለ ፤ ከፋፈለ ። ቆመ ፡ ማእከሎሙ ፡ ወአስተራሐቆሙ ። አስተራሕቅዎሙ ፡ ዘዘ ፡ ዚኣሆሙ ፡ (፩ነገ ፡ ፪ ፡ ፲፭ ። ዳን፭ ፡ ፶፭ ። ዘፍ፴፪ ፡ ፲፯) ።

**መስተራሕቅ፤** የሚያራርቅ ፤ የሚራራቅ ፤ ተራራቂ ፡ በመራራቅ ፡ በልዩነት ፡ ያለ ። በበዓላት ፡ አው ፡ በጊዜያት ፡ መስተራሕቃት ፡ (ፊልክ ፡ ፸፱) ።

**ርሒስ ፤ ሶት ፤ (ርሕሰ ፡ ይርሕስ ፡ ይርሐስ ፤ ርሕፀ ። ዕብ ፡ ወሱር ፡ ራስ ፤ ረጠበ ። ዐረ ፡ ረሸ ፤ ረጨ)** ፤ መራስ ፤ መረስረስ ፤ መርጠብ ፡ መለስለስ ፤ መርከት ፤ መለዘብ ፤ ውሃ ፡ መጥገብ ። ይርሕሱ ፡ አድባር ፡ እምደሞሙ ፡ (ኢሳ፴፬ ፡ ፫ ። ስንክ ፡ ታኅ፲፯) ።

**ርሑስ ፤ (ሳን ፡ ሳት ፡ ሕስት)** ፤ የራሰ ፡ የለሰለሰ ፤ ርጥብ ፤ ልሕሉሕ ፤ ውሃ ፡ ጠገብ ። ሰላም ፡ ለርእስኪ ፡ በቅብዐ ፡ ቅዳሴ ፡ ርሑስ ። ምድር ፡ ርሕስት ፡ ወጥልልት ፡ እማይ ፡ ትወልድ ፡ ዕፄያተ ፡ ብዙኀ ። አቅረበ ፡ ኀቤሁ ፡ ኅብስተ ፡ ይቡሰ ፡ ወርሑሰ ፡ በማይ ፡ ወላዕሌሁ ፡ ዘይት ፡ ወጼው ። ሕፍነ ፡ ፀተር ፡ ዘርሑስ ፡ በማይ ፡ (ደራሲ ። አፈ ፡ ተ፳፱ ። ፊልክ ፡ ፻፴፪ ። ስንክ ፡ ጥቅ፴) ።

**አርሐሰ** ፤ አራስ ፤ አሰራሰ ፤ ነከረ ፤ አረጠበ ፤ አረከ ፡ አጠገበ ። ያርሕሰሙ ፡ ነፍኒፍ ፡ ወጠለ ፡ ገዳም ። እስከ ፡ ይሙሕዝ ፡ ሀፋ ፡ ከመ ፡ ማየ ፡ ወያርሕስ ፡ ምድረ ፡ ኀበ ፡ ቆመ ። ወበአንብዐየ ፡ አርሐስኩ ፡ ምስካብየ ። (ኢዮ ፴፰ ፡ ፳ ። ገድ ፡ ተክ ። መዝ ፡ ፮ ። ሉቃ ፯ ፡ ፴፰) ።

**አርሓሲ** ፤ **መርሕስ** ፤ የሚያርስ ፤ የሚያረጥብ ፤ ነካሪ ።

**ምርሓስ** ፤ ማራሻ ፤ መንከሪያ ፤ ዕቃ ፡ ቦታ ።

**ርኅበ** ፤—ሰፊ ፡ ኾነ ፤—ርሒብ ፡ ርሕበ ።

**ርኂብ** ፤ **በት** ፤ **(ርኅበ ፡ ይርኅብ ፡ ይርኅብ ። ዕብ ፡ ራዔብ ፤ ዐረ ፡ ረዐበ ፡ ሰፋ)** ፤ መራብ ፤ በረኀብ ፡ መያዝ ፤ መጠውለግ ፤ ባዶ ፡ ሆድ ፡ መኾን ፤ ምግብ ፡ መፈለግ ፤ ልብላ ፡ ልብላ ፡ ማለት ፤ ለመብል ፡ መሠየት ፤ መጕምዠት ። ወመጽአ ፡ እምሐቅል ፡ ርኂቦ ። ብፁዓን ፡ እለ ፡ ይርኅቡ ፡ ወይጸምኡ ። ርኅብኩ ፡ ወአብላዕክሙኒ ። ተናገራ ፡ ድመት ፡ በልሳኒ ፡ ሰብእ ፡ ወትቤሎ ፡ ምንተ ፡ ትፈቅድ ፡ ወይቤላ ፡ ይርኅበኒ ፤ ወወሀበቶ ፡ ኅብስተ ፡ (ኩፋ ፡ ፳፱ ። ማቴ ፭ ፡ ፮ ። ፳፭ ፡ ፴፭ ። ስንክ ፡ መጋ ፲፮) ። በርኅበ ፡ ፈንታ ፡ ተርኅበ ፡ ይላል ፤ ስሕተት ፡ ነው ፤ አያሰኝም ።

**ርኁብ** ፤ **(ባን ፡ ባት ፡ ኅብት)** ፤ የተራበ ፤ የተቸገረ ፤ ራብተኛ ፤ ራብ ፡ የያዘው ፤ ምግብ ፡ ያረዘው ። እስመ ፡ ርኁብ ፡ ሀገር ። ርኁባኒሆሙ ። ነፍስ ፡ ርኅብት ፡ (፬ነገ ፡ ፯ ፡ ፬ ። ማር ፰ ፡ ፫ ። ኢሳ ፵፱ ፡ ፲) ።

**ረኃብ** ፤ **አው ፡ ረኃብ** ፤ በቁሙ ፤ ራብ ፤ የምግብ ፡ ዕጦት ፤ ቀጠና ፤ ችጋር ፡ ባሕርያዊ ፡ ሕማም ፤ ጠባይዓዊ ፡ ሕግ ፡ በግድ ፡ ምግብ ፡ የሚያስፈልግ ። ይጠፍኡ ፡ በረኃብ ። ወአምጽአ ፡ ረኃበ ፡ ለብሔር ። ወተወክፈ ፡ ረኃበ ፡ እስመ ፡ ረኃብሰ ፡ አልቦቱ ፡ ኀጢአት ። ኣመጽእ ፡ ረኃበ ፡ እክል ፡ (ዮዲ ፯ ፡ ፲፬ ። መዝ ፡ ፻፬ ። ሃይ ፡ አበ ። ዓሞ ፰ ፡ ፲) ።

**አርኀበ** ፤ አስራበ ፤ ምግብ ፡ ነሣ ፤ ረኀብ ፡ አመጣ ። ምግብ ፡ አስፈለገ ፤ ልብላ ፡ ልብላ ፡ አሰኘ ፤ ረኃቡ ። አርኀበከ ፡ ወእምዝ ፡ መና ፡ ሴሰየከ ። አርኅብዎ ፡ ወአጽምእዎ ፡ (ዘዳ ፰ ፡ ፫ ። ፫ነገ ፡ ፳፱ ፡ ፳፯) ።

**መርኅብ** ፤ የሚያስርብ ፤ አስራቢ ።

**ርኂው** ፤ **ዎት** ፤ **(ርኅወ ፤ ረኀወ ፡ ይርኁ ፡ ይርኀው ። ርሕበ)** ፤ መከፈት ፡ መስፋት ፤ ክፍት ፡ ሰፊ ፡ ባዶ ፡ መኾን ። ኅዋን ፡ ተመልከት ፤ የዚህ ፡ ክፊል ፡ ነው ። መጽሐፍ ፡ ግን ፡ በርኅወ ፡ ፈንታ ፡ ተርኅወ ፡ ይላል ፤ ስሕተት ፡ ነው ። በዝሉ ፡ ጊዜ ፡ ይትረኀዉ ፡ አናቅጽኪ ። ትርኅው ፡ አስራብ ፡ ሰማይ ። ወከነ ፡ ዝ ፡ ምክንያተ ፡ ተርኅዎታ ፡ ለሀገር ፡ (ኢሳ ፷ ፡ ፲፩ ። ዘፍ ፯ ፡ ፲፩ ። ዮሴፍ) ።

**ረኃዊ** ፤ **(ዊት ፡ ውያን ፡ ያት)** ፤ የሚከፈት ፤ የሚከፋፈት ፤ ተከፋች ።

**ርኁው** ፤ **(ዋን ፡ ዋት ፡ ኁት)** ፤ የተከፈተ ፤ ክፍት ፤ ሰፊ ፤ ግልጥ ፤ ባዶ ፤ ኅዋ ። ርኁው ፡ ሞኅትየ ። ይረክብዎ ፡ ርኁወ ። ሞኅት ፡ ርኁት ። መሰክው ፡ ርኁዋት ። ርኁው ፡ ሎሙ ፡ መኳኒ ፡ ትዕግሥትየ ፡ (ኢዮ ፴፩ ፡ ፴፪ ። ዮሴፍ ። ራእ ፫ ፡ ፰ ። ሔኖ ፸፪ ፡ ፮ ። ሱቱ ፡ ዕገዘ ፪ ፡ ፲፪) ።

**አርኀወ** ፤ ከፈተ ፤ አስከፈተ ፤ ገለጠ ፤ ሰበረ ፡ ድል ፡ አደረገ ። አርኀወት ፡ ሞኅተ ። አርኅዋ ፡ ለታቦት ። አርኀውከ ፡ ሰማየ ። አርኀወ ፡ ሀገረ ፡ (ጦቢ ፰ ፡ ፲፫ ። ኩፋ ፡ ፩ ። ኢሳ ፴፱ ፡ ፩ ። ዮሴፍ) ።

**መርኆ** ፤ **(ብ ፡ መራኁት ፤ ታት)** ፤ መክፈቻ ፤ መከፈቻ ፤ ማስከፈቻ ። ነሥኡ ፡ መርኆ ፡ ወአርኀዉ ። እሙንቱ ፡ እለ ፡ ይእኅዙ ፡ መራኁተ ፡ ቤተ ፡ እግዚ ፡ (መሳፍ ፡ ፫፭ ። ፩ዜና ፡ ፱ ፡ ፳፯) ።

መርኆ ፡

**ርኅጸ** ፤—ወዛ ፡ ላበ ፤—ርሕፀ ።

**ርኅቀ** ፤—ራቀ ፡ ወገደ ፤—ርሕቀ ።

**ራኅርኆ** ፤ **ኆት** ፤ **(ራኅርኀ ፡ ይራኀርኅ ፡ ይራኅርኅ ። ዐረ ፡ ረኀ ፤ ረኅረኀ ። ዕብ ፡ ራካኽ)** ፤ መራራት ፤ መግራት ፤ መለዘብ ፤ መለስለስ ፤ መርጠብ ፡ ልሕሉሕ ፡ መኾን ፤ እንደ ፡ ሳንባና ፡ እንደ ፡ ጕበት ። መጽሐፍ ፡ ግን ፡ በራኅርኀ ፡ ፈንታ ፡ ተራኅርኀ ፡ ይላል ፤ አያሰኝም ፤ የተሳሳተ ፡ ነው ። ተራኅርኀ ፡ ሎቱ ፡ ወሖረ ፡ ኀቤሁ ። ኢተራኅርኀ ፡ አሐዱሂ ፡ በላዕሌሁ ። ዘአሣኒየ ፡ ግዕዘ ፡ ይጸንዕ ፡ ፍቅሩ ፡ ወይትራኀራኅ ፡ ላዕሌሁ ፡ ልበ ፡ ኵሉ ። ተራኅርኆተ ፡ መንፈስ ፡ ቅዱስ ። አዘዝኒ ፡ ንሕነሂ ፡ በእንተ ፡ ተራኅርኆ ፡ ወምሕረት ፡ (ዮሴፍ ። አፈ ፡ ተ፲፩ ። ፈላስ ። ያዕ ፡ ዘእል ። ፈ ፡ መ ፡ ፬ ፡ ፪) ።

**ርኅሩኅ** ፤ **(ኃን ፡ ኃት ፡ ርኅት)** ፤ በቁሙ ፤ የራራ ፤ የገራ ፤ ገር ፡ ርሩ ፤ ወላላ ፤ ዐዛኝ ፤ መሓሪ ። ዘቦ ፡ ተፋቅሮ ፡ ርኅሩኅ ፡ ወተዐጋሢ ፡ ውእቱ ። መፍቀሬ ፡ ሰብእ ፡ ወርኅሩኅ ። ኮነ ፡ ትሑተ ፡ ወርኅሩኀ ፡ ልብ ፡ (ፍ ፡ ነ ፡ ፵፭ ። ጥበ፲፪ ፡ ፲፱ ። ዮሴፍ) ።

**ርኅራኄ** ፤ በቁሙ ፤ መራራት ፤ ርሩነት ፤ ገርነት ፤ ገራምነት ። ናሁ ፡ ጸንዐ ፡ ርኅራኄነ ፡ ላዕለ ፡ ውሉዶሙ ። ሃይማኖትነ ፡ ሃይማኖተ ፡ ምሕረት ፡ ወማህል ፡ ወርኅራኄ ፡ (ዮሴፍ ። ፈ ፡ መ ፡ ፲፭ ፡ ፫) ።

**አራኅርኀ** ፤ አራራ ፤ አስራራ ፤ አግራራ ፤ አለዘዘበ ፤ መከረ ፡ አስተማረ ፤ ገር ፡ አደረገ ። ዘቲ ፡ መጽሐፍ ፡ ታራኅርኅ ፡ ጠባይዒከ ፡ ወታሤኒ ፡ ግዕዘከ ። ከመ ፡ ያራኅርኅ ፡ ልበ ፡ እግዚእ ። ታራኅርኅ ፡ ልቦ ፡ ላዕሌየ ፡ (ፈላስ ። መቃ ። ዮሴፍ) ።

**ረጢብ** ፤ **በት** ፤ **(ረጥበ ፡ ይረጥብ ፡ ይርጠብ ። ዕብ ፡ ራጣብ ። ሱር ፡ ራጤብ ። ዐረ ፡ ረጢበ)** ፤ መርጠብ ፤ መለምለም ፤ ርጥብ ፡ ውኃማ ፡ መ

ቅን ። ርጥባን ፡ መስጠት ፤ መቀበት ፤ አደጋ ፡ ለወደቀበት ፡ (ዐማርኛ) ።

**ርጡብ** ፤ (በን ፡ በት ፡ ጥብት) ፤ የረጠበ ፤ ርጥብ ፤ ለጋ ፤ ለምለም ፤ ውሃማ ፤ ደማም ፤ ጭቃ ። ጸሃ ብስ ፡ ዕፀ ፡ ርጡበ ። አነጻ ፡ ባሕም ፡ ርጡብ ። ዕፀመ ፡ ምጋሁ ፡ ተረክበ ፡ ምስለ ፡ ደም ፡ ርጡብ ። መሬት ፡ ርጡብ ፡ እብን ፡ ይቡስ ። ሉብዕተ ፡ እደሁ ፡ ለርጡብ ፡ (ሕዝ፲፯ ፡ ፳፬ ። ሉቃ፳፫ ፡ ፴፩ ። ገድ ፡ ተክ ። ስንክ ፡ ጥቅ ፮ ። ሠኔ፲፱ ። ሱቱ ፡ ዕገዜ ፡ ፺፱) ።

**ርጥበት** ፤ በቁሙ ፤ መርጠብ ፤ አረጣጠብ ፤ ርጥብነት ፤ ርጥባን ። ይቡስ ፡ ዕፀ ፡ ዘአልቦ ፡ ርጥበት ። ብከመ ፡ እሳት ፡ ያየብስ ፡ ርጥበተ ፡ ዕፀ ፡ (መቃ ። ፊልክ ፡ ፺) ።

**አርጠበ** ፤ አረጠበ ፤ አስረጠበ ፤ ርጥብ ፡ አደረገ ። ኣረጥብ ፡ ዕፀ ፡ ይቡሰ ፡ (ሕዝ፲፯ ፡ ፳፬) ።

**ተረጥበ** ፤ (ዐማርኛ) ፤ ተረጠበ ፤ ተቀበለ ፤ ርጥባን ፡ ቀለብ ፡ አገኘ ።

**ርጢን** ፤ (ናት ። ጽር ፡ ሬቲኒ ። ዐረ ፡ ራቲን ። ሱር ፡ ሬጢኒ) ፤ ጥሩ ፡ ሙጫ ፤ ዕጣን ፤ የ ዕጣን ፡ ዐይነት ፤ ከታወቁ ፡ ዕንጨቶች ፡ የሚገኝ ። ፈውስ ፤ መድኀኒት ፤ ከሙጫ ፡ ጋራ ፡ የሚቀመም ፤ በሙጫ ፡ ወ ለባ ፡ የሚለወስ ። አልቦኑ ፡ ርጢን ፡ ውስተ ፡ ገለዓድ ። ርጢናት ፡ እምሉማት ፡ ወጽሩያት ፡ (ኤር፰ ፡ ፳፪ ። ፊ ፡ መ ፡ ፩ ፡ ፱ ። ዘፍ፴፯ ፡ ፳፭ ። ሕዝ፳፯ ፡ ፲፯) ። ባለቅ ኔዎች ፡ ግን ፡ ረጠን ፡ ብለው ፡ ይገሳሉ ።

**ረዪም** ፤ ሞት ፤ (ረየመ ፡ ይረይም ፡ ይ ሪም ። ትግ ፡ ሬመ ። ዕብ ፡ ራም) ፤ ልዒል ፤ ዐ ፊግ ፤ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ማለት ፤ መርዘም ፡ ወደ ፡ ላይ ፡ መው ጣት ፤ ማረግ ፤ መራቅ ፡ መምጠቅ ፤ መላቅ ፡ መብለጥ ፤ ለላይ ፡ መቀመጥ ፤ ላይኛ ፡ ራስ ፡ ጫፍ ፡ ጕንጮ ፡ መጨ ረሻ ፡ መኾን ፤ እንደ ፡ ጕልላት ። ለዐለን ፡ ተመልከት ፤ የ ጸሀ ፡ ንረ ፡ ቤት ፡ ነው ።

**ሬማ** ፤ (ማት ። ዕብ ፡ ራማህ) ፤ ልዕልና ፡ ምጥቀት ፡ ርዝመት ። ከፍ ፡ ያለ ፡ ቦታ ፤ አዳጋ ፡ ቍሊልታ ፤ ተራራ ፡ ኵረብታ ፤ ደርብ ፡ ሰገነት ፤ የተራራ ፡ ላይ ፡ ሜዳ ፤ ስተት ፡ ያለ ፤ የተንጣለለ ። ሐነጽከ ፡ ለከ ፡ ብሔ ፡ ወገበ ርከ ፡ ለከ ፡ ሬማ ፡ ሐነጽከ ፡ ሬማተከ ፡ (ሕዝ፲፮ ፡ ፳፬ ። ፴፭) ።

—፤ ስመ ፡ አህጉር ፤ በብንያምና ፡ በንፍታሌም ፡ ዕፃ ፡ ያሉ ፡ (ኢያ፲፰ ፡ ፳፭ ። ፲፱ ፡ ፴፱ ። ኤር፴፩ ፡ ፲፭ ። ማቴ ፪ ፡ ፲፰) ።

—፤ ስማይ ፤ የሰማይ ፡ ስም ፤ በኢዮርና ፡ በኤረር ፡ መካ ከል ፡ ያለ ፤ ከሦስቱ ፡ ዓለመ ፡ መላእክት ፡ አንዱ ፤ የጠፈር ፡ ሦስተኛ ። በዲኒ ፡ ሀገረከሙ ፡ ሀገረ ፡ ሚልሲት ፡ ሬማ ። ፀሓዩ ፡ ቅዱሳን ፡ ዘሬማ ። ምሕላዩ ፡ ሰማዕ ፡ እም ሬማ ። ገዜ ፡ ዕርገት ፡ ውስተ ፡ ሬማ ፡ (ደራሲ ። አዋል ። ድጓ) ።

**አርያም** ፤ (ማት) ፤ የራማ ፡ ብዙ ፤ ራማት ፡ አርያም ፡ አንድ ፡ ወገን ፤ አርያማት ፡ የብዙ ፡ ብዙ ። መጽ ሐፍ ፡ ግን ፡ አርያምን ፡ እንደ ፡ ራማ ፡ ባንድ ፡ ብቻ ፡ አ ድርጎ ፡ ይናገራል ።

—፤ ልዕልና ፤ ምጥቀት ፤ ላዕል ፤ መልዕልት ። ሐነጸ ፡ መ ቅደሶ ፡ በአርያም ። እለ ፡ ይነብሩ ፡ ውስተ ፡ አርያም ። ከመ ፡ ያስርር ፡ ውስተ ፡ አርያም ፡ ዕጉሊሁ ፡ (መዝ ፸፯ ። ኢሳ፴፯ ፡ ፱ ። ዕን፪ ፡ ፱) ።

—፤ ሰማይ ፤ ሰማየ ፡ ሰማያት ፤ መጨረሻ ፡ ሰማይ ። ዐረገ ፡ ውስተ ፡ አርያም ፡ ጼዊወከ ፡ ጼዋ ። እስከ ፡ ትለብሱ ፡ ኀይለ ፡ እምአርያም ። ወለከ ፡ ንፌኑ ፡ ስኩቴተ ፡ እ ስከ ፡ አርያም ። እምቅድመ ፡ ይሕንጽ ፡ አየራተ ፡ ወ አርያማተ ፡ (መዝ ፡ ፷፯ ። ሉቃ፳፬ ፡ ፵፱ ። ቅዳ ፡ ግሩ) ።

—፤ የድጓ ፡ ቃል ፡ ትምርት ፤ ኹለተኛ ፡ ክፍል ፡ ከውዳሴ ፡ ማርያም ፡ (ስንክ ፡ ግንቦ፩) ።

**አርያማዊ** ፤ ላዕላዊ ፤ ሰማያዊ ፤ ዘሰማይ ። ፀ ሓየ ፡ ጽድቅ ፡ አርያማዊ ። አርያማዊት ፡ መቅደስ ፡ (ሳታ ። ደራሲ) ።

**ረይዮ** ፤ ዮት ፤ (ረየዐ ፡ ይሬይዕ ፡ ይረ ይዕ ። ዐረ ፡ ራዐ) ፤ መገራት ፤ መቅጣት ፤ ማስሮጥ ፡ ማስኬድ ፤ ማስተማር ፡ ማስለመድ ፤ ማቅናት ፤ ማሠል ጠን ፡ የከብት ፡ የሰው ። አንዘ ፡ ይረይዮሙ ፡ ለሰማዕ ያን ፡ (አፈ ፡ ድ፲፱) ።

**ረያዒ** ፤ (ዒት ፡ ዕያን ፡ ያት) ፤ የሚገራ ፤ ገሪ ፤ ቀጭ ፡ አስተማሪ ። ረያዔ ፡ አፍራስ ፡ (አዋል) ።

**አረየዐ** ፤ **አስተረየዐ** ፤ አሰለፈ ፤ አስጠረረ ። ያስተረይዮሙ ፡ ለመስተጋድላኒሁ ፡ (አፈ ፡ ድ፳፭) ።

**ተረየዐ** ፤ ተገራ ፤ ተማረ ፤ ተሠራ ፡ ተቀጣ ፤ ለ መደ ፤ ገራም ፡ ኾነ ። ፈረስ ፡ ዘኢተረየዐ ። እልክቱ ፡ ኢተረየዑ ፡ ወኢተመከሩ ፡ ወኢያእመኑ ፡ ሠናየ ፡ እ ምነ ፡ እኩይ ። እመሰ ፡ ተረየዐ ፡ ኅሊና ፡ ልብነ ፤ በም ንትኬ ፡ ይትረየዓ ፡ ኅሊናቲነ ፡ (ሚራ፱ ፡ ፰ ። አፈ ፡ ድ፰ ። ተግ፰) ።

**ርዩዕ** ፤ (ዓን ፡ ዓት ፡ ይዕት) ፤ የተገራ ፤ ገር ፤ ገራም ፤ ምሁር ፡ ግሡጽ ፤ ልሙድ ።

**ርያዔ** ፤ መገራት ፤ መገሬት ፤ አገራር ፤ ግሪ ፤ ግ ራት ፤ ተግሣጽ ፡ ትምርት ፤ ቅጣት ።

**ሬስ** ፤ (ዕብ ፡ ሬሽ) ፤ ስመ ፡ ፊደል ፤ ዕሥ ራዊ ። ርእስ ፡ ማለት ፡ ነው ፡ (መዝ ፡ ፻፲፰ ፡ ፻፶፫) ። ባማ ርኛ ፡ ግን ፡ ሬሶ ፡ ሬሳ ፡ ማለት ፡ ነው ። የሙት ፡ ዘር ፡ ሊሉ ፡ ወልደ ፡ ሬስ ፡ እንዲሉ ።

**ርዥ** ፤ ንጉሠ ፡ አዕዋፍ ። ......ወህሎ ፡ አሐዱ ፡ ዖፍ ፡ ዘይሰመይ ፡ ርዥ ፡ በሀገረ ፡ ሲን ፡ ውሳጤ ፤ ተ ብህለ ፡ ከመ ፡ ስበ ፡ ይሰርር ፡ ይከድና ፡ ለሀገር ፡ በክ ንፌሁ ፡ ወይወርድ ፡ ዲበ ፡ ዕጓለ ፡ ነገደት ፡ ይመሥጥ ፡ ወያበልዖሙ ፡ ለውሉዱ ። ወይቤ ፡ አሐዱ ፡ ነጋዲ ፡ ርኢኩ ፡ በአሐዱ ፡ ደሴት ፡ እምደሰያተ ፡ ሲን ፡ ክል

ሔተ ፡ አንቀቅሖ ፡ ከመ ፡ ከልኤቱ ፡ ደባትር ፡ ዐበይት ፡ ዘውእቱ ፡ አንቀቅሖ ፡ ዘርዘ ፡ (ጊ ፡ ወ ፡ ሐ ፡ ገ፹፩) ።

**ረኪብ** ፤ በት ፤ (ረከበ ፤ ረከበ ፡ ይረክብ ፡ ይርከብ ። ዕብ ፡ ራኪብ ። ሱር ፡ ርኪብ ። ዐረ ፡ ረኪበ) ፤ መስረር ፤ ወደ ፡ ከብት ፡ ላይ ፤ ወደ ፡ ባሑርና ፡ ወደ ፡ መርከብ ፡ መውጣት ፤ መጫን ፡ መቀመጥ ፤ ተቀምጦ ፡ መኼድ ። መዝለል ፡ መከመር ፡ ፈጥ ፡ ማለት ፤ በላይ ፡ መኾን ፤ መታዘል ፤ ማግኘት ፡ መድረስ ፤ መንካት ፡ መያዝ ፡ መዳሰስ ፤ የወንድና ፡ የሴት ፡ የገንዘብ ፤ ሰሌላም ፡ ይኾናል ። ንሥምከዎ ፡ ወኢረከብክዎ ። ደቂቀሙ ፡ ኢይረክቡ ፡ ንዋዮሙ ። ንግእ ፡ ዘይረክበከ ። ለዘረከበ ፡ ይርከቦ ። ረኪበ ፡ መድፍን ። ረከብዎ ፡ ውዱቀ ። ከመ ፡ ዝ ፡ ረከብኩ ፡ ጽሑፈ ፡ ውስተ ፡ መጻሕፍት ፡ (ማሕሮ ፡ ፪ ። ኢዮ፴፩ ፡ ፲፱ ። ማቴ፰ ፡ ፲፱ ። ዮሐ፲፱ ፡ ፳፱ ። ሚሊ፵ ፡ ፲፰ ። ፩ነገ ፡ ፩ ፡ ፫ ። ኩፋ ፡ ፳፩) ። ረከብናሆሙ ፡ ይሰክቡ ፡ ኅቡረ ። ረከብናኻ ፡ በዝሙት ፤ ያዘ ፡ (ዳን፩ ፡ ፴፰ ። ዮሐ፰ ፡ ፬) ።

**ረከቢ** ፤ (ቢት ፡ ብያን ፡ ያት) ፤ የሚሰር ፤ ሰራሪ ፤ የሚያገኝ ፡ አግኚ ። ረካቢሆን ፡ ለኄራት ፡ (ምሳ ፲፯ ፡ ፰) ።

**ርኩብ** ፤ (ዕማርኛ) ፤ በቁሙ ፤ የኮርቻ ፤ ክንፍ ፤ ወደ ፡ ላይ ፡ መውጫ ፤ መቈናጠጫ ፤ መረጋገጫ ። (ግጥም) ፤ ርካቡ ፡ ምን ፡ አለኝ ፡ ወይስ ፡ ዘለበቱ ፤ እኔን ፡ የገደለኝ ፡ ቅናቱ ፡ ቅናቱ ።

**ራኩብት** ፤ (ባት ። ዐረ ፡ ረኩበት) ፤ የግመል ፡ ወሳብሪ ፤ ባዝራ ፤ ድንጉላ ፤ ሯጭ ፡ ጋላቢ ። ራኩብ ፡ ባን ፡ የወንድ ፤ ት ፡ የሴት ። ዕደው ፡ እለ ፡ ይጼዐኑ ፡ ራኩብተ ፡ (፩ነገ ፡ ፴ ፡ ፲፯) ።

**መርከብ** ፤ (ብ ፡ መራኩብ ። ዐረ ፡ መርከብ ። ሱር ፡ ማርከብታ) ፤ በቁሙ ፤ ሐመር ፤ የባሕር ።

**መርኩብ** ፡ (ዕብ ፡ ሜርካብ) ፤ ሠረገላ ፤ ፈረስ ፡ የሚያሮጠው ፤ ሰው ፡ የሚቀመጠው ።

**መራኩብት** ፤ (ዕብ ፡ ታኂም) ፤ አክይስት ፤ ግሩማን ፡ አራዊት ፤ የሚሰሩ ፡ የሚወረወሩ ፡ (ኢሳ፲፫ ፡ ፳፪) ።

**አርከበ** ፤ ጫነ ፤ አስጫነ ፤ አስቀመጠ ፤ አፈናጠጠ ። አስገኘ ፤ አስረከበ ፤ ሰጠ ፤ አስጨበጠ ። ትሕትና ፡ ዘምስለ ፡ ትዕግሥት ፡ ታረክብ ፡ ንጹርያተ ። ብዝኀ ፡ ስታይ ፡ ኢያረክብ ፡ ንደሰ ፡ ወኢያንጥእ ፡ ቍስለ ። ታረክቦሙ ፡ ሕይወተ ፡ (ማር፩ ፡ ፩ ። ሚሊ፴፱ ፡ ፴ ። ሄርማ) ።

**ተረክበ** ፤ ተረክበ ፤ ተቀበለ ። ተገኘ ፤ ተያዘ ፤ ተመረመረ ። እምአይቴ ፡ ተረክበት ፡ ጥበብ ። ብእሲት ፡ እንተ ፡ ተረክበት ፡ በዝሙት ። ለእመ ፡ ተረክበ ፡ ካህን ፡ በሰሪቅ ። ስጢር ፡ ውእቱ ፡ ዘኢይረከብዎ ፡ በኅሊና ፡ (ኢዮ፳፰ ፡ ፲፪ ። ዮሐ፰ ፡ ፫ ። ቄድር ። ቅዳ ፡ ኢ.ጺ.) ። ፅ ፡ ሀሎ ፡ በማለት ፡ ፈንታ ፡ ተረክበ ፡ ይላል ፤ ስሕተት ፡ ነው ። ወተረክበ ፡ ለሰሎሞን ፡ አርባዕቱ ፡ ምእት ፡ አፍራስ ፡ (፪ዜና ፡ ፱ ፡ ፳፭) ።

**ተራከበ** ፤ ተረካከበ ፤ ተገናኘ ፤ ተጋጠመ ፤ ተሳሳመ ፤ አንድ ፡ ኾነ ። በዕለ ፡ ወነደይ ፡ ይትራከቡ ፡ ኅቡረ ። ተራከቡ ፡ ለቀትል ። ጊዜ ፡ ተራከቦቱ ፡ ምስለ ፡ ብእሲቱ ። ወይትራከብ ፡ ቃላቲሆሙ ፡ ምስለ ፡ ጽራሕ ፡ ብካየ ፡ ጸላእት ፡ (ምሳ፳፪ ፡ ፪ ። ፳ዜና ፡ ፲፱ ፡ ፱ ። ፈ ፡ መ ፡ ፲፩ ፡ ፪ ። ጥበ፲፰ ፡ ፲) ።

**ርኩብ** ፤ (ባን ፡ ባት ፡ ክብት) ፤ የተገኘ ፤ የተፈጠረ ፤ የተገናኘ ፤ ግንኙ ፤ ኅብብር ። ዮም ፡ ርኩብ ፡ መስቀል ። ወክነፊሆሙ ፡ ስሩሓን ፡ ወርኩባን ፤ እኑዛት ፡ ወርኩባት ፡ (ድጓ ። ፪ዜና ፡ ፫ ፡ ፲፫ ። ፫ነገ ፡ ፯ ፡ ፴፩) ። በርኩብ ፡ ፈንታ ፡ ርኩባዊ ፡ ይላል ፤ አያሰኝም ። ግዕዛት ፡ ርኩባውያት ፡ (ፍ ፡ ነ ፡ ፵፫ ፡ ፲፱) ።

**ርክበት** ፤ (ታት) ፤ ማግኘት ፤ መገኘት ፤ አገኛኘት ፤ ባሕርያዊ ፡ ሀብት ፤ ዕድል ። ርክበተ ፡ ንዋይ ። ርክበተ ፡ ወልደሙ ። ርክበተ ፡ አዕፀምት ። ዘአስተፋጠነ ፡ ፈውሶተ ፡ ሕማሙ ፡ እምቅድመ ፡ ይስአን ፡ ርክበታተ ፡ መድኀኒታቲሁ ። ኅሊናቲሁ ፡ ወኀይላቲሁ ፡ ወርክበታቲሁ ፡ ዘውስጥ ፡ (ፍ ፡ ነ ፡ ፵፪ ፡ ፳ ። ስንክ ፡ ኅዳ፳፱ ። ጥር፲፱ ። ግንዘ ። ፍ ፡ ነ ፡ ፵፩) ።

**ረክብ** ፤ ማግኛ ፤ መገኛ ፤ መገናኛ ፡ ቀን ፤ በዓል ፤ የትንሣኤ ፡ ፳፭ኛ ፤ የበዓለ ፡ ኀምሳ ፡ እኩሌታ ፡ ረቡ ፡ የሚውል ። ዋዜማ ፡ ዘረክበ ፡ ካህናት ፡ (ድጓ ። ዮሐ፳፩ ፡ ፲፱) ።

**ሩካቤ** ፤ በቁሙ ፤ መገናኘት ፤ ግንኙነት ። ሩካቤ ፡ ዘበሕግ ። ሩካቤ ፡ ርስሐት ። ለእመ ፡ ረስሐ ፡ በሩካቤ ፡ ምስለ ፡ ብእሲቱ ፡ (ቅዳ ፡ ሕር ። ቀሌ ። ፈ ፡ መ ፡ ፲፱ ፡ ፱ ። ጥበ፯ ፡ ፪ ። ዲድ ፡ ፴፩) ።

**ምርካብ** ፤ (ባት) ፤ ማግኛ ፤ መገኛ ፤ ማስገኛ ፡ ቦታ ። ደመ ፡ ወዝ ፤ ምንዳ ፤ የሙያ ፤ የጕልበት ፡ ዋጋ ፤ ጥቅም ፤ ትርፍ ፤ በሥራ ፡ የሚገኝ ። ዘኢ ፡ የሐርስ ፡ እንዘ ፡ ይሴሴ ፡ ምርካቦ ፡ (፳፬ቆሮ ፡ ፱ ፡ ፲ ፡ ፲፱ ። ግብ፲፱ ፡ ፴፭) ።

—፤ ሐሳብ ፤ ጥበብ ፤ ነገር ፤ ምስጢር ፤ ከልብ ፡ የሚገኝ ። ምርካብ ፡ ዘልብ ፡ ውፁእ ፡ (ቄር ፡ ጸላ) ።

**አስተርከበ** ፤ (የአርከበ ፡ ድርብ) ፤ አቀረበ ፤ አስነካ ። ወአስተርከቡ ፡ ወዐጸሩ ፡ ውስተ ፡ አፉሁ ፡ (ዮሐ፲፱ ፡ ፳፱) ።

—፤ ተወ ፤ ዝም ፡ አለ ፤ ልብ ፡ አደረገ ፤ ነቃ ፡ ተጋ ፡ ተዘጋጀ ። አስተርከቡ ፡ ወአእምሩ ። ዘኢያስተረክቡ ፡ ትርጕሞተ ፡ ቅዱሳት ፡ መጻሕፍት ። መፍትው ፡ ለነ ፡ ንጻሙ ፡ ወናስተብቍዕ ፡ ወናስተርክብ ፡ በጾም ፡ ወበጸሎት ። ያስተርክብ ፡ ለጸሎት ። አስተርክቦተ ፡ በጸሎት ። እመሰ ፡ ፈቀደ ፡ ሰብእ ፡ አስተርክቦ ፡ ይትዋካሕ ፡ ምስሌሆሙ ፡ (መዝ ፡ ፵፩ ። ቀሌ ። ግንዘ ። ኪዳ ። ቄር) ። በረከበ ፡ ፈንታ ፡ አስተርከበ ፡ ይላል ። ዳግመኛም ፡ ዕሩቅ ፡ ወዘ ፡ በቱ ፡ በማለት ፡ ፈንታ ፡ ያስተረክብ ፡ ይላል ፤ ኹሉም ፡ ስሕተት ፡ ነው ። እስመ ፡ ኢያስተርክቡ ፡ ወመ

